# ወንጌል ቅዱስ

ዘእግዚእነ ወመድኃኒነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።
የጌታችን የመድኃኒታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ
ወንጌል ።

ከቀድሞ አባቶች ጀምሮ ሲወርድ ሲዋረድ የመጣው ንባብና
ትርጓሜው
(በአንድምታ)

ተኀትመ ዝንቱ መጽሐፍ በ፲ቱ ወ፪ ዓመተ ሢመተ
ፓትርያርክነቱ ለብፁዕ ወቅዱስ አባ ጳውሎስ ፓትርያርክ
ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ ሊቀ ጳጳስ ዘአክሱም
ወዕጨጌ ዘመንበረ ተክለ ሃይማኖት።

በ፲፱፻፺፰ ዓ.ም
በትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት ታተመ።
አዲስ አበባ



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ
ሊቀ ጳጳስ ዘአክሱም ወእጬጌ ዘመንበረ ተክለ ሃይማኖት

**መግለጫ፡—**

# አርባዕቱ ወንጌላውያን

አበው "ቢቃል ያለ ይረሳል በመጽሐፍ ያለ ይወረሳል" እንዲሉ ከአሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ሁለቱ ፣ ከሰብዓ አርድእት ሁለቱ በመንፈስ ቅዱስ ተመርጠው ቅዱስ ወንጌልን በመጻፋቸው አራቱ ወንጌላውያን ተብለው ተሰይመዋል ። እነሱም ቅዱስ ማቴዎስ ፣ ቅዱስ ማርቆስ ፣ ቅዱስ ሉቃስ ፣ ቅዱስ ዮሐንስ ናቸው ።

ቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ "ይደልዎ ለዘያነብብ ቅድመ ይዝክር ስሞ ለበዓለ መጽሐፍ ወእምዝ ይምሐር ወያንብብ" እንደ አለው (ተግሣጽ 8· ገጽ 99) ስለ አራቱ ወንጌሎች ከመጻፋችንና ከመናገራችን አስቀድሞ ስለ አራቱ ወንጌላውያን የሕይወት ታሪክ በአጭሩ ልንገልጽ እንወዳለን ።

## 1· ሀ/ ቅዱስ ማቴዎስ

በዕብራይስጥና በአረማይስጥ ቋንቋ ማቴዎስ ማለት ሀብተ እግዚአብሔር ወይም የእግዚአብሔር ስጦታ ማለት እንደ ሆነ ይነገራል። በአሥራ ሁለቱ ሐዋርያት የስም ዝርዝር ውስጥ በሁለተኛውና በሦስተኛው ማለትም በማርቆስና በሉቃስ ወንጌል በተራ ቁጥር ሰባተኛ ሲሆን ስሙም ማቴዎስ በመባል ተመዝግቦአል ። (ማር፣ 3· 16–19 ፣ ሉቃ፣ 6· 14–16) ራሱ በጻፈው ወንጌልና በሐዋርያት ሥራ ደግሞ በተራ ቁጥር ስምንተኛ ሆኖ ማቴዎስ በመባል ተመዝግቦአል ። (ማቴ·10፡2–4 ፣ የሐ·ሥ·1፣13) ሌዊ ለሐዋርያነት ከመመረጡ በፊት የተጠራበት ስሙ ሲሆን ማቴዎስ ደግሞ ለወንጌል አገልግሎት ለሐዋርያነት ከተጠራ በኋላ የተጠራበት ስሙ ነው ።

### ለ/ የመጀመሪያ ሥራው

ቅዱስ ማቴዎስ ለሐዋርያነት ከመጠራቱ በፊት ሥራው (ቢቀ መጽብሐን) ቀራጭ ነበር ። በሐዲስ ኪዳን የትምህርት አገላለጽ ቀራጮች እንደ አመንዝሮች ፣ ዓመፀኞች ሌቦች ይቆጠሩ ነበር ። (ሉቃ·18፣ 1 1–12) በዚህ አንጻር ማቴዎስ ቀራጭ እንደ መሆኑ መጠን የዘመኑ የሃይማኖት ሰዎች ይጠሉት ነበር ። ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ማቴዎስን በመቅረጫው ቦታ አገኘውና "ተከተለኝ" በማለት ስለ ጠራው ሁሉን ትቶ ተከተለው። (ማቴ· 9፡9) ቀራጩ ማቴዎስ ሐዋርያና ወንጌላዊ ሆነ ፤ መደቡ ከአመንዝሮችና ከአመፀኞች ጋር የነበረው ሌዊ ከአሥራ ሁለቱ ቅዱሳን ሐዋርያት ጋር ተቆጠረ ። ከአራቱ ወንጌሎች የመጀመሪያውን ወንጌል ጌታ ካረገ በስምንተኛው ተፈጽሞ ዘጠነኛው ሲጀመር ፤ ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዓመት በዕብራይስጥ ቋንቋ ጻፈ ።

### ሐ/ ምልክቱ፡—

ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ ከአብርሃምና ከዳዊት ዘር መወለዱን ለማስረዳት ከአብርሃም እስከ ቅድስት ድንግል ማርያም ድረስ በሰፊው ስለጻፈ ከጥንት ጀምሮ ማቴዎስ በገጸ ሰብእ ተመስሎአል ። ከሦስቱ ወንጌላውያን ይልቅ በማቴዎስ ወንጌል ክርስቶስ ወልደ እጓለ እመሕያው ፣ የሰው ልጅ በመባል ብዙ ጊዜ ስለተጠራ ለማቴዎስ የገጸ ሰብእ ምልክት ከአሰጡት ምክንያቶች አንዱ ነው ።

## 2ኛ· ሀ/ ቅዱስ ማርቆስ

ቅዱስ ማርቆስ ሐዋርያና ወንጌላዊ ፣ እንደዚሁም ሰማዕት ነው ። ከዚህም ጋር የእስክንድርያ ቤተ ክርስቲያን መሥራች አባት ነው ። ወንጌላዊው ቅ/ማርቆስ ኢየሩሳሌም ውስጥ ክርስቲያኖች በቤቷ ለጸሎትና ለትምህርት ይሰበሰቡ የነበረችው የማርያም ልጅ ሲሆን አባቱ አርስጦሉስ ፣ አጎቱ በርናባስ ነበሩ ። ቅዱሳን ሐዋርያት ሁል ጊዜ በእናቱ ቤት እየተሰበሰቡ ጸሎት በማድረግ ፈጣሪያቸውን ያመሰግኑ ነበር ። (የሐ· 12፣12) እናቱ ማርያም እጅግ የከበረች ባለጸጋ እንደነበረችም በመጽሐፈ ስንክሳር ተጠቅሶአል ። ቅዱስ ማርቆስ በመጀመሪያ ዮሐንስ እየተባለ ይጠራ ነበር እናቱም ልጇን ማርቆስን በዕብራይስጥና በዮናናውያን ቋንቋ እያስተማረች እንዳሳደገችው ይታመናል ። ቅዱስ ማርቆስ በወጣትነት ዘመኑ የጌታን ትምህርት ሰምቶ ልቡ ስለተነካ ሁሉንም ነገር ትቶ የክርስቶስን ወንጌል መንግሥተ ሰማያት ለመስበክ ቆርጦ ተነሳ ። ጌታ ካረገ በኋላ ቅዱስ ማርቆስ ከቅዱስ ጴጥሮስ ጋር በመሆን ወንጌልን በማስተማሩ ቅዱስ ጴጥሮስ ልጄ እያለ ይጠራዋል ። (1· ጴጥ፣5፣12) ከጌታ የሰማውንና የተማረውን ጽፎአል ። ወንጌሉም ከእሱ በኋላ በእሱ ስም ተጠርቶአል ። ወንጌሉን የጻፈበት ዘመን ጌታ ከዐረገ አሥራ አንደኛው ተፈጽሞ አሥራ ሁለተኛው ሲጀመር ፤ ቀላውዴዎስ ቄሳር በነገሠ በአራተኛው ዓመት ሲሆን የጻፈበትም ቋንቋ ሮማይስጥ ነው ።

### ለ/ ምልክቱ፡—

ቅ/ማርቆስ በአንበሳ ተመስሎአል ። ምክንያቱም አንበሳ በቅዱስ መጽሐፍ ለእግዚአብሔር ፣ ለሰዎችም

ምልክት እንደሆነ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶአል ፡፡ በኦሪት ዘፍጥረት ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከይሁዳና ከንጉሥ ዳዊት ዘር እንደሚወለድ ተተንብዮአል ፡፡ (49·9–10) በነቢዩ በሆሴዕ እግዚአብሔር አንበሳ ተብሎ መጠራቱን እናያለን (13፡7) መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አሸናፊው የይሁዳ አንበሳ ተብሎ መሰየሙን በራዕየ ዮሐንስ ተጽፎአል ፡፡ (5፡5) በእስራኤላውያንና በዕብራውያን ዘንድ በዙፋንና በበትረ መንግሥት ላይ የአንበሳ ምልክት ይገል ነበር ፡፡ (1·ነገ፡7·29–36 ፤ 10· 19–20) ፡፡ ቅዱስ ማርቆስ በአንበሳ የተመሰለበት ዐቢይ ምክንያት ደግሞ በግብጽ የነበሩትን የአንበሳ ጣኦታት በስብከቱ አጥፍቶ አንበሳ ዐንበሳ የተባለውን ክርስቶስን በመስበኩ ነው ፡፡

## 3ኛ· ሀ/ <u>ቅዱስ ሉቃስ</u>

ወንጌላዊው ሉቃስ እንጾኪያ ውስጥ የግሪክ ወገን ከሆኑ ቤተሰቦች ተወልደ ፤ ጌታ ካረገ በኋላም ቆይቶ ከቅዱስ ጳውሎስ ጋር አብሮ ወንጌልን እንዳስተማረ ተጠቅሶአል (2 ጢሞ፡ 4፡4) ሐኪምም እንደነበረ ተጽፎአል ቆላስይስ 4·14 ፡፡ በስሙ የሚጠራውን ወንጌልና የሐዋርያትን ሥራ የጻፈው ወንጌላዊው ሉቃስ ነው ፡፡ ጌታ ከሙታን ተለይቶ ሞትን ድል አድርጎ በተነሣበት ቀን በፍኖተ ኤማሁስ (በኤማሁስ መንገድ) ጌታችን ከተገለጸላቸው ከሁለቱ ደቀመዛሙርት አንዱ ቅዱስ ሉቃስ እንደሆነ የቤተክርስቲያን ሊቃውንት ያስተምራሉ ፡፡ (ሉቃስ 24· 13 –32) ፡፡ ወንጌሉንም የጻፈበት ዘመን ጌታ ከዐረገ ሃያ አንድ ዓመት ተፈጽሞ ሃያ ሁለተኛው ሲጀመር፤ ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በአሥራ አራተኛው ዓመት በዮናኒ ቋንቋ ነው ፡፡

ለ/ <u>ምልክቱ</u>፡–

ወንጌላዊው ሉቃስ በላህም ይመሰላል ፡፡ መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በከብቶች በረት መወለዱን ፤ በዕለተ ልደቱም የከብት እረኞች ከመላእክት ጋር መዘመራቸውን ከሌሎች ወንጌላውያን ሠፋ አድርጐ ስለሚተርክ ነው ፡፡ (ሉቃ፡ 2· 8–18) ከዚህም ሌላ ላህም በብሉይ ኪዳን የመሥዋዕት እንስሳ ሲሆን ሉቃስም የክርስቶስን መስዋዕትነት በፍሪዳ ምሳሌ ጽፎአል ፡፡ (ሉቃ·15፡ 22–24) ላም የቀንድ ከብት ነው በዚሁ መሠረት ወንጌላዊው ሉቃስ ክርስቶስ ቀርነ መድኃኒት እንደሆነ ነቢዩ ዘካርያስ የተናገረውን ትንቢት በማብራራት ስለጻፈ የላህም ምልክት እንደተሰጠው መተርጒማን ሊቃውንት ይናገራሉ ፡፡

## 4ኛ· ሀ/ <u>ወንጌላዊው ዮሐንስ</u>

ጌታ ይወደው የነበረው የዘብዴዎስ ልጅ ዮሐንስ በፍልስጥኤም ከፍልስጥኤምም ውጪ ክርስትና እንድትስፋፋ ያደረገ ጌታ በመስቀል ላይ ሳለ እመቤታችንን እንዲያገለግላት አደራ የተቀበለ የእመቤታችን የአደራ ልጅ የሆነ ነው ፡፡ (ዮሐ· 19፡26) ከዚህም ጋር ከቅዱስ ጳውሎስ ዕረፍት በኋላ ከኢየሩሳሌም ወደ ኤፌሶን ሄዶ በትንሿ እስያ ወንጌልን የሰበከ በሮማዊው ቄሣር በዶሚቴያኖስ ዘመነ መንግሥት ወደ ፍጥሞ ደሴት ተሰዶ በእስር ቤት ሳለ ራእይን የጻፈ ከዶሚቴያኖስ ሞት በኋላ ወደ ኤፌሶን ተመልሶ "ልጆቼ እርስ በርሳችሁ ተፋቀሩ" እያለ ያስተማረ በስሙ የሚጠሩትን ወንጌሉን እና ሦስቱን መልዕክታት እንዲሁም ራዕይን የጻፈ ፤ ንባቤ መለኮት የሚል ስም የተሰጠው ሐዋርያ ነው ፡፡ ወንጌሉንም ጌታ ከዐረገ በሠላሳ ፤ (በሠላሳ አምስትም የሚሉ አሉ) ፡፡ ኔሮን ቄሣር በነገሠ በስምንት ዓመት በዮናኒ ቋንቋ ጻፈ ፡፡ በልሳነ ጽርዕ የሚልም አብነት አለ፡፡

ለ/ <u>ምልክቱ</u>፡–

ወንጌላዊው ዮሐንስ በንስር ተመስሏል ፡፡ በሥነ እንስሳት (እሞሮች) ጥናት ሊቃውንት እንደሚነገረው ንስር ከሌሎች አዕዋፍ ሁሉ ተለይቶ ወደላይ መጥቆ ይበራል ፡፡ በላይም ሆኖ በመሬት ላይ ያሉትን ረቂቃን ነገሮችን አጣርቶ መመልከት ይችላል ፡፡ ወንጌላዊው ዮሐንስም ወንጌሉን ሲጽፍ ከወንጌላውያኑ እጻጻፍ በተለየ በምሥጢረ ሥላሴ ይጀምራል ፤ በለሥጋዌም ሲጽፍ ወደላይ መጥቆ በማሰብ ቅድመ ዓለም ስለነበረው ቃል ይተርክና "ያ ቀድሞ የነበረው ቃል ሥጋ ሆነ" በማለት ይጽፋል (ዮሐ· 1፡14) ፡፡ ንስር ወደላይ እጅግ መጥቆ እንደሚበርና ወደምድር ሲመለከት ረቂቃን የሆኑትን ነገሮች መመልከት እንደሚችል ፣ ዮሐንስም ረቂቅና ጥልቅ የሆነውን ትምህርት ያስተምር ነበር ፡፡ እነዚህም ፡ "እግዚአብሔር ፍቅር ነው" ፡ "እግዚአብሔር ብርሃን ነው" ፡ "ክርስቶስ ሕይወት ነው" የሚሉትና የመሳሰሉት ናቸው ፡፡

ስለዚህ ከቀደሞ አባቶቻችን ሊቃውንት ሲወርድ ሲዋረድ ከእኛ የደረሰውን የአራቱን ወንጌሎች የአንድምታ ትርጓሜ መምህራን እንዲያስተምሩበት ፣ ደቀመዛሙርት እንዲማሩበት ፣ ምእመናን እምነታቸውን በስፋትና በጥልቀት እንዲረዱበት ቢያቀርብ መንፈሳዊ ደስታ ይሰማዋል ፡፡

መስብሐት ለእግዚአብሔር

ትንግሌ ዘጉባኤ ገ/ሔት ፡፡

በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ፩ አምላክ።

## ታሪክ

ይህን መጽሐፍ አዋንዮስ አውሳብዮስ ተናግረውታል። እነዚህስ መነሻታቸው ከሠለስቱ ምእት በፊት ነውን ወይስ በኋላ ቢሉ በፊት ነው። ይህ በምን ይታወቃል ቢሉ ከሠለስቱ ምእት በኋላ የተነሡ ሊቃውንት ከመዝ ይቤሉ አበዊነ ከመዝ ይቤሉ አጋእዝቲነ ከመዝ ይቤሉ መምሕራኒነ እያሉ ሠለስቱ ምእትን ያነሣሉ እሊህ ባለማንሣታቸው። ያለ ከሠለስቱ ምእት በኋላ የተነሡ ሊቃውንት እንዲህ እያሉ ሠለስቱ ምእትን ማንሣታቸው በሃይማኖት ቢከራከሩ ጉባኤ ቢያቆሙ ነው። እኒህ አለማንሣታቸው በሃይማኖት ባይከራከሩ ጉባኤ ባያቆሙ ነው። መነሻታቸውም ከሠለስቱ ምእት በኋላ ነው። ይህን ስለ ስስት ነገር ተናግረውታል።

መጀመሪያውን ግብር ተዳግሞ ብለውታል ግብር ተዳግሞ ይባላል። ለኦሪት ግብር አላት። በተዳሚ ገብረ እግዚአብሔር ሰማየ ወምድረ ትላለች ለወንጌል ምን ግብር አላት እንዳይሉ ከሦስቱ አካላት አንዱ አካል ሰው እንደሆነ ትናገራለችና ይህን ለመናገር ወካልዑ በቍዔት ይላል። ፪ተኛውን በቍዔት ብለውታል በቍዔት ይባላል ለኦሪት በቍዔት አላት እስራኤል ፪፻ ከ፲፭ ዘመን ኑረው ከግብፅ እንደወጡ ትናገራለች ለወንጌል ምን በቍዔት አላት እንዳይሉ ነፍሳት ፶፻ ፭፻ ዘመን በገሃነም ኑረው እንደወጡ ትናገራለችና ይህን ለመናገር ወሣልሱ ሥርዓት ይላል፤ ሶስተኛውን ሥርዓት ብለውታል ሥርዓት ይባላል፤ ለኦሪት ሥርዓት አላት እመኒ እንዘ ትነውም ወእመኒ እንዘ ትነቅሕ እመኒ እንዘ ትነብር ወእመኒ እንዘ ትትነሣእ፤ እመኒ እንዘ ትቀውም ወእመኒ እንዘ ተሐውር ኢትርሳእ ተዘከርተ እግዚአብሔር አምላክኪ በኵሉ ጊዜ ወበኵሉ ሰዓት ትላለች፤ ለወንጌል ምን ሥርዓት አላት እንዳይሉ ያእቲኬ እንብዕቱ በኵሉ ጊዜ ትላለችና ይህን ለመናገር፡ ወራብዑ ስም ይላል ፬ተኛውን ስም ብለውታል ስም ይባላል፡ ለኦሪት ስም አላት ኦሪት ትባላለች፤ ለወንጌል ምን ስም አላት እንዳይሉ ወንጌል ትባላለችና ይህን ለመናገር፡ ወኃምሱ መሠረት ይላል፡ አምስተኛውን መሠረት ብለውታል መሠረት ይባላል፡ ለኦሪት መሠረት አላት አስገኝዋ ጌታ ጸሐፊዋ ሙሴ እንደሆነ ትናገራለች ለወንጌል ምን መሠረት አላት እንዳይሉ አስገኝዋ ጌታ እንደሆነ አራት ጸሐፍት እንደጻፏት ትናገራለችና ይህን ለመናገር፡ ወሳድሱ ምስማክ ይላል ስድስተኛውን ምስማክ ብለውታል ምስማክ ይባላል ለኦሪት ምስማክ አላት ለእመ ንቀብክ ኦሪተክ ትፀልዕ ከራሚ ከራሚክ ወይሰፍፍ ማኅበብተ ወይንከ ወትሬኢ ውሉደ ውሉድከ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትውልድ ትላለች፡ ለወንጌል ምን ምስማክ አላት እንዳይሉ ከአርአያ እግዚአብሔር አስጥታ ታከብራለችና ይህን ለመናገር፡ ወሳብዑ አርእስተ ነገር ይላል ሰባተኛውን ክፍለ ነገር ብለውታል ክፍለ ነገር ይባላል፡ ለኦሪት ክፍል አላት አራት ወገን ሆና ተጽፋለች፤ ለወንጌል ምን ክፍል አላት እንዳይሉ አራት ወገን ሆና ተጽፋለችና ይህን ለመናገር፡ ይህ አንድ ወገን ነው፡ ሁለተኛ ባዳሬሽ ገብቶ ወይ እልፍኝ ማለፍ አርክብ ተረግጦ ወይከርቻ መውጣት እንዲመች መቅድሙን ተምሮ ወይወንጌል ሲገቡ ይመቻልና። ከማያውቁት አገር የሚያውቁትን ሰው ቢያገኙት ደስ እንዲያሰኝ፡ መቅድሙን ተምሮ ወይወንጌል ሲገቡ ደስ ያሰኛልና፡ ፪ቱን አንድ ወገን አድርገህ ፪ት በል። ሶስተኛም ለመጻሕፍት መልክ ለመስጠት ዓቢዩን በቀይ፡ ንዑሱን በጥቁር፡ ዘሩን በነጥብ ለመለየት፤ ሐዋርያት በዘላን አዋንዮስ አውሳብዮስ በቋሚ ይመስላሉ፡ ዘላን ላሙን ነድቶ አምጥቶ አስረክቦ ይሄዳል እንጂ ላሙን አርዶ ሥጋውን አወራርዶ ይህ ብልት ይህ ነው ብሎ አያስረክብም ቋሚ ግን ከዘላን ተቀብሎ ላሙን አርዶ ሥጋውን አወራርዶ ይህ ብልት ይህ ነው ብሎ ለየ

ር ቀጽር ያስረክበል እንዳይሠረቅ። ዘላን ላሙን ነ ድቶ አምጥቶ እንዲያስረክብ ሐዋርያትም አራት አ ድርገው ጻፉ እንጂ ይህን ያህል ዓቢይ ምስራፍ ይ ህን ያህል ንዑስ ምዕራፍ ይህን ያህል ዘር ብለው አልጻፉም ፡ ቋሚ ከዘላን ተቀብሎ ላሙን አርዶ ሥ ጋውን አወራርዶ ይህ ብልት ይህ ነው ብሎ ሰፍሮ ቀጽሮ እንዲያስረክብ እንዳይሠረቅ፡ አሞንዮስ አውሳብዮስም ይህን ያህል ዓቢይ ምዕራፍ ይህን ያህል

ንዑስ ምዕራፍ ይህን ያህል ዘር ብለው ይጽፉሉና ስለዚህ ሐዋርያት በዘላን አሞንዮስ አውሳብዮስ በ ቋሚ ይመስላሉ ።

በስመ አብ ።

በአብ ስም አምነን አብን ወላዲ ብለን ።

ወወልድ ።

በወልድ ስም አምነን ወልድን ተወላዲ ብለን ።

ወመንፈስ ቅዱስ ።

በመንፈስ ቅዱስ ስም እምነን መንፈስ ቅዱስን ሠራጺ ብለን ።

፩አምላክ ዘለዓለም ።

ምንም ለአጠይቆ አካላት ሶስት ብንል በባሕርይ በ ሕልውና አንድ አምላክ ብለን አምነን ንቀድም ። አንድም አብን በልብ ወልድን በቃል መንፈስ ቅ ዱስን በእስትንፋስ መስለን፡በባሕርይ በሕልውና አ ንድ አምላክ ብለን አምነን ።

ንቀድም በረድኤተ እግዚአብሔር ።

በእግዚአብሔር አጋዥነት እንጀምራለን ።

ሐተታ እግዚአብሔርን አጋዥ ካላደረጉ እግር አ ስተምር አነብ እተረጉም አጽፍ እደጉስ ቢሉ አ ይቻልምና ሁላኬ ፍድፋዴ እንተ ይገብሩ ብእሲ ኢትትፌጸም ዘእንበለ በረድኤተ እግዚአብሔር በ ከመ ቃሉ ለእግዚእን ወዘእንበሌየሰ አልቦ ዘትክሉ ገቢረ ወኢምንትኒ እንዲል ። አብ ወወልድ ወመ ንፈስ ቅዱስ ዘለዓለም ። እሐዱ ዘለዓለም አምላክ ዘለዓለም ብለህ ግጠም ። አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ዘለዓለም አለ በሶስትነታቸው ርባዔ የለባቸ ውምና ። እሐዱ ዘለዓለም አለ በአንድነታቸው ም ንታዌ የለባቸውምና ። አምላክ ዘለዓለም አለ ከዚ ህ ዓለም ንጉሥ ሲለይ ። የዚህ ዓለም ንጉሥ አ ንዱ ሲያልፍ አንዱ ሊተርፍ ነው ። ሥላሴ ግን ቅ ድመ ዓለም ማዕከለ ዓለም ድኅረ ዓለም ንጉሥ

ናቸውና ። ሎቱ ስብሐት ። ክብር ይግባውና ይትባረክ ስሙ ።

ስሙ ይክበር ይመስገንና ።

ወይትለዓል ዝክሩ ።

በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና ።

ወፍጽምናሁ ።

ሕልውናው አንድነቱ ከፍ ከፍ ይበልና ።

ዘእምኔሁ ሚመተ ኵሉ ኃይል ።

የመላእክት ሹመት ከሱ የሚገኝ።ሠያምያነ መላእክ ት ኀራን እንዲል ። አንድም የቀሳውስት ሹመት ከ ሱ የሚገኝ።ወውእቱ ዘይሠይሞሙ ለሰብእ ዛቲ ም ዓርግ እንዲል ። እንድም የነገሥታት የመኳንንት ሹመት ከሱ የሚገኝ።እእምር ከመ ልዑል ይኴንን መንግሥተ ደቂቀ እጓለ እመሕያው ወለዘፈቀደ ይሁ ብ እስመ ኢይሰየም መኰንን ዘእንበለ እምኀበ እ ግዚአብሔር እንዲል ።

ወቦቱ ተፍጻሜተ ኵሉ ስዕለት ።

የልመና ሁሉ ፍጻሜ በሱ የሚሆን ወኢይትከሃል ያቅርቡ ወኢምንተኒ ዘእንበለ በአራቅያናሁ ለወል ድ እንዲል ።

ወኀቤሁ ምብጻሐ ኵሉ አስተብቍዖት ።

የምልጃ ሁሉ መዳረሻ ወደሱ የሚሆን ። ሐተታ ጻድቃን መላእክት ቢያማልዱ ፍጻሜው ወደሱ ነ ውና ። ስዕለት አስተብቍዖት የሚለው እንደምን ነ ው ቢሉ ስዕለት የሚለው በሰባቱ በዐሥራ ሁለቱ በ ሃያ አራቱ ጊዜያት የሚጸለየው ነው አስተብቍዖ ት የሚለው ሰው ስለሚሻው ነገር ግብር ገብቶ ቀ ኖና ይዞ የሚያመለክተው ነው ።

በጽሒፈ መቅድመ አርባዕቱ ወንጌላት ቅዱሳት ።

ንቀድም ጽሒፈ በ በግዕዝ ቦታ የገባ ነው አንተ ለ ኢቀባዕከኒ በዘይት ርእስየ ስምሑራን ልብ በቀ በብ ። ቀስተ ዮናታን ኢተቀብዓት በቀብዕ ዘእንበለ በደመ ኃያላን ። አራት ወንበያት ወወንጌል ሰበኩ በክርስቶስ እንዲል ። የአራቱ ወንጌል መቅድም ሰ ሁቱን ከፍሎ መጻፍን እንጀምራለን ። አንድም በ ን ስለ ማውጣት በመጻፍ እንጀምራለን በቃል መ ጀመር አለና ። እንድም ወታቀንተኒ ኃይለ በጸብዕ እንዲል በጽሒፍ ጊዜ ረድኤተ እግዚአብሔርን መ ጠጋትን ለነገራችን ጥግ እናደርጋለን ።

ወእሠርቱ አቅማራት ።

ዐሥሩን ስንጠረዥ መጻፍንም እንጀምራለን፤አንድም ስንጠረዥን መቅድም አድርግ ፤ የአራቱ ወንጌል መቅድም የሚሆን ዐሥሩ ስንጠረዥ መጻፍን እንጀምራለን ፤ አንድም ጽሒፍን አውርድ ፤ ጽሒፈ መቅድመ ፲ቱ አቅማራት ፤ የዐሥሩ ስንጠረዥ መቅድም የሚሆን ሰባቱን ክፍል መጻፍን እንጀምራለን ሐተታ ምኑናት መጻሕፍተ ዕጻ መጻሕፍተ ደብዳቤ እሉና ከዚያ ሲለይ ከቡራት እስ ፤ ርኩሳት መጻሕፍት ጥንቁላ እሉና ከዚያ ሲለይ ንጹሐት እለ በበሳመ እግዚአብሔር አብ አሜን ።

እግዚአብሔር አንድ ቢያደርገን ፤ ሐተታ አእላፈ እስራኤል አንድ ቢያደርጋቸው ንሴብሖ እንዳሉ፣ ሠለስቱ ምእት ሊቃውንት ነአምን በ፩ዱ ፣ አምላክ እንዳሉ ።
ወእምድኅረ ዝንቱ ፤

በሰላመ እግዚአብሔር አብ ብሎ ነበርና እግዚአብሔር አብ አንድ ካደረገን በኋላ፣ አንድም ንቀድም በረድኤተ እግዚአብሔር ብሎ ነበርና በእግዚአብሔር አጋዥነት ከጀመርን በኋላ ፤አንድም በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ብሎ ነበርና በሦስቱ ስም ካመንን በኋላ ።

ይሜኒ ዘይቀድም መቅድመ ነገር ፍሡሕ ፤
ዘይቀድምና መቅድም አንድ ወገን ፤ ነገር ወንጌል ናት ፣ሥነ ዜና ለዘለዓለም እንዲል ፤ ፍሡሕ እላት መጽድቃንስ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ትላለችና ፤ የወንጌልን መቅድም መጻፍ ይመቻል ፤ አንድም እየራሱ ለማውጣት የወንጌልን የመቅድሙን መቅድም መጻፍ ይመቻል ።

ወያትኩት ዐቱ እንብቦቱ ርቱዕ ።

የቱና መምሕሩ የሚገለጽበት ።

አኰቴት ለእግዚአብሔር ።
ክብር ይገባውና ። ስዋሬ

ባሕርዩን በባሕርዩ የሚሰውር ሰውር ብከ ዕበይከ ለሊከ ወሰ ተከደንከ ወሰሊከ ከ፦ያከ አንጦላዕከ እንዲል ፣ አንድም ትዱሳንን በክብር የሚሰውር ወይ ሰውር ኀሩያን በደመና እንዲል ፣ አንድም ጻድቃንን ከመከራ የሚሰውር እስመ ሰወርከኒ ወረዳእከኒ እንዲል ። ወከዳኒ ።

ወንፍስ በሥጋ ከባቴ አበሳ ።

ነባቢ ፣ ቃል ። ወከሃሊ
አካላዊ ፣ አንድም ነባቢ ፣ ለይኩን ለይኩን ብሎ የተናገረ ፣ ወከሃሊ፣ያንኑ ማድረግ የተቻለው ሐተታ እሱ ተናግሮት ሳይደረግ የቀረ የለምና ወእምከመ ወጽአ ቃል ይትገበር ግብር እንዲል፣አንድም ነባቢ እመርዳለሁ እወለዳለሁ ብሎ ያናገረ ፣ ወከሃሊ ያንኑ ማድረግ የተቻለው ። አንድም ነባቢ ለማይ ወምድር የኅልፍ ብሎ የተናገረ ወከሃሊ ያንኑ ማድረግ የሚቻለው ። ሕያው ።

ሕያው ለራሱ ፣ ወማኅየዊ ።
ማኅየዊ ለሌላው ፣ ወመዋኢ ።

መዋኤ ኃጢአት እስመ ንጹሐት ጠባይዓቲሁ ለእግዚአብሔር ዘእንበለ ነውር እንዲል ፣ አንድም መዋኤ ሥርዓት ወያፈልስ ሥርዓተ ውስተ ሥርዓት እንዲል እምሥርዓትም ይላል ። አንድም መዋኤ ሕሊናት እስመ ሕሊና ይደክም ወየሐጽር እምአእምሮተ እግዚአብሔር እንዲል ።

ዘእንቅሐ አልባቢነ ኀበ ዝክሩ ።
በልብ ወደመታሰቡ በቃል ወደመነገሩ ልቡናችንን ያነቃቃ ፣
ወመርሐ ልሳናቲነ ኀበ አኰቴቱ ወስብሐቲሁ ።
እሱን ፈጽሞ ወደማመስገን አንደበታችንን መርቶ ያደረሰ ። አኰቴተ ስብሐቲሁ ይላል ጌትነቱን ወደ ማመስገን አንደበታችንን መርቶ ያደረሰ ።

ንሴብሖ እንከ በእንተ ዘወሀበነ እምነ ሠናያት ኂሩቱ በቸርነቱ ከሚገኝ ከበጐ ነገር ወገን ስለሰጠን እናመስግነው ። ሐተታ ሠናያት ያለው ልጅነት ነው ሀብተ ክቡ መንፈስ ቅዱስ ውእቱ እንዲል ።

ወናዕዝዞ እንበይነ ዘጸገወነ እምዕበየ ጸጋቲሁ ፣ በለጋስነቱ ከሚሰጠው ክብር ወገን ስለሰጠን እናመስግነው ፣ ዕበየ ጸጋ ያለው ልጅነትን ገንዘብ አድርጎ እስከ ክፍን እሳት ያለው ማዕርግ ነው ።

ወንቀድስ ስሞ ክቡረ ቀድሶቶ ድልወ ።
ክቡር ስሙን የሚገባ ምስጋና እናመስግነው ። ሐተታ ባንድነቱ ምንታዌ ፣ በሦስትነቱ ርባዔ ሳንቀላቅል ። አንድም ሰሙን ጻድቅ ቢሉት ሐሰት ። ባዕል ቢሉት ንዴት ፣ ኃያል ቢሉት ድካም ፣ ይስማማዋል እሱ ግን ጻድቅ ዘአልቦ ሐሰት ፣ ባዕል ዘአልቦ ንዴት ኃያል ዘአልቦ ድካም ነውና ።

በእንተ ዘከሠተ ለነ እምነ ምሥጢራተ ሃይማኖት በተዋሕዶተ ባሕርዩ ለሊሁ ።

ከሠተ ለሊሁ በባሕርይ አንድ መሆኑን ከማመን ምስጢር ወገን ስለገለጸልን እናመስግነው ፣ ሐተታ በከፊል ተናገረ የወማኒ የማዕከላዊ የፍጹም አለፍ ቦኑ እምነቶሙ ዘመ እምነተ አብርሃም እንዲል ።
ወትሥልስተ አካላቲሁ ።
በአካል ሦስት መሆኑን ። ወገጻቲሁ
በቅርጽ ፣ ወመልክዑ ፣ በገጽ ፣ ወአሳሬሁ
አንድ አድራጊውን ከማመን ምሥጢር ወገን ስለገለጸልን እናመስግነው ወእስራ ፪ቱ ሐሳዊያተ እንዲል
ወንስብሖ ስባሔ ፍጹመ ።

ፈጽመን እናመስግነው ።
በእንተ ዘወሀበነ ቦቱ ፤
ከፃሁ ሲል ነው አብ ቢሉ ልጁን ስለሰጠን ወልድ ቢሉ አካሉን ለተዋሕዶ ስለ ሰጠልን ሥጋውን ደሙን ስለ ሰጠን ፤

ወበእንተ ዘአዕተተ እምኔነ ኵሎ ምግባረ ዕልወታ በዘአምጽአ ቦቱ ውስተ ወንጌሉ ቅዱስ

ሰው ሁኖ በሠራት በወንጌል ዘእምነ ወዘተጠምቀ ይድኃን ባለው ኢትጥዓምን ፤ ኢትልክፍን ስለአባለ ፈልን ፤ እንድም አዳምና ሔዋን ያመጡትን ፍዳስ ለአራቀልን ፈጽመን እናመስግነው በግብራቸው ዕልወታት አላቸው ።

ወቦቱ አስተርአየት ተእምራቲሁ
ድውይ መፈወሱ
ወተከሥተት መንክራቲሁ ጋኔን ማውጣቱ
ወኃይላቲሁ
ሙት ማንሣቱ የተገለጸችበት
ወስብሐት ሎቱ ክብር ይግባውና
ይዕበይ ክብሩ
ጌትነቱ ይክበር ይመስገንና
ወይትለዓል ዝክሩ
በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና
ወፍጽምናሁ
ሕልውናው አንድነቱ ከፍ ከፍ ይበልና

ወምስለ ዝንቱ ኵሉ ከመ እስትጉቡእ ዘይትፈቀድ ኀበ ጥያቄሃ ወፈቂድ ኀቤሃ ውስተ ኵሉ መጽሐፍ ጂቱ ይህም ይህ ነው ከዚህ ጋራ ብዚህ ላይ እሷን ከሹ ዋት ከመረመሯት ዘንድ ልቡና የሚሻው ነገር ሁሉ እንደ ተሰበሰበ ሁኖ እስ ፲ ጸሎዓተኒ ማንሻ ። እንድም ይህም ይህ ነው ከዚህ ጋራ በዚህ ላይ እሷን ከሹዋት ከመረመሯት ዘንድ ልቡና የሚሻው ነገር ሁሉ በሰባቱ ክፍል እንደተሰበሰበ ሁኖ እሷን በጽ ፈት ወደመሻት ወደማሰብ ማለት እሷን ወደመጻፍ ወናሁ ጸውዐተኒ መፍቅድ ኀበ ኃሢሠ ዘከሮታ ። እሷን በጽሕፈት ወደመሻት ወደማሰብ ፈቃድ ንጉሥ ፈቃደ ነፍስ ፈቃደ መንፈስ ቅዱስ አነሣሣችኝ መፍቅድ ዐፀባ ይላል አብነት ቁርጽ ፈቃድ ፤ የላይ ቤት አማርኛ እገባሪ ፈቃድ ።

ወጽሕፈቱ ውስተ ዝንቱ መጽሐፍ ንጹሕ ከመ ይኩን ብጽሐተ ስረባሕ ።

ዘፈቃደ ሥጋ ንጹሕ የሚሆን በወንጌል አጠገብ ይህ መቅድም መጻፉ ለወንጌል መዳረሻ ሊሆን ነው ሐተታ ። ይህማ በሌላ ተጽፎ ተምረውት ቢገቡ ይከሊከልናልን ብሎ ፤ ጽሕፈቱ በዝንቱ ፤ ከፈቃደ ሥጋ ንጹሕ የሚሆን የመቅድም መጻፍ ለወንጌል መዳረሻ ሊሆን ነው ።
ወመርሐ ስዘየኃሥሥ ዘይትፈቀድ ።

የሚወደደው የሚሻው ምሥጢር ለሚሻ ደቀ መዝሙር መርሀ ሊሆን ነው ።
ወዛቲ ይእቲ ግብር ቀዳማዊ ።

ይህ ነው መጀመሪያውን ግብር ቀዳማዊ ብለውታል ግብር ቀዳማዊ ይባላል ።
ወካልዑ በቁዔት ።

ሁለተኛውን በቁዔት ብለውታል በቁዔት ይባላል ወዳግሙ ይላል ።

ወሣልሱ ሥርዓት
ሦስተኛውን ሥርዓት ብለውታል ሥርዓት ይባላል
ወራብዑ ስም
አራተኛውን ስም ብለውታል ስም ይባላል ፤ ስምዮት ትእምርት ይላል አብነት ።
ወኃምሱ መሠረት ።

አምስተኛውን መሠረት ብለውታል መሠረት ይባላል እምአይቴ ይላል አብነት ።
ወሳድሱ ምስማክ ።
ስድስተኛውን ምስማክ ብለውታል ምስማክ ይባላል
ወሳብዑ እርእስተ ነገር ።
ሰባተኛውን ክፍለ ነገር ብለውታል ክፍለ ነገር ይባላል ።
ግብር ቀዳማዊ ።
መጀመሪያውን ግብር ቀዳማዊ ብለውታል ግብር ቀዳ ማዊ ይባላል ፤ አያይዞ ለመንገር ደገመው ።
ወግብሩሰ ለዝንቱ መጽሐፍ ማሕየዊ ።
ማሕየዊ የሚሆን የዚህ የመጽሐፍ ሥራው ።
ከመ ይርባሕ ቦቱ ሕይወተ ሕይወት ዘለዓለም ለደ ቂቀ ዕጓለ እመሕያው ።
ጌታ ለደቂቀ ዕጓለ እመሕያው የዘለዓለም ድኅነትን ያስገኘበት ዘንድ ፤ ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው የዘለዓለም ድኅንነትን ያገኙበት ዘንድ ነው ፤ ለደቂቀ ዕጓለ እመ ሕያው የዘለዓለም ድኅነት ይገኝበት ዘንድ ነው ፤
ወበጺሐቶሙ ኀበ ፈጣሪሆሙ ።
ወደፈጣሪያቸው መድረሳቸውን ፤ ተላጽቆቶሙ ከፈጣ ሪያቸው ጋራ አንድ መሆናቸውን ፤ ተመስሎቶሙ ፈጣሪያቸውን መምሰልን ያገኙበት ዘንድ ነው ፤ ሁሉ ንም ያስተረጉማል ።
በቃል ፤ ባነጋገር ፤
ወበምግባር ።
በሥራ ሁለት አርእስት ተናገረ ለሁለቱም ያመጣል በቃልሰ እስመ ውእቱ ይጼውዕ ወይስሕብ ኀበ አእ ሮተ እግዚአብሔር ።
በቃል ያልሁት እግዚአብሔርን ወደማወቅ ያደርሳ ልና ስለዚህ ነው ።
ይትባረክ ። ይክበር ይመስገንና ።
ወይትለዓል ዝክሩ ።
በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና በተዋሕዶተ ባሕርዩ ።

በባሕርይ አንድ መሆኑን ።
ወመለኮቱ ።
በአገዛዝ በጌትነት አንድ መሆኑን ።
ወትሥልስተ አካላቲሁ ።
በአካል ሦስት መሆኑን ።
ወገጻቲሁ ። በገጽ ።
ወመልክኡ ። በቅርጽ ሦስት መሆኑን ።
ወአግሬሁ ።
አንድ አድራጊውን ወደግወቅ ያደርሳልና ስለዚህ ነው ፣ ወእመረ ፀተ ህላዊያተ እንዲል ።
ወያጨይቅ ተሥጉተ ፩ዱ ሕላዌ እምፎቱ ሕላዌያት ከሦስቱ አካላት የአንዱን አካል ሰው መሆኑን ያስረዳልና ስለዚህ ነው ።
ወተዋሕዶቶ በዘተሰብአ ቦቱ ።
ከተዋሐደው ሥጋ ጋራ አንድ አካል አንድ ባሕርይ መሆኑን ያስረዳልና ስለዚህ ነው
ወይዜኑ ኀዳጠ በተሐውሶቱ ወበአንሶስዎቱ ውስተ ዓለም እምጊዜ ልደቱ እምቅድስት ድንግል ንጽሕት እስከ ጊዜ ተንሥአቱ ወዕርገቱ ውስተ ሰማያት ንጽሕት ከምትሆን ከእመቤታችን ከተወለደ ዠምሮ እስከሚነሣበት እስከሚያርግበት ድረስ በዚህ ዓለም ሠላሳ ሦስት ዓመት ከአራት ወር ከዐሥር ቀን መኖሩን ያስረዳልና ስለዚህ ነው ።
ወበምግባርሰ ፤
ቃል ላለው ጨርሶ ምግባር ላሰው አመጣ በምግባርም ያልሁት ።
እስመ በተግሣፃቲሁ ልዕልት ይወስድ ኀበ ምግባራት ሠናያት ወፍጹማት ወመሥመርያት ።
እንሰ እብለከሙ ባለው ፍጹማት ወደሚሆኑ ምግባራት ያደርሳልና ስለዚህ ነው ።
ወጽድል ትርፍት ወክብርት ።

ፍጽምት ክብርት ወደምትሆን ወደገድለ ልቡና ያደርሳልና ስለዚህ ነው ።

ወበኪዳኑ እንተ ጸርሐ ባቲ ወይቤ እመቦ ዘዐቀበ ቃልየ ይገብር ግብረ ዚአነ እገብር ወዘየዓቢ እምኔሁ ይገብር ።

እመቦ ዘዓቀበ ቃልየ ባለው ወበአስፍዎተ ኪዳኑ ይላል አብነት በወንጌል እመቦ ዘዓቀበ ቃልየ ባለው ያደርሳልና ስለዚህ ነው ።

ወዓዲ ትከውኖ ሕይወተ ዘለዓለም ፤
ዳግመኛ በዚህ ዓለም ብቻ ተአምራት አድርጋለት እንደ ጋን መብራት ሁናበት አትቀርም በወዲያው ዓለም የዘለዓለም ድኅነትም ታሰጠዋለች ።
ወዘከሙትሰ ፤
በዚህ ዓለም ብቻ ተአምራት አድርጋለት እንደ ጋን መብራት ሁናበት እንዳትቀር በወዲያውም ዓለም የዘለዓለም ድኅነትን እንድታሰጠው የሚያስታውቅ የሚያስረዳ ነገር ።

ላዕለ እለ ገብሩ ትእዛዞ አስተርአየት ላዕለ እደዊሆሙ ተአምራት ወመንከራት ወኃያላት ዓቢያት ፤ ላዕለ እደዊሆሙ ለእለ ገብሩ ትእዛዞ ፤ ሕጉን በፈጸሙ በሕጉ በጸኑ በሐዋርያት ቃል በሐዋርያት ሥልጣን ጋኔን ማውጣት ሙት ማንሣት ተደረገ ።
እስከ ውእቶሙ ከሠቱ አዕይንቶ ዕውራን ፣

ዕውራንን እስከ ማብራት ደርሰው ፣ እስመ ፣ ውእቶሙ ከሠቱ ዕውራን ፣ ዕውራንን አብርተዋልና ፣ ወአንጽሑ እለ ለምጽ ፣

ልሙጻንን እስከማዳን ደርሰው አድነዋልና ።
ወሞእዎ ለሞት ።

ሞትን ድል እስከ መንሣት ደርሰው ድል ነስተውታልና ፣ ሐተታ ሞእዎ አለ ቢያም ይፈውሱበታል ቢገድል ያሥነሡብታል ኃጢአት ቢያሠራ ስርየት ይሰጡበታልና ፣

ወከብረት ነፍሶሙ በውስተ ዓለማት ፀኤቲ ዘዝየ ወዘከሐ ።

ሰውነታቸው በወዲህም በወዲያም ዓለም ከበረች ሐተታ ፣ በወዲህ አማልከት ተመሰሉ ሰብአ ወወረዱ ኀቤነ ብለዋችዋል ፤ በወዲያውም ወሀሎ ይትዌሰክ ሥነ በዲበ ሥን ይለዋል ።
ወእምፍርሃተ ቃሉ ርኁቁ ጻድቃን እምነ ምግባራት ምኑናት ወፍትወተ ዓለም ርኁቀት ጥቀ ።
ወይወድይዎሙ ውስተ እቶነ እሳት ያለውን ነገር ከመፍራት የተነሣ ጻድቃን ከዓለማዊ ግብር ፈጽመው ተከለከሉ ፣ አንድም ወበፍርሃተ ቃሉ አርኃቀ ይላል ። ወይወድይዎሙ ውስተ እቶነ እሳት ባለው ነገር ጌታ ጻድቃንን ከዓለማዊ ግብር ፈጽሞ ከለከለ አንድም ወፍርሃተ ቃሉ ይላል ፣ ወይወድይዎሙ ውስተ ፣ እቶነ እሳት ያለውን ነገር መፍራት ጻድቃንን ከዓለማዊ ግብር ፈጽማ ከለከለች ፣ አንድም ቃሉ፣ ባለው ፣በቀሉ ይላል ዕፄሁ ዘኢይነውም ወእሳቱ ዘኢይጠፍእ ያለውን ነገር ከመፍራት የተነሣ ጻድቃን ከዓለማዊ ግብር ፈጽመው ተከለከሉ ፤ አንድም እንዲህ ባለው ነገር ጌታ ጻድቃንን ፈጽሞ ከለከለ ፤ አንድም እንዲህ ያለውን ነገር መፍራት ጻድቃንን ከዓለማዊ ግብር ፈጽማ ከለከለች ፣
ወተግኀሡ እምነጽሮታ ወዘከሮታ ፣

በዓይን ከማየት በልብ ከማሰብ ፈጽመው ተከለከሉ ወጸርየት አልባቢሆሙ ። ሰውነታቸው እንደ ፀሐየ ፊሳ ማሰት ፀሐይ እንደወደቀበት ዕንቍ ጸራችላቸው ። ወተጠበበት ሕሊናሆሙ

ልቡናቸው ተራቀቀችላቸው ።

እስከ በጽሑ ኀበ ሥርዓት ዘመላእክት ፣
ወደ መላእክት እነዋወር እስኪደርሱ ድረስ
ወበተግሣጻቲሁ ፣ እንሰ እብለከሙ ባለው

ወበተካይዶቱ ፡ እመቦ ዘዓቀበ ቃልየ ባለው ወበነገሮቱ ፡
ወጻድቃንስ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ፡
ረሰዮሙ ለደቂቀ ዕጓለ እመሕያው ተመሳልያነ ኀበ ፈጣሪሆሙ ።
ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው ፈጣሪያቸውን እንዲመስሉ ልጹቃን ፡ ከፈጣሪያቸው ጋራ አንድ እንዲሆኑ ። ብጹሐን ፡ ወደ ፈጣሪያቸው እንዲደርሱ አደረጋቸው ፡
ከመ ይግበሩ ምግባራቲሁ ወይረሱ መንግሥቶ ፡
ሥራውን ሠርተው ክብሩን ይወርሱ ዘንድ ።

፪ተኛ ጉባኤ ።

ወካልኡ በቊዔት ።

ሁለተኛውን በቊዔት ብለውታል በቍዔት ይባላል ወዳግሙ ይላል አብነት ፡
ወበቊዔተ ዝንቱ መጽሐፍ ንጹሕ ፡

ከፈቃደ ሥጋ ንጹሕ የሚሆን የዚህ መጽሐፍ በቊዔቱ በቊዔትነቱ ፡
ካዕበ እሰመ ውእቱ በዘይትነበብ እምኔሁ ያጤይቅ አጥርዮ መድኀኒቱ ለአዳም ።

በዘይትነበብ ካዕበ ፡ በቊዔት ካዕበ ፡ ያጤይቅ ካዕበ ብለህ ግጠም ፡ እሱ ሁለተኛ በሱ በሚነገረው ነገር ሁለተኛ የአዳምን ድኅነት ማግኘቱን ሁለተኛ ያስረዳልና ስለዚህ ነው ፤ አጥርዮ መድኀኒቱ ባለው ግብረ መድኀኒቱ ይላል አብነት ፡ የአዳምን የድኅነቱን ሥራ ያስረዳልና ስለዚህ ነው ።
ወዘርዑ ፡
የልጆቹንም ድኅነት ማግኘታቸውን ያስረዳልና ስለዚህ ነው ።
እምፄዋዌ ሰይጣን ርጉም ፡
ርጉም ከሚሆን ከሰይጣን ምርኮኝነት የአዳምን ድኅነት ማግኘቱን ልጆቹም ድኅነት ማግኘታቸውን የድኅነቱን ሥራ የድኅነታቸውን ሥራ ያስረዳልና ስለዚህ ነው ።

ወተፈድዮቶሙ ሀየንተ ኀጕለት ዕረፍተ ሠናየ ፡ ባስ ጉዳት ፈንታ በጎ ዕረፍት ማግኘታቸውን፡ዘከመ ተፈድዩ ፡ ብጐ ዕረፍትን እንዳገኙ ይናገራልና ስለዚህ ነው ፤ ዕረፍተ ሠናይተ ፡ ገነተ ሠናይተ ፍኖተ ሠናይተ ፡ ግዕዘ ሠናይተ ፡ ገድለ ሠናይተ ይላል አብነት ፤
ወዓርጉ እምጸናፌ ጽልመት ኀበ ብርሃን ልዕልና የሰው ዳርቻ እንዲሉ ፤ ልዩ ከሚሆን ጨለማ ዳርቻ ልዕልና ወዳለው ብርሃን መውጣታቸውን ፤ ዘከመ ዓርጉ ፡ እንደወጡ ይናገራልና ፡ ስለዚህ ነው ።
ሐተታ ፡ ልዩ ያለው የዚህ ዓለም ጭለማ በዓይነ ሥጋ ይታያል የወዲያው ግን ለዓይነ ነፍስ እንጂ ለዓይነ ሥጋ አይታይምና ።

ወፈግዑ በጣዕመ ፡ ግእዛን እምድኅረ ነበሩ በመሪር ኃዘን ግብርናት ፡

ለዲያብሎስ መገዛት ባመጣው በጽኑ ኃዘን ከኖሩ በኋላ ጣዕመ ግዕዛንን አግኝተው ተድላ እንዳደረጉ ይናገራልና ስለዚህ ነው ።

ወዘኮነስ ከመ ዲያብሎስ ኮነ ሊቀ ዓቢየ በውስተ መላእክት ።

የሆነስ ሆነና ቀድሞ ዲያብሎስ ሊቀ መላእክት አጋዜ መንጦላዕት እንደ ነበረ ስማኝ ልንገርህ ፡ ያል ተያያዘ ፤ እንድም ለዲያብሎስ መገዛት ባመጣው በጽኑ ኃዘን ከኖሩ በኋላ ጣዕመ ግእዛንን አግኝተው ተድላ ማድረጋቸው እንደምን ነው ትለኝ እንደሆነ የዚህስ ነገር ዲያብሎስ ቀድሞ ሊቀ መላእክት አጋዜ መንጦላእት እንደነበረ ስማኝ ልንገርህ ።
ወቦበ ተዓደወ እመካኑ በስሕተት ወወፅአ እምትእዛዘ ፈጣሪሁ ዘውሱን ሎቱ ።

በስሕተት ከቦታው በወጣ ጊዜ ፍጡር ነህ ቢሉት ፈጣሪ ነኝ ባለ ጊዜ ከተወሰነለት ከፈጣሪው ትእዛዝ ወጣ ማለት ቀድስ ቢሉት ቀድሱኝ አለ ወድቀ ማኘሻ ፤ እንድም ፍጡር ነህ ቢሉት ፈጣሪ ፡ ቀድስ ቢሉት ቀድሱኝ ባለጊዜ ።
ወድቀ እመንበሩ ።
ከሹመቱ ተሻረ ከልዕልናው ተዋረደ ።

ወወድቁ ምስሌሁ ኵሎሙ ሠራዊቱ እለ ገብሩ ፈቃዶ ነህ ያሉት ሁሉ ከሱ ጋራ እንደሱ ወደቁ ፡
ወወድቀ ውስተ ምድር ከመ ይግበር ባቲ በከመ ፈቀደ በትዕቢቱ ወበትዝኅርቱ ።

በትዕቢቱ በትዝኅርቱ የወደደውን ያደርግባት ዘንድ ወደዚህ ዓለም ወደቀ ለመሐመድ ልጁ መቃብር ሊባርክለት መካ እስጥንቡል ወደቀ
ታሪክ ጌታ መላእክትን በነገድ መቶ በከተማ ዓሥር አድርጎ ፈጥሮ ተሰውራቸው ባሕርዩ ረቂቅ እን ደሆነ ለማጠየቅ ካልሹኝም አልገኝም ሲል መላ እክትም እእምሮ አላቸውና ተመራመሩ እምአይቴ መጻእነ ወመኑ ፈጠረነ ለሊነኑ እምኀበ ርእስነ ተፈ ጠርነ ወሚመ እምካልዕ ብለው ዲያብሎስን ከሁሉ አልቆት ፈጥሮት ነበርና ወደላይ ቢያይ ድምፅ አጣ ወደታች ቢያይ ሁሉ ከበታቹ ሁኖ አየ እኔ ፈጠርኋችሁ ልበላቸው ብሎ አሰበ አስቦም አል ቀረ እኔ ፈጠርኋችሁ አላቸው ። መላእክትም በቦታ እንደሆነ እኛ ከበታቻችን ያሉትን አልፈጠርና ቸው በምን ምክንያት ፈጠርኋችሁ ይለናል ፈጥረህ አሳየን እንበለው ብለው አሰቡ አሰበውም አል ቀሩ በቦታ እንደሆነ እኛ ከበታቻችን ያሉትን አል ፈጠርናቸው በምን ምክንያት ፈጠርኋችሁ ትለ ናለህ ፈጥረህ አሳየን አሉት ሊፈጥር እጁን ከእሳት አገባው ፈጀው ዋይ ብሎ ጮኸ ፈወሰው ። እፍ

እሮ አምላክ ቢሆን ነው እንጂ ውሳጣዊ አምላ ክግ ቢሆን ስትል ነው ባላለኝም ነበር ብሎ አሰበ ፤ ይህን ያሰበት ልቡን ተሰማው ፈጀው ዋይ ብሎ ጮኸ መላእክት ተናወጹ ይህ ስሑት ፍጥረት ፈጽሞ ሳያስታቸው ልገለጽላቸው ብሎ እሉ በግያይበት በምሥራቅ በኩል አንስ አቤ እግዚአብሔር ለይኩን ብርሃን ብሎ የኀሑን ብር ሃን ፈጠረላቸው የብርሃን ኀርፍ አፈሰሰላቸው እሱ ንም ተድጥ እፈጥራለሁ ብለህ እጅህን ከእሳት አግኘው ፈጀህ ዋይ ብለህም ጮህህ ፈወስኩህ እፍእቱ አምላክ ቢሆን ነው እንጂ ውሳጣዊ አም ላኩግ ቢሆን ምን ስትል ነው ባላለኝም ነበር አል ኝኝ ብሎ ሁለተኛ ፈውሶ ዛሬ ነገሥታት መኳንንት መላታቸውን በርጥብ ቁርበት ጠቅልለው ገደል እንዲጥሉ ባደረው ጭለማ አጐናፀፎ ከኢየሩሳ ሌም ለግያሚት አውርዶ በኢዮር ካሉ መላእክት ያርቀታል እስከ ረቡዕ ከዚያ ይሰነብታል በዕለተ ሠሉስ የተፈጠሩ አዝርዕትን አትክልትን ዕፀዋትን አይቶ እንዲህ አድርጎ ፍጥረት ማከናወን ለዚህም እንጂ ገር እንርለት ይሆናል አለ ።

ወደኝው እንደሆነ በዚህ ዓለም ሳንርህ አለው ለእግ ዴክውን ግን ነቡትን አለው ፤ በዕለተ ረቡዕ ፀሐይ [illegible] ተፈጠሩ ይገ አይተው [illegible] አምስትን ሊሉት ፤ አንዱ ዕደው እምዝንቱ ሕሊና ፤ እኔ ከግመ ኳ ውዑእ ነኝ አላመሰገንም ይሆንላትሁስ እን ደሆነ ሁለተኛ አድርጋትሁ አመስግኑኝ አላትው ወይም አያይዞ አራት አለቆች አሉት።ከሚካኤል ከገብርኤል ዘንድ ላካቸው ኢየሩሳሌም ለማያዊት ቢሏተው ምስቱ ሰማያት አይመስሏትም እኛም ከውኘት በቀር ያገኘነው ነገር የለም ። ገዢ ነኝ የሚለውን ወግተን እጅ እናድርጋት ብሎ ላከ። ከት እይንተ ንጉሥ እንደገ፥ እብድ ውሻ አድርገው እብድ ውሻ አስመስለው ለደዷትው ። መጥተው ነገሩት ሚካኤል ገብርኤል ቢሏትሁ በኔ ዘንድ ቁም ነገ ርን ናቸው እንደ ቀለም ጼጸ እሳት እንጂ እይደሉ ብሎ ሰልፎ ተነሣ እሱ እቀብ የወጣሁ ይመስለ ዋል ቁልቁል ይወርዳል ። ጐየ እግዚእ ምስለ አር ያሙ ሰማዩን ጠቅሎ ተመለሰ ብሎ አዝምሮ ተመ ለሰ ። መላእክት ይህን ሰምተው ይህ ስሑት ፍጥ ረት እስከ መቼ ድረስ በፈጣሪው ሲታበይ ይኖራል ብለው ገጠሙት ድል አደረጋቸው ። ሁለተኛ ገጠ ሙት ድል አደረጋቸው ። ፈቃድህ ባይሆን ነውን ብለው አመለከቱ ። ፈቃድስ ፈቃዴ ነው ድል የሚ ነግበትን ግብር ታውቁ ብዬ ነው ብሎ የብርሃን ትእ ምርተ መስቀል ሰጣቸው እሱን ባየ ጊዜ ከዚህ

በታች ወርዷል ፤ ነው አይገባውም ያሉ አሉ ፤ ነው ብሎስ አይገባውም ማለት አይመችም ብሎ እኛም እንደሉ ነን ያሉ አሉ ፤ ከሱ በቀር ፈጣሪ ነኝ ያለም የለ ብሎ ነው ይገባዋል ያሉ አሉ ይሆን አይሆን ብለው የተጠራጠሩ አሉ ። ሳይመራመሩ የቀሩ አሉ ነው ይገባዋል ያሉ አብረውት ወርደዋል ፤ ይሆን አይሆን ብለው የተጠራጠሩ በዚህ ዓለም ቀርተዋል ሳይመራመሩ የቀሩ በአየር ቀርተዋል ክብር ይሁና ቸው ብሎ እፎ ፈቀደ ኀበ ፈቀደ ።
ከወደደ ዘንድ እንደምን ወደደ ፤

እስመ ሥልጣኑ እንተ ተፈጥረት ምስሌሁ ኢተዓተ ተት እምኔሁ ።
ፍጡር እንደሆነ የሚያውቅባት በተፈጥሮ የተሰጠ ችው ግዕዛን አልተነሳችውምና ።
ወእምዝ ተከሥተ ሎቱ ድኀረ ክብረ መንበሩ እንተ ሀለወ ባቲ አምጣና ወክብራ ፤ አምጣና ወክብራ ለክብረ መንበሩ እንተ ሀለወ ባቲ ከሹመቱ ከተሻረ ከማዕርጉ ከልዕልናው ከተዋረደ በኋላ ቀድሞ የነበረባት የማዕርጉ ደግነት ተገለጸችለት ።

ወተዘከረ ፍሥሐ ወኃሤተ እንተ ኮነ ይትፌሣሕ ባቲ ምስለ መላእክት ወሊቃናት ወሥልጣናት ሰማያው ያን ፤

ስመ ነገድ ከመላእክት ጋራ ያደርገው የነበረውን ተድላ ደስታውን አሰበ ።

በብዝኀ ታላቲሆሙ ወኅብረተ ዜማሆሙ ፤ በነገራቸው ብዛት በምስጋናቸው አንድነት ሐተታ የነገር ብዛት ቅዱስ ውዱስ ስቡሕ ዕዙት ሃሌ ሉያ ማለት ነው ይህ ሁሉ በምሥጢር አንድ ነው ።
ወዘይፈደፍድስ እምኔሃ ፍሥሐ ወኃሤት ልዕልተ ወምዕዝተ እንተ ታቄርብ ኀበ እግዚአብሔር ይት ለዓል ዝከሩ ።

በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና ይል ቁንም ወደ እግዚአብሔር የምታደርስ ቀመስጠ ነበረችው ያቺን አሰበ ። ሐተታ ተቀብቷል ቢሉ የተ መቸ አልተቀባም ቢሉ ቢጸና ።
ወዘረከቦሂ ድኀረ ውእቱ እምድቀታት ።
ከዚህ በኋላ ከድቀታት ወገን ያገኘውን አሰበ ፤ ሐተታ ድቀታት ብሎ አበዛ ከኢየሩሳሌም ሰማያዊት ወደ ኢዮር ከኢዮር ወደዚህ ዓለም ከዚህም በታች አውርዶታልና ።

ወጽልመተ እንተ ገልበበቶ ወበዓፁ ላዕሌሁ ፤ ከጸናችበት እሱም ከጸናባት ከድንቁርና ወገን ያገኘ ውን አሰበ ድቀታት ላለው ዋዌ ፤ እንድም ለላይኛው ልዕልተ ምዕዝተ ላለው ዋዌ የጸናችበትን የጸናባ ትን ድንቁርናውን አሰበ ፤
ወህየንተ ብርሃን ዘመላእክት ትፍሥሕት በእርእያ ለይጣናዊት ርኩሰት ።

ደስ ብሏቸው የሚኖሩ መላእክት ስላገኙት ብር ሃን ፈንታ በምታጌይፍ ባላጋራነት መልክ እንዳለ ፀውቆ ፤
ወሐለየ በትዕቢቱ ወበትዝኅርቱ ወይቤ እስመ ይፈ ቅድ እግዚአብሔር እግብአትየ ከመ ያንብረኒ ኀበ ዘቀዳሚ ንብረትየ እንተ ተዓተተት እምኔየ ወእ ምእሊአየ ።
በትዕቢቱ በትኅዝርቱ አስቦ ወይም እንጂ ወይም አኮን ከኔ ከወገኖቼም ከተለየች ወደ ቀደመች ማዕ ርጌ ሊመልሰኝ ይወድ ይሆናል አለ ፣
ወአእመረ እግዚአብሔር ይትለዓል ዝከሩ ሕሊናሁ እኩየ ወትዕቢቶ ፣
በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና ክፉ አሳቡን ትዕቢቱን ዐውቆ ፣
ወእፎ ኃደገ ምግባራተ ሠናያት ።
በጐ ምግባራትን እንደተወ አውቆ ፣
እንተ ይእቲ ትሕትና ወየዋሃት ወድኂን እምኃጢ አት ።
ምግባራት ሠናያት የተባሉም ትሕትና ወየዋሐት ድኂን እምኃጢአት ናቸው ። ሐተታ ትሕትና ባለ ፈው መጻጸት ። የዋሃት ከሚመጣው መጠበቅ ። ድኂን ለሁለቱም ነው ።

ዘለፎ እግዚአብሔር በፈጠረ ብእሲ ዝልፈት ከሠተ አዳምን በመፍጠሩ መዝለፍን ዘለፈው ግሳፈርን አሳፈረው ማስወተትን አስወተተው ።
በእሡንዮ ፍጥረቱ ለአዳም ።

አዳምን አከናውኖ በመፍጠሩ ፤ እንደ ብርጭቆ የሚ ያንጸበርቅ እንደ ጽጌያት የሚያሸበርቅ አድርጎ በመ ፍጠሩ ይህስ ቁም ነገር አይደለም ዐዋቂ አድርጎ በመፍጠሩ ፤

እስመ ውእቱ ለሐኮ እምጽጉ ጠባይዕ ።
ከአራቱ ባሕርያት ፈጥሮታልና ።

ወይእቲ እሳት ወነፋስ ማይ ወመሬት ።
አራቱ ባሕርያት የተባሉ እሳት ነፋስ ማይ መሬት ናቸው ።

ሥጋ ዘፍጹም ቆሙ ።

ቁመቱ ድልድል የሚሆን አካሉ እንደ ድንክ አያ ጥር እንደ ረዓይት አይረዝም ።
ዘቦቱ ጽቱ ኃይል ።

ሁለት ግብር ሁለት ባሕርይ ያለው አድርጎ በመ ፍጠሩ ።

ኃይለ ዘርዕ ። የዘር ግብር የዘር ባሕርይ ።
ወኃይለ እንስሳ ።
የደመ ነፍስ ግብር የደመ ነፍስ ባሕርይ ።
ወኃይለ በቈላትስ በሁከቱ ነፍስ ይነውኅ ወይማስን የዘር ግብር የዘር ባሕርይ ነፋስ እየወዘወዘው

ያድጋል ነፋስ እየወዘወዘው ይደርቃል ፈርሶ በስብሶ ይቀራል ።

በከመ ዕውቅ ዝንቱ ውስተ ኵሉ አጽናፈ ምድር ይህ በአራቱ ማዕዘን ታውቆ እንዳለ ።

ወኃይልሰ እንስሳዊት ሀውክት ይእቲ በሥምረት የእንስሳ ግብር የእንስሳ ባሕርይ ልብሳ ልብሳ በማ ለት ፈቃድ የምትነሣሣ ናት ።
ወይእቲ ባ እምነ አእምሮ ።

ወለይእቲ ሲል ነው ለሷም ከዕውቀት ወገን አላት ወከፈላ ምክረ እምጥበብ ለስገኖ እንዲል ።
ዛይእቲ እንስሳዊት ያቺውም እንስሳዊት ናት ወውስቴታ ይትረከብ ነጸሮ ።

በርሷም ማየት ይገኛል ፣ ሐተታ ማየት በሁሉ አለ ይልቁንም ጉጉት የባሕር ድመት በሌሊት ያያሉ ።
ወሰሚዕ ።
መስማት ይገኛል ። ሰሚዕ በሁሉ አለ ይልቁንም በቅሎ ንቁሕ ነው ።
ወጣዕም ።

ጣዕም ይገኛል ፣ ጣዕም ሁበሉ አለ ይልቁንም ፈረስ አህልና ዐፈር ቢሰጡት ፣ የሰጡት እንደሆነ ዐፈሩን እየተወ እህሉን ይበላል ።
ወአጼንዎ ።

አጼንዎ ይገኛል ። ሐተታ አጼንዎ በሁሉ አለ ይል ቁንም የሜዳ አህያ ፣ ወይቀውም ሐለስትዮ ማዕ ከለ አድባር ወያበቁዕ እንፎ እንዲል ፤ ከተራራ ላይ ወጥቶ አፍንጫውን ከፈት ከፈት ያደረገ እንደሆነ የማር የውኃ ጣዕም ይመጣለታል የሦስት ቀን መን ገድ ገሥግሦ ሄዶ ማሩን በልቶ ውኃውን ጠጥቶ ዕለቱን ተመልሶ ከቦታው ገብቶ ያድራል ።
ወገሢሥ ።

ገሢሥ ይገኛል ፣ ገሢሥ በሁሉ አለ ይልቁንም ዝን ጀሮ በትር ቈርጦ እስከ መማታት ይደርሳል ፤ የላይ ቤት አማርኛ በችሐበችሆ ይላል ።
ወዓዲ ተንሥኦ ወነቢር ።

አፍ ቁጭ አፍ ቁጭ ማለት ይገኛል ቡኽር አታ ርፍም ። እንድም እናበህ ተንሥኦ ነቢር መቀመጥ ያለበት መነሣት ይገኛል ። ውሻ ድመት በኋላ እግራ ቸው ይቀመጣሉ በፊት እግራቸው ይቆማሉ ።
እንሳሕስሖ ።

እንሳሕስሖ ይገኛል ። እንሳሕስሖ በሁሉ አለ ይል ቁንም ጥርኝ አታርፍም ።
ወኀድዓት ።

ኀድዓት ይገኛል ፣ ኀድዓት በሁሉ አለ ይልቁንም አንበሳ ። በሬም ያግዛል ።
ወፍትወት ።

ፍትወት ይገኛል ፡ ፍትወት በሁሉ አለ ይልቁንም ሰገኖ ፡ ሰገኖ ታበዝኅ ፍትወተ ወእምከመ ኢፀንሰት ኢትበልዕ ማዕረ እንዲል ፡፡
ወወሊድ ፡፡
ወሊድ ይገኛል ፡ ወሊድ በሁሉ አለ ይልቁንም ነማ ያለሽል አታድርም ፡፡
ወሙዓት ፡፡
መዓት ይገኛል ፡ መዓት በሁሉ ፡ አለ ይልቁንም ግሥላ ታንቆ ይሙታባሽ ያሏት እንደሆነ ታንቃ ትሞታለችና ፡፡
ወማህል ፡፡ ማህል
ይገኛል ፡፡ ማህል በሁሉ አለ ይልቁንም ዘሆን ፡ ዘሆን ሆይ ዘሆን ሆይ ያሉት እንደሆነ መንገድ ይመራል
ወሕማም ፡፡

ሕማም ይገኛል ፡፡ ሕማም በሁሉ አለ ይልቁንም ነብር ዓይን ሕመም ይጸናበታል ፡፡
ወተበቅሎ ፡፡

ተበቅሎ በሁሉ አለ ይልቁንም ግመል እፕብቆ የመታትን እስከ ስድስት እስከ ሰባት ዓመት ድረስ አትረሳውም ስፍራ ሲመቻች ገደል ገፍታ ትጥለዋለች ባጥ ብላ ትረግጠዋለች ፡፡
ተፈሥሖ ፡፡

ተፈሥሖ በሁሉ አለ ይልቁንም ቀበሮ ፡ ዱሮ ዘመን ቀበሮ ጣዝማ ያገኘ እንደሆነ ሲዘል በታው ይጫፋው፤ ነበር ዛሬ ግን እጁን ጭኖ የሚዘል ሁኑዋል የጊዜውን ከፋት መናገር ነው ፡፡

ወኃዘን ፡፡ ኃዘን በሁሉ አለ ይልቁንም ዖፈ መንጢጥ ባሏ የሞተ እንደሆነ ወበዕፍራ ትቤጽር ልሳና ይላል ፊቷን ጸፍታ እንደበቷን ሰንጥቃ ትኖራለች ፡ ሌላ መጥቶ ልድረሰብሽ ያላት እንደሆነ ያን ታሳየዋለች ቢመለስ ይመለሳል የተጋፋት እንደሆነ ከወገኖቹዋ ትጠጋለች ያድኑዋታል ፡
ነዊም ፡፡ መኝታ በሁሉ አለ ይልቁንም እሆ የያዘውን ከመጣል ይደርሳል ፡፡

ወነቂሕ ፡፡ መንቃት በሁሉ አለ ይልቁንም ቆቅ ፡ ያን ቆቅ ያሉ እንደሆነ ይህን በቅሎ
ሕይወት ፡፡ ሕይወት በሁሉ አለ ይልቁንም ዖፈ ፊንክስ የሚባል ዖፍ አለ ባሯት ባሯት መቶ ዘመን ይታደሳልና ፡፡ ይህስ የታወቀ ነው ብሎ እንደ ፎገራ እሞራ ጥርቱ የተላለፈ እንደሆነ ጭሮ መብላት አይሆንለትም ከዕንጨት ከድንጋይም ቀመታው እንደሆነ ይተካከልለታል ጭሮ ይበላል ፡፡
ወመዊት ፡፡ ሞት በሁሉ አለ ይልቁንም አይጥና ድንቢጥ ጭላት የበልጉ ለመኸር የመኸሩ ለበልግ አይገኙም ፡፡

ወኵሎሰለ ዝንቱ በከመ ይትረከብ ዝበሙስተ እንስሳ ነሳሳለችና ይህን የሞሰስ ሁሉ በእንስሳት ባሕርይ እንዳለ በሰውም በእንስሳ ባሕርዩ ይህ ሁሉ አለ ወዓዲ አከበሮ በንፍሐት ዘይእቲ ማኀተመ ሕይወት መንፈሳዊት እንተ ባቲ አከበሮ እምኵሉ ፍጥረት ዘታኀተ ሰማይ ፡፡

ከአራቱ ባሕርያት አዋሕዶ ፈጠረው ብሎ ነበርና ዳግመኛ ባራቱ ማዕዘን ካለ ፍጥረት ለይቶ ባከበረበት የሥጋ ሕይወት የደመ ነፍስ ሕይወት በምትሆን በነባቢት ነፍስ አከበረው ፡፡

ወትትዓወቅ በኃይለ ንባብ ፡
ምሥጢር በመናገር ትታወቃለች ፡፡

ዛይእቲ አርአያ ገጹ ለእግዚአብሔር ወእምሳሊሁ ይቺውም የእግዚአብሔር መታወቂያው ናት ምሳሌውም ናት ፡፡
በከመ ይቤ መጽሐፍ ፡
መጽሐፍ ንግበር ሰብአ በአርዓያነ ወበአምሳሊነ እንዳለ ፡፡

ወይእቲ ዘኢትትለከፍ ፡
የማትያዝ የማትዳሰስ ናት ፡
ወዘኢግብርት ፡፡ ግብር እምግብር ያልተፈጠረች ናት ፡፡ እንድም አጥብቅ ፡ ያያገብሯት ናት ፡፡
ሀላዊት ፡ ነዋሪት ናት
ወዘኢመዋቲት ፡ የማትሞት ናት ፡
ኵናኔተ ሥጋ ወኃይሉ ፤
ሥጋን ደመ ነፍስን የምትገዛ ናት እንድም ሥጋን የምትገዛ ናት ወኃይሉ ጠበቃው ናት
በእንተ ዘኮነት እሐተ ውስተ ኵሉ ፡
በፈቃድ አንድ ስለሆነች ፡፡

ወባቲ ይትረከብ ጥበብ ዘየሐለብ ልብ ወየኃሪ ፡
ልብ የሚሻው ጥበብ በሷ ይገኛል ፡፡
ወእእምሮ አዝማናት ፡፡

ፀሐይ መጸው ክረምት ፀጋይ ማወቅ በሷ ይገኛል ይህንስ እንስሳትም ያውቁታል ብሎ ዓዝማነ መንግሥት ስማያትን ማወቅ ይገኛል ፡፡

ወመካናት ፡፡ ቆላ ደጋን ማወቅ በሷ ይገኛል ፡ ይህንስ እንስሳትም ያውቁታል ብሎ ቆላ ገሊነም ደጋ መንግሥት ሰማያት ማወቅን በሷ ይገኛል ወኵላ ምግባራት እንተ ትከውን በዘይእቲ ላዕሌሁ የሚሠራው ሥራ ሁሉ እሱን ተዋሕዳ ባለች በሷ ነው ፡ እንድም እሷን ተዋሕዶ ሳለ በሥጋ የሚሠራ ሥራ ሁሉ ባቲ ይትረከብ ፡፡

በሥልጣን ባሕታዊት ፡፡ በዕውቀት ልዩ ናትና ሥዕልት ዘእንበለ ገቢር ፡፡
ግብር እምግብር ሳይሆን የተፈጠረች ናት ፡፡

ወገብረ ላቲ ሥልጣነ በውስቴታ ትግበር በከመ ኀረየት እንዘ አልቦ ዘይኪንና ወዘይኄይላ ፡፡

የሚገዛት የሚያዛት ሳይኖር የወደደችውን እንደወደደች ታደርግ ዘንድ አእምሮ ጠባይዕን ሳለባት ። ኲሎ ይኩን ሠናያቲሃ ወእኪያቲሃ በሥምረተ ሕሊናሃ ።

ፀጎኒቷም ክፋቷም በፈቃደ ይሆን ዘንድ ።
በአምሳለ መላእክት ።

ሠናያቲሃ በአምሳለ መላእክት ፤ በሚካኤል በገብር ኤል አምሳል ።

እኪያቲሃ በአምሳለ መላእክት ብለህ ግጠም ።
በአጋንንት አምሳል ይሆን ዘንድ ።
ወተፈጸመ ፍጥረቱ ለአዳም በዝንቱ ግብር ።

የአዳም ተፈጥሮ በዚህ ተፈጸመ ።
ዘቦ ውስቴቱ ፫ቱ ኃይል ።
ሦስት ግብር ሦስት ባሕርይ ባለው ።

ኃይለ ዘርእ ። የዘር ግብር የዘር ባሕርይ ባለው ።
ወኃይለ እንስሳ ።

የደመ ነፍስ ግብር የደመ ባሕርይ ባለው ።
ወኃይለ ንባብ ።
የነባቢት ነፍስ ግብር ባለው ። ይቀየን

ሦስተኛ ጉባኤ ።

ወአልበሶ አልባሰ ብሩሃ ።

ከአራቱ ባሕርያት ፈጥሮ ከእንስሳት ከአራዊት ለይቶ በነባቢት ነፍስ አከበረው ብሎ ነበርና ልጅነትን ሰጠው ፤ እስመ አልበሰክኒ ልብሰ ትፍሥሕት ወልብሰ መድኃኒት እንዲል ።

አካሉን ሲያይ ብሩህ አለ ፣ ህብሩን ሲያይ አልባስ ብሎ አበዛ ፣ ከዚህ ዕለቱን አስመስሎታል አክሲማርስ በ፵ ቀን ብሎ ለይቶ ተናግሯል ።

ወገብረ ሎቱ ሥልጣነ ለርእሱ ።
ሥራ ሠርቶ ሊጠቀምበት መንፈሳዊ ዕውቀትን ሰጠው ።
ወአኀጥዖ ሞተ ።
በዓቂበ ሕግ እንዳይሞት አደረገው ።
ወረሰዮ ሥሉጠ ላእለ ኲሉ ፍጥረት ዘታሕተ ሰማይ በአራቱ ማዕዘን ያሉትን ፍጥረት አሰገዛው ፣ ወአወልጠኖ ፣ አራቱ ማዕዘን ባሉ ፍጥረት አሠለጠነው ወፈጠረ ሎቱ እምሥጋሁ ረድኤተ ።
ከአካሉ ልትረዳው ፈጠረለት ፣ በአቅሉ ክበደ ዋዕይ ልጅ በማስገኘት አንድም እሱ የአፍአውን እሷ የውስጡን በማከናወን ።
ወሰመያሔዋን ።
ሔዋን ሕዋን አላት ፤ ሕይወት ማለት ነው እንደግብሯስ ሞት በተባለች በተገባት ነበር ሕያዋን ጸድቃን ከሷ የሚወለዱ ስለሆነ ሕይወት አላት ።
ወአንበሮሙ ውስተ ገነተ ዔዶም ጽባሒዊ ።

መወደድ ባለው በምሥራቅ በኩል በገነት አኖራቸው አንድም ፤ ጽባሒዊ መወደድ ባለው በገነት ምሥራቅ አኖራቸው አራት ማዕዘን አለውና ።

ወወሀቦሙ ይትፈሥሑ በኲሉ ሠናያት አምላካውያት ዘእንበለ ክልዓት ።

ወሀቦሙ ዘእንበለ ክልዓት ፣ ከአምላክ በሚገኘው ነገር ሁሉ ደስ ይላቸው ዘንድ ያለመከልከል ሰጣቸው ይትፈሥሑ ዘእንበለ ክልዓት ያለመከልከል ደስ ይላቸው ዘንድ ።

ወወሰነ ሎሙ ትእዛዘ በእንተ አሐቲ ዕፅ ባሕቲታ ፣ ስለ አንዲት ዕፅ ብቻ ትእዛዝ ወሰነባቸው ።
ወይእቲ ዕፅ እንተ ታሌቡ ሠናየ ወእኩየ ።
ያቺም ዕፅ ባይበሏት በጐ ቢበሏት ክፉ የምታስታውቅ ናት ።

ከመ ኢይብልዑ እምኔሃ ።
ወሰነ ከመ ኢይብል እምኔሃ ከሷ እንዳይበሉ ትእዛዝ ወሰነባቸው ።

ሐተታ ፤ የገዥና የተገዥ ምልክት የዓቂበ ሕግ ምልክት ጾምንም በዚህ ነገረው ።
እስመ አመ ይበልዑ እምኔሃ ሞተ ይመውቱ ።
ከሷ የበሉ እንደሆነ የሞት ሞት ይሞታሉና ብሎ ወለእመ ሰምዑ እንከ ትእዛዞ ይከውኖሙ ሕይወተ ዘለዓለም ።

ትእዛዙን ቢጠብቁ የዘለዓለም ድኅነት ይሆናቸዋል ብሎ ።
አንድም ትእዛዙን ጠብቀው ቢሆን የዘለዓለም ድኅነት በሆናቸው ነበር ።
ወለእመሰ ተዓደው ይከውኖሙ ሞተ ።
ትእዛዙን ግን ቢያፈርሱ ሞት ተፈረደባቸው ።
ወሶበ ርእየ ሰይጣን ዕበየ ስብሐቲሁ ወክብራቲሁ ሰይጣን የራሱን ደግ ክብሩን ፣ ደግ ጌትነቱን ባየ ጊዜ ውብርሃነ ዘይትዓፀፍ ቦቱ ።

ተሰጥቶት የነበረውን ጸጋውን ባየ ጊዜ ።
ወርእየ ርእሶ በርእሱ እምድኅረ ክብር ወሢመት ዓባይ ።

ከሹመቱ ከተሻረ ከልዕልናው ከተዋረደ በኋላ ራሱን በራሱ በመረመረ ጊዜ ወድቀ አንድም መልስ የአዳም ደግ ክብሩን ደግ ጌትነቱን ባየ ጊዜ ለአዳም የተሰጠውን ጸጋውን ባየ ጊዜ አዳም ከተሾመ ከከበረ በኋላ የራሱን ክብር በአዳም ላይ ሁኖ ባየ ጊዜ ወድቀ በድቀተ ቅንዓት ።

ቅንዓት ባመጣው ድቀት ወደቀ ደንገፀ በድንጋጼ ቅንዓት ፣ ቅንዓት ባመጣው ድንጋጼ ደነገፀ ፣ ኃዘን ባዘነ

ቅንዓት ተከሠ በትካዝ ቅንዓት፤ ኃዘን ትካዝ ባመ ጣው ቅንዓት አዘነ ፤ ወድቀ መውዴቀ ውዱቅ ይላል ፤ መውዴቅ ዲያብሎስ ውዱቅ አዳም ነው አዳምን ያሳተ ዲያብሎስ ወደቀ ድል ሆነ ።

ወቀብጸ ተስፋሁ ። ተስፋ ቆረጸ
በእንተ ዘኢፈቀዶቱ እግዚአብሔር ኪያሁ ፤
እግዚአብሔር እሱን ባለመሻቱ ፤
ወኢያግብአ ውስተ ዘቀዳሚ መንበሩ ፤
ወደተደመ በታው ወደቀደመ ማዕርጉ ባስመመሰሉ
ወኢተርፈ ሎቱ እምነ ዘይእኅዝ ዘእንበለ ዘያሰግዶ ሰብእሲ ከመ ያውዕአ እምፈቃዶ ፈጣሪሁ ።

ወይም እንጂ ይመልሰኝ ይሆናል ብሎ ነበርና አዳ ምን ከፈጣሪው ትእዛዝ ያወጣው ዘንድ አዳምን ከሚ ያስትበት ግብር በቀር ከያዘው ከረዘዘው የቀረለት የለም ።
ወነሥአ ሎቱ ተኃይሎተ ዘበእኪት ፤

የበጐ መበረታታትአለና የከፉ መበራታታትን አደረገ
ወመንሱተ ወልታ
ወልታ መንሱተ ሲል ነው አዳምን ድል የሚነሳበ ትን ጋሻ አነገበ ።

ወመጽአ መንገለ ብእሲ በውእቱ ተኃይሎት ጸዋግ በከፉ መቢራታት ወደአዳም መጣ ፤ ሐተታ ፤ አዦን ዮስ አውሳብዮስ በገነት እንዳሉ ሁነው ይጽፋሉ ወእምጽእሂ ለውእቱ ንዋይ እምኢየሩሳሌም እንዳለ ነቢይ በኢየሩሳሌም ሳለ በባቢሎን እንዳለ አድርጎ ፤ በእንተ ምክንያት ዘያወፅእ ቦቱ እምገድል ሠናይት ከበጐ ግብር ስለሚያወጣበት ምክንያት እምገነት ሠናይት እምፍናት ሠናይት እምግእዝ ሠናይት እም ዕረፍት ሠናይት ይላል ።
ወጸንሆ እንከ ።

ሸመቀበት ሰው በጠላቱ እንዲሸምቅ ጦሩን ሰንግሎ ጋሻውን ወልውሎ፤ አንድም ድል የሚነሣበትን ግብር ዐወቀ ፤ አንድም የሚለያዩበትን ጊዜ ጠበቀ ። በከመ የአምሮን ጸላዒ ለጊዜያት ለነኒ ይደልወነ ከመ ናእምር ድካሞቲነ እንዲል ።
ወናሁ ውእቱ ምስለ ረድኤቱ ተሠልጡ ውስተ ኵሉ ዕፀወ ገነት ።

ተሠልጡ ካለ ውእቱ ወረድኤቱ ምስለ ረድኤቱም ካለ ተሠልጠ ቢል በቀና ነበር ልማደ መጽሐፍ ነው ሴሊት ምስለ መዓልት ይትካፈልዎ ለዘመን በዕ ሪና ።
ከንቶ ይትናገሩ ፩ዱ ምስለ ካልዑ እንዲል ፤ እሷ እሱ በገነት ባለው ዕፅ ሁሉ ሠልጥነው ነበር ።
ዘእንበለ እሐቲ ዕፅ ባሕቲታ እንተ ከልአ እምኔሃ ። እሷን አትብላ ብሎ ከከለከለው ካንዲት ዕፅ በቀር ወተፈሥሐ እንከ ዓቢየ ፍሥሐ ።
ፈጽሞ ደስ አለው ።

ወአእመረ ከመ በውእቱ ዕፅ ይመውእ ።
በዕፀ በለስ ድል እንዲነሣው ዐውቋልና ።
ወያወዕአሙ ለአዳም ወለሔዋን እምፍግዓሆሙ ።
አዳምና ሔዋንን ከተድላቸው ከደስታቸው እንዲለ ያቸው ፤ አንድም ተድላ ደስታ ከሚያደርጉባት ከገነት እንዲያወጣቸው ዐውቋልና ፤
ወተኀብአ እንከ ውስተ ሥጋ ከይሲ ።
በሥጋ ከይሲ ተሰወረ ።
ወረሰያ ምክንያተ ለኃጉል ።
ለጉዳት ምክንያት አደረጋት ፤ ታሪክ እንስሳት አራ ዊት ከአዳም ዘንድ ሄዱ ስለምን ቢሉ ስም ለመሰየም ስምስ ተሰይመዋል እስከዚያ ወጹት ኑረው ብሎ ለዶጅ ጥናት ሄደው አርደህ ብዓን አሉት ። ምን አጥፎ በገነት ባለ ዕፅ ሁሉ አሠልጥናኛል ፤ እናንተስ ባሳ ትሁበት ያርባተሁ ያብዛተሁ ያስፋፉተሁ ብሎመርቆ ሰደዳቸው ፤ ዲያብሎስ ከመንገድ ቆይቶ ወጹተ ሄዳ ችሁ ኑራችኋል አላቸው ። ከአዳም ከጌታተን አሉት አዳም ጌታችሁ ምን ይመስላል አላቸው ከሠሌዶ ሰባት እጅ ያበራል አሉት በዚያውስ ላይ ይህን ያህል ደስታ ምን ተገኘ፤ል አላቸው ። እንዲህ ብን ሰው እንዲህ አለን ሞት ቢቀርልን አሉት ። ያቺን ዕፅ ቆርጦ ማን ከፉ ባገበልኝ ነበር ብሏል ። በሌላው ቀን ሲሄዱ አገኛቸው ወጹት ትሄዳላችሁ አላቸው ከአዳም ከጌታቴን አሉት ። አስከተሉኝ አላቸው ። አዳም ጌታችን መልክ መልካም ነው አንተ መልክ ጥፉ ብለው ትተውት ሄዱ ። አብርል አዝርል የሚ ባሉ የገነት አዕዋፍ መጡ አስከትሉኝ አላቸው አዳም ጌታችን መልካም አንተ ክፉ ብለው ጥለውተ ሄዱ ። እባብ መጣተ የገመል ወሳብሬ ታህል ነበር ወዴት ትሄጃለሽ አላት ወደ አዳም ወደ ጌታዬ አለ ችው ፤ አስከትይኝ አላት አዳም ጌታዬ መልካም ነው አንተ ከፉ ነህ አይሆንም አለችው ። ከፉ ከሌለ መል ካም በምን ይታወቃል መሰሎሻል ። በዚያውስ ላይ ባንቺ እንጂ አምር የስም ብሎ በውዳሴ ከንቱ ጠለ ፋት ፤ አስከትላው ሄደች ቁልቁለቱን ጨርሰው እዳ ገቱ ደረሱ ፤ የቆላ መንገድ እንጂ ካልተዋወቁበት አይሆንም እየተዛዘልንእንውጣው አላት እሽ አችሰው ነይ ልዘልሽ አላት ጥቂት እልፍ አድርጎ በጽሐ በፂ ሥግው ሆነ ፤ ከአዳም ዘንድ ሄደ ጸሎት ይዞ አገኘው አስቀድሞ በዚህ ድል ነሣው በሐኬ ንጉሠ ሰማያት ወምድር አለው ፍልጥ አርዌ ምድር ፤ ንጉሠ ምድር ነኝ እንጂ ንጉሠ ሰማያት ፈጣሪዬ ነው አለው ። ሔዋን ወዴት ናት አለው ፤ ከዚያ አለተ አለው ቢሄድ ሥራ ፈትታ አገኛት በዚህ ድል ነሣት ።
ወአስተርአያ ለሔዋን በነገር ጥዑም ዘምሉእ ጕሕ ሉት ከዳት ተንኮልን በተመላ ደስ በሚያሰኝ አነጋ ገር ሔዋንን ተናገራት ፤ በሐኪ ንግሥተ ሰማይ ወም ድር አላት ደስፈቅ አላት ፤

ወይቤላ በእንተ ምንት ይቤለክሙ እግዚአብሔር ኢትብልዑ እምኵሉ ዕፀው ዘውስተ ገነት ።

ለይቼ የጠየቅኋት እንደሆነ ታውቅብኛለች ብሎ በገነት ካለው ዛፍ ሁሉ አትብሉ ያላችሁ ስለምንነው አላት ፤
ወትቤሎ ንበልዕሰ እምኵሉ ዕፀው ዘውስተ ገነት

በገነትስ ካለ ዕፅ ሁሉ እንበላለን ፤
ወባሕቱ ፍሬ ዕፅሰ ዘውስተ ገነት ይቤለነ እግዚአብሔር ኢትብልዑ እምኔሃ ። ነገር ግን በገነት እንዲት ዕፅ አለች እሷን አትብሉ ብሎናል ።
ከመ ኢትሙቱ ሞተ ፤

ያው ቅሉ ነፍሳን አይደለም የሞት ሞት ትሞታላችሁ ብሎ ነው እንጂ አለችው ፤
ወይቤላ አኮ ሞተ ዘትመውቱ ።

ጣዖቱን ይሰብካል የሞት ሞት ትሞታላችሁ ብሎ አይደለም ፤
ወባሕቱ የአምር እግዚአብሔር ከመ ሶበ በላዕክሙ እምኔሃ ይትከሠታ አዕይንቲክሙ ወትከውኑ ከመ አምላክ ።

በበላችሁ ጊዜ የአምላክነት ዕውቀት እንድታውቁ እንደ አምላክ እንድትሆኑ ያውቃልና ፤
ወትአምሩ ከመ ሠናየ ወእኩየ ።

የሰውነት የአምላክነት ዕውቀት እንድታውቁ ያውቃልና ስለዚህ ነው እንጂ የሞት ሞት ትሞታላችሁ ብሎ አይደለም ።
ወአፍትዋ ከመ ትብላዕ እምውእቱ ዕፅ ፤
ዕፀ በለስን ትበላ ዘንድ አስወደዳት ልብላ ልብላ አሰኛት ።
ወታብልዖ ለአዳም ፤
ለአዳም ታበላው ዘንድ ፤
ከመ ይኩኑ ዘየአምሩ ሠናየ ወእኩየ ።

የሰውነትን የአምላክነትን ዕውቀት ያውቁ ዘንድ ፤
ወሶበ ጸንዐ ኀበ ነገሩ ጸንዓ ላዕሌሃ ፍትወተ ጥዕመት ምስለ ሕሊና ትዕቢት ፤
ነገሩን በተቀበለች ው ጊዜ አምላክ እሆናለሁ በማለት ልብላ ልብላ የማለት ፈቃድ አደረባት ። ልብላ አሰኛት ፤

ወአፍጠነት ወበዓልት እምይእቲ ዕፅ ፤
ፈጥና ቆርጻ በላች ።
ወአብልዓቶ ለአዳም ፤
ለአዳምም አበላችው ። ሐተታ ነገሩን እንደ ተቀበለችው አውቆ የአምላክነት ነገር እንዲህ አይደለም የተቀዳደማችሁ እንደሆነ ያገደኛችሁ ይቀርባትኋል ለርሱ በቀኝ እጅሽ ላንቺ በግራ እጅሽ ቆርጠሽ አንድ ጊዜ ጉረሺት አላት ። የሷ ሲነግት አይቶ እሱ ያመልጠኛል የሱ ሲነግው አይታ እሷ ታም ልጠኛለች ብሎ ፥ ዛሬም ሴቶች ይህ አብነት ሁኖ ባቸው ብቀኝ እጃቸው ለባሎቻቸው እያሳለፉ በግራ እጃቸው ይበላሉ ።
ወወጽኡ እምትእዛዘ እግዚአሙ ወተዓደው አምነ ገሩ ፤
ከፈጣሪያቸው ትእዛዝ ወጡ ፤
ወቦኑ ቀታልያነ ርእሶሙ ፤
ራሳቸውን አጥፊ ሆኑ ።
ወተሰዱ እምድረ ገነት ኀበ ምድረ ሕማም ፤

ከገነት ወደ ምድረ ፋይድ ወረዱ ፤ ሐተታ ምድረ ፋይድ ማለት ምድረ ኃጣር ወመርገም ምድረ ድን ጋጼ ወረዓድ ማለት ነው ።
ወእርእያ ኀሱም ወኅሱር ፤
ከፉና መልካም ቀይና ጥቁር አጭርና ረጅም ቀጭ ንና ወፍራም ወደሚፈጠርበት ።
ወሲሳየ ኃዘን ።

ቢያገኙት ቋንጣን ቢያጡት ቀጠና ወደሚሆንበት ወፈትሐ ላዕሌሆሙ በሞት እስከ ለዝሉፉ ፤

አምስት ሺህ አምስት መቶ ዘመን እስኪፈጸም በሞተ ሥጋ ላይ ሞተ ነፍስን ፤ በርደተ መቃብር ላይ ርደተ ገሃነምን ፈረደባቸው ።
ወእምድኅረ ተዓርቁ እምልብሰ ብርሃን ዘቲአጽፉ ቦቱ ።

ከተሰጣቸው ከጸጋቸው ከተለዩ በኋላ ፥ አንድም የተ ሰጣቸው ጸጋቸውን ባጡ ጊዜ ።
ተኃፍረ አዳም እምእግዚአብሔር ፤
ከእግዚአብሔር የተነሳ አዳም ፈራ ፤ ሐተታ ስኩና ብእሲ እያሰማ ቢመጣ አዳም ፈርቶ ከእንጨት ውስጥ ተሰውሮ ተገኝቷል ።
በእንተ ተዓድዎቱ ።
ከትእዛዙ ስለወጸ ፈራ ።
ወናሁ ቀደመ ቃል ከመ ነፍስ ነባቢት እንዘ አልቦ ዘይኬንና ወዘይጌይላ ፤
ተኃፍረ ብሎ ነበርና በምን አውቆ ትሉኝ እንደ ሆነ ። የሚገዛት የሚያዛት ሳይኖር ነፍስ አዋቂት እንደሆነች አስቀድሞ ተነግሯል ወዝብረ ላቲ ሥል ጣነ በውስቴታ ከመ ትግበር ዘከመ ኃረየት ተብሎ ወለአመሰ ነበረት በትእዛዙ እምኮነት ብርሀት በብ ርሃነ ትእዛዙ ፤
ትእዛዙን ጠብቃ ኑራ ቢሆን ትእዛዙን ቢጠብቁ በሚገኝ ብርሃን ትእዛዙን በመጠበቅ ብርሃን ብር ሀት በሆነች ነበር ።
ወሶበ ጸንዐት እንከ ኀበ ተዓድዎተ ነገሩ ጸልመት በጽልመተ ተአድዎ ።
ትእዛዙን ግን ቢያፈርሱ ፤ ትእዛዙን ቢያፈርሱ በሚ መጣ ጨለማ ። ትእዛዙን በማፍረስ ጭልማነት ጨለ መች ማለት ። ትእዛዙን ቢያፈርሱ በሚመጣ ድን ቁርና ደነቁረች ።

እስመ እልቦ ዘይኄንና ወዘይጌይሳ በውስተ ፈቃደ
ኅፅሴሃ ፤
በፈቃዷ የሚያዛት የሚገዛት የለምና ፤ እመ ነበረት
ለበጎው ፤ የሚያዛት የሚገዛት ሳይኖር ሶበ ጸነት
ለክፉው ፤
ወበእንተ ዝንቱ ይረክቦ ለብእሲ ገነት ፤
ገነተ ሲል ነው ፤ መገናኘት የጋራ ከሆነ ብሎ እን
ዲህ አለ እንጂ ። በስዚህ አዳም ገነትን ይወርሳል ።
ሶበ ሞቅሐይጤ እምኢኩይ ውስተ ሠናይ ወገቢሮቱ ።
ከክፉ ወደ በጎ ቢመለስ በጐውን ወደ ማድረግ ቢመ
ለስ ፤ ገነትን ይወርሳል ፤

ወሶበ ጸነ እምሠናይ ኀበ እኩይ ወገቢሮቱ ፣
ከበጎ ወደክፉ ቢመለስ ክፉውን ቢያደርግ ፤
ደለዎ ሁነኔ ፤
ሞት ተፈረደበት ።
ወበጸኒኖቱ ለአዳም ኀበ ፈቃደ ሰይጣን ወተዓድ
ዎተ ፈጣሪሁ ኮነ እንከ ገብሮ ለሰይጣን ፤
አዳም የሰይጣንን ነገር በመቀበሉ ከፈጣሪው ትእዛዝ
በመውጣቱ የሰይጣን ተገዢ ሆነ ።
ወታሕተ ሥልጣኑ ፤
ከሥልጣኑ በታች ሆነ ፤

ወተርፈ ውስተ ምድር ኅዙነ ወትኩዘ ፤
በዚህ ዓለም ያዘነ የተከዘ ሁኖ ኖረ ፣ አንድም ኮነ
ገብሮ ለሰይጣን ታሕተ ሥልጣኑ፤ከሥልጣኑ በታች
ሁኖ የሰይጣን ተገዢ ሆነ ። ወተርፈ ፤ በዚህም ዓለም
ያዘነ የተከዘ ሁኖ ኖረ ፤
በእንተ ዘገብረ ተዓድዎተ ፤ ከፈጣሪው ትእዛዝ
ስለወጣ ።
ወዓለወ ትእዛዘ ፈጣሪሁ ፤
የፈጣሪውን ትእዛዝ ስላፈረሰ ፤
ወእምንዳቤ እንተ ረከቦ ፤
ካገኘው ጸዋትወ መከራ የተነሣ ፤
እምኃዘን ወእምእውያት ፤
ከኃዘን ከልቅሶ የተነሣ ፤
ወከኢወ እንብዕ ውዑይ ።

ቁጡ እንባን ከማፍሰስ የተነሣ ። ሐተታ ቁጡ እንባ
ዓይን ከማጥፋት ያደርሳል ። አንድም ውዑይ እንባ
ከማፍሰስ የተነሣ ።
ሪስዓ ገነተ እንተ ነበረ ባቲ ፤
የነበረባትን ገነትን ዘነጋ ።
ወእልቦቱ ካልዕ ሕሊና ዘእንበለ ብካይ ላዕለ ኃጢ
አቱ ፤

በኃጢአቱ ከማዘን ከማልቀስ በቀር ማዘን ማልቀስ
ነው እንጂ ሌላ ግዳጅ አልነበረውም ፤ ሐተታ አዳ
ምን የቤተ ፈት ልማድ አላገኘውም ቤተ ፈት
በዚህ ጊዜ እበላ እጠጣ እለብስ አጌጥ የነበረ ቀረ
ብኝ ብሎ ያዝናል ፣ እሱ ግን የማይገባ ሥራ ሠርቼ
ፈጣሪዬን አሳዘንሁት ብሎ ነው እንጂ በገነት
ሳለሁ አደርገው የነበረው ተድላ ደስታ ቀረብኝ ብሎ
አይደለምና በኃጢአቱ ከማዘን ከማልቀስ በቀር
በኃጢአቱ ማዘን ማልቀስ ነው እንጂ ግዳጅ አል
ነበረውም አለ ፤
ወእስመ እግዚአብሔር ይትለዓል ዝክሩ ንስሐሁ
ወገዓሮ ብዙኃ ወምንዳቤ እንተ ረከቦ ተማኅለ ላዕ
ሌሁ ወምሕሮ ።
በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና
እላበጀሁም ማሰቱን ብሶ መጨነቁን ጸዋትወ መከ
ራውን አይቶ ይቅር አለው አዘነለት ፤
ወፈቀደ ያድኅኖ እምዳኅጹ በእንተ ፪ ገጸት ።
ስለ ሁለት ነገር ከፍዳው ሊያድነው ወደደ ፣
፩ዱ በእንተ ንስሐሁ ፤
ከሁለቱ አንዱ እላበጀሁም በማለቱ ነው ፣
ወገዓረ ብካዩ ለኃሚሠ ሥርየት ፤
ኃጢአቱ ሊሠረይለት ኃጢአቱን ሊያሥተሰርይለት
እያለቀሰ በመጨነቁ ነው ።

ወረሲአቱ ገነተ ወፍግዓሁ ወተድላሁ ፤
ገነትን በመዘንጋቱ ተድላው ደስታውን በመዘን
ጋቱ ነው ።

ወካልዕስ በእንተ ዘተሕተ ውእቱ ተትሕቶተ
ወካልዕሂ ሲል ነው ሁለተኛውም እሱ ፈጽሞ ስለ
ተዋረደ ነው ።
ወዓዲ አጥረየ ሰይጣን መዊዓ ወኃይለ ላዕለ አዳም
ወቀነዮ ፤
ዳግመኛ ሰይጣን በአዳም ላይ ኃይልን መዊዕን ገን
ዘብ አደረገ ።
ወኮነ ጼዋሁ ፤ ምርኮው ሆነ

ወኮሉ ዘርዑ ምስሌሁ ፤
ልጆቹም ከሱ ጋራ እንደሱ ተገዙ ።
ወተሰልጠ ሰይጣን ዲቤሆሙ ለእስግዶ በብዙኅ ግብ
ራት ። አሳታቸው ብሎ ነበርና ዳግመኛ
በብዙ ነገር ለማሳት ሰይጣን ሠለጠነባቸው ።
ወመንክራት ትልዋት ፤
ቀጽሎ ቀጽሎ በሚደረግ በምትሐት ተአምራት ፤
አንድም ወመንክራት ትልዋተ ይባል ። ቀጽሎ ቀጽሎ
እራድፎ እራድፎ በሚመጣ መከራ ሠለጠነባቸው
ወቦ እምኔሆሙ ዘመሐረ ከመ ፍጥረት ተፈጥረት
እምኀበ ርእሳ ባሕቲታ ዘእንበለ ሠራዒ ወገባሪ ።
ከርሳቸው ወገን ፍጥረት ያለ ሠራዒ ያለ መጋቢ
ከባሕርይዋ እንደ ተፈጠረች ያስተማረ አለ እን ማኒ
ወቦ እምኔሆሙ ዘመሐረ ከመ ፀሐይ ወወርህ ወከ
ዋክብት አሙንቱ እለ ፈጠሩ ዓለመ ፤

ሰማይ ምድርን የፈጠሩ ፀሐይ ጨረቃ ከዋክብት
እንደሆኑ ያስተማራቸው አሉ ። ጽርዓውያን ፀሐይ
ጨረቃን ስባቱን ከዋክብት ያመልኩ ነበር ።

ወቦ ዘመሐረ ከመ አምልኮ አራዊት ወእንስሳ ይእቲ
ፍኖት በአማን ጥይቅት ፤

አምልኮተ አራዊት አምልኮተ እንስሳ በውነት የተ
ረዳት ሃይማኖት እንደሆነች ያስተማራቸው አሉ ።
ወባቲ ይትረከባ ፈቃዳት ።
የሚሹት ነገር በሷ እንዲገኝ ።
ወይትፌጸማ ባቲ ስእለታት ።

ልመናም በሷ እንዲገኝ ያስተማራቸው አሉ ። ሐተታ
ግብጻውያን ላም ያመልኩ ነበር ባቢሎናውያንም
ዘንዶ ያመልኩ ነበር ፥

ወአርስእሙ እግዚአብሔርሃ አምላኮሙ ።
ፈጣሪያቸው እግዚአብሔርን አስካዷቸው ።

ወቦኡ ውስተ ልጎተ ርስእት ፤ ወደ ፍጹም
ዝንጋኤ ገቡ ፤

ወተመንኖት ወተቀንዮት ለብዙኅ ኃጢአት ዘዘዚአሁ
ልዩ ልዩ የሚሆን ለብዙ ኃጢአትም ወደ መገዛት
ወደ መናቅ ገቡ ።

አምቅትለት ፤ ነፍስ ከመግደል ወገን
ወእምዝሙት ወሐሰት ወሐሜት ።
ከዝሙት ከሐሰት ከሐሜት ወገን አንዱ ብቻ ሠር
ቶት አይቀርምና በከፊል ተናገረው ።
ወአፆእት ።
ሰውን እግዚአብሔርን ከመበደል ወገን ፤
ወትዕግልት ። ከቅሚያ ወገን
ወእምልኮተ ጣዖት ዘግብረ እድ ፤
የሰው እጅ ሥራ የሚሆን ጣዖትን ከማምለክ ወገን
ወክሂደ እግዚአብሔር ፤
እግዚአብሔርን ከመካድ ወገን ።
ወዘይመስሎ ለዝንቱ ።

ነማማለትና ይህን ከመሰለ ወገን ለብዙ ኃጢአት ወደ
መገዛት ገቡ ።
ወኮኑ ስይጣናት ውኩላነ ፤
ሰይጣናት ቁራኞች ሆኑ ።
ወሥሉጣነ በአዳም ወበኵሉ ዘርዑ ውስተ አሕጉሎ
በአዳም በልጆቹም ሁሉ በቁራኝነት የሠለጡኑ ሆኑ
ከመ ጺውዋን ፤

ምርኮኞች እንደመሆናቸው ፥ እንድም ማራኪ በም
ርኮኞቹ እንዲሠለጥን ።

ወለዘሞት እምኔሆሙ የአሥሩ ነፍሶ ውስተ ሲኦል
ይህም ሊታወቅ ከላቸው ወገን የሞተውን ሥጋውን
በመቃብር ነፍሱን በሲኦል በገሃነም ተቁራኝተው
ይኖሩ ነበር ። አሜሃ ይትፌነዋ ነፍሳት ውስተ ገሃነም
እስከ ይመልእ አብያተ ሞት እንዲል ።

ወኮነ በሙ ዝንቱ ግብር ለዝሉፉ እስከ ተፍጸሜተ
፶፻ ወ፭፻ ዓመት እምፍጥረቱ ለአዳም ፤

አዳም ከተፈጠረ ጀምሮ አምስት ሺህ አምስት መቶ
ዘመን እስኪፈጸም ድረስ ቁራኝነት ፈጽሞ ተደረገ
ባቸው ።

## አራተኛ ጉባኤ ።

ወፈቀደ እግዚአብሔር አድኅኖተ ዓለም በማህሉ
ወበምሕረቱ ።
በይቅርታው በቸርነቱ ብዛት እግዚአብሔር ዓለምን
ማዳን ወደ ፤
ወርእየ ተግባረ እደዊሁ እለ እምጽእሙ እምተኃጥ
ጥኦ ኀበ ተረክቦ ፤

ካለመኖር ወደ መኖር እምኀበ እልቦ ኀበ ቦ ከኢ
ምንት ወደምንት አምጥቶ የፈጠራቸውን ፍጥረቶ
ቹን አይቶ ። እንድም እምኃጢዕ ኀበ ረኪብ ይላል
አብነት ካጣ በኋላ ያገኛቸውን ፍጥረቶቹን አይቶ ፥
ወእከበሮሙ ላዕለ ኵሉ ፍጥረት ዘታሕተ ሰማይ
ከሰማይ በታች ባሉ ፍጥረታት ሁሉ እንዲሠለጡና
ቸው አይቶ ።
ከመ በዝኃት ወፈድፈደት ኀበ ተጼውዎተ ሰይጣን
ወደሰይጣን ምርኮኝነት መሄዳቸው ፈጽማ እንደጸ
ናት ዐውቆ ።
ወቀንዮቱ መሪር ፤
ወደጽኑ እገዛቱ መሄዳቸው እንደጸናች ዐውቆ ።
ምሕሮሙ በዕበየ ሣህሉ ወምሕረቱ ወኂሩተ ሠና
ይቱ ፤
በይቅርታው በቸርነቱ ብዛት አዘነላቸው ።
ወፈትሖሙ እመዋቅሕቲሁ ፤
ከቁራኝነቱ አዳናቸው ።
ወእምጼዋዌሁ ማኅጉሊ ፤

ጥፋት ካለበት ምርኮኝነቱ ፥ ወእምጼዋዌ ማኃጉሊ
ይላል ። ሰይጣንን በግብሩ ማኃጉሊ አለው ከሰይጣን
ምርኮኝነት ፈትሖሙ አዳናቸው ።
በዘይሜኒ ጽድቁ ወርትዑ ።

ባማረ በተወደደ ፍርዱ አዳናቸው ። ወበድልወት
ኮነ ኰነኔ እግዚአብሔር ወአድኃነነ በፍትሐ ጽድቅ
ወርትዕ እንዲል ። ጌታ የገደልክ ገደልክ የበደልክ
በደልክ በቃህ አላለምና በካሳ ብኋል እንጅ ፤
ወኢኃደጎሙ ውስተ ኃጉል ለዝሉፉ በዕደ ሰይጣን ።
በሰይጣን እጅ እንደተያዙ ሊቀሩ በቁራኝነት
ፈጽሞ አልተዋቸውም ።
ወኢሞአ በኃይሉ መዋኢት ፤
በእምላክነቱ ድል አልነሣውም ።
ወኢኃየሎ በክሂሎቱ ።
በከሃሊነቱ አልተዋጋም አልሠለጠነበትም ።
ወኢበምንትኒ እምዕበዩ ፤

ከጌትነቱ ወገን በምንም በምን በአምላክነቱ ድል
አልነሣውም ።

እላ በትሕትናሁ ወፍትሐ ጽድቁ በትሩፋተ ምሥ
ጢር እንግዳ ።
እንግዳ በሚሆን ተዋርዶ በሠራው ሥራ ነው እንጅ
በዘየዓቢ ጥበቡ እምነ ኵሉ ጥበብ ወልባዌ ።
ከጥበብ በሚበልጥ ጥበቡ ከእውቀት በሚበልጥ ዕው
ቀቱ ፤ ሐተታ ዓለምን ከፈጠረበት ጥበቡ ሰው
ሁኖ ማዳኑ ይበልጣልና ።
ቀዳማዊ ዘውእቱ እምቀዲሙ ዘእልቦ ጥንት ቃለ
እግዚአብሔር ፤ ቀዳማዊ ጥንት
የነበረ በዚህ ጊዜ ተገኘ የማይባል እካላዊ ቃል ፤
ዘቦቱ ኵሉ ኮነ ።
ሁሉ በሱ ሕልውና በሱ አንድነት የተፈጠረ ።
ወዘእንበሌሁሰ አልቦ ዘኮነ ወኢምንትኒ እምዘኮነ
ያለሱ ሕልውና ግን ምንም ምን የተፈጠረ የሌለ
እስመ ቃለ ኵሉ ፍጥረት ትመስል ፍጥረታት ።
የሰው ሁሉ ቃል እንጅ የሰው ሁሉ ቃልእኮን ባሕር
ይዋን ትመስላለች ፡ እንድም የሰው ሁሉ ቃል
ባሕርይዋን ትመስላለች እኮን ፤ ወእምጣ
ናሰ እስመ ቃለ ሰብእ ሐማሚት ወጸም ሐያዪት ።
መጠኑዋ ግን የሰው ቃል ደካማ የምትጸወልግ ናትና
ወሕይወታ ምሉዕ በከመ ንሬእያ እምተማትሮትነ
ዘበዓቡዕ ፤ በረቂቅ ተዋሕዶው ባለ
በሥጋ እነዋወሯ ተጠልፎ ኸያጅ ነውና ።
ኃላፊት ወማሳኒት ፤
ያኑ እንድናውቅ ኃላፊ ጠፊ ናትና ፡
ወሐዋሪት ኀበ ተኃጥእ ፡
ከመናር ወዳለመኖር እምኀበ ቦ ኀበ አልቦ ከምንት
ወደ ኢምንት ኸያጅ ናትና ። ወቃለ እግዚአብሔርሰ
ልዕልት ፡ እካላዊ ቃል ግን
ከዚህ ሁሉ የራቀች ናት ።

ይእቲኬ እርዓያ ገጹ ፡ እግዚአብሔር
አብን በመልክ የምትመስለው በባሕርይ የምት
ተካከለው ናት ።

ቀዳሚት ወፈጣሪት ። ቀዳማዊት ፈጣሪት ናት
ወሕያውት ለዓለም ህላዊት ።
ለዘላለሙ ሕያውት ባሕርያዊት ናት ።
ወነባሪት ዘኢትማስን የማትለወጥ ነባሪት ናት
ወሶበ ኮነት ይእቲ ቃል ፈጣሬተ ወሕያውተ ወባሕ
ርያዊተ ነባሬተ ለዓለም ይደሉ እንከ በዛቲ ግብር
ባሕርያዊት ትሰመይ ሕላዌ አካለ ።

እንዲህ እንዲህ ከሆነች ባሕርያዊት በምትሆን በዚ
ህች ሥራ ፤ ሕላዌ ፡ አካል ባሕርይ ልትባል ይገባል
እስመ ትርጓሜሃ ለሕላዌ በኀበ መምህራን ነባብያን
በጥይቅና ።

እስረድተው በሚተረጉሙ በመምህራን ዘንድ የሕ
ላዌ ትርጓሜ አካል ነውና አካል ባሕርይ ነውና ባሕ
ርይ ልትባል ይገባል ፤
ውእቱ ዘአልቦ እሡር ለባሕርይ ፤

ባሕርዩ የማይመረመር እርሱ ፤
ፈቀደ በፈቃደ አቡሁ ወበሥምረተ መንፈሱ ቅዱስ
ከመ ይቤዙ ኵሎ ነፍሳተ እለ ሙቁሐን ኀበ ጽል
መተ ሞት ወጥንቃቃተ ሲኦል ።

በባቱ ፈቃድ በመንፈስ ቅዱስ ፈቃድ ሞት ባመጣው
ጨለማ ተግዘው የነበሩ ነፍሳተን በሲኦል ምቶግ
ግነት ያሉ ነፍሳትን ሊያድን ወዷልና ።
በሕላዌሁ ቅዱስ ፤
ከአብ ከመንፈስ ቅዱስ በተለየ አካሉ ፤
ወኀቢአ ብርሃነ መለኮቱ ዘኢይትከሃል ከመ ያስተ
ርኢ በተሠግዎቱ እመንፈስ ቅዱስ ወእማርያም
እምቅድስት ድንግል ።

በፈቃደ አቡሁ ወበሥምረተ መንፈሱ ቅዱስ በተ
ሠግዎቱ ። ባባቱ ፈቃድ በመንፈስ ቅዱስ ፈቃድ
ከመንፈስ ቅዱስ ከፋይነት ከመቤታችን ተከፋይነት
የተነሣ ሰው በመሆን ኀብአ ፤ እንድም በግብረ መን
ፈስ ቅዱስ ከእመቤታችን ከሥጋዋ ሥጋ ከነፍሷ ነፍስ
ነሥቶ ሰው መሆኑ ሊታይ የማይቻል ብርሃነ መለ
ኮቱን በሥጋ ሰወረ ።

ከመ ይቅረብ እምኔሁ ጸላዒ ወይብጻሕ ኀቤሁ ፡
ይቅረብ ያለውን ይብጻህ እምኔሁ ያለውን ኀቤሁ
እለው ጸላዒ ዲያብሎስ ወደሱ ይደርስ ዘንድ እን
ድም ሰው ከመሆኑ የተነሣ የሰውነት ሥራ ከመሥ
ራቱ የተነሣ ወደርሱ ይቀርብ ዘንድ ወደርሱ ይደርስ
ዘንድ ። ወያምስሎ ከመ ካልዓን ሰብእ እለ ውስተ
ጼዋሁ በምርኮኝነት እንዳሉ እንደ ሌሎች ሰዎች
ያደርገው ዘንድ ።
ወያስተጌብሮሙ ግብሮ ፡

ሥራውን የሚያሠራቸውን ያስመስለው ዘንድ ሥራ
ውን እንደሚያሠራቸው ያደርገው ዘንድ ወያስተ
ጌብሮ ግብሮ ። ሥራውን የሚያሠራውን ሰው ያስ
መስለው ዘንድ ።

ወኢይፍራህ እምነ ዕበዩ ወመንከራቲሁ ሶበ ርእየ
ከተአምራቱ ከጌትነቱ ወገን ባየ ጊዜ እንዳይፈራ
ወበከመ ኮነ እንከ ሰይጣን በጉሕሉት ተኃብዓ ውስተ
ሥጋ ከይሲ ።

ኮነ ያለውን ተኃብአ ብሎ አመጣው ፤ ሰይጣን በተ
ንኮል በሥጋ ከይሲ እንደ ተሠወረ ።

እስከ ተሠልጠ ወጸንዓ ላዕለ ፍጥረትነ እምቀዳሚ
ከጥንት ዠምሮ በባሕርያችን እስኪሠለጥን ድረስ
ሐተታ ተሠልጠ ጸንዓ ማለቱ ግን ሥጋን በመቃብር
ነፍስን በገሃነም ተቆራኝቶ ይኖር ነበርና ነው ከማሁ
ኮነ ድኅነትነ እማዕሰር በተሰውሮተ ቃለ እግዚ
አብሔር በዘመድነ ።

እኛም ከፍዳ መዳናችን ቃለ እግዚአብሔር በባሕር
ያችን በመሰወሩ ሆነ ።

ወበተዋሕዶቱ ቦቱ ፤
ሥጋን በመዋሐዱ ሆነ ፤
እስከ ቤዘወነ እምኔሁ ፤ ከሱ እስኪያድነን
ወአደኃነነ በፍትሐ ጽድቅ ወርትዕ ።
በፍትሐ ጽድቅ በፍትሐ ርትዕ አዳነን ። ሐተታ እን ዳለፈው ።

ወኮነ ከመ ኵሉ ሰብእ ዘእንበለ ኃጢአት ባሕቲታ ፤
ከብቻዋ ከኃጢአት በቀር እንደ ሰው ሁሉ ሆነ ፣
ወነነ ኵሎ ከመ ሰብእ እንደ ሰው ሁሉን ሆነ ።
ወእምድኅረ ዝንቱ ወእምቅድሜሁኒ ኢተዓርቀ እመ ንበረ ስብሐቲሁ ።

ከፅንስ በኋላ ከልደት በፊት ዘጠኝ ወር ካምስት ቀን በማኅፀን ሳለ ከጌትነቱ መንበር አልተለየም ። እን ድም ከልደት በኋላ ሠላሳ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር፣ ከልደት በፊት ዘጠኝ ወር ከአምስት ቀን ከጌትነቱ መንበር አልተለየም ።

ወኢያንከር እንከ ወኢፎዱሂ እምዝንቱ ነገር ፤
ከዚሀ ነገር የተነሣ አንድ ስንኳ አያድንቅ እንዳያደንቅ ወኸሕነኒ ምድራውያን እለ ፍጡራን ኢንእምር ፍጥ ረተ ነፍስነ ነባቢት እምውስጠ ወሰነ ሥጋነ ።
ምድራውያን ፍጡራን የምንሆን እኛ የሥጋ ሕይ ወት ከምትሆን ከደመ ነፍስ ጋራ ተዋሕዳ ያለች የነባ ቢት ነፍሳተንን ባሕርይንስ እንኳ ዐናውቅም ።
በእንተ ዘትሰፍሕ መልዕልተ ሰማያት ።
ወደ ሰማይ የምትደርስ ስለሆነች ፤ ትደርስም እንደ ሆነ አትደርስም እንደሆነ ዐናውቅም ።

ወትሬኢ ኃይላተ ሰማያውያን ወፍጥረታተ ሉዓላው ያን ሰማያውያን መላእክትን ሉዓላውያን ፍጥረታትን የምታይ ስለ ሆነች ። ታይም እንደሆነ አታይም እንደሆነ አናውቅም ።
ዘርእዩ ዳንኤል ነቢይ ወዮሐንስ ወልደ ዘብዴዎስ ወካልዓንሂ ።
እነ ዳንኤል እነ ዮሐንስ እነ ሕዝቅኤል ያዩትን ፣ በኪመ ርእዩ ይላል ። በኪመ ባለቤቶችን ማምጣት ነው እነ ዳንኤል እነ ዮሐንስ እነ ሕዝቅኤል እንዳዩ ።
ወኢትትአኃዝ ላቲ ነፍስ ወኢበምንትኒ እምግዘፈ ሥጋ ።
ከሥጋ ግዘፍ የተነሣ ነፍስ በምንም በምን አትገታም ወኢይትበሐል እንከ እፎ ተዋሐደ ቃል በሕላዌ ሥጋ ወኢተዓርቀ እመንበረ ስብሐቲሁ ።
እንዲህ ከሆነ አካላዊ ቃል በባሕርየ ሥጋ እንደምን ተዋሐደ ከተዋሐደስ ከጌትነቱ መንበር እንደምን አል ተለየም አይባልም ።
ወሶበ ኮነ ከመዝ ለነፍስተ ፍጡራን ወእፎ ፈድፋደ ይኪውን ማዕከለ ፍጥረት ሸወጣሪሃ ፤
ለፍጡራን ባሕርይ እንዲህ ከሆነ በፍጥረትና በፈጣ ሪዋ ዘንድ የቱን ያህል መበላለጥ ይኖር ይሆን ።
ወእምድኅረዝ ከሠተ ኃይሎ ወዕበዮ ።

ወእምድኅረ ዝንቱ ወእምቅድሜሁኒ ኢተዓርቀ እመ ንበረ ስብሐቲሁ ብሎ ነበርና ከተወለደም በኋላ ከሃሊነቱን ጌትነቱን ገለጠ ።
ወዓዲ በተአምራት ።

ከሠተ ፣ ዓዲ ዳግመኛም በተአምራት ገለጠ ።
እንተ ገብረ በከሚተ አዕይንተ እውራን ።

እውራንን ከማብራት ወገን ባደረገው ተአምራት ፤
ወአንጽሖ እለ ስምጽ ። ልሙፃንን ከማንጻት ወገን
ወአንሥአተ መፃጕዓን ።

ደዌያቸው የጸናባቸውን ከማዳን ወገን ፣
ወአውፅኦተ አጋንንት እምድውያን ።
ከሕሙማን አጋንንትን ከማውጣት ወገን ።
ወአሕይዎ ሕሙማን ዘዘዚአሁ ሕማሞሙ ።
ደዌያቸው ልዩ ልዩ የሚሆኑ ሕሙማንን ከማዳን ወገን ።

ወገሥጾ ነፍሳት ። ነፋሳትን ከመገሠጽ ወገን
ወሐዊር ዲበ ማይ ። በወኃ ላይ ከመሄድ ወገን
ወአጽግቦ አእላፋት እምኅ ኅዳጥ ኅብስት ።

እምስት እንጀራ አበርክቶ ለአምስት ሽሀ ሰው ከማ ብላት ወገን ።
ወአንሥኦተ ምውታን እመቃብራት ።
ሙታንን ከመቃብራት ከማሥነሣት ወገን ። ሐተታ ያሥነሣ አንድ አልዓዛርን አይደለምን ቢሉ ፣ መጽ ሐፍ ስም ካልጠራ ማብዛት ልማዱ ነውና ። አንድም በተአምረ ኢያሱስ እነ አብርሃምን ነቢያትን ሁሉ አሥነሥቷል ይላል ።
ወዘይመስሎ ለዝንቱ ።

ይህን የመሰለ ሁሉ ባደረገው ተአምራት ከሠተ ጌትነቱን ገለጸለ ።
ወገብረ ዘንተ ተአምራተ በእንተ ብዙኅ ግብራት ስለ አራት ነገር ይህን ተአምራት አደረገ ።
አሐቲ እምኔሃ ከመ ይነጽር ሰይጣን ዕበዮ ወከሂሎቶ ካራቱ አንዱ ሰይጣን ጌትነቱን ከሃሊነቱን ያውቅ ዘንድ ነው ፣
ከመ ይኩን ምክንያተ ለዘሀለወ ውእቱ ከመ ይግ በር ቦቱ ከመ ኵሉ ሰብእ ጽሩዓን ።

እርሱ እንደ ዕሩቅ ብእሲ አድርጎ በሱ ያደርግበት ዘንድ ስላሰው ነገር ምክንያት ሊሆን ነው ።
ወካልዕታሂ ከመ ይኩን ተበቅሎተ ለእለ ርእዩ ዘንተ ተአምራተ ወኢተለውዎ ወርኅቁ እምኔሁ ወአስተር አይዎ በከሕደት ወበዕልወት በፍትሐ ጽድቅ ወርትዕ ሁለተኛ ተአምራቱን አይተው ባላመኑ መፈራረጃ ይሆን ዘንድ ነው ፣

ወሣልስታ ከመ ይኩን ጽንዓ ለእለ የእምኑ ቦቱ ፣ ሦስተኛም ላመኑበት ኃይል ይሆናቸው ዘንድ ነው ኃይለ ስተጋድሎቶሙ ።

ለመዋጋት ጽንዕ ይሆናቸው ዘንድ ነው ።
ወራብዕታዊ እስመ ትመርሆሙ ይእቲ ለእለ ተመ
ይጡ እምኃጉል ወተሰው ጽድቀ ።

አራተኛም ከክሕደት ወደ ሃይማኖት ከኃጢአት ወደ ጽድቅ ለተመለሱ መሪ ትሆናቸዋለችና ስለዚህ ነው
ወዘቦነ ይገብር ምግባራተ ዘይደሉ ለሰብእ ።

ለሰው የሚሰማማ ሥራ ይሠራ የነበረ ማለት ለሰ
ውነቱ የሚሰማማ ሥ ይሠራ የነበረ ።

እምኀዘን ፡　　ያዝን የነበረ ፡　　ወፍርኃት
ይፈራ የነበረ ።　ወረሀብ ፡　　ይራብ የነበረ
ወንዋም ፡　　ይተኛ የነበረ ።　ወጸዊረ ጽእለታት
ስድቡን ታግሦ ይቀበል የነበረ ።
ወዘአምሳለ ዝንቱ ።　　ነሣሣለትና ይህን
የመሰለ ሥራ ይሠራ የነበረ ።

እስመ ፈቀደ ውኑቱ በዝንቱ ከመ ይንሥት ጥበቦ
ለሰይጣን ።

በዚህ የሰይጣንን ጥበብ ሊያፈርስበት ስለወደደ ነው
እንድም ወዷልና ስለዚህ ነው ።
እስመ ውእቱ ኮነ ሶበ ይሬኢ ተአምረ ወመንክረ
ይፈርህ ወይቴክዝ ።

ኮነ ያሰውን ይሬኢ ብሎ አመጣው እሱ ተአም
ራቱን ባየ ጊዜ ይፈራ ያዝን ነበርና ።
ወይርሕቅ እምትውክልና ቦቱ ወተሣልቆት ላዕሌሁ
እሱን እቆራኛለሁ ከማለት በሱ ከመዘበት ይርቅ
ነበርና ።
ወእመ ርእየ ምንተኒ እምነ ሕጸታት ወጽርዓታት
ይትፌሣሕ ።
የሰውነት ሥራ ባየበት ጊዜ ግን የላሜ ልጅ ያው
ራዬ ውላጅ ብሎ ደስ ይለው ነበርና ።
ወይትኤበይ ።　　ይታበይ ነበርና ።
ወይትመየጥ ኀበ ትውክልና ቦቱ፤
እሱን እቆራኛለሁ ወደማለት ይመለስ ነበርና ፤
ኪመ ሙቁሕ ውስተ እዴሁ ።
በእጁ እንደ ተያዘ አድርጎ ፡
ወምእ እንከ ።　　ድል ነሣው ፡
ወነሥተ ጥበቢሁ በዛቲ ገጸት ንሥተታት ዘዘዚአሃ
ኮለንታሃ ብይንተ ።
እየራሱ እየራሷ የነሳ የተረዳ መለየትን በተለዩች
የፈረሡች በምትመስል በሰውነቱ ሥራ ጥበቡን አፈ
ረሠበት ።
ወተኪሥተት ሎቱ ተመውአቱ ፡
ድል መሆኑ ተገለጸችለት ።
ወጸርዓት ጥበቡ ።　　ጥበቡ ዛገች ።
ወጽዕቀቶ ቦቱ ስሕተቱ ወምክንያቱእምተቃርኖተ
ተአምራተ ብሩሃት ወንሥተታት ከሡታት ።
የጎላ የተረዳ መፍረስን የፈረሱ የሚመስሉ ተአ
ምራትን ከመቃወሙ የተነሣ ስሕተቱ ምክንያቱ

ወለሌ አሰኘችው ፡ ሐተታ የሰውነቱን ሥራ ሲሠራ
የአምላክነቱ የፈረሰ ይመስላል ፡ የአምላክነቱን ሥራ
ሲሠራ የሰውነቱ የፈረሰ ይመስላልና ያንንም ንሥ
ተታት ፡ ያንንም ንሥተታት አለ ።
ወኮነት ልማድ ንብርተ ለካህናተ አይሁድ ።

ለካህናተ አይሁድ የለመደች ሥርዓት ነበረች ፤ እን
ድም ኮነት ልማድ ንብርተ ፤ ሥርዓት የጸናች ሁና
ነበረች ።
ኪመ ይፍትሑ ላዕለ ጊጉያን ።

በበደለኞች ይፈርዱ ዘንድ ፡
ቀተልት ወሠረቅት ወፈያት በስቅለት ።
ነፍስ በገደሉ ሞትን በሠረቁ ግርፋትን ፡ በወምበዴ
ስቅለትን ይፈርዱ ዘንድ የቀረው ቅጣቱ ስልት
ስልት አለው ለወምበዴ ግን ስቅለት ነው ።

ወእልሆሰሰ ሎሙ ፀራዊ ከመ ዝንቱ ውእቱ ኢየ
ሱስ ዘነሠተ ሕገ ወገብረ ተአምራተ ወመንክራተ
በዕለተ ሰንበት ።

ሥርዓት አፍርሶ ቅዳሜ ተአምራትን ያደረገ ኢየሱስ
ክርስቶስ እንደሆነ ጸላዒ ዲያብሎስ ሹክ አላቸው
ዝንቱ ብእሲ ዘኢየዓቅብ ሰንበተ ኢኮነ እምእግዚ
አብሔር እንዲሉ አደረጋቸው ።

ወኮኑ ሎቱ አርድእት ብዙኃን እምነ አይሁድ ፤
ከአይሁድ ወገን ብዙ ደቀ መዛሙርት እንዳሉት
ሹክ አላቸው ፡ ናሁ ኵሉ ዓለም ተለዎ ድኀሬሁ ኢተ
አምሩኑ ከመ አልቦ ዘንበቍዕ እንዲሉ አደረጋቸው
ወእምከመ ተሰምዓ ዝ ግብር ከመዝ ይተልውዎ
አይሁድ ኵሎሙ በእንተ ዘርእዩ እምዕበየ ተአምራት
ዘላዕሌሁ ።

ተአምራቱ የታወቀ የተነገረ እንደሆነ በሥልጣኑ
ካደረገው ከተአምራቱ ብዛት ወገን ፡ እንድም ከፍ
ጹም ተአምራቱ ወገን ስለ እዩ መላው አይሁድ
እንዲያምኑበት ሹክ አላቸው ። ዝንቱ ብእሲ ብዙኀ
ተአምረ ይገብር ወእመ ኀደግናሁ ከመዝ ይመጽኡ
ሰብአ ሮሜ ወይነሥኡ ብሔረነ ወሕዝበክነኒ እንዲሉ
አደረጋቸው ።

ወኢትረከቡ ላዕሌሁ ጌጋየ ዓቢየ ዘእንበለ ዘተንግሩ
ለጲላጦስ መኰንን ።
ለጲላጦስ ከመንገር በቀር ለሞት የሚያበቃው ነገር
አታገኙበትም አላቸው ።
እስመ ዝንቱ ገብረ ዲቤሁ ዕርፈተ ላዕለ እግዚአብ
ሔር ወላዕለ ንጉሢ ።

ሰንበትን በመሻሩ ላይ እግዚአብሔር ነኝ ንጉሥ
ነኝ አለ ብላቸሁ ለጲላጦስ ከመንገር በቀር ለሞት
የሚያበቃ በደል አታገኙበትም ።
እስመ ውእቱ ይብል በ ጊዜ ከመ ወልደ
እግዚአብሔር ውእቱ ፤　　ወልደ እግዚአብሔር

ነኝ ይላልና ወልደ እግዚአብሔር ነኝ አለ ብላችሁ ፣ ወቦ ጊዜ ከመ ንጉሠ አይሁድ ውእቱ ።

የአይሁድ ንጉሥ ነኝ ይላልና የአይሁድ ንጉሥ ነኝ አለ ብላችሁ ፣ እንድም እየራሱ ለማውጣት ወልደ እግዚአብሔር እንደሆነ የሚናገርበት ጊዜ አለና እግዚአብሔር ነኝ አለ ብላችሁ ።
ንጉሥ እንደሆነ የሚናገርበት ጊዜ አለና ንጉሥ ነኝ አለ ብላችሁ ስቁማር ከመንገር በቀር ሌላ በደል አታገኙበትም ።
ወንሕነሰ አልብነ ንጉሥ ዘእንበለ ቄሣር ፤

ለኛስ ከቄሣር በቀር ያለቄሣር ሌላ ንጉሥ የለንም እንዲሉ አደረጋቸው ሐተታ እንዲሁም ባሉ ጊዜ በሥጋቸው ቄሣር በነፍሳቸው ዲያብሎስ ሰልጥኖባቸዋል ።
ወናሁ ፈታሕነ ላዕሌሁ በሞተ ስቅለት ።

ስቅሎ ስቅሎ እንዲሉ አደረጋቸው ።
ወተሰምዓ ነገር ከመ ጲላጦስ ተሰጥዎሙ በዘፈትሑ ቦቱ ላዕሌሁ ወእውሥኦሙ ለሊሁ በሥምረቱ ።
ስቅሎ ቢሉት ጲላጦስ ሊያድነው ወዶ ምንተ እኩየ ገብረ በዘይመውት ብሎ እንደመለሰላቸው ታውቋል ተነግሯል ።
ወመጠወ ነፍሶ ለሞት በፈቃዱ ኅሪት ከመ ይቤዝዎ ለአዳም እምሞት ።
አዳምን ከሞት ያድነው ዘንድ ባማረ በተወደደ ፈቃዱ ነፍሱን ከሥጋው ለየ ።
እስመ ሞትሰ እምደለዎ ለአዳም ስቁለ ዘበኃጣር ፣ ጩርቅ ታጥቆ ግንድ ተሸከሞ ተዋርዶ ተሰቅሎ መሞት ለአዳም በተገባው ነበር ። እንድም ተዋርዶ ተሰቅሎ መሞትስ ለአዳም በተገባው ነበር ታሪክ ሌላሳዕ መምሩን ኤልያስን ሸኝቶ የዮርዳኖስን ተሻግሮ ኢያሪኮ ገብቶ ሲያስተምር ሰው በዛ ጉባዔ ሰፋ ደቃ መዛሙርቱ ጸበበነ ማኅደር ንዑ ንግዝም ዕፀ ወንሕነፅ ካልዓ ማኅደረ ብለው ሄዱ እሱም መምህረ ትሕትና ነውና አብሯቸው ሄደ በዮርዳኖስ ዳር ሲቆርጡ ወተነጽላ ማኅጼሁ ወቦአ ውስተ ማይ እንዲል ከዛቢያው ወልቆ ብረቱ ከውኃ ገባ ወዝኒ ኀቡይ እግዚእየ ፣ ጌታዬ ይህም የተውሶ ጠፋ ተጨርሶ አለው ፣ የገባበትን አሳየኝ አለው አሳየው ቅርፍት ዕፀ ቀርፎ እመሳቅሎ ከውኃው ላይ ቢጥለው የማይዘግጠው ቅርፍት ዘግጦ የዘገጠውን ብረት ይዞት ወጥቷል ። እንደዚህም ሁሉ ሕማም ሞት የማይገባው ጌታ ሙቶ ሞት የሚገባው አዳምን የማዳኑ ምሳሌ ጥምቀትም የሞቱ ምሳሌ ነውና ።

በእንተ ዘተዓደወ ትእዛዘ ፈጣሪሁ ።
ከፈጣሪው ትእዛዝ ስለወጣ ፣
ወኮነ ቀታሌ ርእሱ ።
ራሱን እጥፊ ስለሆነ ።
እስመ በፈቃዱ አስተዳለወ ሞተ ለርእሱ

ወዶ ራሱን እጥፊ ሁኑዋልና ፣ እንድም ራሱን ለመጉዳት ሞትን አስፈርዷልና ።

መዘዕውቅስ ለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ኢኮነ ምጽአቱ ወተሠግዎቱ ዘእንበለ ከመ ይፈጽም ዘረከቦ ለአዳም ።
ጌታተን ኢየሱስ ክርስቶስ ሰው መሆኑ አዳምን ያገኘውን ነገር ለመፈጸም ነው ለሌላ እንዳይደለ የሚያስታውቅ የሚያስረዳ ነገር ፤

በጽድቁሰኬ አምጽአ ሞተ ላዕለ ርእሱ ዘድልው ላዕለ አዳም ።
በአዳም የተፈረደ ሞትን በራሱ አደረገው ።
ወተወከፎ እንከ ውስተ ሥጋሁ ።
በሥጋው ተቀበለው ።
ዘውእቱ ጠቢእቱ ፤
ያውም ጭከናው ነው ፣ ዘውእቱ ጠባይዒሁ ይላል ባሕርዩ በሚሆን በሥጋ ተቀበለው ።
አበከ ቤዘዎ እሞት ፤
አዳምን ከሞት እስኪያድነው ፤

ከመ ይከሥት ለነ በውእቱ ፍኖተ ትሩፋት ፤
በዚህ የትሩፋትን ሥራ ይገልጽልን ዘንድ ።
እስመ ውእቱ መጠወ ነፍሶ ለሞት እምድኅረ ተመከሮቱ ውስተ ዓውደ ምኵናን ።

እሱ ባደባባይ በመከራ ከተፈተነ በኋላ ተሰቅሎ ነፍሱን ከሥጋው ለይቷልና ።

ወኢተረከበ ሎቱ ጌጋይ ወኢነውር ለዘይትኬነን ቦቱ ፣
ነገር ግን ይሙት ብቃ በሚፈረድበት ገንዘብ ይፈረድበት ዘንድ ነውር በደል አልተገኘበትም ።
ወበእንተዝ ኮነ ጲላጦስ ሰማዕተ ።
ነውር በደል ስላልተገኘበት ጲላጦስ መሰከረ ።
ወይቤሎሙ ለሕዝብ እስመ ዝንቱ ብእሲ ንጹሕ ወጻድቅ ውእቱ ወኢተረከበ ላዕሌሁ ኃጢአት ።
ጻድቅ ንጹሕ ነውና ኃጢአት አልተገኘበትምና ።
ነሥአ ማየ ወተሐፅበ እደዊሁ ወይቤ ንጹሕ አነ እምደሙ ለዝ ብእሲ ጻድቅ ወኄር ።

ወይቤሎሙና ይቤ እንድ ወገን በዚህ ሰው ደም ከሚመጣ ፍዳ ንጹሕ ነኝ ብሎ ውኃ አስመጥቶ ባደባባይ ታፀበ ።
በከመ ሰምዓ ኮነ መጽሐፍ ።
ወንጌል ነሥአ ማየ ወተሐጽበ እደዊሁ ብሎ እንደ ተናገረ ፣ ታሪክ በእፅራኅ እስራኤል ልማድ ከሀገርና ከሀገር መካከል ሰው ሙቶ የተገኘ እንደሆነ ያ ሰው ለሞተበት ሰፍራ አቅራቢያ በሚሆን አገር ያሉ ሰዎች ውኃ በመንቀል ይዘው ጊደር ነድተው ከበረሃው ይወርዳሉ ፣ ቋንጃዋን ይመቷታል ትወድቃለች የዚህን ሰው ደም እኛ አላፈሰስነም ያፈሰሰውንም አላየንም ብለው ይታፀባሉ ከገዳዩ ወገን

ሲደርስ መወየብ ይጀምራል ከገዳዩ ሲደርስ ፈጽሞ ደም ይሆናል ። ምእመናንም ጥምቀትን ገንዘብ ማድ ረጋቸው መናገር ነው ።
ወሶበ ኮነ ከሃሌ ኵሉ ግብር በእንተ ተሠግ ዎቱ በፍጥረትነ ፈቀደ ሐሚመ ሀየንተ ከሂሎቱ ፤ ባሕርያትንን ስለ ተዋሐደ ሁሉንም ማድረግ የሚ ቻለው ቢሆን የከሃሊነቱ ለውጥ የከሃሲነቱ ፈንታ ከሃሊ ሲሆን ወዶ መከራውን ተቀበለ ።
ወተትሕተ ሀየንተ ልዕልናሁ ።

የልዕልናው ለውጥ ፡ የልዕልናው ፈንታ ልዑል ሲሆን ተዋረደ ።
ወሞተ ሀየንተ ኃይሉ ።
የኃያልነቱ ለውጥ ፡ የኃያልነቱ ፈንታ ኃያል ሲሆን ሞተ ወእርኅመ ማንሻ ። እንድም ከሃሊ ባለው ከሃሌ ይላል ባሕርያችንን ስለ ተዋሐደ ሁሉን ማድረግ የሚቻለው እሱ ወዶ መከራ ስለ ተቀበለ ስለተዋ ረደ ከሞተ ፤
ወእፎኑመ ንሕነ ምንዳን ወጽቡሳን ወምስኪናን ዘኢ ንትመሰል ቦቱ ፤
ምንዳን ጽቡሳን ምስኪናን የምንሆን እኛ በመከራ እሱን የማንመስል እንደምን ይሆን ።

ሶበሰ ኮነ እግዚእነ ሞፆ ለሰይጣን በኃይሉ መዋ ኢት እምኢኮነ መንከረ ።
ኮነ ያሰውን ሞፆ ብሎ አመጣው ሰይጣንን ጌታ ችን በአምላክነቱ ድል ነሥቶት ቢሆን ባልተደነ ቀም ነበር ።
ወእምኮነት ዘውስቴቱ ትሩፋት ዘኢሰብሕት ወዘኢ ውድስት ፤
ሥራው ያልከበረች ያልተመሠገነች በሆነች ነበር እንድም እምኢኮነት ዘስብሕት ባልተመሠገነችም ነበር ።
ትሩፋትሰ ስብሕት ዛቲ ይእቲ ፤
የምትመሠገንስ ትሩፋት ይህች ናት ፤
መዓት ላዕለ ዝንቱ ገጽ ምንክር እንግዳ ወዕጹብ ግብ ።

ፈጽሞ ድንቅ እንግዳ በሚሆን በሰውነቱ ሥራ ድል መንሣት ነው ።
ዘቦቱ ኮነ ፍኖት ሰፉረ ወልብው ።
ፍኖት ለኀበ አቡሁ እንቀጽ ዘመንገለ ወላዲሁ የሚ ባል ጌታ ሰው ሆኖ ባጭር ቁመት በጸባብ ደረት ተወሰኖ በታወቀበት በሰውነት ሥራ ድል መን ሣት ነው ፤
እስከ ኃሠሠ እምኔነ ለበዊዕ ውስተ ዝንቱ እንቀጽ ጽቡብ ።

ከኛ ወገን እንዱም አንዱ እያንዳንዱ ወደ ትሩ ፋት ለመግባት እስኪሻ ድረስ ፤
ወእቶሙ ውሑዳን እለ ይበውእ ውስቴታ ፤
ወደ ትሩፋት የሚገቡ ማለት ትሩፋት የሚሠሩ ጻድቃን ጥቂት ናቸውና ።
ወሶበ ፈቀደ ከመ ይመጡ ነፍሶ ለሞት በሥምረቱ ኅሩያዊት ፈቀደ እንከ ሰይጣን ሞቅሐታ በፍሥሐ ወበሐሤት ።
ባማረ በተወደደ ፈቃዱ ነፍሱን ከሥጋው ሲለይ በወደደ ጊዜ ሰይጣን ፈጽሞ ደስ ብሎት እቁራኛ ስሁ ብሎ ቀረበ ።

ወገሠጸ እግዚአብሔር ።
ወግድ ከኔ ፤ ከኔ ምን አለህ አለው ።
ወቀፈጸ ዘእምላዕሌሁ ምክዳን ።

ከአምላክነቱ ብርሃን ጥቂት ብልጭ አደረገለት ። ሒተታ በጸባብ መስኮት ብርሃን እንዲገባ ይላሉ ይህስ ይበዛል ብሎ የምጣድ ብልጭልጭታ ያህል ፤ ወርእየ ኃይላተ ሰማይ ድንጉጸነ በእውደ መስቀሉ ቅዱስ ።

መላእከትን በመስቀሉ ዙሪያ እንደ ሻሽ ተነጽፈው እንደ ቅጠል ረግፈው እንደ ግንድ ተረብርበው አየ ። እንድም ድኅናን ይላል አምላክን ክርስቶስ እያሉ ሲሰግዱ ሲወድቁ ሲነሡ አየ ።
ወተጠብለለ በሦዌ ፀዋግ ወፍርሃት ፍድፉድ ፤

በጽኑ ፍርሃት ተያዘ ።
ወተጠየቀ ከመ ወልደ እግዚአብሔር ውእቱ በእ ላንቱ ራእያት ።
ወቀፈጸ እምላዕሉ ምክዳነ ወርእየ ኃይላተ ሰማይ ድንጉጻነ በዓውደ መስቀሉ ባለው ነገር ወልደ እግ ዚአብሔር እንደሆነ አወቀ ተረዳ ።

ወእምሰምዐ እንተ ሰምዓ ኮነ አብ እምሰማይ በከሠተ እመ ጊዜ ጥምቀት በፈለገ ዮርዳኖስ በተጠመቀ ጊዜ አብ ከሰማይ መጽቶ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ በጉባዔ በዮርዳኖስ ከመሠከረለት ምስክርነት የተነሣ ፤
ወዓዲ በላዕለ ደብረ ታቦር ፤
ዳግመኛ በደብረ ታቦር ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ከመሠከረለት ምስክርነት የተነሣ ።
ወእምዝ ልህበ ልህበተ እምኔሁ ።

እቁራኛስሁ ብሎ ከመቅረቡ የተነሣ ፤ የባሕርይ ልጅ መሆኑን ከማወቁ የተነሣ መጋልን ጋለ መቀኩ ሰን ተኩሰ ፤
ወተረፈ ቅውመ ኀበ ውሣጤ ነፍሳት ዘኢይክል ያንቀሰቅል ፤
በእሳት ዛንጀር ታሥሮ በነፋስ አውታር ተይዞ ወዲ ያና ወዲህ ማለት የማይቻለው ሆኖ ቁሞ ቀረ ።
ወኮነት ምግባራቲሁ ኵላ ወተቃውሞቱ ዘምስለ እግዚእነ ሥዕልተ በቅድሜሁ ።
የሚሠራው ሥራ ሁሉ ከጌታ ጋራ የሚቃወመው መቃወም ሁሉ በፊቱ እንደ ሥዕል እንደ መስታ ዋት ተሥሎ ተቀርጾ ታየችው ።

ዘከመ ተቃውሞቱ አንተ ተቃወመ ወትዕግልተ
እንተ ተዓገለ ።

እንደ ተቃወመው መቃወም እንደ ቀማው ቅ ምያ
ያለ ።

እንዘ ያስተናትን ዘይመጽእ ኅዕሌሁ እመቅሠፍት
በእን ቲአሃ ።

ስለ ስድቡ ከመቅስፍት ወገን በሱ የሚመጸበትን
ሲያወጻ ሲያወርድ እንደ ትቢያ ያበነኝ እንደ ጢስ
ያተነኝ ይሆንን አያለ ።

ወሕምዝ ተዘከረ ክብራተ እንተ ኮነት ሎቱ ቀዳሚ
ምስለ መላእክት ።
ከዚሆ በኋላ ከመላእክት ጋራ ያደርጋት የነበረች ክብ
ሩን አሰበ ። ሐተታ ተቀብቷል ቢሉ የተመቸ
አልተቀባም ቢሉ ቢጸና ።

እስመ ውእቱ በሥምረቱ ጸነ እስከ ወድቀ ወኃደገ
ሎቱ እግዚአብሔር ሥልጣኖ እንቲአሁ ይግበር
ባቲ ዘፈቀደ ።

በሥምረቱ ብሎ ነበርና በምን ዐውቆ ትሉኝ እን
ደሆነ የወደደውን እንደ ወደደ ያደርግባት ዘንድ
በተፈጥሮ የተሰጣትውን ግዕዛንኑ አልነሣውም ።
ውውእቱ ከሃሊ በነሚእታ እምኔሁ ።
ግዕዛኑን ነስቶ እንደ ሥዕል እንደ እንስሳ ሊያደር
ገው የሚቻለው ሲሆን ።
ወምግባራቲሁ እንተ ቀደመት ኅዕሌሁ ዘምስለ አይ
ሁድ ።
በአይሁድ አድሮ ሲሠራው የነበረውን ሥራውን አስበ
ወተአግሦተ እግዚአብሔር ኅዕሌሁ ዘበእንቲአሃ።
ምንም ዘዘድለው እግዚአብሔር ታግሦት እግዚአ
ብሔር እቡን መታገሡን አስቦ ።
ወእስተዓበየ መጠነ ይፈድዮ ለወልደ እግዚአብሔር
ለወልደ እግዚአብሔር የሚከሰውን ካሳ አበላለጠ
ስማይ ወዘውስቴቱ ።
ሰማይ የኔ ገንዘብ ሁኖ በሰማይ ያሉ ፍጥረታትም
የኔ ገንዘቦተ ሁነው ፣ እንድም ከመ ሰማይ ወከመ
ዘውስቴቱ እንደዚሁ ሰማይ ያለ ሌላ ሰማይ ኑሮ
ያየኔ ገንዘብ ሁኖ በዚህ በማይ እንዳሉ ፍጥረታት
በዚያም ኑረው እኒያ የኔ ገንዘቦች ሁነው ።
ምድር ወዘዲቤሃ ፣
ምድር የኔ ገንዘብ ሁና በምድርም ያሉ ፍጥረታ
ትም የኔ ገንዘቦተ ሁነው ፣ እንድም ከመ ምድር
ወከመ ዘውስቴቱ ፣ እንደዚሁ ምድር ያለ ሌላ ምድር
ኑያ የኔ ገንዘብ ሁና በዚህ ምድር እንዳሉ ፍጥረታት
በዚያም ኑረው እኒያ የኔ ገንዘቦች ሁነው ።
ኢይከውኑ አምጣነ ቀዊሞቱ ቅድመ ጲላጦስ ቅጽ
በተ ዓይን ኀድግስ ዘኮነ ቅድመ ዝንቱ ወድኅሬሁኒ
ከዚህ አስቀድሞ ከእንግዲህም ወዲህ የሚደረገ
ውን ተወውና ዓይን ተከድኖ እስኪገለጽ ድረስ

በጲላጦስ ፊት ስላቆምሁት ካሣው ሊሆኑት አይበ
ቁም ብሎ አበላለጠ ።

ወሶበ አእመረ እግዚአብሔር ሕሊናሁ አቅለለ ሎቱ
ዕፀበ ወላህበ ።
እንዲህ ማለቱን እግዚአብሔር ባወቀ ጊዜ አስራ
ቱን አላላለት ግለቱን አቀዘቀዘለት ።
ከመ ይኩን ቀዊሞቱ በፍድየት ህየንተ ፈቃደ
ሥምረቱ ።

ወዶ ነፍሳትን አለቃለሁ ማለቱ በካሣ ይሆን ዘንድ
በግድ ቀማኝ እንዳይል ። እንድም ጌታ ስለ ወደደ
ለት እናወሩ በዚህ ዓለም ይሆን ዘንድ ።
ወሶበ ፈትሐ እማዕሰሩ ወጠፍአ ላህቡ ወቆመ
ቅድመ እግዚእነ እንዘ ይገርር ወይሰግድ ወያስተ
በቍዕ ።

አስራቱን ባላላለት ግለቱን ባቀዘቀዘለት ጊዜ እየተ
ገዛ እየሰገደ እየማለደ በጌታ ፊት ቆመ ።
ከመ ይዕትት እምኔሁ ሙስና ።
ጥፋቱ ይርቅለት ዘንድ ። እንድም ያእትት ይላል
ጥፋቱን ያርቅለት ዘንድ ።
ወያብሖ ለነቢር ውስተ ምድር ።
በዚህ ዓለም ለመኖር ያሰናብተው ዘንድ ።
ወያንሥእ እደ'ሁ እምነ እዳም ወዘርዑ ።
እሱም ቍራኝነት ከአዳም ከልጆቹ ያርቅ ዘንድ ።
እለ ተጋብኡ ውስተ ሞቅሕ በፈቃድ ዘእንበለ
አእምሮ ።

ሳያውቁ ወደው በሠሩት ኃጢአት ። እንድም በነቢብ
በገቢር ሳይሆን በሐልዮ በሠሩት ኃጢአት በቍ
ራኝነቱ ካሉ ከአዳም ልጆች ቍራኝነትን ያርቅ
ዘንድ ፤
ወተሠጥወ ስእለቶ ። ልመናውን ተቀበለው።
ወአዕረጎሙ እግዚአብሔር ለአዳም ወለዙሉ ዘርዑ
እምሲኦል ። አዳምን
ልጆቹን ከሲኦል ወደ ገነት አወጣቸው ሐተታ
ዲያብሎስም ፈጽመህ ካጠፋሽኝማ ያንተስ ጠላት
የኔስ ወዳጅ በምን ይታወቃል ከፈቃድህ የወጣ
ፍርፋሪ ለቅሜ ልኑር ብሎ ለምኖታል ።
ወአግብአ ኀበ ዘቀዳሚ ንብረቱ ውስተ ገነተ ፍግዓ
ተድላ ደስታ ወደሚያደርግበት ወደ ቀደመ ቦታው
ወደ ቀደመ ማዕርጉ መለሰው ።
ወእኀለፎሙ ለጻድቃን ምስሌሁ እምኃጕል፤
ጻድቃንን ከሱ ጋራ እንደሱ ከሲኦል አውጥቶ ገነት
አገባቸው ።
ኀበ ፍትሐ ጽድቅ ወርትዕ፣ ቀድሞ ፍትሐ
ጽድቅን ፍትሐ ርትዕን ወደሰሙባት ኋላ በፍትሐ
ጽድቅ በፍትሐ ርትዕ ወደ ወጡባት አገባቸው
ወኃደገሙ ለአኩያን ህየ ውስተ ትውክልና ፤
አኩያን ነፍሳትን ግን በሲኦል በቁራኝነት እንዳሉ
ተዋቸው ።

ምስለ መላእክቲሆሙ እስከ ዕለተ ደይን ፡
ከእለቆቻቸው ከአጋንንት ጋራ ፡ እንደዚሁም ከፈርዖን
ከሄሮድስ ጋራ እስከ ዕለተ ምጽአት ድረስ በሲኦል
ተቀቸው ።

ወእምድኅረዝ ተንሥአ እሙታን ከመ ይምሐረነ
ተንሥኦ ሥጋቴኒ እምድኅረ ሞት ።

አጋንንትን ድል ነሥቶ ነፍሳትን ከሲኦል አውጥቶ
ብት ካሣ ወልድ የኛን ትንሣኤ ያበረዳ ዘንድ
ተነሣ ።          ለግሀል ወለደይን ወለፍትሕ ፡
ግልጽ ፤ ለጻድቃን የሚደረገው ፡ ደይን በኃጥአን የሚ
ፈረደው ፡ ፍትሕ የወል ነው ።
መንገደ ሙቅተ ሰማያት ፤
ወተንሥአ ወአርገ ተን ዓረገ ፤

ከመ ያብዕ ለነ ዕርገተ ጻድቃን ንጹሐን እምድኅረ
ትንሣኤ ኅበ መንግሥት ዘድልው ሎሙ ።
ዕርገት እምድኅረ ትንሣኤ ፤ ከትንሣኤ በኋላ ጻድቃ
ቃን በሥጋም በመንፈስ በሥጋ በብርሃን ወደ ተዘጋጀ
ቸላቸው ወደ መንግሥተ ሰማያት መግባታቸውን
ያበረዳ ዘንድ ዓረገ ።
ወእምዝ ፈነወ ሎሙ መንፈስ ቅዱስ ።
ዓረገ ባሥረኛው ቀን መንፈስ ቅዱስን ሰደደላቸው
ከመ ንትመራሕ ቦቱ ኅበ ሐዊረ ፍኖት ፤
ወደ ትሩፋት ሥራ እንመራበት ዘንድ ማለት ትሩ
ፋት እንመራበት ዘንድ ።
እንተ ትመርሕ ኅበ ሕይወት ወመድኃኒት ፤

ፍኖት ላለው ወደ ደገኛው ልጅነት ወደ ትንሣኤ
ዘለክብር የምታደርስ እለ ፤ ፈነወ ላለው ዋዌ ፡ የዓረ
ፍትን ልጅነት ወደ ደገኛው ልጅነት የሚያደርስ
እለው ፤                    ወናሁ ተጠ
የቀ ወጸንዓ በቀዓተ ዝንቱ መጽሐፍ ንጹሕ ፡
ከፈታደ ሥጋ ንጹሕ የሚሆን የዚህ መጽሐፍ በቀ
ዓት በቀዓትነቱ ታወቀ ተረዳ ።
ውበዘን ተኃሥሶ መፍቅድ ኅበ አንብቦቱ ለዘከነ
ልብዎ ወማዕምረ ።

ብልሀ እስተዋይ የሆነ ደቀ መዝሙር ከተመለከተው
ዘንድ ልቡና የሚሻው ብዙ ምሥጢር አለበት ።

ስድስተኛ ጉባኤ ፤

መግለጡ ሥርዓት ፤
ምስተኛውን ሥርዓት ብለውታል ሥርዓት ይባላል
ወሥርዓት ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ፤
ክቡር የሚሆን የዚህ መጽሐፍ ሥርዓቱ ፤
ይእቲኬ አንብቦቱ በኵሉ ጊዜ ፡

ዘው ጊዜ በኵሉ ጊዜ ይላል ሁልጊዜ እሱን መመ
ልከት ነው እመኒ እንዘ ትነውም ወእመኒ እንዘ
ትነቅሕ እመኒ እንዘ ትነብር ወእመኒ እንዘ ትትና

ግእ እመኒ እንዘ ትቀውም ወእመኒ እንዘ ተሐ
ውር ኢትርሳዕ ተዘክሮተ እግዚአብሔር አምላክነ
በበኵሉ ጊዜ ወበኵሉ ሰዓት እንዲል ፡

ወኃዲገ ሕሊናት ለዓቂበ አቅማሪሁ ወተአምሪሁ ፡
ስንጠረዡን ቁራኛውን ለማወቅ ሕሊናትን ጨልጦ
ገርኝቶ መስጠት ነው ፡ እንድም መብል መጠጥን
መተው ነው፤እንድም ሕሊናትን፡ማጽናት ነው ኃዲ
ገነ ጥንተ ነገሩ እንዲል ፤

ወተአዝዞ ቦቱ ፡              በሱ ጸንቶ መኖር ነው
በጠይቆ ወበገቢር ወቀዊም በኵሉ ትእዛዛቲሁ ፡
በመረዳት ፡ በሥራ በትእዛዙ ሁሉ ጸንቶ መኖር ነው
በቃል ፡                              ባነጋገር፥
ወበምግባር ፡                          በሥራ ፡
ወተመያይጠ ኅበ ጽንዓቱ ፡

ከጸናም ዘንድ መላልሶ መመልከት ነው ፡ ለእመ
ረከብከ ቀለመ ጸዋግ ተመያየጥ ዐሥርተ ወክልኤተ
ጊዜያተ ወኢትፍቅድ ኃሊፈ ቀጽል እምኔሁ እን
ዲል ፡
ወምሳሌያቲሁ ዘምሱል ኅበ ትርጓሜያት ፡
የተመሰለውን ምሳሌውን ወደ ትርጓሜ ሲያፋልሱ
መኖር ነው ፤ እንድም ዘምሉስ ይላል አብነት ወደ
ትርጓሜ የተመለሰውን ምሳሌውን ማወቅ ነው ፡
ዘጽሕፍት ፡                         በብራና ፡
ወዕውቅት ፤               በልቡና ታውቃ ያለች
ወበውእቱኬ ይትበየን ለአንባቢ መሴልየ ኵሉ
ኃይለ ቃሉ ፤

በዚህም ለተመልካች ደቀ መዝሙር የነገሩ ምሥጢር
ብልት ብልቱ ይታወቃልና ስለዚህ ነው ፡ እንድም
ምሊላየ ኵሉ ኃይለ ቃሉ ይላል የነገሩ ምሥ
ጢር መለያያ መለያያው ይታወቃልና ስለዚህ ነው
በብሩሀ ብያኔ ፡              በኅላ በተረዳ መለየት
ወይነሥእ በእስተብዮቀ ጥይቅና ወተፍጻሜተ ዘሀሉ
ውስቴቱ ፡

በሱዋ ያለውን በመመልከት ዕውቀትን በመረዳት
ገንዘብ ያደርጋልና ስለዚህ ነው ፤
እስከ ደኅሪት ነገር ፡
ኅብዕ አርእስተ ነገር ያለው እስኪፈጸም ድረስ እን
ድም መላው እስኪፈጸም ድረስ ።
ወናሁ ተጠየቀ ሥርዓቱ ፡

የዚህ መጽሐፍ ሥርዓቱ ታወቀ ተረዳ ፤ እንድም
ወጸንዓት ንበቱ ይላል እሱን በመመልከት ጸንቶ
የመኖሩ መጽናት ታወቀ ተረዳ ወጸንዓት ንብረቱ
ይላል እሱን በመመልከት መኖሩ ታወቀ ተረዳ ፤
ወራብው ትእምርት ፡
አራተኛውን ስም ብለውታል ስም ይባላል ስምዮቱ
ትእምርት ይላል ፡
ወትእምርተ ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ወንጌል ።

ክቡር የሚሆን የዚህ መጽሐፍ ስሙ ወንጌል ነው
ወንጌል ብሂል በልሳነ ጽርእ ወትርጓሜሁ ስብከት
ወንጌል ማለት በጽርእ ቋንቋ ብሥራት ስብከት
ማለት ነው ።
እስመ ተሰብከ ውእቱ

ወልደ እግዚአብሔር እንደነገሠ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ እንደጠፋ ተናግራለችና ወንጌለ መንግሥት እንዲል ወደ ግእዝ ቢመልሱት ወንጌል ማለት ስብከተ ማለት ነው እለ ።

በእንተ ትስብእተ ቃለ እግዚአብሔር በዘመድነ
በኛ ባሕርይ ቃለ እግዚአብሔር ሰው መሆኑን ተና
ግሯልና  እንድም ሰው መሆኑ ተነግሮበታልና
ወኀድረተ መንፈስ ቅዱስ ላዕሌነ ወውስቴትነ ፥
መንፈስ ቅዱስ በኛ ማደሩን ተናግሯልና ። እንድም
መንፈስ ቅዱስ በኛ ማደሩ ተነግሮበታልና ። ላዕሌነ
ወውስቴትነ ማለቱ በነፍስ በሥጋ ሲል ይደጋግመዋል
ዓዲ ይቤ ዛቲ ብሥራት እንተ ባቲ ደሰዎሙ ለውሉደ
ሰብእ ከመ ይኩኑ ታቦተ ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር ማደሪያ ለመሆን ምእመናን የነቁ
በት የተጉባት ወንጌል ደግ ሕግ ናት ።
ወማኀደረ መቅደሱ ። ልዩ ማደሪያው ይሆኑ ዘንድ
ወኮነ ሎሙ ዘይበዝኅ ክብር በክብረ ዝንቱ ዕበይ ።
በወንጌል ደገኛ ፍጹም ክብር ተሰጣቸው ።
አ ለዝንቱ ክብር ዓቢይ ወኂሩት ዘአንበለ መሥፈ
ርት ።

ፍጹም የሚሆን ይህ ክብር ልክ መጠን ወሰን ድን
በርየሌለው ቸርነቱ ምን ይረቅ ምን ይጠልቅ አ ወዮ
እንደምን ያለ ረቂቅ ነው ። እንድም ፍጹም ለሚሆን
ለዚያ ክብር ወሰን ድንበር ስሌለው ለቸርነቱ እንክሮ
ይገባል ።
ወዜነወነ ካዕበ ተማህሎተ እግዚአብሔር ልዑል ለደ
ቂቀ ዕጓለ እመሕያው ።
ልዑል እግዚአብሔር እኛን ይቅር ማለቱን ነግሮና
ልና ።
ወሰርየ ጌጋይ ።
ተኃድገ ለከ ኃጢአትከ ተኃድገ ለኪ ኃጢአትኪ
ማለትን ።
ወአብጥሎ ኵነኔያት ።

ኢትጥዓም ኢትልክፍን ኢትግሥሥን ማሳለፉን ።
ወሰቢረ ሦከ መስሐቲ ጸላዒ ።
ዲያብሎስ የሚያሠራቸው እኩያት ፍትወታት ኃጣ
ውእን ድል መንሣቱን ።
ወድከሞተ ትዝሀርቱ ።
ዲያብሎስን በምስቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል መን
ሣቱን ነግሮናልና ።
ወዓዲ ዘበቍዓነ ቦቱ በጸውዖትነ ውሉደ ፤
በጸውዖቱ ውሉደ ብሎ ውሉድ እኛን በመጥራቱ
እኛን የጠቀመንን ጥቅም ነግሮናልና  እንድም

ውሉድ ይላል ውሉድ እኛ እሱን በመጥራታችን የጠ
ቀምነውን ጥቅም ነግሮናልና ።
ወፍግዓ ዘድልው ለነ ውስተ መንግሥተ ሰማያት
ወሕይወት ለዝሉፉ ።

በማያልፍ ሕይወት በመንግሥተ ሰማያት ተዘጋጅቶ
ልን ያለ ተድላችንን ነግሮናልና ፤ ወሕይወተ ይላል
ፍግዓ ላለው ። በመንግሥተ ሰማያት ተዘጋጅቶልን
ያለ ተድላችንን የማያልፍ ሕይወታችንን ነግሮናልና
ስለዚህ ነው ።
ወናሁ ተበየነ ትእምርቱ ።
እነሆ ስሙ ታወቀ ተረዳ ፤
ወምክንያተ ስሙ ።
ወንጌል የተባለበትም ምክንያት ታወቀ ተረዳ ።

ወኃምስ መሠረት ፤ እምስተኛውን
መሠረት ብለውታል መሠረት ይባላል ። እምእይቱ
ይላል አብነት ፤
ወመሠረተ ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ፤
ክቡር የሚሆን የዚህ መጽሐፍ መሠረቱ መሠረትነቱ
በኀበ እግዚአብሔር ዓቢይ ወ እዚዝ ።
ዓቢይ እዚዝ የሚሆን እግዚአብሔር ነው ።
ወኮኑ ሎቱ ፬ቱ ጸሐፍት ፤
አራት ጸሐፍት አሉት ፤
፪ቱ እምኔሆሙ ዘእምሐዋርያት ፲፪ቱ ወ፪ቱ እለ ኃረ
ዮሙ እግዚእነ እምዙሉ አርድእት ወሰመዮሙ ሐዋ
ርያት ፤
ከአራቱ ሁለቱ ከአምስት ገቢያ ሰው መርጦ ክሾማ
ቸው ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ወገን ናቸው ፥
ወውእቶሙ ማቴዎስ ወዮሐንስ ፤
ሁለት የተባሉትም ማቴዎስ ዮሐንስ ናቸው ፤
ወ፪ቱ እምኔሆሙ እምአርድእት ማርቆስ ወውእቱ
ዘኮነ ረድአ ለጴጥሮስ ፥

ከሁለቱ አንዱ የጴጥሮስ ደቀ መዝሙር ማርቆስ ነው
ወካልኡ ሉቃስ ወውእቱኒ ዘኮነ ረድአ ለጳውሎስ ፤
ከሁለቱ አንዱ የጳውሎስ ደቀ መዝሙር ሉቃስ ነው
ወጸሐፉ እንከ ወ ስተ ኵሉ አህጉር ርኁቃት ፥

በቦታ ተለያይተው በርኁቃት አህጉር ጻፉ ። ሐተታ
ማቴዎስ በፍልስጥኤም ጀምሮ በህንድ ይጨርሰዋል
ወጠና በፍልስጥኤም ወፈጸማ በህንድ እንዲል
ማርቆስ በግብጽ በሮምም ይላል ሉቃስ በመቄዶንያ
ዮሐንስ በኤፌሶን ሁነው ጽፈዋል ፤
ወበአዝማን ውሉጣት ፥
በልዩ አዝማን ጻፉ ፤ ሐተታ ማቴዎስ ጌታ ካረገ
ስምንተኛው ተፈጽሞ ዘጠነኛው ሲጀመር ቀላው
ዴዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዘመን ፤ ማር
ቆስ ጌታ ካረገ ዐሥራ እንደኛው ተፈጽሞ ዐሥራ
ሁለተኛው ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ
ባራተኛው ዘመን ፤ ሉቃስ ጌታ ካረገ ሀያ አንድ ተፈ
ጽሞ ሀያ ሁለተኛው ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር

በነገሠ ባሥራ አራተኛው ዘመን፤ ዮሐንስ ጌታ ካረገ በሠላሳ በሠላሳ አምስትም ይላል ፤ ኔሮን ቄሣር በነገሠ በሰባት በስምንትም ይላል ። ሰባት ቢሉ ሲፈጽም ስምንት ቢሉ ሲጀመር ፤

ወጸሐፉ በልሳን ዘዘዚአሁ ፤　　ልዩ ልዩ በሚሆን ቋንቋ ጻፉ ፤ ሐተታ ማቴዎስ በዕብራይስጥ ፤ ማርቆስ በሮማይስጥ ሉቃስና ዮሐንስ በዮናኒ ፤ ዮሐንስን ለይቶ በልሳነ አርእ የሚል አብነት ይገኛል እንደ [illegible] እንደ [illegible] ጥቂት ጥቂት የልሳን መለያየት [illegible] ውስተ ፍጻሜ አሐዱ ፤
[illegible] የነገራቸው ምሥጢር ፩ ሆነ [illegible] ፤
[illegible] ነገር [illegible] ነው ።
[illegible] ፤

[illegible] እንድ [illegible] ወንጌል ደገ ሕገናት ፤
[illegible] ወንጌል [illegible] ተነገረች ፤

[illegible] ፤　　በብራና ተጻፈች
[illegible] ፤　　በልቡና ተቀረጸች
[illegible] ተወልዶ ወተሌልዮ ፤
ጥቂት ጥቂት ከመለወጥ ከመለየት በቀር ጥቂት መለወጥ መለየት ሳይቀር አንድም እንደ ማቴዎስ እንደ ማርቆስ መለየት መለወጥ ሳይኖር ያለመለወጥ ያለመለየት ፤
[illegible] ነበረ መሠረቱ ኀበ ባዕሉ ፤

[illegible] ባለቤቱ እንደሆነ እነሆ ታወቀ ተረዳ ፤
[illegible] ፤　　አራት ጸሐፍት እንዳሏት ታወቀ ተረዳ ተነገረ ፤
[illegible] ምስግክ ፤
[illegible] ምስማክ ብለውታል ምስማክ ይባላል [illegible] ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ፤
[illegible] የሚሆን የዚህ መጽሐፍ መከዳነቱ ፤

[illegible] ለአይ ግብር ይሜኒ ወለአይ ገጽ እመክፈ [illegible] ዘይፈቅድ ልብ ወየኃሪ ።
[illegible] ጥበብ እድል ወገን ከሥራ ክማናቸ [illegible] ክነገር በማናቸውም ነገር ይመች እንደሆነ [illegible] ምስግክ ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ወፈቂዶቱ [illegible] ኀበ ተጠብቦተ ልብ ፤

[illegible] የሚሆን የዚህ መጽሐፍ መከዳነቱ እሱን መ[illegible] ልቡናን ወደማራቀቅ ያደርሳልና ስለዚህ ነው [illegible] ማኅበረት ሉዓላዊ ወአስተጋብእ በተ[illegible] ዘበውስቴታ ይበጽሕ ኀበ በቀ[illegible] ።
[illegible] እዝናት በእሷ ያለውን በመመልከት ወደ [illegible] ያደርሳልና ስለዚህ ነው ።
[illegible] ውስቴታ ምልአተ ወተፍጻሚተ [illegible] ደቀ [illegible] ዕውቀትን መረዳትን ገንዘብ ያደርጋልና ስለዚህ ነው ። አንድም ይትፈቀድ በሷ ያለ ዕውቀት መረዳት ይገኛልና ስለዚህ ነው ።
ወውእቱ እስመ ነገር እምላካዊ አመ ነሚእቱ ወአፍልሶቱ በሕሊና ሠናይ ይፈልስ ውስተ ነፍሳት ንጹሐን እሙን ልባዌ ኀበ ተወክፎ ።
እሱም እምላክ ያስተማረው የአምላክን ነገር የሚናገር ወንጌል መሆኑ እበሳበታለሁ እጠግበታለሁ ሳይል በሚያስተምርበት ጊዜ ደቀ መዝሙር እሾም በታለሁ እሸለምበታለሁ እከብርበታለሁ ሳይል በሚማርበት ጊዜ መምር እንዳያውቅ ከመሆን ደቀመዝሙር እንዲያውቅ ወደመሆን ደርሶ ይገልጻልና አንድም እምነ ለባዊ ኀበ ተወካፊ ከአስተዋይ መምር ወደብልህ ደቀመዝሙር ደርሶ በንጹሐት ነፍሳት አድሮ ይኖራልና ስለዚህ ነው ።
ወይመርቅ ውስቴትነ ሥርቀተ እስከ ይቀውም ውስቴትነ እምነ እርእያ እግዚአብሔር ቆመተ ዘበአማን ከአርአያ እግዚአብሔር አስጥቶ በኛ ዘንድ ፈጽሞ እስኪረዳ በኛ ሥገለጽን ይገለጻልና ስለዚህ ነው ። በአስተርክቦ ልቡናዊት ፤

ልቡናን አንድ በማድረግ በአስተርክቦ ልቡና ይላል ሕሊናን አንድ በማድረግ ።

ዘውእቱ ሊቀ ኵሉ ትሩፋት ፤　　ይኸውም የትሩፋት አበጋዝ የሚሆን ሕሊና ነው ።
ወሶበ ኮነ ውእቱ ክማሁ ኮነ እንከ ንሕነኒ ድልዋነ ለነሚአ መንፈስ ቅዱስ በረድኤት እምላካዊት ወበእንተ ዝንቱ ይደሉ ላዕሌነ ንብረት ለዝሉፉ በንጽሕና ወበኂሩት ።
እንዲህ ከሆነ ከአምላክ ዘንድ በሚገኝ ረድኤት መንፈስ ቅዱስን ለመቀበል ነቅተን ተግተን ስለዚህ በንጽሕና ጸንቶ መኖር ይገባናል ።
እንተ ባቲ ኮነ ድልዋነ ለተመጥዎ ሕግ እምላካዊ ወመንፈሳዊ ፤　　አምላክ ያስተማረውን መንፈስ ቅዱስ ያጻፈውን ሕግ ለመቀበል በበቃንበት በረድኤት እምላካዊት ኮነ ድልዋነ ለመንፈስ ቅዱስ ፤ ዘቦቱ ኮሉ ነበበ በልሳን ዘዘዚአሁ ውስተ ኵሉ አጽናፈ ዓለም ፤
ሰው ሁሉ በሰባ አንድ ቋንቋ በአራቱ ማዕዘን የተናገረበት ብሎ ለሕግ ቀጸለ አንድም በአራቱ ማዕዘን ያለ ሰውን ሁሉ በሰባ ሁለት ቋንቋ ያናገረው በተሰፋ መንፈስ ቅዱስ ።
በተሰፋ መንፈስ ቅዱስ በሀብተ መንፈስ ቅዱስ በፍተ መንፈስ ቅዱስ ይላል አብነት በመንፈስ ቅዱስ አጋዥነት ፤ ዓዲ እንቅሐነ ፈጣሪ ኀበ አእምሮ ቅድምናሁ ወተድኅሮቱ ።
ዳግመኛ ፈጣሪ ቀዳማዊነቱን ደኃራዊነቱን ወደ ማወቅ አነቃቃን ።
ይትባረክ ወይትለዓል ፤　　ይክበር ይመስገን በልብ መታሰቡ በቃል መነገሩ ከፍ ከፍ ይበልና ፤ ወኀበ ልሒኮተ ፍጥረቱ መንክር ።

ድንቅ የሚሆን ፍጥረቱን በልጅነት ማደሱን ወደ ማወቅ እነቃቃን ።
ወተከሥቶ ልቡና ጥበቡ ልዕልት ወብርህት ፤

ልዕልት ብርሀት የምትሆን የሥጋዌን ዕውቀት መገ ለጽን ወደማወቅ እነቃቃን ፤
ወናሁ ተከሥተ ምስማከ ዝንቱ መጽሐፍ ፤
እነሆ የዚህ መጽሐፍ መከዳንቱ ታወቀ ተረዳ ፤
ለአይ ገጽ ወለአይ ግብር ይኄይስ
ከሥራ ብማናቸውም ሥራ ከነገር በማናቸውም ነገር ይመች እንደሆነ ።

## ስባተኛ ጉባኤ

ወሳብዕ አርእስተ ነገር ፤
ሰባተኛውን ክፍለ ነገር ብለውታል ክፍለ ነገር ይባላል
ወአርእስተ ነገረ ዝንቱ መጽሐፍ ክቡር ፤
ክቡር የሚሆን የዚህ መጽሐፍ የነገሩ ክፍል ፤
እስመ ይእቲ ብይንት፤ የተለየች ናትና
ወውስቴታ ብያኔ ክሡት ፤

በዪም የጎላ የተረዳ መለየት አለና ስለዚህ ነው
በቃል ፤ በነገር ፤ ወበገቢር፤ በሥራ
ሁለት አርእስት ተናገረ ። ለሁለቱም ያመጣል ፤
ቢቃልሰ እስመ ይእቲ ትነግር በኢንተ ልደቱ ለእግ ዚእን ወመድኃኒነ እምእግዝእትነ ማርያም ድንግል ንጽሕት ወአንሶስዎቱ ውስተ ዓለም ፤
በቃል ያልሁት ንጽሕት ንዕድት ክብርት ከምትሆን ከመቤታችን መወለዱን በዚህ ዓለም ፴ ሦስት ዓመት ከአራት ወር ከዐሥር ቀን መኖሩን ትናገራለችና ስለዚህ ነው ።
ወትኤዝዝ ኀበ ምግባራት ንጹሐት ወመሥመርያት ንጹሐት መሥመርያት የሚሆኑ ምግባራትን ታዛ ለትና ስለዚህ ነው ፤
ወታሌቡ ዓዲ በጥይቅና ተስፋ በውሂበ ሕይወት ፤
ዘለዓለም ዘድልው እምነ ሠናያት ደኃርያት ፤
ዳግመኛ በኋላ ዘመን ከሚገኝ ከበጐ ነገር ወገን ተዘ ጋጅቶ ያለውን የማያልፈውን ድኅነት በመስጠት የተስፋውን መረዳት ታስረዳዋለችና ስለዚህ ነው።
ወታዜክር ፈሪሃ ዘነኔ ወበቀል ዘበጽድቅ ፤
በእውነት የሚደረግ ፈሪሃ ዘነኔን ፈሪሃ በቀልን ታሳ ስባለችና ስለዚህ ነው ፤
በአምግን ምግባራተ ሃይማኖት ፤
በሚሠሩት ሥራ መጠን ፤
ወአንቀስቅሶ ውስተ ዓለም ኃላፊ ፤
ልብሰ አንጽቶ ሠናፊልን እንስርቶ አምሞ ጠም ጥሞ መንደር ለመንደር በመዞር መጠን ፤
ወፈቂድ ኀበ ነገር እኩይ ፤
ከፉ ነገርን በመውደድ ታዜክር እንድም ከፉ ነገ ርን በመውደድ መጠን ፤
ወሕሊናት ርኩሳት ፤
ጉዳት ያለበትን ነገር በመውደድ መጠን ፤

ወቃላተ ጕሕሉት ፤
ከዳት ተንኮል ያለበትን ነገር በመውደድ መጠን ታዜክር ፤
እስከ ተፍጻሜተ ዝንቱ ፤
ሳብዕ አርእስተ ነገር ያለው እስኪፈጸም ፤
ወኀበ ማኅለቅቱ ፤ መላው እስኪፈጸም
ወበገቢርሰ እስመ ለለ፩ዱ እምሰባክያን ክፈለ ምዕ ራፈ ዚአሁ እምዕራፈ ካልኡ ፤

ቃል ላለው ጨርሶ ገቢር ላለው አመጣ ፤ በገቢር ያል ሁት ከአራቱ ወንጌላውያን እንዱም አንዱ እያለ አንዱም አንዱ ከባልንጀራው ምዕራፍ የራሱን ለይ ቷልና ፤

እምነ ፍኖት ነዊህ ወኅጺር ፤
ረጅሙን ከረጅም አጭሩን ካጭር ፤ እንድም ረጅ ሙን ካጭር አጭሩን ከረጅም ።
ዘእንበለ ኃይለ ቃል ፤

ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ካለው በቀር በዚህ አይለያዩም
ወተአምራት ፤ በረከተ ኅብስትን ፤
ወስምዓት ፤ ጾራ ፤
ወትእዛዛት ፤ አንስ እብለክሙ ፤
ወምሳሌያት ፤ ምሳሌ ዘርዕ ከነዚህ በቀር
ወፈቃደ ኵሎሙ ዘበውስቴታ ፩ እሙንቱ ፤

በሱዋ ያለ የሁሉ ፈቃድ አንድ ነው ። እንድም ፈቂድ ዘበውስቴታ በሱዋ ያለውን በመሻት ሁሉ አንድ ናችው ።

ኁልቈ አርእስት ነገራት ዘ፬ቱ ወንጌላት ሰባክያን በዘናመጽእ በክፈለ ምዕራፋተ ኃይለ ቃል ፤
የአራቱን ወንጌል የዓቢይ ምዕራፍ ቍጥር የነገ ሩን ምስጢር ምዕራፍ በመክፈል ጊዜ በምናመጣው አለ ። እንድም ክፍለን ክፍለን በምናመጣው አለ ።
ወኵሉ ነገር እምኔሆን ውስተ ቀዳሚሃ

ዓቢይ ምዕራፍ በመጀመሪያው ነው ያውም በሚ መጣው ነው ፤ ንኡስ ምዕራፍ ቀጥሎ በሚመጣው ነው ለሁለቱ ሁሉ ፤
ብያኔ ሮማዊ ፪፻፲ወ፬ አርእስት ፤
ሮማዊ ቍጥር ሮማዊ አቈጣጠር ሁለት መቶ ዐሥራ ዘጠን አርእስት ነው ፤
ማቴዎስ ፷ወ፰ አርእስት ፤
ማቴዎስ ስሳ ስምንት አርእስት ነው ፤
ማርቆስ ፵ወ፰ አርእስት ፤
ማርቆስ አርባ ስምንት አርእስት ነው ፤ ስሳና አርባ መቶ ስምንትና ስምንት ዐሥራ ስድስት ነው ፤ ዐሥራ ስድስትን ይዘህ ሂድ ።
ሉቃስ ፹ወ፫ አርእስት ።
ሉቃስ ሰማንያ ሦስት አርእስት ነው ፤ አሥራ ስድ ስትና ሦስት ዐሥራ ዘጠኝ ።
ዮሐንስ ፳ አርእስት ።

ዮሐንስ ሃያ አርእስት ነው ። ሃያን ከሰማን ያላይ ብትደርበው መቶ ይሆናል ። ሁለት መቶ ዐሥራ ዘጠኝ ያለው ይህ ነው ።

ኍልቈ አርእስት ንኡሳን አንተ ተሠርዓ አቅማር እንበይነ ዚአሃ ዘአንበርዋ አበው ቅዱሳን አሞንዮስ ወአውሳብዮስ በረከተ ጸሎቶሙ የሃሉ ምስሌነ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ልመናቸው ክብራቸው ይደርብንና አበው ቅዱሳን ሐዋርያት የተናገሯት አሞንዮስ አውሳብዮስ የጸፏት ሰሌዳ ሰንጠረዥ የተጻፈላት ፡ እንድም አበው ቅዱሳን አሞንዮስ አውሳብዮስ አድርግ ፡ አበው ቅዱሳን አሞንዮስ አውሳብዮስ የጸፏት ሰሌዳ የጻፉላት ሰንጠረዥ የተጻፈላት የንኡስ ምዕራፍ ቍጥር ፲፻ ወ፩፻ ፳ ወ፩ አርእስት ፡ ሺህ መቶ ስሳ አምስት ነው ።

ማቴዎስ ፫፻ ፶ ወ፭ አርእስት ፡

ማቴዎስ ሦስት መቶ አምሳ አምስት ነው ። አምስት ባለው ስድስት ይላል ከውስጥ አግብቶ ሲዘራው አምስት ያለ እንደሆነ አንድ ወገን አድርጎ ስድስት ያለ እንደሆነ የመጨረሻውን ምዕራፍ ከሁለት ከፍሎ ነው ።

ማርቆስ ፪፻ ፷ ወ፮ አርእስት ፡

ማርቆስ ሁለት መቶ ሠላሳ ስድስት አርእስት ነው ሦስት መቶና ሁለት መቶ አምስት መቶ ፡ አምሳ ሠላሳና ሰማንያ አምስትና ስድስት ዐሥራ አንድ ።

ሉቃስ ፫፻ ፵ ወ፪ አርእስት ፡

ሉቃስ ሦስት መቶ አርባ ሁለት አርእስት ነው ። አምስት መቶና ሦስት መቶ ስምንት መቶ ከአርባው ዐሥሩን ነሥተህ ከዘጠና ላይ ስትደርበው መቶ ይሆናል ። ዘጠኝ መቶ ሠላሳ ሦስት ቢል ።

ዮሐንስ ፪፻ ፴ ወ፪ አርእስት ።

ዮሐንስ ሁለት መቶ ሠላሳ ሁለት አርእስት ነው ፤ ሺህ ከመቶ ይሟል ሠላሳና ሠላሳው ስሳ ነው ፡ ሁለትና ሦስት አምስት ነው መላው ሺህ ሦስት መቶ ስሳ አምስት ነው ።

ወኍልቈ ምዕራፋት ዓበይት በመጽሐፈ ቀብጥ ፡ የዓቢይ ምዕራፍ ቍጥር በቅብጥ አቈጣጠር ። ሐተታ ቋንቋው ቅብጥ ነውና በመጽሐፈ ቅብጥ አለ ፡ አኝ ድም የገ የጸ ጸያፍ አለባቸውና ግብጽ ሲሉ ቅብጥ ይላሉ ፤ በግብጻውያን አቈጣጠር ።

፪፻ ፹ ወ፮ ምዕራፍ ።

ሁለት መቶ ሰማንያ ስድስት ምዕራፍ ነው ።

ማቴዎስ ፻ ወ ፩ ምዕራፍ ፡

ማቴዎስ መቶ አንድ ምዕራፍ ነው ፡

ማርቆስ ፶ ወ ፬ ምዕራፍ ፡

ማርቆስ አምሳ አራት ምዕራፍ ነው ።

ሉቃስ ፹ ወ፮ ምዕራፍ ፡

ሉቃስ በማንያ ስድስት ምዕራፍ ነው ።

ዮሐንስ ፵ ወ ፭ ምዕራፍ ፡

ዮሐንስ አርባ አምስት ምዕራፍ ነው ፡ ሐተታ አንድና አራት አምስት አምስትና አምስት ዐሥር ። አርባና አምሳ ዘጠና ፡ ዐሥሩን ከዘጠና ብትደርበው መቶ ይሆናል ። ሉቃስ አዳለው ። ሁለት መቶ ሰማንያ ስድስት ያለው ይህ ነው ።

ወሶበ አንከ ዘከርነ በእምጣንነ ዘበጽሐት ኀቤሁ ክሂል እምእሔድሮ ውስተ መጽሐፍ እስትጕቡዕ ጓቱ አንተ አቅደምናሃ ቀዲሙ ንቅትለኬኒያሃበከመ ሠርዑ አበው አሞንዮስ ወአውሳብዮስ እምአቅሚራት በተሰጠችን አእምሯችን በደረሰችበት መጠን አስቀድመን በተናገርነው በሰባቱ ክፍል የተሰበሰበውን በማሳጠር አሳጥረን ከተናገርን በኋላ ኪዚያ ኪያሐ አሞንዮስ አውሳብዮስ እንደጻፉ አሥሩን ቀመረ ፤ ሰንጠረዥ እንጻፍ ።

በዚህ መጽሐፍ ግን ንኡስ ምዕራፍ ፩፻ ፲፩ ነው ። ማለት ፡ ማቴዎስ ፻፳፮፤ ማርቆስ ፹፮ ፡ ሉቃስ ፻፴፩ ። ዮሐንስ ፳ ፤ ዓቢይ ምዕራፍ ደግሞ ፹፱ ነው ። ማለት ማቴዎስ ፳፰ ፡ ማርቆስ ፡ ፲፮ ። ሉቃስ ፳፬ ። ዮሐንስ ፳፩ ነው ።

በእንተ አኀብሮ ዘአርባዕቱ ወንጌላት ቅዱሳት ። የአራቱ ወንጌላውያንን ነገር ለማስተባበር ። ወረሰይዋ በማኅለቅት ።

ሳብዕ አርእስተ ነገር ያለው ሲፈጸም አደረጓት ። በመትልወ ኀብረተ ቃሎሙ ።

የዘራቸውን አንድነት ቀጽሎ ቀጽሎ በመጻፍ አደረጉት ፤ ሐተታ በመጀመሪያው አራቱ የተባበሩበትን በሁለተኛው ሦስቱ በሦስተኛው ሦስቱ የተባበሩበትን ፲ቱ አቅማር ተጠየቀት ጥቃ ። ዐሥሩ ሰንጠረዥ ታወቀ ተረዳ ።

ወላቲ ፲፻ ፶ ወ፭ መስመር ።

ለሷም ስድስት መቶ አምሳ አምስት መስመር አሏት ሐተታ ን ሰ ምዕራፍ በዛ መስመር አነበሳ ቢሉ ንኡስ ምዕራፍ እንደ ሰው እንደ እህል መስመር እንደ ቤት እንደ ውድማ ነው ፡ ባንድ ቤት ብዙ ሰው ባንድ ውድማ ብዙ እህል እንዲኖር ። ባንድ መስመርም ብዙ የንኡስ ምዕራፍ አኃዝ ይጻፋልና አምስት ባለው በዘጠነኛው ሰንጠረዥ ዐሥራ ዘጠኝ ይላል ፤ ይህን ዘጠኝ ያለ እንደሆነ ዘጠነኛውን ሀያ ይላል ።

ቀመር ቀዳማዊ ማቴዎስ ወማርቆስ ሉቃስ ወዮሐንስ ፸ ወ፪ መስመር ።

አራቱ የተባበሩበት መጀመሪያው ሰንጠረዥ ሰባ ሁለት መስመር ነው እንዲህ እያልህ ሂድ ።

ቀመር ዳግማዊ ማቴዎስ ወማርቆስ ሉቃስ ፪፲ወ፪
መስመር ፡፡
ሦስቱ የተባበሩበት ለሁለተኛው ሰንጠረዥ መቶ
ዐሥራ ሁለት መስመር ነው ፤ መቶ ሰማንያ አራት
ይሆናል ፡፡
ቀመር ሣልስ ማቴዎስ ወሉቃስ ወዮሐንስ ፳ ወ፩
መስመር ፡፡
ሦስቱ የተባበሩበት ሦስተኛው ሰንጠረዥ ሃያ አንድ
መስመር ነው ፡ ሃያውን ከሰማንያ ላይ ስትደርቢው
መቶ ይሆናል ፤ አራትና አንድ አምስት ሁለት መቶ
አምስት ፡፡

ቀመር ራብዕ ማቴዎስ ወማርቆስ ወዮሐንስ ፳ ወ፮
መስመር ፡፡

አራተኛው ሰንጠረዥ ሦስቱ የተባበሩት ሃያ ስድ
ስተ መስመር ነው ፤ አምስተና ስድስት ዐሥራ አንድ
ሃያና ዐሥራ አንድ ሠላሳ አንድ ሁለት መቶ ሠላሳ
አንድ ፡፡

ቀመር ኃምስ ማቴዎስ ወሉቃስ ፹ ወ፫ መስመር
ሁለቱ የተባበሩበት አምስተኛው ሰንጠረዥ ሰማ
ንያ ሦስት መስመር ነው፤ሠላሳና ሰማንያ መቶ ዐሥር
ሦስትና አንድ አራት ሦስት መቶ ዐሥራ አራት
ቀመር ሳድስ ማቴዎስ ወማርቆስ ፵ ወ፰ መስመር
ሁለቱ የተባበሩበት ስድስተኛው ሰንጠረዥ አርባ
ስምንት መስመር ነው ፤ ማርቆስና ሉቃስን አጠግባ
ሁሉንም እንዲህ እያልህ ሂድ ፤ ዐሥርና አርባ አምሳ
አራትና ስምንት ዐሥራ ሁለት ፡፡ ሦስት መቶ ስሳ
ሁለት ፡፡

ቀመር ሳብዕ ማቴዎስ ወዮሐንስ ፯ መስመር ፡
ሁለቱ የተባበሩበት ሰባተኛው ሰንጠረዥ ሰባት
መስመር ነው፤ሁለቱን ከሰባት ላይ ስትደርበው ዘጠኝ
ይሆናል ሦስት መቶ ስሳ ዘጠኝ ማቴዎስ እስከ
ሰባት ይዘምታል ከዚህ በታች የለውም ፤

ቀመር ሳምን ማርቆስ ወሉቃስ ፲ ወ፫ መስመር ፤
ሁለቱ የተባበሩበት ስምንተኛው ሰንጠረዥ ዐሥራ
ሦስት መስመር ነው ሦስት መቶ ሰማንያ ሁለት
ይሆናል ፡፡

ቀመር ታስእ ሉቃስ ወዮሐንስ ፲ ወ፱ መስመር
ሁለቱ የተባበሩበት ዘጠነኛው ሰንጠረዥ ዐሥራ
ዘጠኝ መስመር ነው ፤ ሁለትን ካሥራ ዘጠኝ ላይ
ቢደርቡት ሃያ አንድ ይሆናል ሃያውን ከሰማንያ
ላይ ቢደርቡት መቶ ይሆናል ፤ አራት መቶ አንድ
ቀመር ዐሥር በዘተሌለዩ ቦቱ ኵሉ ለለአሐዱ
አሐዱ እምሰባኪያን ፪፻ ፶ ወ፬ መስመር ፡፡
ከአራቱ ወንጌላውያን አንዱም አንዱ እያንዳንዱ
የተባበሩበት ዐሥረኛው ሰንጠረዥ ሁለት መቶ
አምሳ አራት መስመር ነው ፡፡ ማቴዎስ ፷ ወ፪
መስመር ማቴዎስ ስሳ ሁለት መስመር ነው ፤

ማርቆስ ፳ወ፩ መስመር ማርቆስ ሃያ አንድ
መስመር ነው ስሳና ሀያ ሰማንያ አንድና ሁለት
ሦስት ሰማንያ ሦስት ፤

ሉቃስ ፸ወ፪ መስመር ፤ ሉቃስ ሰባ ሁለት መስ
መር ነው ፤ ሰባና ሰማንያ ፡ መቶ አምሳ ፤ ሦስትና
ሁለት አምስት ፤ መቶ አምሳ አምስት ፤ ዮሐ
ንስ ፺ወ፱ መስመር ፡ ዮሐንስ ዘጠና ዘጠኝ
መስመር ነው በዘጠኝ ላይ አምስትን የደረቡ እንደ
ሆነ ዐሥራ አራት ይሆናል ፡፡ ዐሥራ አራትና ዘጠና
መቶ አራት ሁለት መቶ አምሳ አራት ሆነ ፤ አራቱ
የተባበሩበት አራት መቶ አንድ የተለያዩበት ሁለት
መቶ አምሳ አራት መላው ስድስት መቶ አምሳ አምስት
ወንጌል ቅዱስ ዘዜነወ ማቴዎስ ቃሉ ፩፻ ወ፯፻
ማቴዎስ ያስተማረው የወንጌል ዘሩ ሁለት ሺህ
ከሰባት መቶ ነው ፡፡

ወንጌል ቅዱስ ዘዜነወ ማርቆስ ቃሉ ፲፻ ወ፬፻ ፤
ማርቆስ ያስተማረው የወንጌል ዘሩ ሺህ ከሰባት፡፡
መቶ ነው ፤ አራት ሺህ ከአራት መቶ ይሆናል ፡፡
ወንጌል ቅዱስ ዘዜነወ ሉቃስ ቃሉ ፩፻ ወ፰፻
ሉቃስ ያስተማረው የወንጌል ዘሩ ሁለት ሺህ ከስ
ምንት መቶ ነው ፤ ስምንት መቶና አራት መቶ
ሺህ ከሁለት መቶ ይሆናል ፡ ሰባት ሺህ ከሁለት መቶ
ወንጌል ቅዱስ ዘሰበከ ዮሐንስ ቃሉ ፩፻ ወ፯፻
ዮሐንስ ያስተማረው የወንጌል ዘሩ ሁለት ሺህ ከሰ
ባት መቶ ነው ፤ ሰባት መቶና ሁለት መቶ ዘጠኝ
መቶ ይሆናል ፡፡

ወኮነ ድሙረ ቃሎሙ ለዓርባዕቱ ወንጌላት ፺፻ ወ፱፻
የአራቱ ወንጌላት የዘሩቸው ቍጥር ድሙሩ ዘጠኝ
ሺህ ከዘጠኝ መቶ ነው ፡፡

ከመ ታእምሩ ኈልቍ ቃላቲሆሙ ለአርባዕቱ ወን
ጌላት ጸሐፍነ ለከሙ በጺጋሁ ለእግዚአብሔር
የአራቱ ወንጌላውያን የዘሩትውን ቍጥር ታውቁ
ዘንድ እግዚአብሔር ገልጾልን ጻፍንላችሁ ፡፡

ወምንባረ ቃሎሙ ለ፬ቱ ወንጌላት ፺፻ ወ፬፻ ፵ ወ፱
አራቱ ወንጌላውያን በዘር የተባበሩበት ግን ዘጠኝ
ሺህ ከአራት መቶ ዓርባ ዘጠኝ ነው ፤ የተለያዩበት
አራት መቶ አምሳ አንድ ነው ፡፡
ወከመዝ ኃብሩ አርባዕቲሆሙ ፤
አራቱ ወንጌላውን በዚህን ያህል ዘር ተባበሩ ፡፡
ዘብእሲ ማቴዎስ ፤

በገጸ ብእሲ የተመሰለ ማቴዎስ ፤
ዘአንበሳ ማርቆስ ፤
በገጸ አንበሣ የተመሰለ ማርቆስ
ዘላህም ሉቃስ ፤

በገጸ ላህም የተመሰለ ሉቃስ
ዘንስር ዮሐንስ ፡

በገጸ ንስር የተመሰለ ዮሐንስ ፤
ዘልዑለ ይሠርር ወልዑለ ይጸርሕ ወልዑለ ይሰብክ ቃለ ወልደ እግዚአብሔር ለዓለመ ዓለም አሜን አካል ከሀልውና ተገልጾለት ንጽሐ ሥጋ ንጽሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና ተሰጥቶት ቀዳሚሁ ቃል ብሎ የተናገረ ዮሐንስ ።

ስምንተኛ ጉባኤ ፤

**አልፈሀ ግፃዌ ሥርዓት በል ፤** ታሪክ የመ**ጻሕፍትን** መልክ ከዚህ ይናገራሉ ፤ ታችኛው ግል**የት ጎዳና ፤ ላይኛው** ገጽ እርእስት ግልየት ጎዳግ፣ **ዳርና ዳሩ ገጽ ምስማክ ግልየት ጎዳና መ**ካከሉ ዓምድ **ሐውልት ግልየት ጎዳና ቀለም የመደቀበት መስመር መስሬ** የሄደበት ሲራክ አራት ጥቁር እምስት ቀይ ነጭ ሁለት ጥቁር ምስት ቀይ ስረዝ ሁለት ጥቁር ነጥብ ይባላል ። **ግጻዌ** ሥርዓት በእንተ ኅብረተ ቃላት የ፬ቱ **ወንጌላት** ።
የአራቱ ወንጌላውያንን ነገር ለማስተባበር የአራቱ ወንጌላውያን የተገለጸ ሥርዓት ይህ ነው ያጌጹ ወደለዎ ለዮሐንስ ግጻዌ እንዲል ።
እንዘ ይትሉ ረድኤተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ክልኤቱ ባሕቲቶሙ ጸሐፉ እንከ ወንጌለ እምሐዋር ያት ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እየቃኛቸው እያገዛ ቸው ከሐዋርያት ሁለቱ ብቻ ወንጌልን ጻፉ ።
ወክልኤቱ እመትሎሆሙ ፤

ሁለቱ ሐዋርያትን ተከትለው ከሚያስተምሩ ከሰባ አርድእት ወገን ናቸው ።
አሐዱ ዘጳውሎስ ፤ አንዱ የጳውሎስ ደቀ መዝሙር ሉቃስ ነው ፤
ወአሐዱ ዘጴጥሮስ ረድአ ዚአሁ ።

አንዱ የጴጥሮስ ደቀመዝሙር ማርቆስ ነው ።
ምስለ ማቴዎስ ወዮሐንስ ጸሐፉ እንከ ወንጌላተ እንዘ ኢየኃሥሡ ክብረ ለርእሶሙ ።
ለራሳቸው ክብር ሳይሹ እንበላበት እንጠጣበት እን ቶምበት እንሸለምበታለን ሳይሉ ከማቴዎስ ከዮሐ ንስ ጋራ ጻፉ እነዚያ እንደጻፉ ጻፉ ።
አላ በከመ ይትፌቀድ ፤

እንደሚወደድ አድርገው ንባቡን አጉልተው ምሥጢ ሩን አርቅቀው ጻፉ ሐተታ የፈላስፎች መጽሐፍ የሆነ እንደሆነ ንባቡ ረቂቅ ጨጨጨ ጀጀጀ ሸሸሸ እያሉ ምሥጢር የለውም ።
ወንጌልሰ ሶበ ተጽሕፈ እሐዱሂ እምአከለ ፤
ወንጌል ካራቱ አንዱ ቢጻፍ በበቃ ነበር ።
ወየአክልሂ ።

እስከ ዕለተ ምጽአት ለልጅ ልጅ ይበቃ ነበር ።
ዳዕሙ አርባዕቲሆሙ ኃብሩ እለ ይጽሕፉ ፤
ወንጌልን የጻፉ አራቱ አንድ ሆኑ እንጂ ፤
ወኮኑ እንዘ ኢይትረአዩ ፤
ሳይተያዩ ጻፉ ።
ወእኮ በ፩ዱ መካን ሀልዎሙ ዘጸሐፉ ፤
ባንድ ቦታ ሁነው አልጻፉም ፤
ወኢሂ ተማከሩ ለአኀብሮ ቃላት ።

ነገሩን ለማስተባበር አልተማከሩም ይህ እንዲህ ይሁን ይህን እንዲህ እንበለው ብለው ፤
ወእልቦ ኃሠሣ ማእከሎሙ ።

በሳቸው ዘንድ መጠያየቅ የለም አልተጠያየቁም ይህስ እምደምን ይሁን ይህንስ እንደምን እንበለው ብለው ዳዕሙ ከመ ዘአሐዱ አፍ ነበቡ ኵሎሙ ።
እንዳንድ ልብ መካሪ እንዳንድ ቃል ተናጋሪ ሁነው አንድ ነገር ተናገሩ እንጂ ።
እሩየ በብሒተ ወርእየተ ዘበአማን ዝንቱ ኮነ ፤
ተለያይተው የጻፉት ይህ ተያይተው እንደጻፉት ሁኖ ተገኘ ።

ወሶበ ኢኮነ ከመዝ ጸላኢ ወኢመኑሂ እምኢአምነ ተለያይተው ጽፈዋት አንድ ሁና ባትገኝስ ማንም ማን መናፈቅ ወንጌል ደግ ሕግ እንደሆነች ባላመ ነም ነበር ።

ወእኮ ድንቀተ ዘኮነ ዘመጠንዝ አኀብሮ ቃላት ፤
ድድቀተ ድድቀተ ይላል ይህን ያህል የነገር ማስተ ባበር የተደረገ በሐሰት በምትሐት አይደለም ።
ወእምኵሉ ሐሜት ወትሕዝብተ ጸላዒ አድኃነት ።
አራት ወገን ሁና ተጽፋ አንድ ሁና በመገኘቷ ከጠላት ጥርጥር ከጠላት ነቀፋ ራሷን አዳነች ሐተታ ወን ጌል ተራ ሕግ ናት ብሎየ ጠረጠራት የነቀፋት የለምና ወፈድፋደ ያከብሮሙ ሰብእ በእንተ ዘጸሐፉ በብሩኅ ይልቁንም ንባቡን አጉልተው ምሥጢሩን አርቅቀው ስለጻፉ ሰው ሁሉ ፈጽሞ ያከብራቸዋል ።
ወጽሕፈቱስ ከመዝ ውእቱ ፤
ጽፈቱም ይህ ነው ።
እስመ አምላክ ኮነ ሰብአ ፤
አምላክ ሰው ሆነ ብለው ነው ።
ወበእንተ ትእምርታት ዘኮነ ፤
ድውይ ፈወሰ ብለው ነው ።
ወመንክራተ ዘገብረ ፣
ጋኔን አወጣሙት አነሣ ብለው ነው ።
ወበእንተ ዘተሰቅለ ወበእንተ ዘተቀብረ ።
ተሰቀለ ተቀብረ ።
ወበእንተ ትንሣኤሁ ወበእንተ ዕርገቱ ።
ተነሣ ዓረገ ።
ወበእንተ ምጽአቱ ።
ዳግመኛ ይመጣል ብለው ነው ።
እስመ ሀለዎ ይኰንን ሕያዋነ ወሙታነ ፤
ሕያዋንን ሙታንን ይገዛ ዘንድ በሕያዋን በሙታን ይፈርድ ዘንድ አለውና ።

ወከመ ዘወሀበ መድኃኒተ በምጽዋት ፤
አብ ቢሉ ልጁን እንደ ምጽዋት አደርጎ ሰጥቷል
ወልድ ቢሉ አካሉን እንደ ምጽዋት አደርጎ ሰጥቷል
አንድም ሥጋውን ደሙን እንደምጽዋት አድርጎ
ሰጠ ብለው ነው ።

ወዘከመ ይቢ ኢያምጻእኩ ካልአ ሥርዓተ ዘይትቃ
ወማ ለብሊት ሕግ ።

አስቀድማ የተሠራች ኦሪትን የምታሳልፍ ሕግን
አልሰራሁም አለ ብለው ነው ። ኢይምበልከሙ ዘመ
ጻእኩ እሰዐሮሙ ለኦሪት ወለነቢያት አለ ብለው
ነው ።

እስመ ወልድ ፍቁር ባሕቲቱ ብሑተ ልደተ ዘከ
መዝ ፤

በልደት ሥሉጥ የሚሆን ፍቁር ወልድ ብቻ ዛሬ ወን
ጌልን እንደሠራ ቀድሞም ኦሪትን የሠራ እሱ ነውና
በእንተዝ ያለው ማንሻ ፤ አንድም በልደት ሥሉጥ
የሚሆን ፍቁር ወልድ ብቻ ቀድሞ ኦሪትን እንደ
ሠራ ዛሬም ወንጌልን የሚሠራ እሱ ነውና ።
ወበእንተዝ ኮነ ዘመጠነዝ አኀብሮ ቃላት ፤
ስለዚህ ይህን ያህል የነገር ማስተባበር ተደረገ ።
ሉቃስ ዝልፈተ አርአየ ፤

ሉቃስ አሌ ለከሙ አብዕልት እስመ ሠለጥከሙ
ትፍሥሕተከሙ በዝንቱ ዓለም ብሎ ዘለፋን ተና
ገረ ።

ከመ ንትመራሕ ነገረ ርትዕ ጽንዕተ ፤
የማትፈርስ እውነተኛ ነገርን እናውቅ ዘንድ ፤
ወዮሐንስ አኀድአ ወከሐ እንዘ ይብል እምላዕሉ
እፃኀበ አቡሁ ወረደ ።
እፃና እፃ አንድ ወገን ዮሐንስ ወልደ ዕጓለ እመ
ሕያው ወረደ እምበማይ ብሎ ጽፎ የመናፍቃ
ንን ክርክር ጸጥ አደረገ ።
እንዘ ክርስቶስ የሐወ ሶሙ ፤
ክርስቶስ እየቃኘችው ዮሐንስ አኀድአ ወከሐ ሉቃስ
ዝልፈተ አርአየ ፤
ወእፃ ካልዓኒሁ ውእቱ አንጎ ፥
ከወንደሞቹ እብልጦ አካል ከሀልውና ተገልጾላት
ንጽሐ ሥጋ ንጽሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና ተሰጥቶት
ቀዳሚሁ ቃል ብሎ ተናገረ ።
ወማቴዎስኒ ዘእምአይሁድ ብዙኃነ አእመነ ፤
ማቴዎስም ከአይሁድ ወገን ብዙ ሰው አሳመነ ።
አንድም ከአይሁድ ወገን የሚሆን የጌታችን ልደት
ለብዙ ሰው አስተማረ አንድም ከአይሁድ ወገን
የሚሆን ማቴዎስም ብዙ አሳመነ ።
ወማርቆስኒ እንዘ ሀሎ ብሔረ ግብጽ አስተብቍዕዎ
አርድእተ ዚአሁ ከመ ይግበር ከመዝ ፤
ማርቆስም በግብጽ ሳለ ደቀ መዛሙርቱ በቃል
ያለ ይረሳል በመጽሐፍ ያለ ይወረሳል ሃብቱ ለደቀ
መዛሙርቶቻቸው እንደጻፉ ጻፍልን ብለው ለመኑት
ማለዱት ።
ወሉቃስኒ ካዕበ በሐዲስ ተናገረ ።
ዝልፈተ አርአየ ሳለው ዳግመኛም ሉቃስ አብዝቶ
ቆጸረ ።
ወእስከ አዳም አልዓለ ፤

እስከ አዳም ደረስ ሐተታ ሌሎች የሚቈጽሩ እስከ
ስድስት እስከ ሰባት ነው እንደሱ አብዝቶ የቈጠረ
የለምና አንድም በሐዲስ ከነበረ ከዮሴፍ ጀምሮ
በብሉይ እስከ ነበረ እስከ አዳም ደረስ ወልደ
ዮሴፍ ብሎ አዳም ወልደ እግዚአብሔር እስከ
ማለት ደረሰ ።
ወአኮ በእሐቲ ማዕዘንት ጽሒፎሙ ዘደፈኑ ፤
ጽፈው ባንድ ቦታ አልተውም ።

አላ በኵሉ ምድር ወበኵሉ ባሕር ሰፍሑ ስምዓተ
ለኵሉ ሰብእ ።

ባራቱ ማዕዘን ሳሉ ሁሉ ጻፉ እንጂ ።
ወእንዘ መቃርዓት ሀልው ይትነበብ ዝንቱ እስከ ዮም
መናፍቃን ሳሉ ወንጌል እስከ ዛሬ ድረስ ይነበባል
ይተረጐማል ።
ወአልቦ ዘአዕቀፈ እምዘጽሑፍ ወኢመኑሂ ፤
ከተጻፈው ጽፈት ማንም ማን የነቀፈ የለም ፤
አንድም አላ በኵሉ ብለህ መልስ ። ባራቱ ማዕዘን
ዞረው ወንጌልን ለሰው ሁሉ አስተማሩ እንጂ አይ
ሁድ መናፍቃንም ሳሉ ሁልጊዜ ይህ መጽሐፍ ይነ
ገራል ትምህርቱንም የነቀፈ የለም ።
እንዘ ታረትዕ ኃይለ እምላክ ከሃሊተ ኵሉ ።
ሁሉን ማድረግ የሚቻላት ኃይል አምላካዊት እያ
ቀናናት ፤
ወፈደፋደ እምኵሉ ።
ይልቁንም ወንጌል ስትጸፍ ፤
ወሶበ ኢኮነ ከመዝ እፎ መጸብሐዊ ወመገልብ
እምጠቡ ከመዝ ፤

እንዲህ ባይሆን መጸብሐዊ ማቴዎስ መግለቦ ሠሪ
ዮሐንስ እንደምን በተራቀቁ ነበር አንድም እፎ
እምጠበ በል በውን በግብር ምክንያት ያሸሸ የነበረ
መጸብሐዊ ማቴዎስ እንደምን በተራቀቀ ነበር ገለቦ
ይላል ትግሬ ሸሸ ሲል ።
ወኢኮነ በምትሐት ወኢበሕልም ዘኮነ ዝ ለአለ በየ
ዋሃት ወበሃይማኖት ያነብብዎ ወየአምኑ ፣
አምነው በሃይማኖት ባለመቃወም ጸንተው ለሚመ
ለከቱት የተደረገ ይህ በሐሰት በምትሐት እይደለም
ወእኮ በሕይወቶሙ ከመ ፤
ማመናቸውም በሕይወተ ሥጋ ሳሉ ብቻ አይደለም
ዓዲ መዊቶሙሂ ፤
ከሞቱም በኋላ ነው እንጂ ።
አኮ ለጅ ወ፩ቱ ሰብእ ወኢለ፪ት ። የጻፉ
ለመቶ ሀያ ቤተ ሰብእ ብቻ አይደለም ።

አሳ ለአህጉር ወለአሕዛብ ወለሕዝብ ወለምድር ወለባሕር ወለዓላዳስ ወለፀር ወለኵሉ ዓለም ። ለሁሉም ነው እንጂ አንድም ለዋቂት ሰው ብቻ አይደለም በባሕር በየብስ በደሴት በሀገር ላሉ ለሕዝብም ለአሕዛብም ነው እንጂ ።
አእመኑ በዛጎን ዘእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ወውስተ መርሶ አብኡ ፤
በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ አጋዥነት አሳምነው ወደመንግሥተ ሰማያት ወደብ አገቡ ።
መዋዎ ኀብረተ ቃላት ቅዱሳት ዘ፬ቱ ወንጌላት ተፈጸመ ።
አራቱ ወንጌላውያን በዘር የተባበሩበትን ጽፎ መስጠት እለቀ ።
ወደ ኋላ ተመልሰህ አውሴብስ በል ፤
አውሴብስ ለቆጵርያኖስ ።

ታሪክ አሞንዮስ አውሳብዮስ ይህን ያህል ዓቢይ ምዕራፍ ይህን ያህል ንኡስ ምዕራፍ ይህን ያህል ዘር ብለው ጽፈው ከተለያዩ በኋላ ብልህ ደቀ መዝሙር የተለያዩበትን የተባበሩበትን ዘር ልወቅ ባለ ጊዜ እንደምን ይሆናል ባሕር ለባሕር ሲዋኝ ይኖራል ብሎ ይህን ሲሻ ቀኖና ገባ ባሥሩ ሰንጠረዥ አምሳል አሥር መሬ አኃዝ ተገልጾለት ይጽፋል ። አውሴብስ ለቆጵርያኖስ የላከው ክታብ ይህ ነው ። ዘአውሴብስ የአውሴብስ ክታብ ለቆጵርያኖስ ትድረስለት እምአውሴብስ ይላል ። ከአውሴብስ የተላከች ክታብ ለቆጵርያኖስ ትድረስለት ፤ ቆጵርያኖስ ካህን ጨዋም ነው ይሉታል ።
ለዘእፈቅር ለእኁየ ፤
ለምወደው ለወንድሜ ለና ለ አንድ ወገን ።

ፍሥሐ ወሰላም ወዳኅና ለከ እምኀበ እግዚአብሔር ከእግዚአብሔር ዘንድ መንፈሳዊ ደስታ ይደረግልህ አሞንዮስ እስክንድራዊ በብዙኅ እስተሐምሞ ወጽሒቅ ገብረ ወኀደገ ለነ ዘቃለ ዘከመ ኃብሩ ፬ቱ ወንጌላውያን ወእምዝ አርአስተ ምንባባት ።

የእስክንድርያው ሰው አሞንዮስ በብዙ ትጋት በብዙ ጻሕቅ አራቱ ወንጌላውያን የተባበሩበትን የተለያዩበትን ፥ አንድም ሰንጠረዡን ቁራኛውን አንድም ዓቢይ ምዕራፉን ንኡስ ምዕራፉን ይህን አንድ ወገን ወእምዝ አርእስተ ምንባባት ዘሩን ጽፎ ተወልን፤ ሐተታ እሱ የሚጽፍ መሬ አኃዙን ነውና አንድ ሁነው የጻፉትን ለሱ ብቻ ለዋቶ ተናገረ ።

ወበአንተዝ እንከ መፍትው ጥንቶ ይትልው ። ስለዚህ ማቴዎስን ሊመለከቱ ይገባል ።
ከመ ኢይኩን ሙሱነ ምንተኒ በተሲወ ንበቱ ። በተመለከቱት ጊዜ አንድ በሚሆኑበት ዘር ልዩ እንዳይሆን ።
ወ፫ቱኒ ኢይትኀደጉ ፥
ሦስቱም እንዳይለያዩ ፥

ከመ እሙንቱኒ ይድኃኑ እምተጸርዖ በንበቱ ። እሳቸውን በተመለከቷቸው ጊዜ ከመለየት ይድኑ ዘንድ ፍጹመ ሥጋ ወመለያልየ ይኩኑ ።

አንደ እንድ ልብ መካሪ እንደ ቃል ተናጋሪ ይሆኑ ዘንድ እንጂ ፥ አንድም ፍጹም ሥጋ ወመለያልይ ፥ አካል ሕዋስ የተፈጸመለት ሰው ይሆኑ ዘንድ ነው እንጂ ።
ወተአምር ለለ፩ዱ ወንጌል መካነ ትእምርቱ ፥ አእምር ሲል ነው ። የያንዳንዱ ወንጌል የሰንጠረዡን ቦታ ዕወቅ ።
ወባሕቱ አማን በዘህልው እምጸማሁ ለቀዳማዊ ብእሲ ዘነገርኑ ስሞ ረከብኩ አነሂ ምክንያተ እንተ ከማሃ ትመበል ሥርዓተ ወሐፈጥኩ ፲ተ ትእምርታተ ጉልቆ ወአንበርኩ ለከ ፤

አሞንዮስ እስክንድራዊ በብዙኅ እስተሐምሞ ወጽሒቀ ገብረ ወኀደገ ለነ ዘቃለ ዘከመ ኃብሩ ፬ቱ ወንጌላውያን ወእምዝ አርእስተ ምንባባት ብለን ስሙን ያነሣነው አሞንዮስ በጻፈበት በኩል እኔም በጾፈት እሷን የምትመስል እንደሷ ያለች አግኝቼ በዐሥር ሰንጠረዥ አምሳል ዐሥሩን መሬ አኃዝ ጽፌ ተውኩልህ ።
ወስመ ይከዎ ለቀዳማዊ አሐደ ።
ወስመይቡ አሐደ ቀዳማዊ ይላል መጀመሪያውን ሰንጠረዥ አንድ አልሁት ።
ወአኀዞ ለቀዳማዊ ፥

የመ ጀመሪያውን ሰንጠረዥ መሬ አኀዘንም አንድ አልሁት ፤ ወአኀዘ ቀዳማዊ ወአኃዞ ለቀዳማዊ ይላል ወውእደ ኃብሩ አርባዕቲሆሙ ቃላተ ማቴዎስ ወማርቆስ ሉቃስ ወዮሐንስ ፤
ወእደ ኃብሩ ይላል ፥ አራቱ በዘር ከተባበሩባት ዘንድ የተባበሩበትን ሰንጠረዥ አንድ አልሁት መሬ አኀዙንም አንድ አልሁት ።
ወውስተ ዳግም ፫ቱ ማቴዎስ ወማርቆስ ወሉቃስ ፥ በሁለተኛው ሰንጠረዥ ሦስቱ የተባበሩበትን ሁለተኛውን ሰንጠረዥ ሁለት አልሁት መሬውንም አኀዘ ሁለት አልሁት ። ወውስተ ሣልስ ሠለስቱ ማቴዎስ ወሉቃስ ወዮሐንስ ሦስቱ የተባበሩበትን ሦስተኛው ሰንጠረዥ ሦስት አልሁት መሬውንም አኀዝ ሦስት አልሁት ።ወውስተ ራብዕ ፫ቱ ማቴዎስ ወማርቆስ ወዮሐንስ ሦስቱ የተባበሩበትን አራተኛውን ሰንጠረዥ አራት አልሁት መሬውንም አኀዝ አራት አልሁት።
ወውስተ ኃምስ ፪ቱ ማቴዎስ ወሉቃስ ።
ሁለቱ የተባበሩበትን አምስተኛውን ሰንጠረዥ አምስት አልሁት ። መሬውንም አኀዝ አምስት አልሁት ።
ወውስተ ሳድስ ፪ቱ ማቴዎስ ወማርቆስ ።
ሁለቱ የተባበሩበትን ስድስተኛውን ሰንጠረዥ ስድስት አልሁት መሬውንም አኀዝ ስድስት አልሁት ።
ወውስተ ሳብዕ ፪ቱ ማቴዎስ ወዮሐንስ ።

ሁለቱ የተባበሩበትን ሰባተኛውን ሰንጠረዥ ሰባት አልሁት መሪውንም አኃዝ ሰባት አልሁት ።
ወውስተ ሳምን ፷ቱ ማርቆስ ዐሉ ቃስ ።
ሁለቱ የተባበሩትን ስምንተኛውን ሰንጠረዥ ስምንት አልሁት መሪውንም አኃዝ ስምንት አልሁት
ወውስተ ታሥዕ ፪ ሉቃስ ወዮሐንስ ፤
ሁለቱ የተባበሩበትን ዘጠነኛውን ሰንጠረዥ ዘጠኝ አልሁት መሪውንም አኃዝ ዘጠኝ አልሁት ፤
ወውስተ ዐሥር ዘዘዚአሆሙ በዐሥረኛው ሰንጠረዥ አንዱም አንዱ እያንዳንዱ የተለያዩበትን ሰንጠረዥ ዐሥር አልሁት መሪውንም አኃዝ ዐሥር አልሁት።
ወከመዝ ውእቱ ሥርዓቱ ዘተሠርዓ ።

አራቱ እንደ ተናገሩ እንደ ጻፉ የተጻፈው ጽፈት ይህ ነው ።

ወነገሩ ለለአሐዱ ወንጌል በጉልቆ አኃዙ ፤
የያንዳንዱ የወንጌል ዘሩ በንኡስ ምዕራፉ አኃዝ ቍጥር ነው ፤ ወይቄጥን እም ቀዳማዊ መጸሐፈ ልደቱ ሲል አንድ ይላል ፡ ወዳግም ወዘሎንኬ ሲል ሁለት ይላል ። ወሣልሥ ለእግዚእነ ሲል ሦስት ይላል እስከ ይትፈጸም መጽሐፉ እንዲህ እያለ ማቴዎስ እስኪፈጸም ፤ አንድም መላው እስኪፈጸም እንዲህ እያለ ይሄዳል ።

ወበ ጉልቈ አኃዙ ቦቱ አኃዝ ዘበሲራኩ ዘያኤምር ውስተ አይ ሥርዓተ ቀመር ሀሎ ።

የተባበሩበት የተለያዩበት ዘር በማናቸውም ሰንጠረዥ ጽፈት እንዳለ የሚያስረዳ በየንኡስ ምዕራፍ አኃዛቸው ቍጥር በሲራኩ የተጻፈ መሪ አኃዝ አለ
ወእምከመ አሐዱ ከመ ውእቱ ውስተ ቀዳማዊ ፤
መሪ አኃዙን አንድ ያለ እንደሆነ በመጀመሪያው ሰንጠረዥ እንደሆነ ይታወቃል ።
ወእምከመ ክልኤቱ ። ከመ ውእቱ ውስተ ዳግማዊ
መሪ አኃዙን ሁለት ያለ እንደሆነ በሁለተኛው ሰንጠረዥ እንደሆነ ይታወቃል ።
ወእምዝ እስከ ይትፈጸም ዐሠርቱ ሥርዓት ፤
ከዚህም በኋላ ዐሥሩ ሰንጠረዥ እስኪያልቅ መሪ አኃዝ እንዲህ እያለ ይሄዳል ።
ወእምከመሰ ፤ አመ ከሠትከ እምአርባዕቱ ወንጌል ካራቱ ወንጌል የሻኸው ኑሮህ ብትገልጽ ።
ወፈቀድከ ታእምር አለ መኑ እሙንቱ እለ ኃብሩ ቃለ ተኃሥሥ ውስተ አቅማሪሁ ወትረክብ ።
በዘር የተባበሩ እነማንም እንደሆኑ ልታውቅ ብትወድ ከሰንጠረዡ ገብተህ ፈልግ ታገኛለህ ፤
እእሚረከ አኃዘ ጉልቊ ዘበሲራኩ ።
በሲራኩ የተጻፈ መሪ አኃዙን ዐውቀህ ፤
ወእሉሂ ውስቴቱ ።
እሳቸውም በሰንጠረዡ ተጽፈዋል ።
ከመ ውስተ ግልየቱ ጉልቈ አኃዙ ለለአሐዱ ወንጌል ዘዘዚአሆሙ ።

እየራስ እየራሳቸው እያንዳንዱ ወንጌል የመሪ አኃዛቸው ቍጥር በግልየቱ እንደ ተጻፈ እሳቸውም በሰንጠረዡ ተጽፈዋል ።
ወዘከመሂ ኃብሩ ቃለ ዘከመ ኃብሩ አርባዕቱ ወሠለስቱ ወክልኤቱ ፤
አራቱ ሦስቱ ሁለቱ የተባበሩበትን እንደ ተባበሩ ።
ወአሐዱሂ ዘከመ ይቤሉ ፤
የተለያዩበትን እንደ ተለያዩ እንደ ተናገሩ ።
ወጸሐፍኩ ውስተ ቀዳማዊ ቀመር ዘከመ ኃብሩ አርባዕቲሆሙ ።

አራቱ እንደ ተባበሩ በመጀመሪያው ሰንጠረዥ ጽፌልሃለሁ ።

ውስተ ግልየቱ ለቀመር ጉልቈ አኃዞሙ ለለአሐዱ ወንጌል ።

በሰንጠረዥም የያንዳንዱ ወንጌል የመሪ አኃዛቸው ቍጥር ተጽፏል ።

ወከማሁ ውስተ ወንጌልሂ ጽሑፍ ጉልቈ አኃዙ ፡ ክማሁ ለማለት ነው የመሪ አኃዛቸውም ቍጥር በወንጌል ተጽፏል ።

በዘየአምርዎ ኀበ ኃብሩ ፬ቱ በሲራከ አኃዙ ወውእደሂ ፫ቱ ወውእደሂ ፪ቱ ወ፩ዱሂ ።

በአኀዘ ሲራኩ ሲል ነው በሲራኩ የተጻፈውን መሪ አኃዙን ዐውቀው አራቱ ሦስቱ ሁለቱ የተባበሩበትን እንደ ተባበሩ ፣ ወ፩ሂ የተለያዩበትን እንደ ተለያዩ ፣ በሚያውቁት ገንዘብ ያውቁት ዘንድ ይህን የሚያውቁበት መሪ አኃዝ ጽፌልሃለሁ ።
ወእሡከመ ረከቡ እንዘ ያነብቡ አኃዘ ዘበሲራኩ ።
ሲመለከቱ በሲራኩ የተጻፈውን መሪ አኃዙን ያገኙ እንደሆነ ፣
ወፈቀዱ ያእምሩ አስማቲሆሙ ለእለ ኃብሩ ።
በዘር የተባበሩትን ስማቸውን ሊያውቁ ቢወዱ ፣
ይኅሥሡ ውስተ አቅማሪሁ ወይረክቡ ፤
ከሰንጠረዡ ገብተው ይፈልጉ ያገኛሉ ።
እስመ ውስቴቱ ጽሑፍ አስማቲሆሙ ።
ስማቸው ከውስጡ ተጽፏልና ።
ወጸሐፍኩ ዓዲ ትእምርተ ውስተ ወንጌል ትእምርተ አኃዝ ዘበሲራኩ ።
ዳግመኛም በወንጌል የአንቀጽ ምልክት ጽፌያለሁ ፡ ኀበ ገብረ ተአምራተ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ተአምራት ካደረገበት ጌትነቱን ሥራ ከሠራበት ዘንድ ፣ ሐተታ ሰንደቅ አላማ ዙፋን መከዳ ድባብ ማሰሪ ይቀርጻል ።
ኀበሂ አዘዘ ወኀበሂ ገሠጸ ባሕረ ወኀበሂ መሐረ ወኀበሂ ነበረ ።
ፃእ መንፈስ ርኩስ ብሎ ካዘዘበት ባሕርን ነፋሳትን ከገሠጸበት ፣ ከተራራ ተቀምጦ ካስተማረበት ሳይ፣

ሐተታ ወምበር መቋሚያ መነሳንስ ድባብ ማሰሬ እንደ ጃንጥላቱ የፍ አድርጎ ይቀርጻል ።
ወትእምርት ኀበ አኃዙ ማዕተበ መስቀል ።

ነገረ መስቀልን ከሚያነሣሣበትቦታ የመስቀል ምል ክት አለ ፤ ሐተታ እንደተ አድርጎ ይቀርጻል ። ነገረ በቀልን ከሚያነሣበት እንደ እግረ ገመል አድርጎ ይቀርጻል ፤ ግመል በቀለኛ ናት አጥብቆ የመታትን እስከ ቢድስት እስከ ሰባትዓመትአትረሳውም ሰፍራ ሲመቻተ ገደል ገፍታ ትጥለዋለች ባጥብሳ ትረ ገጠዋለች ። ነቢያትን ከሚያነሣበት ጋ ጋ ጋ እያለ ይጽፋል ። ጋጋና ማለት ነው ። ጋ ጋ ኛ አስቢነጋ እየሙኙ እንዲያድር ነቢያትም ጌታ እስኪወለድ ትንቢት ተናግረዋልና ፤ እንድም ጋጋኛ ቀን ደጋ ወጥቶ ሲሞህ ይውላል ሌሊት ቀላ ወርዶ ያድራል። ነቢያትም ሲያል መውረድ አልቀረላቸውም በእደ እግዚአብሔር ተጠብቀዋል እንጂ ፤ ሐዋርያትን ከሚያነሣበት ጌ ጌ ጌ እያለ ይጽፋል ። ባለጌ ማለት ነው ። ባለጌ ባለርስት ነው ፤ ሐዋርያትምየመ ንግሥተ ሰማይ ባለቤቶች ናቸውና ፤ ይህንንም በነጭ በጥቁር በቀይ ይቀርጸዋል፤ ቀይ ደማቸውን ያፈሰሱና ጥቁር መከራቸው ጽኑዕ ነውና ፤ ነጭ ዋጋ አላቸውና ፍሥሐ ወሰላም ለነ በክርስቶስ ፤

በክርስቶስ የሚገኝ ፍቅር አንድነት ይደረግልን ፤ በስመ እግዚአብሔር መሐሪ ወመስተሣህል ስብሐ ሐት ለእግዚአብሔር ማዕርገ ወንጌል ወዝማሬ ዘበ አማን ።

ስብሐት ወዝማሬ ብለህ ግጠም ፤ወንጌልን ላከበረ ለእግዚአብሔር የባሕርይ ክብር ይገባዋልና ፤ መሐሪ መስተሣህል በሚሆን በእግዚአብሔር ስም እምነው ጸሐፍዋ ፬ቱ ወንጌላውያን አራቱ ወንጌላውያን ጻፉት በተአምራት ግሁዳት እምኀበ ኵሎሙ ሐዋርያት፤ በሐዋርያት ዘንድ በተገለጸ ተአምራት ።

ወመንክራት መዋኤ ኵሉ ሕሊናት ወቴክሥተ ቦቱ ጽድቅ ሃይማኖት ።

ሕሊናትን ድል የሚነሳ የሚያሳምን አንድነቱ ሦስ ትነቱ በተገለጸበት በተአምራት ወንጌልን ላከበረ፤ ወአስተኃፈረ ቦቱ ሰሕተተ ሰይጣናት ።
ኢተጥዓምን ኢትልከፍን ኢትግሥሥን ያሳለፈበት ወንጌልን ላከበረ ።
ወአፍለስ ፍጥረተ እግዚአብሔር ኀበ አምልኮቱ እምድኅረ አምልኮ ጣዖት ።

ሰውን ሁሉ ከአምልኮተ ጣዖት ወደ አምልኮተ እግዚአብሔር ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ በመለሰበት በተአምራት ወንጌልን ላከበረ ። አንድም የመለሰባት ወንጌልን ላከበረ ።
ወዬወወ ቦቱ ዌዋዌ ዘይወስድ ኀበ ሕይወት ዘለ ዓለም ።

ወደማያልፍ ሕይወት የሚያደርስ ምርኮኝነትን የማረከባት ወንጌልን በተአምራት ላከበረ ፤ አንድም ወደማያልፍ ሕይወት የሚያደርስ ምርኮኝነት የተማረ ኩባት ወንጌልን ላከበረ ፤ ሐተታ ለሞት የሚሆን የነ ብልጣሶር ምርኮ አለና እንዲህ አለ ።

ወአድኃነ ሰብአ እምከህደት ወእምተታልዎተ ፀር ወሞተ ኃጢአት ።

ሰውን ከክህደት ከሰይጣን ምርኮኝነት ቍራኝነት በኃጢአት ከሚመጣ ፍዳ ያዳነባት ወንጌልን በተ አምራት ላከበረ ።

ወፈጸመ ሕገ ርትዕ በሕገ ትሩፋት ፤
ኢትቅትልን በኢታምጽእ ኢትዘሙን በዘርእይ ያሳለ ፈባት ወንጌልን ፤
ወሠርዓ ተፋቅሮ ፤

ተፋቀሩ በበይናቲክሙ የምትል ወንጌልን ወም ሕረተ ፤ ብፁዓን መሐርያን የምትል ወንጌልን ወአሠንዮ ፤ ሠናየ ግበሩ ለኵሉ ያለባት ወንጌልን ወገዲፈ ጥሪት ።

አሰመ ትፈቅድ ትኩን ፍጹመ ሑር ወሢጥ ንዋየከ ያለባት ወንጌልን ፤

ወትሕትና ብፁዓን ትሑታን ያለባት ወንጌልን ፤ ወንጽሐ ።

ብፁዓን ንጹሐነ ልብ ያለባት ወንጌልን በተአምራት ላከበረ ።

ወለዝንቱ መጽሐፍ ቅዱስ ዘያበርሃ ቦቱ ነፍሳት ከመ ከዋከብት ወጽጌያት ።

ነፍሳት እንደ ከዋክብት የሚያበሩባትንእንደጽጌያት የሚያሸበርቁባትን ወንጌልን ?

ወለሊሁ ሕገ መድኃኒት ለኵሉ ነፍሳት ፤
የድኅነት ሥራ የሚሆን ወንጌልን ፤
ወነቅዓ ሕይወት ለዘይትጌበሮ እምነ ኵሉ አንጋድ ከነገደ ካም ከነገደ ሴም ከነገደ ያፌት ተወልደው ለሚሠሩት የድኅነት መገኛ የሚሆን ወንጌልን ፤
ጸሐፍዋ ፬ቱ ወንጌላውያን ።
አራቱ ወንጌላውያን ጻፉት ።
በአህጉር ሊሉያን ፤

ቢቦታ ተለያይተው ጻፉት ፤ ሐተታ ማቴዎስ በፍል ስጥኤም ፤ ማርቆስ በግብጽ በሮምም ይላል ሉቃስ በመቄዶንያ ዮሐንስ በኤፌሶን ሁነው ጽፈዋል ።
ወበአዝማን ውሉጣን ።

በዘመንም ተለያይተው ጻፉት ፤ ሐተታ ማቴዎስ ጌታ ባረገ ስምንት ተፈጽሞ ዘጠነኛው ሲጀመር ቀላ ውዲዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዘመን ማር ቆስ ፤ ጌታ ባረገ ዐሥራ አንድ ተፈጽሞ ዐሥራ ሁለ

ተኛው ሲጀመር፤ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በአራተኛው ዘመን ፥ ሉቃስ ሀያ አንደኛው ተፈጽሞ ሀያ ሁለተኛው ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ ባሥራ አራተኛው ዘመን ፤ ዮሐንስ ጌታ ባረገ በ፴ በ፴ አምስትም ይላል ። ኔሮን ቄሣር በነገሠ በስባት ዓመት በስምንትም ይላል ፥ ሰባት ቢሉ ሲፈጸም ስምንት ቢሉ ሲጀመር ።

ወውእቶሙ ማቴዎስ ወማርቆስ ሉቃስ ወዮሐንስ፤ አራት የተባሉም ማቴዎስ ማርቆስ ሉቃስ ዮሐንስ ናቸው ።

ወስማቴዎስ ስሙ ሌዊ ፥

የማቴዎስ ስሙ ሌዊ ነው ሌዊ ይባላል ።

ወትርጓሜሁ ኅሩይ ፡ ትርጓሜው ም ኅሩይ ይባላል ወውእቱ ዘእምነገደ ይሳኮር ዘእምሀገረ ናዝሬት ፤ ትውልዱ ነገዱ ከነገደ ይሳኮር ናዝሬት በሚባል አገር ነው ።

ስመ አቡሁ ዲቁ ፥ አባቱ ዲቁ ይባላል

ወስመ እሙ ካሩትያስ ፥ እናቱ ካሩትያስ ትባላለች

ወሶበ ተጋብኡ ኅቤሁ ጉባኤ ብዙኅ እምእይሁድ

ዘጸውእሙ ወእለሂ አምኑ ወተጠምቁ ወኃሠሡ እምኔሁ ከመ ያስተጸንዕ አልባቢሆሙ ዘእአመኖሙ ቦቱ በቃል ወበመጽሐፍ ዘዜነዎሙ በልሳነ ዕብራይ ስጥ ወተሠጥወ ስእለቶሙ ።

ያስተማራቸው ያሳመናቸው ያጠመቃቸው ከይእሁድ ወገን የሚሆኑ ብዙ ምእመናን ተሰብስበው በቃል ያለ ይረሳል በመጽሐፍ ያለ ይወረሳልና ብለው በቃል በዕብራይስጥ ያስተማራቸውን በመጽሐፍ ጽፎ ያስረዳቸው ዘንድ ጸፍልን ባሉት ጊዜ ልመናቸውን ተቀበላቸው ፤ በቃል ዘእአመኖሙ ቦቱ

በልሳነ ዕብራይስጥ ያስተጸንዕ አልባቢሆሙ በመጽሐፍ ብለሀ ግጠም ።

ወወጠነ ጽሒፈ ዝንቱ መጽሐፍ በፍልስጥዔም ወፈጸማ በሀንድ ዕብራይስጣዊ ።

በፍልስጥዔም ጀምሮ በሀንድ ፈጸማት ፥

እመ ተስዱ እርድእት እምድረ ይሁዳ በቀዳሚት ዓመት እመንግሥተ አቅሎንድዮስ ቄሣር ።

ምእመናን ከይሁዳ ወጥተው በሄዱ ጊዜ ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዘመን አቅሎንድዮስ ቀላውዴዎስ ይለዋል ።

ወይእቲ በራብዕት ዓመት እምዓመተ ዕርገት ቅድስት ይችውም ጌታ ባረገ ስምንተኛው ተፈጽሞ ዘጠኛው ሲጀመር ነው ።

ወኮነ ስምዓ በሀገረ ብስባሬ ውጉረ በአብን አመ ፲ቱ ወ፪ቱ ለጥቅምት ፥

በጥቅምት ባሥራ ሁለት ቀን ብስባራ በምትባል አገር በደንጊያ ተመትቶ በሰማዕትነት ሞተ ። ወተቀብረ በቅርጣግና ዘቄሣርያ ።

የቄሣርያ ክፍል ዕፃ በምትሆን በቅርጣግና ተቀበረ ወሰዛቲ ብሥራት ተርጐማ ዮሐንስ ወልደ ዘብዴዎስ በሀገረ እልእንባን ።

የማቴዎስ ወንጌልን ዮሐንስ ወንጌላዊ በእልእንሳን አስተምሯታል ።

ወሰበከ ባቲ በሀንድ ወበኢየሩሳሌም ፥

ኪያሃ ሲል ነው ፤ እሷን በሀንድ በኢየሩሳሌም አስተማረ ።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር ለዓለመ ዓለም አሜን ፥ እስጀምሮ ላስጨረሰን ለእግዚአብሔር ለዘላለሙ ክብር ይግባው ።

ብሥራተ ማቴዎስ ሐዋርያ ፩፥ እም፲ ወ፪ቱ ሐዋር
ያት ጸሎቱ ወበረከቱ የሀሉ ምስለ ፍቁሩ
ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ይህ ቃል የሙሴ ምስት ቃል ነው ጥንተ ነገሩ
እንደምነው ቢሉ እግዚአብሔር እምቅድመ ዓለም
በልብ የመከረውን በነቢያት ያናገረውን ለመፈ
ጸም ሥጋ ሆነ ፡ ሥጋም ሁኖ ሕግ ጠባይዓዊን ሕግ
መጽሐፋዊን ሲፈጽም አደገ ሕግ ጠባይዓዊ በየ
ጥቂቱ ማደግ ነው ። ልህቀ በበሕቀ እንዘ ይትኤዘዝ
ለአዝማዲሁ እንተ ይእቲ አሙ እንዲል ፤ ሕግ
መጽሐፋዊ ሕገ ኦሪትን መፈጸም ነው ። እግዚአ
ለኦሪት ገብረ በሕገ ኦሪት ከመ ይሣየጦሙ ለእለ
ውስተ ኦሪት ወገብረ በሕገ ኦሪት እንዲል ፤
ሕገ ኦሪትን መፈጸም እንደምነው
ቢሉ በ፰ ቀን ቤት ግዝረት መግባት
በ፵ ቀን ዕጓለ ርግብ ዘወገ ማዕነቅ ይዞ ከቤተ መቅ
ደስ መግባት ካመተ ሦስተ ጊዜ ለገቢረ በዓል መው
ጣት ነው ። ፫ተ ጊዜያተ ለለዓመተ ለያበተርኢ ተባ
ዕትከ እንዲል ። በቀሩት ግን ከ፳ ዓመት ዘታተ
እንዳይወጡ ሥርዐተ ተሠርቶባቸዋል እሱ ግን አሥራ
ሁለተ ዓመት ሲሆነው ወጥቷል ፡ መውጣቱ በግ
ብተማር ነው እንጂ ለሌላ አይደለምና ፡ እንዲህ ለኀዲሀ
እያለ ፴ ዘመን ቢመላው በዮሐንስ እጅ ተጠምቆ
ልጅነቱን አስመስክሮ ገዳም ሄደ ። ገዳም ሄዶም
፵ መዓልት ፵ ሌሊት ጾመ መዋዕለ ጾሙ ሲፈጽም
ሰይጣን በ፫ ነገር ተፈታተነው ፡ ዘበበተ በተዐቢተ
በፍቅረ ንዋይ በስበት ቢመጣበተ በተዕግሥተ
በተዕቢት ቢመጣበተ በትሕትና በፍቀረ ንዋይ
ቢመጣበት በአሊዓ ንዋይ ድል ነሣው ፡
ሦስቱ አርእስተ ኃጣውአ የሚያስኙ እሊህ
ናቸው ። ዛሬም በሊህ ድል ለነሣ ሰው የቀሩት ኃጣ
ውአ ሊይቆሙለትም ከዚህ በኋላ ምድረ እሥራኤል
ገብቶ ትምህርተ ታምራተ ጀመረ የአይን ታምራት
አይተው የቃሉን ትምህርተ ሰምተው ካሥር እሀ
ጉር ከብዙ መንደር ተሠጸጽተው ያምበተ ገዚያ
ያህል ሰዎች ተከተሉት ከሊህ መቶ ሃያ ቤተ ሰብእ
ይመርጣል አበቀድሞ አሥራ ሁለቱን ሐዋርያተ ።
ወረሰየ እምሰብእ ዚአሁ ሐዋርያት እንዲል ፤ ቀየሎ
ስባ ሁለቱን አርድእት ። አርአየ ወኃረየ ካልዓን ሰብእ
እንዲል ፤ ፸ም ይባል በአኃዝ ቀጥሎም ሠላሳ ስድስ
ቱን ቅዱሳት አንስት መቶ ሃያ ቤተ ሰብ የሚያሰኙ
እሊህ ናቸው ፡ በሊህ ትምህርት አይከፈልባቸውም
ካደረበት ያድራሉና ። የቀሩት ግን ሲማሩ እየዋሉ
ምሽት ይከለክላቸው ነበር ። ሳሥራ ሁለቱ ነገደ
እሥራኤል በየፃቸው እየገባ ወር ወር ይሰብካቸው
ነበር ሦበት ዓመት ከሦስት ወር አስተምሮ ትምህርቱ

በምር ሲረዳለት ለመድኃኒተ ዓለም በቀራንዮ ተሰ
ቀለ ወገብረ መድኃኒተ በማእከለ ምድር ኢይደልዎ
ለነቢይ መዊት በአፍአ ዘእንበለ በኢየሩሳሌም እን
ዲል ፤ ተሰቅሎም በሞቱ ዓለምን አድኖ ፫ መዓ
ልት ሦበት ሌሊት በከርሠ መቃብር አድሮ ተነሣ ።
እበመ ውእቱ ቀሰፈነ ወይፌውሰነ ውእቱ አቀ
ሰለነ ወይሜርየነ ወያሐይወነ በሰኑይ መዋዕል ፤
ወአመ ሣልበት ዕለት ንትነሣእ ። ወእመ ሣልሰት
ዕለት ሦጣ ለነፍስ ውስተ ሥጋሁ እንዲል ፤ ተነ
ሥቶም መጽሐፈ ኪዳንን ፵ ቀን ለሐዋርያት አስተ
ማረ ። ጉባኤ ሠርቶ ግን ያስተማራቸው ሦስት ቀን
ነው ። የትንሣኤ የእግብአተ ግብር የጥብርያዶስ
ወዝንቱ ሣልሱ ለአግዚእነ እንዘ ያስተርአዮሙ
ለአርዳኢሁ እምድኅረ ተንሥአ እሙታን እንዲል ።
በበዛው መናገር ነው እንጂ ሳንዱም ለሁሉቱም ለሦ
ስቱም ባለሟሎቹ ሳይገለጽላቸው አይውልም እያ
ድርም ነበር ፵ው ቀን ሲፈጸም አንተሙስ ንበሩ
ሀገረ ኢየሩሳሌም እስከ ትለብሱ ኃይለ እምአር
ያም ብሎ አዟቸው ዓረገ ። ባረገ ባሥረኛው በተነሣ
ባምሳኛው ቀን መንፈስ ቅዱስን ሰደደላቸው ። አበበ
ዚያ ወጹት ኑሮ ቢሉ ባሥረኛው መዓርግ የገዛን
እና ነበርንና ከጥንተ ቦታተን እንደመለሰን ለማጠ
የቀ ። እንድም በዘጠኙ ከተማ ያሉ መላእክተ ሥጋ
ዌውን ያላወቁ ነበሩና ለጊዜ ቢያስተምር ይህማ እን
ዳኦሆን ፈጣሪ ፍጡር ይመስል እንዱን ሥራውን
ቢሠራ ባንዱ ይዘበበልበታል ወዲያስ ቢያስተም
ራቸው ወጹህስ ቢሰድባቸው ይማነውናል ብሎ
ሐተታ ከቀደመው ይገባል ። እንድም አሥሩን
ቃላተ ፲ን ሕዋሳተ ጠብቄ ስጠኋችሁ
እናንተም ብተጠብቁ ፡ ይሰጣችኋል በማለት
ሐዋርያትም መንፈስ ቅዱስን ተቀብለው ፍሩሃን
የነበሩ ጥብዓን ሆኑ ። ከዛልየት ታደሱ በአእምሮ
ጉለመሱ ምሥጢር ተረዱሙ ፤ ፩ድ ቋንቋ ያውቁ
የነበሩ ፸፩ ቋንቋ ተጨመረላቸው ፡ ዓመት በገዛ
ረተ መኗናቸው ኢየሩሳሌምን አስተማሩ ወነበሩ
ዓመተ ፍጽምተ በኢየሩሳሌም እንዲል ። ከዚህ
በኋላ ፡ ሐሩ ወመሐሩ ያላቸውን ነገር ያውቃሉና
ዕፃ በዕፃ ዛለው ይህነን ዓለም ተካፍለው ለማስተ
ማር በሚወጹበት ጊዜ ምድረ ፍልስጥኤም ለማቴ
ዎስ በዕፃ ደረሰው ፡ ከዚህ ገብቶ
ጌታ ከፅንስ ጀምሮ ያደረገውን ታምራት
ያስተማረውን ትምህርት የሠራውን ትሩ
ፋት ቢነግራቸው እሥራኤል ናቸውና ከአሪት ወደ
ወንጌል ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ ቶመ
ለሱ አመኑ ተጠመቁ ። ትምርት ካልደረሰበት ለማዳ
ረስ ወጥቶ በሚሄድበት ጊዜ በቃል ያለ ይረሳል
ብመጽሐፍ ያለ ይወረሳልና ጻፍልን ብለውት በዚህ

ምክንያት ይጽፋል ፤ አንድም እሱ እንደ አባትነቱ ከራሱ አንቅቶ ይጽፍላቸዋል ። አንድም በኢየሩሳሌም የነበሩ አይሁድ እስጢፋኖስን በደንጊያ ወግረው ከገደሉ በኋላ እስጢፋኖስ ነበር እንጂ ። ባፍና በመጣፍ የማይቻል የቀሩትንስ ሐዋርያት መበተን አይሳነንም ብለዋል ፣ ሐዋርያትም ይኸን ሰምተው እንክስ ንትመየጥ መንገለ አሕዛብ ብለዋል ፤ ያመኑት እኛ ሐዲሳን አትክልት ነን ካልጻፋችሁልን እንደምን ይሆናል ብለዋቸው በዚህ ምክንያት ይጽፋል አንድም ያላመኑት አይሁድ ያመኑትን ክርስቶስን ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም ነው ትሉ ታላችሁ እንጂ ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም መሆኑን እስኪ በፍሬታችሁ ቀጽራችሁ አስረክቡን ብለዋቸዋል አሳትውም በዕውቀተ ፍጹማን አይደሉምና ከማኅበር ግብተ ማስረጃ ቢባናችው ይልኩብኋል ። ሶቤሃኬ ተንሥአ ማቴዎስ ዘመተንሥአተ ማይ ላዕለ እሳተ እንዲል ተናዶ ተነሥቶ በዚህ ምክንያት ይጽፋል አጻጻፉም በስዕት ነገር ነው ክፍለ ዘመኑን ለመናገር ፤ በዘር ዘሩካቤ ተወለደ ብለውታልና ዘእንበለ ይትቃረቡ ተረክበት ፅንሰተ እመንፈስ ቅዱስ ለማለተ ዮሐንስ የአብዮ ብለውታልና ዘኢይደልወኒ ፅጹር ቶታነ አሣዕኒሁ እምእገሪሁ ለማለት ፤ በብዔል ዜቡል ያወፅኦሙ ለአጋንንት ብለውታል በመንፈሰ እግዚአብሔር ያወፅኦሙ ለአጋንንት ለማሰት ፩ዱ እምነቢያት ብለውታልና እግዚእ ነቢያት እንደሆነ ለማጠየቅ ፤ መዋዕለ ጽሒፈት ማቴዎስ ጌታ ካረገ በሦንት ቢሉ ሲፈጸም ዘጠኝ ቢሉ ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዓመት ማርቆስ ጌታ ካረገ ዐሥራ አንድ ቢሉ ሲፈጸም ዐሥራ ሁለት ቢሉ ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ ባራተኛው ዐመተ ። ሉቃስ ጌታ ካረገ ሀያ አንደኛው ተፈጽሞ ሀያ ሁለተኛ ሲጀመር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ ባሥራ አራት ዓመተ ። ዮሐንስ ጌታ ካረገ በሠላሳ በሠላሳ አምስትም ይላል ኔሮን ቄሣር በነገሠ በሰባት ቢሉ ሲፈጸም በስምንት ቢሉ ሲጀመር ። ጸሐፍቱም ሁለቱ ከሐዋርያት ሁለቱ ከአርድእት ናቸው ። ሐዋርያት ጨርሰው እንዲጽፉት ያላደረገ ሁለቱን ከአርድዕት ያጻፈ ስለምን ቢሉ ስለ ክብረ አርድእት ። ጨርሰው ሐዋርያት ጽፈዋት ቢሆን አርድእት ለማስተማር በወጡ ጊዜ እኒህማ የአፍአ ሰዎች እንጂ ናቸው የውስጥማ ሰዎች ቢሆኑ ደጊቱን ሕገ ወንጌልን ባላጻፉቸውም ነበር ብለው አይሁድ ትምርታቸውን ከመቀበል በተከለከሉ ነበርና ፣ ያውስ ቢሆን ጨርሰው አርድእት እንዲጽፏት ያላደረገ ሁለቱን ከሐዋርያት ያደረገ ስለምን ቢሉ ስለ ክብረ ወንጌል ፣ ጨርሰው አርድእት ጽፈዋት ቢሆን ይህችማ እንጂ ተርታ ሕግ ናት ። ደጊቱማ ሕግ ምሥጢረ ታምራትን በቤተ ኢያኤሮስ ምሥጢረ መንግሥትን በደብረ ታቦር ምሥጢረ ምጽአትን በደብረ ዘይት ምሥጢረ ጸሎትን በጌቴሴማኒ ባዩ አዕማደ ምድር በተባሉ በልበ ሐዋርያት እንጂ ቀርታለች እያሉ አይሁድ ደገኛይቱን ሕገ ወንጌልን ከመቀበል በተከለከሉ ነበርና ፣ ያውስ ቢሆን ጸሐፍቱን ከፍ ብሎ አምስት ስድስት ዝቅ ብሎ ሁለት ሦስት ያላደረገ አራት ያደረገ ስለምን ቢሉ ጌታ ባራት በአራት ወገን የሠራው ብዙ ሥራ አለና በዚያ መስሎ ለመናገር በዚያውስ ላይ ሥርዓተ ምድር ተሠርዓ በሥርዓተ ሰማይ እንጂ ይላል ፣ በሰማይ አራት ጸወርተ መንበር ኪሩቤል አሉ ። ምንው ይጸውር ድዱ ወይነብር ጠፈረ ሆኑ አንጉዝ ውስተ እዴሁ ለጽናፌ ዓለም በአራሁ እንዲል ። እሱ ይሸከሟቸዋል እንጂ እሳቸው ይሸከሙታል ቢሉ ። ዘፈቀደ የሚገለጽላቸው መንበሩን ተሸክመው የሚታዩ የሚቀድሱት በጸጋ የሚያድርባቸው ስለሆነ እንዲህ አለ እንጂ የሚሸከሟቸውስ እሱ ነው ። እሊህም ገጸ ብእሲ ገጸ አንበሳ ገጸ ላህም ገጸ ንስር ናቸው ። ማቴዎስ በገጸ ብእሲ ይመሰላል ። ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም እያለ ሥጋዊ ልደቱን ይጽፋልና ማርቆስ በገጸ አንበሳ ይመሰላል አንበሳ ኑሮው ከሰው ርቆ በምድረ በዳ ነው ከዚያ ሁኖ ጣሕሩን በሰማ ጊዜ አንስሳት ይገሠጻሉ አራዊት ይደነግጣሉ ። ማርቆስም ከትምርተ ምድረ በዳ በምትሆን በግብጽ ቀዳሚሁ ለወንጌል እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ብሎ ባስተማረ ጊዜ ምእመናን ተገሥጸዋል አጋንንት መናፍቃን ደንግጸዋልና ፣ ዳግመኛም አንበሳ ለላህም ጌታው ነው ይሰብረዋል ። እሱም ከግብጽ አምልኮተ ላህምን አጥፍቷልና ፣ ከትምርተ ምድረ በዳነቷንም ከዚህ ይናገራሉ ፣

ቀድሞ ሙሴ አሮን ኋላም እለ ኤርምያስ ወርደው ቢያስተምሯት አልተጠቀመችም ፍጹም ጥቅሟ በማርቆስ ነውና ፤ ሉቃስ በገጸ ላህም ይመሰላል ። አምጽኡ ላህመ መግዝእ ወጥብሑ ንብላዕ ወንትፈግሕ ምስሌሁ ዕያለ ምሳሌውን ይጽፋልና ዮሐንስ በገጸ ንስር ይመስላል ንስር በእግሩ ይሸከረክራል በክንፍ መጥቆ ይበራል በእግር እንዲያሽረክር እሱም እንደ ወንድሞቹ ወልደ እጓለ እመሕያው ወረደ እምሰማይ ብሎ ይጽፋል ። በክንፍ መጥቆ እንዲበር እሱም አካል ከሀልውና ተገልጸለት ቀዳሚሁ ቃል ብሎ ተናግሯልና ። አንድም እንስር ዘኸሙር በብርሃን አዕይንቲከ እንዲል ፤ የንስር ዓይኑ ጽሩይ ነው ሽቅብ ወጥቶ ረቦ ቁልቁል በተመለከተ ጊዜ የበናፍጭ ቅንጣት ታህል ሥጋ ብትሆን አትሰወረውም ያችን አንሥቶ ይመገባታል ። እሱም አካል ከሀልውና ተገልጾለት ንጹሐ ሥጋ ንጹሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና ተሰጥቶት ቀዳሚሁ ቃል ብሎ ተና

ገሯልና አቃወማቸውንም ከዚህ ይናገራሉ ገጸ ብእሲ
አቀዋወሙ በምሥራቅ ፊቱ ወደ ምዕራብ ። ገጸ
አንበሳ አቀዋወሙ በምዕራብ ፊቱ ወደ ምሥራቅ ።
ገጸ ላህም አቀዋወሙ በሰሜን ፊቱ ወደ ደቡብ ፤
ገጸ ንስር አቀዋወሙ በደቡብ ፊቱ ወደ ሰሜን ፤
ማቴዎስ ጽፎ ለማርቆስ ደቀ መዛሙርት ፤ ማር
ቆስ ጽፎ ለማቴዎስ ደቀ መዛሙርት ፤
ሉቃስ ጽፎ ለዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ዮሐ
ንስ ጽፎ ለሉቃስ ደቀ መዛሙርት መስጠታቸ
ውን መናገር ነው ። ወንጌል በጥንተ ስብከት
የደረሰችበትን መናገር ነው እንጂ ኋላስ ከሁሉ ደር
ሳለች ። በ፬ቱ አፍላጋት ይመስላሉ ። እሊህ ከገነት
ካንድ ከዕፀ ሕይወት ሥር ነቅተው ውኀነታቸውን
ይህን ዓለም ዙረው አጠጥተው ዕፀዋትን ከይብ
ሰት ወደ ልምላሜ ከልምላሜ ወደ ጽጌ ከጽጌ ወደ
ፍሬ ያደርሳሉ ። አራቱ ወንጌላውያንም ወንጌልን
ካንድ ከጌታ ቱምረው ይህን ዓለም ዙረው አስተም
ረው ምእመናንን ከይብሰተ ኃጢአት ወደ ልምላሜ
ንስሐ ከልምላሜ ንስሐ ወደ ጽጌ ትሩፋት ከጽጌ
ትሩፋት ወደ ፍሬ ክብር ያደርሳሉና ፤ እኒህም ኤፌ
ሶን ግዮን ጤግሮስ ኤፍራጥስ ናቸው ። ኤፌሶን
ፈለገ ሀሊብ ነው ። ርስትነቱም የሕፃናት ርስት ነው
ማቴዎስ በዚህ ይመስላል ። ከመ ሀሊብ ሀለብክኒ
ወከመ ግዕት አርጋዕከኒ እንዲል ። በዘር የሚመ
ለዱ የነገሥታትን ልደት ይጽፋልና ፤ ዳግመኛ ሄሮ
ድስ ያስፈጃቸውን የሕፃናትን ነገር ይናገራልና ፤
ግዮን ፈለገ ወይን ነው ርስትነቱም ቢጾሙ ቢሰ
ለዩም ሥራቸውን ደስ ብሏቸው የሚሠሩ ሰዎች
ርስት ነው ። ማርቆስ በዚህ ይመስላል ። ወይን
ያስተፌሥሕ ልበ ሰብእ እንጂ ይላል ወንጌሉን
ሁሉን ደስ በሚያሰኝ በዕርገት ይጨርሳልና ። በዚ
ህስ ሁሉም ይተባበሩበታል ብሎ ቅብዓ ትፍሥሕት
መንፈስ ቅዱስ በሚሰጥበት በጥምቀት ይጀምራ
ልና ፤ ጤግሮስ ፈለገ መዓር ነው ርስትነቱም ጸዊረ
ነገር የሚቻላቸው ሰዎች ርስት ነው ። ሉቃስ በዚህ
ይመስላል ። መዓር እንጂ ከቡድ ነው ። እሱም አባ
ስረይ ሎሙ እስመ በዘኢየአምሩ ይገብሩ በትዕግ
ሥትክሙ ታጠርይዋ ለነፍስክሙ እያለ ከቡድ
ከቡድ ነገር ይጽፋልና ፤ ኤፍራጥስ ፈለገ ዘይት ነው፤
ርስትነቱም የሰማዕታት ርስት ነው ። ዮሐንስ በዚህ
ይመስላል ዘይት ጽኑዕ ነው ። እሱም ጽንዑ እስመ
አነ ሞእክዎ ለዓለም እያለ ይጽፋልና ። ዘይት ብሩህ
ነው የሰውን ልቡና በትምህርቱ ብሩህ ያደርጋልና
ዳግመኛም ዘይት አራቱን ሽቱ ስቦ በመዓዛ አንድ
ያደርጋቸዋል ፤ እሱም ወንድሞቹን በምሥጢር
ይበዘብዛቸዋልና ነቅዓቸውንም ከዚህ ይናገራሉ ፤
ቦ ዘይወፅእ እምሥራቅ ወየሐውር ለምዕራብ ከመ
ይስቂ ዘህየ ። ቦ ዘይወፅእ እምዕራብ ወየሐውር ለም
ሥራቅ ከመ ይስቂ ዘህየ ፤ ቦ ዘይነቅዕ እምሰሜን
ወይሠወጥ ለደቡብ ከመ ይስቂ ዘህየ ። ቦ ዘይነቅዕ
እምደቡብ ወየሐውር ለሰሜን ከመ ይስቂ ዘህየ እን
ዲል ። ማቴዎስ ጽፎ ለማርቆስ ደቀ መዛሙርት ፤
ማርቆስ ጽፎ ለማቴዎስ ደቀ መዛሙርት ፤ ሉቃስ
ጽፎ ለዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ፤ ዮሐንስ ጽፎ ለሉ
ቃስ ደቀ መዛሙርት መስጠታቸውን ወንጌል በጥ
ንተ ስብከት የደረሰችበትን መናገር ነው እንጂ ።
ከዚህ በኋላስ ከሁሉ ደርሳለች ፤ በ፭ቱ ነፋሳተ ምሕ
ረት ይመስላሉ ፤ ፭ቱ ነፋሳተ ምሕረት ፤ ለሰው ሕይ
ወት ጽንዕ ይሆናል ፤ ሕይወት ለመሆናቸው እስመ
ነፋሳት ነፍሳቲሆሙ ለማያት እስመ እምሁከተ ነፋ
ሳት ንስሕቦ ለቁመተ ሥጋነ ፤ እስመ ነፋስ
ያገዝፎ ለፍሬ እንዲል ጽንዕ ለመሆናቸው ወገብረ
አዕማደ ሰማይ በነፋስ ። ወይዔምድ በነፋስ እሉ
አሙንቱ እለ ይረብብዋ ለልዕልና ሰማይ ይላል ።
እኒህም በነፈሱ ጊዜ ለሰው አምስት ነገር ይመጣ
ለታል ፤ ጠል ዝናም ሕይወት በረከት ፈውስ ፤
አራቱ ወንጌላውያንም ባስተማሩ ጊዜ ለሰው አም
ስት ነገር ይገኛልና እንደ ጠል ትምህርት እንደ ዝናም
ሥጋው ደሙ እንደ ሕይወት ሕይወት መንፈሳዊ
እንደ በረከት በረከት መንፈሳዊ ፤ አንድም መሳውም
በረከተ ኀብስትን ይጽፋሉና እንደ ፈውስ ፈውስ
መንፈሳዊ አንድም ፈውስ ንስሐ ፬ቱ ነፋሳተ ምሕ
ረት ያለሙትን የሚያጠፉ ያለመለሙትን የሚያደ
ርቁ ፭ ነፋሳተ መዓት አሉ ። እሊህም በነፈሱ
ጊዜ በሰው አምስት ነገር ይመጣል ፤ ይብሰት ሐሩር
ድምሳሴ አንበጣ አናኩዕ ፬ቱ ነፋሳተ ምሕረት ያለ
መለሙትን የሚያደርቁ ያለሙትን የሚያጠፉ ፭ት
ነፋሳተ መዓት እንዳሉ ። ፬ቱ ወንጌላውያንም ያስተ
ማሩትን የሚያስከዱ ያለሙተ የሚያጠፉ ፤ ፭፤ ቤተ
አይሁድ አሉ ። ኃጥአን መጸብሐን ፤ ጸሐፍት ፈሪሳ
ውያን ሰዱቃውያን ረበናት መገብተ ምኩራብ ሊቃነ
ካህናት ሞላሕቅተ ሕዝብ ፤ አልመተ ዝዕላን የሚል
አብነት ይገኛል መላሕቅተ ሕዝብ ማለት ነው እኒሀ
ባስተማሩ ጊዜ በሰው ፭ ነገር ይታዘዛል ። እንደ ይብ
ሰት ይብሰተ አእምሮ እንደ ሐሩር መከራ እንደ
ድምሳሴ ደጋግ ሰዎች በሥጋቸው ክፉ ሰዎች በነፍ
ሳቸው የሚጎዱ ሁነዋል ። እንደ አንበጣ ዓላዊ ንጉሥ
መናፍቅ ጳጳስ እንደ አናኩዕ ብዝኃ ሠራዊት ፤ ፭ቱ
ነፋሳተ መዓት በ፬ቱ ነፋሳተ ምሕረት ተወስነው ተገ
ተው እንዲኖሩ የ፭ ቤተ አይሁድም ትምህርት በ፬ቱ
ወንጌላውያን ትምህርት ተወስኖ ተገቶ ይኖራልና
ባራቱ ባሕርያት ይመስላሉ ካራቱ ባሕርያት የወጣ
ፍጥረት የለም ከ፬ቱ ወንጌላውያንም ትምህርት የወጣ
የለምና በ፬ቱ መዓዝነ ዓለም ይመስላሉ ከ፬ቱ መዓ
ዝነ ዓለም የወጣ ፍጥረት የለም ካራቱ ወንጌላውያንም
ትምህርት የወጣ የለምና በ፬ቱ ከዋክብት ይመስላሉ
ሕልመልሚሌክ ምልክኤል ምልኤል ናርኤል ይባ

ለሉ ። እሊህ ዓመቱን ካራት ይከፍሉታል ዘጠና
አንድ ቀን ከ፲፰ ኬክሮስ ፺፩ ቀን ፤ ካሥራ አምስት
ኬክሮስ ይደርሳቸዋል ፀሐይን ተከትለው ሥጋዊ
ምግብ ይመግባሉ አራቱ ወንጌላውያንም ዘመኑን
ካራት ተካፍለው ፀሐየ ጽድቅ ኢየሱስ ክርስቶስን
ተከትለው መንፈሳዊ ምግብና ይመግባሉና ባራቱ
ክፍለ ዘመን ይመስላሉ ፣ ጸደይ ከረምት መፀው
ሐጋይ ናቸው ጸደይ ወርኃ ዘርዕ ፣ ነው ። ማቴዎስ
በዚህ ይመስላል ምሳሌ ዘርእን ከሁሉ ይልቅ
እምልቶ ፣ አስፍቶ አብዝቶ ጽፋልና ዳግመኛም
ወርኃ መሬት ነው ። እሱም ምድራዊ ልደቱን ይጽ
ፋልና ከረምት ወርኃ ማይ ነው ። ማርቆስ በዚህ
ይመስላል ፣ እሱም በጥምቀት ይጀምራልና መፀው
ወርኃ ነፋስ ነው ። ሉቃስ በዚህ ይመስላል በአም
ሳለ ነፋስ የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስን ነገር መንፈስ
እግዚአብሔር ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ ወኃይለ ልዑል
ይጼልለኪ እያለ ይጽፋልና ፣ ሐጋይ ወርኃ እሳት
ነው ። ደረቅ ነው ዮሐንስ በዚህ ይመስላል መስ
ተፃርር መስተቃርን የሌለበት ደረቅ ቃል ፤ ቀዳሚሁ
ቃል እያለ ይጽፋልና ባ፬ቱ አንስተ ያዕቆብ ይመ
ስላሉ ልያ ባላ ዘለፋ ራሄል ይባላሉ ። ማቴዎስ በልያ
ይመስላል ። በመጀመሪያ እንደወለደች እሱም ከሁሉ
አስቀድሞ ይጽፋልና ማርቆስ በባለ ዓመተ ራሄል
ይመስላል ። ከልያ ቀጽላ እንደወለደች ከማቴዎስ
ቀጽሎ ይጽፋልና ። እሷ እመቤቷን አህላ መስላ
እንደወለደች እሱም ቀዳሚሁ በማለት ጌታው ዮሐ
ንስን ይመስላልና ። ሉቃስ በዘለፋ ዓመተ ልያ ይመስ
ላል ከባላ ቀጽላ እንደወለደች ከማርቆስ ቀጽሎ ይጽ
ፋልና ። እሱዋ እመቤቷን አኽላ መስላ እንደወለ
ደች ምንም እሱ ሽቅብ እሱ ቁልቁል ቢቆጥሩ
ልደተ አበውን በመቍጠር ጌታው ማቴዎስን ይመ
ስላልና ። ዮሐንስ በራሄል ይመስላል ከሁሉ በኋላ
እንደወለደች ከሁሉ በኋላ ይጽፋልና ። እሱዋን
ፍቅርት በኀበ ያዕቆብ ይላታል ። እሱንም ረድእ
ዘያፈቅሮ ይለዋልና ፣ በ፬ ብሔረ ነገሥት በ፰ቱ ብሔረ
አረት ይመስላሉ ይህ ሁለት አራት ይሆናል እንዲህ
ያለስ ብዙ አለ ብሎ ሙሴ አራት አድርጎ የጻፈውን
ኃይለ ቃሉን አወጻጽቶ አንድ አድርጎ ጽፎ ዳግም
ሕግ ብሎታል ። ወንጌልም አራት ሁና ተጽፋ አንድ
ሕግ ለመባሏ ምሳሌ ነውና በ፰ እቀብተ ቤተመቅደስ
ይመስላሉ ፬ት ፰ት ይሆናሉ እንዲህ ያለስ ብዙ
አለ ብሎ ፰ት ፬ት ይሆናሉ ሁለቱ ከውስጥ ሁነው
ተወካፍያነ መባዕ ናቸው ፯ቱ በአፍአ ሁነው ኢይባዕ
ሞጻብዊ ወአሞናዊ እስከ ግልስ ወራብዕ ትውልድ
ያለውን ይጠብቃሉ አራቱ ካምስቱ አራቱ ከስድስቱ
አራቱ ከሰባቱ ቆመ ብእሲ ይሆናሉ ፣ እኒህ ካምስት
ቦታ ሁነው የማይገባውን እንዳይገባ እንዲከለክሉ
አራቱ ወንጌላውያንም ፰ቱን አእማደ ምሥጢር ፤
እስተምረው ከምእመናን ልቡና ክህደት ኑፋቄ እን
ዳይገባ ይከለክላሉና ፤ በ፬ መሠረታተ ቤተ መቅደስ
ይመስላሉ ፥ ከታች ድልድሉ ሰባት ክንድ ነው በዚ
ያው ላይ ባ፰ት ሰው ቁመት ልክ በዚያ ላይ በ፯ት
ሰው ቁመት ልክ በዚያ ላይ በ፯ት ሰው ቁመት ልክ
በዚያ ላይ ቤተ መቅደስ ታንጿል በቤተ መቅደስ
ላይ ብርሃን ሰፍሮ ይታይ ነበር ። ፬ መሠረት
ያ፬ቱ ወንጌላውያን ። መቅደስ የምእመናን ። ብር
ሃን የጌታ ምሳሌ ። ፬ቱ ወንጌላውያን ባስተማሯቸው
በምእመናን ጌታ ለማደሩ ምሳሌ ። በ፬ቱ
ገጸተ ኵሉሕ ባራቱ ገጸተ ታቦት ይመስላሉ ።
ወንጌል ለሆግዕና ባራት መዓዝን ትነበባለችና ይህስ
ሁሉ መዓዝነ ዓለም ካለው ይገባል ብሎ ወንጌል
መሠረቷ ስለ አራት ነገር ነውና ። ለጥምቀት ለተ
ክሊል ለፍታት ለቍርባን ። መዋዕለ ጽሕፈት ተና
ግረናል ። አገርም ማቴዎስ በፍልስጥኤም ጀምሮ
በህንድ ጨርሱዋል ። ወፈጸማ በህንድ እንዲል ። ማር
ቆስ በግብጽ በሮምም ይላል ። ሉቃስ በመቄዶንያ
ዮሐንስ በኤፌሶን ። ልሳንም ማቴዎስ
በዕብራይስጥ ማርቆስ በሮማይስጥ ሉቃስና ዮሐንስ
በዮናኒ ። ዮሐንስን ለይቶ በፅርእ ይላል እንደ በቅላ
እንደ ሐማሚን ጥቂት ጥቂት የልሳን መለያየት ነው፣
ወንጌልሂ ሶበ ተጽሕፈ ፩ዱ እምእከለ ወየእከ
ልሂ ይላል ፣ ወንጌል ካራቱ አንዱ ቢጻፍ በበቃ ነበር
ለልጅ ልጅም ይበቃ ነበር ይህስ እንዳይሆን
ካንዱ የሌለው ካንዱ አለ ፣ ካንዱ ያለው ካንዱ
የለም ብሎ ሶበ ተጽሕፈ ፩ዱ ። አራቱ አንድ ሁኖ
ቢጻፍ በበቃ ነበር ፣ ለልጅ ልጅም ይበቃ ነበር ቦታ
አንድ ሳያደርጋቸው ዘመን ሳያገናኛቸው ቋንቋ ሳያ
ጋጥማቸው አራት አድርገው ጽፈውት አንድ ሁኖ
ቢገኝ የእግዚአብሔር ነገሩ የመንፈስ ቅዱስ ምሥ
ጢሩ እንደሆነ ሊታወቅ አራት አድርገው ጽፈውታል
እንጂ ሶበ ተጽሕፈ ፩ዱ እም እከለ ወየእከልሂ ፤
ከዚህም ሥጋዊ ምግብናን ከሦስት እንደከፈለ መን
ፈሳዊ ምግብና ከሦስት ከፈለ ሰው ከተወለደ ጀምሮ
እስከ ሃያ ዓመት ያለው ምግበ ነፋስ ነው ብር ብር
እያለ የሚሠራውን አያውቅም ። ወኢይከል ያእምሮ
ዘውስተ ነፍሱ እንዲል ። ከሃያ እስከአርባ ያለው
ዘመን ምግበ እሳት ነው ማወቁን ያውቀዋል እየተ
ናደደ ይሠራዋል ። ከአርባ እስከ ስሳ ያለው ምግበ
ማይ ነው ሰውነቱ እየደከመ ይሄዳል ፣ ተመልሶ የሕ
ፃንነቱን ሥራ ልሥራ ቢል አይቻለውም ከተወለደ
እስከ ሃያ ዘመን ያለው ከአዳም እስከ ሙሴ ያለው
ዘመን አበው ነው ። የሚሠራውንም ሥራውን እን
ዳያውቀው ጽድቅና ኃጢአት ተለይቶ አይታወቅም
ነበር ምንም እነ ሄኖክ እነ ኢዮብ አንድ አንድ ሰዎች
ቢያውቁት ፣ ዛሬ ከቤተ መንግሥት የተመከረውን
ምክር ሁለት ሦስት ባለሟሎች ቢያውቁት እንጂ

ሙቱ እንዲያመተው ፤ ከሃያ እስከ አርባ ያለው ዘመን አራት ነው ፤ እየተናደደ ዐውቆ እንዲሠራው በአራትም ጽድቅና ኃጢአት ተለይቶ ታውቋል። ሰው እልክ እየገባ የሚሠራው ሁኑዋልና ፤ ወኃ የሰ ገቡ ሕገ ኃጢአት ዘውስተ አባልየ ወፄወወኒ መንገሌሁ እንዳል ካርባ እስከ ስሳ ያለው ዘመን ወንጌል ነው ፤ ሰውነቱ እየደከመ እንዲሄድ ኃጢአት ወጥቷል ። ወደከመ ሕጉ ለኃጢአት እንዳል ተመልሶ የኃጢነቱን ሥራ ልሥራ ቢል እንዳይቻለው መንገሌንም ሊለውጣት የተቻለው የለምና ። ይኸን አርባዕት ፫ ፯ ሰጥተዋል በምን ምክንያት ቢሉ ሰማትልተያናስ መክስምያናስ የሚባሉ ሁለት ዓላውያን ነገሥታት ተነሥተው አብያተ ጣዖታት ይትረኃዋ አብያተ ክርስቲያናት ይትዓፀዋ ብለው ዐዋጅ ነገሩ ። አብያተ ክርስቲያናት ተተኩሱ መጻሕፍት ረለሱ ። ከምእመናንም ወገን የሚሞቱት ሞቱ የሚፈልሱትም ተሰደዱ ። ዘመኑም አርባ ዘመን ነው [illegible] የቀንዋ ዘመን ሰገዐታት ብለው [illegible] መናፍቅ ፒዮማናት ራትዕ ንጉሥ ቈስጢናስን እንዲሞላቸው ወገድ ዓዋጅ መስለው አብያተ ክርስቲያናት ይትረኃዋ አብያተ ጣዖታት ይትዓፀዋ ብሉ ፤ በዘመኑ

አርዮስ ወልድ ፍጡር በመለኮቱ ብሎ ተነሣ ። በዚህ ምክንያት ጉባኤ በኒቅያ ይሁን ብሎ ዐዋጅ ነገረ። ሦስት መቶ ዐሥራ ስምንት ሊቃውንት ተሰብስበው አርዮስን አውግዘው ለይተው ሃይማኖት መልሰው እጽንተው በሚለያዩበት ጊዜ ለመጻሕፍት ሁሉ አርእስት ሰጥተዋል ። መልእክተ ያዕቆብ መልእክተ ጴጥሮስ መልእክተ ዮሐንስ መልእክተ ይሁዳ መልእክተ ጳውሎስ ፤ ብሥራተ ማቴዎስ ብሥራተ ማርቆስ ብሥራተ ሉቃስ ብሥራተ እብ ፤ ትሩፍ ረድእ ተናጋሪ በመለኮት ዮሐንስ ወልደ ዘብዴዎስ ፍቁረ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ብለው ስለምን ቢሉ የጻሐፊው ደግነት የታወቀ እንደሆነ የመጽሐፉም ፥ ደግነት ይታወቃል ብለው ይደልዎ ለዘያነብብ ቅድመ ይዝክር ስሞ ለበዓለ መጽሐፍ ወእምዝ ያንብብ ወይምሀር እንዲል ። ወንጌል ብሥራት ስብከት ቢል አንድ ነው ፡ ወንጌል ብሂል ቢልሳነ ጽርእ ወትርጓሜሁ ሰብከት እንዲል ፡ ዲያብሎስ እንደተሻረ ወልደ እግዚአብሔር እንደነገሠ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ እንደጠፉ ትናገራለችና ልምናው ክብሩ ይደርብንና ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ ማቴዎስ የጻፈው ወንጌል ይህ ነው፡፡

## የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል
## ቅዱስ ማቴዎስ እንደ ጻፈው ።

### ምዕራፍ ፩ ።

፩ መጽሐፈ ልደቱ ለእግዚእነ ኢየሱስ
ክርስቶስ ።

ወንጌላውያን ሲጽፉ ራሳቸውን መሠረት አያ
ደርጉም ሌሎች ግን ራሳቸውን መሠረት ያደር
ጋሉ ምንም የሚገልጽላቸው መንፈስ ቅዱስ
ቢሆን የሚጽፉ ከራሳቸው አንቅተው ነውና
ዳግመኛ ካንድ አገር ሁነው ጽፈው ወደ አንዱ
አገር ይሰዱታልና ። ወንጌላውያን ግን የሚ
ጽፉ ጌታ የተናገረውን ነው እንጂ ከራሳቸው
አንቅተው አይደለምና በመካከል ሁነው ይጽ
ፋሉና ፤ ዳግመኛ ምንም አንዱም አንዱ ወሀሎ
፩ዱ ብእሲ ቢል ነገር ለማያያዝ ነው ።

፪ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ የልደቱ ቍጥር
ይህ ነው ። ጸሐፊዮ ለብእሲ ከመ ዘሞተ ወበ
ውእቱ መዋዕል ወፅአ ትእዛዝ እምኀበ አው
ግስጦስ ቄሣር ከመ ይጸሐፍ ኵሉ ዓለም እን
ዲል ፣ እንድም የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ
የልደቱ ወግ ታሪክ ይህ ነው፤ ስማ ለዳቤር ትካት
ሀገረ መጽሐፍ እንዲል ፣ የወግ የታሪክ ሀገር
ሲል ፣ ወግ የነትእማርን የነራኬብን የሩትን
ያመጣል ። ታሪክ ወለእግዚእነ ኢየሱስ ክር
ስቶስ ከመዝ ውእቱ ልደቱ ብሎ ያመጣል ፣
ልደቱ ለእግዚእነ አለ ፣ ብዙ ልደታት አሉና
ከዚያ ሲለይ ፣ ልደተ አዳም እምድር ልደተ
ሔዋን እምገቦ ። ልደተ አቤል እምከርሥ ልደተ
በግዕ እምዕፅ ፣ ልደተ ሙታን እመቃብር አለ።
እኒያ አውጭ ይሻሉ ። እሱ ግን በገዛ ሥልጣኑ
ነውና ፣ የልደቱን ነገር ብቻ ይናገራልና መጽ
ሐፈ ልደቱ አለ ምነው ቢሉ ፣ መጽሐፍ ባንድ
መጀመር ኋላ ብዙ ማምጣት ልማድ ነው ።
ከዚያ ሁሉ አሪት ዘልደት ይላል። የሥነ ፍጥ
ረትን ብቻ ተናግሮ ይቀራልን መጽሐፈ ልደቱ
ባለው በጥቂር አንድ ይላል የንኡስ ምዕራፍ
አኃዝ ነው ፤ ማቴዎስ መጽሐፈ ልደቱ ማር
ቆስ አንተ ውእቱ ወልድየ ፣ ሉቃስ ወይመስ
ሎሙ ወልደ ዮሴፍ ዮሐንስ ቀዳሚሁ ቃል
ያለውን ሁሉም የጌትነት ነገር ከሆነ ብሎ
አራቱ የተባበሩበት ሲል ፩ዱ ይላል ፣ ፫ቱ
ቢል ማርቆስን አውጥቶ ፣ በሦስተኛው ሰንጠ
ረዥ ማርቆስ ስምና ፤
ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም ሉቃስ ም ፫፡ቍ፡፴፩
የዳዊት ልጅ የአብርሃም ልጅ ከነገሥታት ዳዊት
ከአበው አብርሃም ብቻ ይወልዱታልና እን
ዲህን አለ ቢሉ ፤ ትንቢት የተነገረ ለኒህ
ነውና ፣ ትንቢትማ ከነገሥታት ለሰሎሞን
አነ እከውኖ አባሁ ወውእቱ ይከውነኒ ወል
ድየ ተብሎ ፤ ከአበውም ለሴም ለይኅድር
እግዚአብሔር ውስተ ቤቱ ለሴም ተብሎ ተነ
ግሮ የለም ቢሉ የሚበዛ የዚህ ነውና ፣ በሚ
በዛው ተናገረ ። እንድም ተስፋ ለተስፋ ሲያ
ነጽር በዘርእ ይትባረኩ ፣ ኵሎሙ አሕዛበ
ምድር ያለውንና ፤ አስመ እምፍሬ ከርሥከ
አነብር ያለውን ተስፋ ለተስፋ ሲያነጻጽር ።
እንድም ዳዊት ሥርወ መንግሥት ነው። አብርሃ
ምም ሥርወ ሃይማኖት ነውና ። አስመ አብ
ርሃም ኮነ ሥርወ ሃይማኖትን ወሃይማኖቶሙ
ለአይሁድ እንዲል ። የዳዊትን ሥርወ መን
ግሥትነት ኋላ ያመጻል፤ እንድም እግዚአብሔር
ፈጣሪያቸውን ዳዊት ንጉሣቸውን ቢያነሣላቸው
ይወዳሉና ወየኃሥሥዎ ለእግዚአብሔር አም
ላኮሙ ወለዳዊት ንጉሦሙ እንዲል ፤ ዳዊትንም
ከመውደዳቸው የተነሣ የነገሠውን ሁሉ ዳዊት
ይሉት ነበር ። ወሶበ ሰምዓ ዘንተ ዳዊት ደንገ
ፀት ነፍሱ ወነፍስ ኵሉ ሕዝቡ እንዲለው
አካዝን ፤ እንድም ያላመኑት ያመኑትን ወልደ
ዳዊት ወልደ አብርሃም መሆኑን ስፍራችሁ
ቈጥራችሁ አስረክቡን ብለዋቸው ነበርና ስለ
ዚህ እንዲህ አለ ፤ ከፍለ ዘመንም ለመናገር፤
በዚያውስ ላይ አብርሃም አይቀድምም ዳዊት
አይከተልም ቢሉ ፤ አባቱን አያውቅ አያቱን
ናፈቀ ይሉኛል ብሎ ለጌታም ከአብርሃም ዳዊት
ይቀርበዋልና ። እንድም እርካብ ተረግጦ
ወደ ኮር መውጣት ባዳራሽ ገብቶ ወደእል
ፍኝ ማለፍ እንዲመች ። ወልደ ዳዊት ብሎ
ወልደ አብርሃም ሲሉ ይመቻልና ። እንድም
ጌታን ወልደ ዳዊት ዳዊትን ወልደ አብርሃም
አለው እንድም ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም
ዋዌ የቀረው ነው ፣ እንድም የጌታ ጥቅል ስሙ
ነው ፤ ዕውራን በሆሣዕና ተማሃለነ ወልደ
ዳዊት እንዳሉ ። ወልደ አብርሃም ብሎ ለጌታ
ቀጸለለት ፣ እንድም ይዞ ለመሄድ ይመቸኝ

ብሎ ይዞት የሚሄድ አብርሃምን ነውና ወደ ኋላ አደረገው ።

፪ አብርሃም ወለዶ ለይስሐቅ ፤

፪ አብርሃም ይስሐቅን ወለደው ።

ከአጋር የተወለደ እስማኤል ከኬጡራ የተወለዱ ፮ቱ ሕፃናት ያሉ አይደለምን ስለምን ይስሐቅን ለይቶ አነሣው ቢሉ ነቢይ የሆነ እንደሆነ ልደተ አበውን ጠንቅቆ ይቆጥራልና መላውን ያነሣል ። ወንጌላዊ ግን የሚሻ የጌታን ልደት ነውና ። የጌታም መወለድ ከይስሐቅ ነው እንጂ ከነዚያ አይደለምና ። አንድም ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ። ትንቢት እምይስሐቅ ይስመይ ለከ ዘርዕ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌ ይስሐቅ መሥዋዕት ሁኖ ቀርቧል ። ጌታም መሥዋዕት ሁኖ ይቀርባልና ወይስሐቅኒ ወለዶ ለያዕቆብ ፤ ይስሐቅም ያዕቆብን ወለደ ። እነዚያስ ዕለት እናት ባያገናኛቸው ነው እኒህማ ዕለት እናት አገናኝቷቸው አንድ ቀን ተፀንሰው አንድ ቀን የተወለዱት ኤሳውን ስለምን ለይቶ ተወው ቢሉ ። ነቢይ የሆነ እንደሆነ ልደተ አበውን ጠንቅቆ ይቆጥራልና መላውን ያነሣል ፤ ወንጌላዊ ግን የሚሻ የጌታን ልደት ነውና ። የጌታም መወለድ ከያዕቆብ ነው እንጂ ከኤሳው አይደለምና ። አንድም ፤ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ። ትንቢት ኮከብ ይሠርቅ እምያዕቆብ ወያእትት ኃጢአተ እምእሥራኤል ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም በጸውየተ ሐዋርያት አብዝተው ያመጣሉ ከዚያው ከፍለው ይናገሩታል ። ያዕቆብ ከወንድሙ ከኤሳው ተጣልቶ ወደ አጐቱ ወደ ላባ ሲሄድ ከምንጭ አጠገብ ደረሰ ። ውኃው ደንጊያ ተገጥሞ አባግዕ ከድንጊያው ሰፍረው ኖሎት ተሰብስበው አገኘ ። ምነው ከፍታችሁ አታጠጧቸውም አላቸው። መላው ኖሎት እንጂ ካልተሰበሰቡ ከፍቶ ማጠጣት አይሆንልንም አሉት ። ውኃው ኩሬ ነው ጠላት ጥቂት ራሱን ሁኖ መጥቶ መርዝ እንዳይበጠብጥበት ለ፵ ለ፷ የሚከፈት ደንጊያ ገጥመው ይሄዳሉ ። እሱ ብቻውን ከፍቶ አጠጥቶላቸዋል ያዕቆብ የጌታ ። ደንጊያው የመርገመ ሥጋ የመርገመ ነፍስ ። ውኃው የጥምቀት ። አባግዕ የምዕመናን ኖሎት የነቢያት የካህናት ምሳሌ ። ወያዕቆብኒ ወለደ ይሁዳሃ ወአኃዊሁ ። ዘፍ ፤ ፳፭ ፤ ፫ ፤ ፳፩ ፤ ፳፭ ፳፱፤ ፴፰ ያዕቆብም ይሁዳን ወንድሞቹን ወለደ የይስሐቅን ልደት በተናገረ ጊዜ እለ እስማኤልን የያዕቆብን ልደት በተናገረ ጊዜ ኤሣውን አላነሣም ከዚህ አሁን ደርሶ ይሁዳሃ ወአኃዊሁ አለ ምነው ቢሉት ጌታ ካሥራ ሁለቱ ነገድ ይወለዳልና ፤ አንድም ነቢይ ቢሆን አባቶቻችንን ከቍጥር አይለያቸውም ነበር ወንጌላዊ ስለምን ለይቶ ተዋቸው ብለው አይሁድ ደገኛይቱን ሕገ ወንጌልን ከመቀበል በተከለከሉ ነበርና አንድም ለምሳሌ ይመቸኝ ብሎ ካሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል ያልተወለደ ምግድረ ርስትን አይወርስም ። ያሥራ ሁለቱ ሐዋርያትንም ትምህርት ያልተቀበለ መንግሥተ ሰማያትን አይወርስምና ያውስ ቢሆን ይሁዳን ለይቶ ማንሣቱ ስለምነው ቢሉ ቅንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም። ትንቢት ኢይጠፍዕ ምስፍና ወምልክና እምእባሉ ለይሁዳ እስከ አመ ይረክብ ዘጽኑሕ ሎቱ ተብሎ ተነግሯል ፤ ምሳሌውን አሁን ያመጣል ። ዘፍ ፵ ፱ ፲ ።

፫ ወይሁዳኒ ወለደ ፋሬስሃ ወዛራሃ እምትዕማር ዘፍ ፤ ፴፰፡፳፱ ፩ዜና ፪፥፬ ፤ ሩት ፬፡፲፰ ፤ ፩ነገ፡፪፥ ፭

፫ ይሁዳም ፋሬስን ዛራን ከትዕማር ወለደ ። የይስሐቅን ልደት በተናገረ ጊዜ ሳራን ፤ የያዕቆብን ልደት በተናገረ ጊዜ ርብቃን ፤ የይሁዳን የወንድሞቹን ልደት በተናገረ ጊዜ እለ ልያን እለ ራሔልን አላነሣም አሁን ደርሶ እምትዕማር አለ ምነው ቢሉ ይህች ምክንያት ያላት ናት ። ይሁዳ ሴዋ የምትባል ሚስት አግብቶ ኤርን አውናንን ሴሎምን ይወልዳል ፤ ኤር ማለት ፀሐይ ማለት ነው አውናን ማለት ወይን ማለት ነው ሴሎም ማለት መስተሳልም ማለት ነው። ለበኲሩ ለኤር ከአሕዝብ ወገን ትዕማር የምትባል ብላቴና እምጥቶ አጋባው አባቴ ማግባቱን ባይፈቅድልኝ ነው እንጂ ማግባቱንማ ቢፈቅድልኝ ከኃያላኑ ከእስራኤል ወገን ያጋባኝ አልነበረምን ብሎ ተጸይፎ የማይደርስባት ሆነ ። እግዚአብሔር ትዕቢት አይወድምና በዚህ ምክንያት ቀሠፈው ። ኋላ በኦሪት የሚሠራው በሕገ ልቡና ተገልጾለት ዓቅም ዘርዓ ለእኁከ ብሎ ለአውናን አጋባው ። እሱም ሥራውን እየሠራ ከዓፄ ዘርዕ በአፍአ ሆነ ልጅ ቢወለድ ለሱ ስሙ መጠሪያ ይሆነዋል እንጂ ለኔ ምን ይሆነኛል ብሎ ፤ እግዚአብሔር ምቀኝነት አይወድምና ቀሠፈው ፤ በሳራ ወለተ ራጉኤል አስማንድዮስ የሚባል ጋኔን በጭንዋ አድሮ ሰባቱን ባሎቿን እንደገደለባት ይህች ብላቴና ልጆቼን ትጨርስብኛለች ብሎ በፊሊጥ ያሳናብታታል ። ሑሪ ቤተ አቡኪ ወንበሪ መበለቲኪ እስከ አመ ይልኅቅ ወልድየ ሰሎም ብሎ ፤ አድጎ ሳለ እንዳላደገ አድ

ርጎ ፣ እሷም እያዘነች ሂዳለች ። ማዘንዋ ግን
ዝሙት ቀረብኝ ብላ አይደለም ፣ እመቤታ
ችን ጌታችን ከቤተ ይሁዳ ይወለዳሉ ሲሉ
ትሰማ ነበርና ፤ ከባለተስፋ ቤት ወጥቼ ሄድሁ
ብላ ነው እንጂ ፤ በዚያ ወራትና ሚስቱ ሴዋ
ሞተችበት ። መዋዕለ ኀዘኑ ሲፈጸም ቴምናታ
ወደምትባል ሀገር በጎቹን ሊያሸልት በሚሄ
ድበት ጊዜ ናሁ ይሁዳ ሐሙኪ የዓርግ ውስተ
ቴምናታ ከመ ይቅርፅ አባግኢሁ ብለው ነገሯት፤
ሴሎም እንዳደገ ያላትም ነገር እንዳልተ
ፈጸመላት ባየች ጊዜ እንዳታስለኝ ላታስው
ብላ ልብሰ ዘማ ለብሳ ጃንጥላ አስጥላ ድንኳን
አስተክላም ቢሉ ክተመላቀለ መንገድ ቆየ
ችው ። እሥራኤል ሴት ሲያዩ አልፎ መሄድ አይ
ሆንላቸውም ነበረና በጁ በዪኝ አላት ። በዚያ
ውስ ላይ ሚስቱ ሦተተበት ማለት ለዚህ ይመ
ቻል ። ምንት ትሁብኒ አስበ ደነስየ አለችው
እፌኑ ለኪ ፩ መሐስዓጠሊ ፣ የፍየል ጠቦት
እልክልሻለሁ አላት ። ሀብኒ አኀዘ መያዣ
ስጠኝ አለችው ። ምን ልስጥሽ ቢላት ፤ ቀለ
በትህን ኩፌትህን ዘንግህን ስጠኝ አለችው
መያዣ ሰጥቶ ተገናኝቶ ይሄዳል ። እሷም ዘማ
አይደለችምና ልብስዋን አሰልባ እንደ ጥንቷ
ተቀመጠች ። የበግ መልከኛው ኢራስ አዶ
ሎማዊ ይባላል ። ይኸን ጠቦት ወስደህ ለዚ
ያች ዘማ ሰጥተህ ገንዘቦችንን ይዘህ ና ብሎ
ላከው ። ቢፈልግ አጣት አይቴ ቤታ ለዘማ እያለ
ይጠይቅ ጀመር ፣ እኛስ በሀገራችን ዘማም
የለብን አሉት ። ተመልሶ አጣኋት አለው ፤
ብታገኛት ትሰጣት ነበር እንጂ ካጣሃትማ ገን
ዘባችን ከኛ ፤ በዚያውም ላይ ዛሬስ የያዕቆብ
ልጆች ጠገቡና አይቴ ቤታ ለዘማ እያሉ ዘማ
ሲፈልጉ ይዞራሉ ሆነ ባሉን ነበር አለው ።
ከሦስት ወር በኋላ ትዕማር መርዓትከ ፀንሰት
በዝሙት ብለው ነገሩን ። በምን አውቀው ቢሉ
ከሦስት ወር በኋላ ፅንስ እየገፋ ጡት እየጠቆረ
ይሄዳልና ። በዚያ ወራት በአሕዛብ ሰልጥኖ
ባቸው ነበረና በደንጊያ ወግራችሁ በእሳት
አቃጥላችሁ ግደሏት ብሎ አዘዘ አድርሱኝ አለ
ቻቸው የማያደርስዋት ሆነ ። እንኪያስ ኀል
ቅት ዘመኑ ዝ ኩፌት ዘመኑ ዝ ሕለት ዘመኑ
ብላችሁ ስጡልኝ አለቻቸው ፤ ወስደው ሰጡት
አይቶ ጸድቀተኒ ትዕማር ረታችኝ ፤ ጸድቀት
እምኔየ ከኔ ይልቅ ተሻለች ከኔ የተነሣ ከበ
ረች ብሎ ተናግሯል ። መንታ እንደፀነሰች
አውቃ በምትወልድበት ጊዜ መወልዲቱን አስ
ቀድሞ የተወለደውን በኩሩን እንድናውቀው
ቀይ ሐር እሠሪበት አለቻት ፤ አስቀድሞ

ዛራ እጁን ስደደ ፈትለ ለይ ሐር አሰረችበት ፣
ፋሬስ እሱን ወደኋላ ስቦ ተወለደ ። ፋሬስ
ማለት ጣሽ ጠምሳሽ ክፍለት ፍልጠት ኃያል
ማለት ነው ፤ ዕጹብ በአንቲአከ ማለት
ነው ፤ ዕጹብ በአንቲአከም ማለት ያየነው
ቀርቶ ያላየነው ወጣ ማለት ነው ። ዛራ ማለት
ወለት ድክምት ማለት ነው ። ደክሞ ተወልዷ
ልና ። ቅድመ ዘርኢናሁ ዝኒ ሠረቀ ማለትም
ነው ። ቀይሕ ፈትለ ለይ ማለት ነው መልከ
መልካም ማለት ነው ዛሀራ ይላል በዓረብ
መልከ መልካም ሲል ይህ ሁሉ ምሳሌ ነው ፣
ይሁዳ የእግዚአብሔር አብ ኤራስ አዶሎማዊ
የቅዱስ ገብርኤል በግዕ የእግዚአብሔር ወልድ
ሕልቀት የሃይማኖት ኩፌት የአክሊለ ሦክ
ሕለት የመስቀል ትዕማር የቤተ አይሁድ ።
ትዕማር ማያዣ ይዛ ቀረች እንጂ ዋጋዋን አን
ዳላገኘች ቤተ አይሁድም ትንቢቱን ተስፋውን
ሰምተው ቀሩ እንጂ በክርስቶስ አላመኑምና
አንድም የምሳሌ ምሳሌ ። ትዕማር የምኩራብ
የቤተ ክርስቲያን ምሳሌ ትዕማር ልጆችን ከአ
ባታቸው ከይሁዳ አገኘች እንጂ ። ከልጆች
እንዳላገኘች ። ቤተ ክርስቲያንም ምዕመናንን
ከአግዚአ ነቢያት ከእግዚአ ካህናት ከክርስ
ቶስ አገኘች እንጂ ። ከነቢያት ከካህናት አላ
ገኘችምና ። አንድም ትዕማር የቤተ ክርስቲ
ያን ምሳሌ ትዕማር ከልጆችም ካባትም ዘርን
እንዳልተጸየፈች ። ቤተ ክርስያንም ከሕዝብ
ከአሕዛብ ከሐቃል ከሀገሬት ከግዙር ከቆላፍ
ያመኑትን ሁሉ ትቀበላለችና ። ለዘመጽአ ኀቤየ
ኢይሰድዶ ወኢያወጽአ አፍአ እንዲል ፣ ፋሬስ
የአሪት ዛራ የወንጌል ምሳሌ ። ዛራ አስቀድሞ
እጁን እንዳወጣ ። ወንጌልም በመልከ ጸዱቅ
ታይታ ጠፍታለችና ። ፋሬስ እሱን ወደ ኋላ ስቦ
እንደ ተወለደ በመካከል ኦሪት ተሠርታለች ።
ዛራ በኋላ እንደተወለደ ወንጌል ኋላ ተሠርታለ
ችና ። አደ ዛራ የቀሳውስት ፈትለ ለይ የሥጋው
የደሙ ምሳሌ ። ይህንስ ለምን ይሻዋል ቢሉ ትዕ
ማር በሃይማኖት እንደከበረች አሕዛብም በሃ
ይማኖት እንዲከብሩ ለማጠየቅ በእስራኤል
ዘለፋ ለአሕዛብ ተስፋ ሊመሆን ። በልደተ ሥጋ
ይመካሉና፣ለኛስ ክርስቶስ ከትዕማር ተወልዶልን
የለም ለማለት ። በዓቂበ ሕግ ይመካሉና የሕግ
አፍራሽ ልጆች አይደላችሁምን ለማለት ።
ክርስቶስ በዳዊት ከበረ ይላሉና ዳዊት በክር
ስቶስ ከበረ እንጅ እሱማ የትዕማር ልጅ አይ
ደለም ለማለት ።

ወፋሬስኒ ወለደ ኤስሮምሃ ፡ ፋሬስም ኤስሮ
ምን ወለደ ። ወኤስሮምኒ ወለደ አራምሃ ።
ኤስሮምም አራምን ወለደ ።

፱ ወአራምኒ ወለደ አሚናዳብሃ ፡ ዘኍ ፡ ፯ ፡ ፲፪።
፲ አራምም አሚናዳብን ወለደ ፡ ወአሚናዳብን
ወለደ ነዓሶንሃ ፡ አሚናዳብም ነዓሶንን ወለደ።
ወነዓሶንኒ ወለደ ሰልሞንሃ ፡ ነዓሶንም ሰል
ሞንን ወለደ ።

፲፩ ወሰልሞንኒ ወለደ ቦኤዝሃ እምራኬብ ሩት ፩
፳፱ ፡ ፩ ነገ ፡ ፲፮ ፩ ።

፲፪ ሰልሞንም ቦዔዝን ከራኬ ብ ወለደ ። በአሪት ባያስ ይለዋል ። ከዚህ ቦዔዝ አለ እንደምነው ቢሉ ላንድ ሰው ሁለት ስም አለው ። አንድም በጽያፍ የገባ እሷንም በአሪት ረዓብ ዘማ ይላታል፡ከዚህ ራኬብ አለ እንደምነው ቢሉ ላንዲት ሴት ሁለት ስም አላት ። አንድም በጸያፍ የገባ ፡ ራኬብ ማለት፡ ዘትትረከብ ለኵሉ ማለት ነው የይስሐቅን ልደት በተናገረ ጊዜ ማራን የያዕቆብን ልደት በተናገረ ጊዜ ርብቃን የይሁዳን የወንድሞቹን ልደት በተናገረ ጊዜ ልያን ራሄልን አላነሣ ከዚህ ደርሶ ስለምን አነሣ ቢሉ ምክንያት ያላት ናት ። ኢያሱ በሰጢን ሰፍሮ ሳለ ካሌብና ሰልሞንን ኢያሪኮን ሰልላችሁ ኑ ብሎ ሰደዳቸው ደጋ ደጋውን ሲሰልሉ አድረው ኢያሪኮ ከቆላው ሲደርሱ ነጋባቸው አሕዛብ አይተው ዐወቋቸው በምን ምክንያት ቢሉ ሲፈሩ አይተው፥ አንድም የጕበኛ ዓይኑ ባካና ነውና ዓይናቸው ሲባክን አይተው ። አንድም በልብሳቸው በአካላቸው እስራኤል ቅርጸ ቀላል ናቸው ልብሳቸውም ነጭ ነው ። አሕዛብ ግን ቁመተ ገፋፋ ልብሰ አዳፋ ናቸውና ። የኢያሪኮ ቅጽሯ ሰባት ነው ራኬብ ሕዝቡን ትቀበል ነበር ፡ ቢሉ ስድስቱን ወደውሥጥ አንዱን ወደውጭ አድርጋ ከስድስተኛው ዛኒጋባ ጥላ ትኖር ነበር መኳንንቱን ትቀበል ነበር ቢሉ ስድስቱን ወደውጭ አንዱን ወደውሥጥ አድርጋ ከስድስተኛው ዛኒጋባ ጥላ ትኖር ነበር ። ገብተው ሰውረኝ አሏት ከሰገነት አውጥታ በቀርከሃ አቴና ጠቅላ አቆመቻቸው ። አንዲመጡ ዐውቃ ፍርፋሪ ጥላ ውኃ አፍሳ ትቆያለች መጥተው የእስራኤል ጕበኞች ካንቺ ገብተዋል ስጭን አሏት ። መግባትስ ገብተው ነበር ሕቀ በደሩከሙ እህል ቀምሰው ውኃ ጠጥተው ሂዱ አለቻቸው ። መግባታቸውን ብታምንላቸው ፡ መውጣታቸውን ያመኑችልን መሰሏቸው ፤ ገብተን እንይ ባይሉ ተመልሰው ሄዱ ። ኋላ ገብታ ትወርሱ ሀገረን ወትቀትሉ ነገሥታቲን አለቻቸው በምን ዐውቅሽ አሏት ። እበመ እግዚአብሔር ወደየ ፍርሃተ ውስተ ልበ ኃያላኒን ። ኃያላኑ ሲፈሩ ሲሸበሩ ያድራሉ ። ላምላ ለስላ የሚከፈተው የብረት ላንቃ ከመዝ ህለወነ ንትረጎው እያለ በገዛ እጁ የሚከፈት ሆነ ። ነገር ግን አሕዛብ ተድላ ሲያደርጉ እኔ አላደረግሁምና ደርባችሁ እንዳታጠፉኝ ማሉልኝ አለቻቸው ። አላቸውም ጠንቅቀው ይምላሉ ። አንች ለኛ እንዲህ ብለሽ ኋላ ለዘመዶችሽ ነግረሽ ፈጣሪያችን በቸርነቱ ቢያድነን ከመሐላ ንጹሐን ነን ከደጅሽ ሰንደቅ አላማ ትከዪበት ከመስኮትሽ ሐር ዝጊበት ሰውሽ ከቅጽር በአፍአ አይውጣ ወጥቶ ቢሞት በኛ ዕዳ የለብንም አሏት። እሷም መከራ ትስዳቸዋለች ፤ አሕዛብና ጕንዳን መንገድ ኪያዘ አይለቅምና ሦስት ቀን በመንገድ አትሂዱ በዱር ሂዱ በመዓልትአትሂዱ በሌሊትሂዱ ብላ መከራ ሰደደቻቸው እንደነገረቻቸው አድርገው ኢያሱ ካለበት ደረሱ፡ እንደምን ሁናችሁ መጣችሁ አላቸው።እንዲህ ያለች ሴት አግኝተን ሰውራ ሰደደችን አሉት ። ከአሕዛብ ወገን እንዲህ ያለች ሴት መገኘቷ ፈቃደ እግዚአብሔር እንጂ ቢሆን ነው ብሎ አልዋለም አላደረም ዕለቱን ተነሥቷል መጀመሪያ አንድ ጊዜ ዞሮ በፈረ ከዚያም ጥቂት ጥቂት አልፍ እያለ ይሰፍራል ፡ እንዲህ እንዲህ እያለ እስከ ስድስት ቀን ይሰነብታል በሰባተኛው ቀን ኃያላኑን በቀኝ በግራ በፊት በኋላ አሰልፎ ካህናቱን ልብሰ ተክህኖ አልብሶ ታቦተ ጽዮንን አሸክሞ ስድስት ጊዜ ዞራችሁ በሰባተኛው የነጋሪት ድምፅ ስትሰሙ አውኩ ደንፋ አላቸው እንዲህ ማለቱ አሕዛብ ቍጡዓን ናቸው ወጥተው ይገጥመኛል ድል አደርጋቸዋለሁ ብሎ ነው ። ስድስት ጊዜ ዞረው በሰባተኛው የነጋሪት ድምፅ ሲሰሙ አወኩ ደነፉ ቅጽሩ ባራት ማዕዘን ፈረሰ ተናደ ፤ አሕዛብን አጥፍቶ ኢያሪኮን እጅ አድርጎ አድሯል ሰልሞን ከዚች ሴት ደጅ ጠኑን አቆመ ፤ ያች ያልኩህ ሴት ይሀች ናት ብሎ ግዳይ ጣለለት ባርኬልሃለሁ አግባት ። ልጅ ትውለድልሀ አለው ። እሱዋን አግብቶ ቦዔዝን ይወልዳል ፡ ይህ ሁሉ ምሳሌ ነው ኢያሱ የጌታ ፤ ኢያሪኮ የምዕመናን ፤ አሕዛብ የአጋንንት ፤ ምሳሌ ። ኢያሱ አሕዛብን አጥፍቶ ኢያሪኮን እጅ እንዳደረገ ። ጌታም አጋንንትን ድል ነሥቶ ምዕመናንን ገንዘብ ለማድረጉ ምሳሌ ፡ መስኮት የከናፍረ ምእመናን ፡ ሐር

የሥጋው የደሙ ፡ ስንደቅ ዓላማ የመስቀል
ራኬብ የአሕዛብ ፤ ብዙ ወንድ ስታወጣ ስታ
ገባ ኑራ ኋላ ባንድ በሰልሞን እንደ ተወሰነች
አሕዛብም ብዙ ኃጢአት ሲሠሩ ብዙ ጣዖት
ሲያመልኩ ኑረው ባንድ በጌታ እምነው ለመ
ኖራቸው ምሳሌ ፡ ሰልሞንና ካሌብ የኦሪትና
የወንጌል ምሳሌ ናቸው ሴላይነታቸው በዚህ
ዓለም እንደሆነ ወንጌልና ኦሪትም የተሠሩ
በዚህ ዓለም ነውና ፤ ይህንስ ለምን ይሻዋል
ቢሉ ፤ ሐተታ እንዳለፈው እንደ ትዕማር በል ።
ወቦዔዝኒ ወለደ ኢዮቤድሃ እምነ ሩት፡ ቦዔዝም
ኢዮቤድን ከሩት ወለደ ። የይስሐቅን ልደት
በተናገረ ጊዜ ሣራን የያዕቆብን ልደት በተና
ገረ ጊዜ ርብቃን የይሁዳን የወንድሞቹን ልደት
በተናገረ ጊዜ እነልያን እነራሄልን እሳነሣ ፡
ከዚህ ደርሶ ይህቶን እነሣ ምነው ቢሉ ። ምክ
ንያት ያላቱ ናት ። አቤሜሌክ የሚባል ካህንም
ጨዋም ነው ቢሉ ሚስቱ ኑኃሚን ትባላለች
ኑኃሚን ማለት ፍሥሕት ጥዕምት ማለት ነው
ልጆቻቸውም መሀሎን ኬልዎን ይባላሉ በረ
ኃብ ምክንያት ደወለ ሞዓብ ተሰደው ሲኖሩ
ለታላቁ ልጁ ለመሀሎን ሩትን ለታናሹ ለኬ
ልዎን ዑርፋን አጋብቷቸው ሲኖር አስቀድሞ
አባት ሞተ ከዚህ በኋላ ልጆቹ ሞቱ ። ኑኃሚን
እንደዚህ ሁና ስትኖር ከእሥራኤል ወገን መን
ገደኛም ቢሉ ነጋዴም ቢሉ ሰው መጣ ሀገ
ራችን እንደምን ሁነዋል ብላ ጠየቀችው ።
ሀገራችንማ ለምቷል ቀንቷል ምን ታጥቆ የወ
ይኑ ዘለላ ጋን ይመላ የስንዴው ዛላ እፍኝ
ይመላ አላት ። ሠናይ ለብእሲ ለእመ ይከውን
መቅብርቱ ውስተ ርስቱ እንዲል ፡ እንኪ
ያስ ከሀገሬ እሞታለሁ እቀበራለሁ ብላ መን
ገድ ጀመረች ሁለቱ ምራቶቿ ተከተሏት ።
አላትና ትተካልናለተ አትሉኝ ፈጅቻለሁ ወልዳ
ታደርስልናለች አትሉኝ አርጅቻለሁ ተመ
ለሱ አለቻቸው ዑርፋ ከሞቱ እቴቴ ምን
አለኝ ካማቴ የምትል ያልታደለች ናትና ስማት
እጅ ነሥታት ተመለሰቱ ። ሩት ግን ከሞተ
እቴቴ ምን አለኝ ካማቴ የማትል ደግ ሴት
ናትና አገርሽ አገሬ ፈጣሪሽ ፈጣሪዬ ነው
ከሞትሽበት እሞታለሁ ከተቀበርሽበት እቀበ
ራለሁ ብላ ተከትላት ሄደች ። የሀገሬ ሰዎች
ይወዷትነበርና ኑኃሚን ኑኃሚን መጣች እያሉ
ተቀበሏት ምን ፍሥሕት ጥዕምት ትሉኛላ
ችሁ መሪር ኀዘንት ትክዝት በሉኝ እንጂ ።
መሊዕየ ወፃእኩ ወዕራቅየ ገባእኩ ፤ ከባል
ከልጅ ወጥቼ ብቻዬን ተመለስኩ አለቻቸው።
በሀገራቸው ሞቱን ካልሰሙ በታውን ለሌላ

አይሰጡበትምና ቤቷን ጠርገውላት ገባች ።
ሩት እየወጣች እየወረደች የሞያ እየዋለች
ትመግባታለች ። ከዕለታት ባንድ ቀን ከቡ
ዔዝ አዝመራ ሄዳ ስትለቅም ቦዔዝ ለሠራ
ተኞች ምሳ አሲዞ መጣ እግዚአብሔር ምስ
ሌከሙ አላቸው ኃይል ይሰጣችሁ ሲል ፡ እሆ
በከመ ቃልከ ፤ እንደ ቃልህ ይደረግልኝ
አሉት ይህች ሴት ወዴት ናት ብሎ ጠየቀ
በምን ምክንያት ቢሉ አሕዛብ መልከ መል
ካሞች ናቸውና በመልኳ ፡ አንድም አጥርቃ
ስትለቅም አይቶ ፤ አንድም ስትፈራ አይቶ
እስራኤል የሆቦ እንድሆነ አራሪ ለማራሪ ማራሪ
ለአዕዋፍ ይተዋሉ ። ከኑኃሚን ጋራ የመጣች
ሞዓባዊት ናት አሉት ለዚችስ ገቢረ ሠናይ
ይገባል ብሎ ጠርቶ ካጠገቡ አድርጎ ከእንጀ
ራው ቆርሶ ከወጡ አጥቅሶ ሰጣት ወዲያው
ሥራት ይሠሩላታል ከእንግዲህ ወዲህ አት
ከልከሏት ከመካከል ገብታ ትልቀም አትቅ
ረጧት የሰበሰበችውን ተሸክማላት ጊዜ ሲያ
ጋጥማችሁም ከምትጠጡት ስጧት ብሎ ይሠ
ራላታል እርሷንም ይመክራታል ። እስራኤል
ቀናተኞች ነን ካንዱ አዝመራ የዋለ ካንዱ
አይውልም ። ትልዊዮን ለአዋልድየ ። አዝ
መራው እስኪከተት ዛሬ ወዴት ውለዋል እያ
ልሽ እየጠየቅሽ ከኔ አዝመራ ዋይ አላት እር
ስዋ ናሁ አሙትከ ረከበት ጥገበ በቅድሜከ
ብላ እጅ ነሣች ። የሰበሰበችውን ይዛ የተረፋትን
በቀሚሷ ኪስ ቋጥራ ሄደች ብትሰፍረው ዐሥር
መስፈሪያ ሁኗል ያሥሩ ቃላት ምሳሌ
ያን ሰጥታት ስትመገብ ዛሬ ከማን አዝመራ
ውለሽ ኑሯል አለቻት ። ከቦዔዝ አዝመራ አለ
ቻት ። አንች ባታውቂው ነው እንጂ ፤ እሱማ
የባልሽ የመሀሎን ርስት ጕልት ያለ በእሱ
እጅ እንጂ ነው አንቺ ለኔ በጕሥራ ብትሠሪ
እኔም ላንቺ በጕሥራ መሥራት ይገባናልና
ዐውድማ የሚጥ ልበትን ቀን ጠይቀሽ ንገሪኝአለ
ቻት።ጠይቃ ነገረቻት ገላዋን አጥባ ሽቱ ዘግባ
ደኅና ልብስ አልብሳ የሴቶች ወግ አድርሳ መክራ
ትሰዳታለች ። እሥራኤል ሲበሉ ቢያዩዋቸው
አይወዱምና ከክምር ሥር ተሠውረሽ እምሽ
ተሽ ሲ ተኛ ቀርበሽ ከእግሩ ሥር ተኚ ።
እንች ማነሽ ይልሻል እኔ ባርያህ ሩት ነኝ
አ ወ ራ ረ ስ አ ቆ ራ ረ ስ ይ ገ ባ ኛ ል ብየ
መጥቻለሁ በዬው ከዚህ በኋላ እምላክ እስ
ራኤል ያለው ይደረግልሻል አለቻት ። እንደ
ነገረቻት እስኪበሉ ከክምር ስር ተሰውራ ቆይታ
ሲተኛ ቀርባ ከእግሩ ስር ተኛች አንቺ ማነሽ
አላት እኔ ባሪያህ ሩት ነኝ አወራረስ አቆራረስ

ይገባኛል ብዬ መጥቻለሁ አለችው ከቀደመው ደግነትሽ የዛሬው ይብሰጥ አረጋዊ ነው ብሰሽ ወደ ሕፃን መልከ ክፉ ነው ብለሽ ወደ መልከ መልካም ድኃ ነው ብለሽ ወደ ባለጠጋ አለ መሄድሽ ነገር ግን ከኔ ይልቅ አወራረስ አቆራረስ የሚገባው አለ ያ ቢያደርገው አደረገው ያ ባያደረገው ሕያው እግዚአብሔርን እንዳ ደርግልሽ ። አሁንም ሰው ሳያይሽ ሂጂ ብሎ እንዳታፍር ፮ መሥፈሪያ ሰጥቶ ሰደዳታል ። የጁቱ ቃላተ ወንጌል ምሳሌ ፣ ሲነጋ ቦዔዝ ሰው ሰብስቦ ባደባባይ ተቀምጦ ያን ሰው ሲያልፍ አይቶ አስጠራው ። የመሀሎን ርስት ጉልት ያለ ባንተ እጅ ነው ይህችን ብላቴና አግብተህ ሰሙን የሚያስጠራ ልጅ አትወልድምን አለው ። ቀዳሚ ተሐምሦ ዘዚአየ ወዳግም ተሐምዎ ዘዚአከ አውነትህ ነው አስ ቀድሞ አወራረስ አቆራረስ የኔ ነው ። ቀጥሎ ያንተ ነው ። ዘዚአየ ተሐምዎ ተሐምው አንተ የኔን አንተ ውሰደው ከሁለት ዛፍ ያለች ወፍ ሁለት ክንፏን ትንደፍ እንዲሉ እኔስ የሁለት ቤት ማተናት የሁለት ልጅ ማሳደግ አይሆንልኝም አለው ፣ እንኪያስ በአራት የሚገባውን አድርገህ ስጠኝ አለው ፣ ጫማውን አውጥቶ ይሰጠዋል ። ጫማ ለእግር ቤዛ እንደ ሆነ ኃይል ቤዛ የሚሆን ልጅ ቀረብኝ ሲል በዚህም ቤተ ፍቱሐን አማዕን ተብለው እስከ ፯ ቤት ድረስ ይሰደቡበታል ጺቅ ይሉበታል ጽቁነህ ፊሉ ፤ ሕዝቡም መርቀው ያጋቡታል። የያዕቆብን ቤት በልያ በራሔል ምክንያት ሰልጅ በክብት እንዳነጹው ያንተንም ቤት በዚች ብላቴና ምክንያት በልጅ በከብት ይነጽልህ ብለው መርቀው ይሰጡታል ። እርስዋን አግብቶ ኢዮቤድን ይወልዳል ። ኢዮቤድ ያለችው ኑኃሚን ናት ኢዮቤድ ማለት መጽንዒ ርስት ጸዋሬ ርስዓን መርሥዒ ኃዘን ማለት ነው ። ይህንስ ለምን ይሻዋል ቢሉ ሐተታ እንዳለፈው እንደ ትዕማር ቢል ። ከዚህም ጌታን ከነዚህ መወለድ አያሳድፈውም እሳቸውን ያጸራቸዋል ያከብራቸዋል እንጂ ፣ ብርሃን ፀሐይ ከሸለል በወደቀ ጊዜ ሸለሉን ያጸራዋል ይስነግለዋል እንጂ ብርሃነ ፀሐይን እንዳያሳድፈው ።

ወኢዮቤድኒ ወልደ ዕሤርሃ፤ ኢዮቤድም ዕሤይን ወለደ ። ወዕሤይኒ ወለደ ዳዊትሃ ንጉሠ ዕሤይም ንጉሥ ዳዊትን ወለደ ፣ ሐተታ ፤ በሚያመጣው ሰሎሞንሃ ንጉሠ ሮብዓምሃ ንጉሠ ፣ አቢያሃ ንጉሠ አይል አሁን ደርሶ ዳዊትሃ ንጉሠ አለ ምነው ቢሉ ፤ ዳዊት ሥርወ መንግሥት ነውና ፤ ሥርወ መንግሥትማ ሳኦል አይደለም ቢሉ ትንቢት የተነገረ ለዳዊት ነውና ትንቢትማ ለሳኦልስ ብንያም ተኩላ መሣጢ ይበልዕ ሲሳዮ በነግህ ተብሎ ተነግሮለት የለም ቢሉ ያንማ እንጂ ወፍና ሠርክ ይሁብ ሳመሳእክቲሁ ባሰው አፍርሶታል ።

፮ ወዳዊትኒ ንጉሥ ወለደ ሰሎሞንሃ እምነ ብእሲተ ኦርዮ ፤ ፪ ነገ ፣ ፲፪ ፣ ፳፬ ።

፮ ዳዊት ንጉሥም ከኦርዮ ሚስት ከቤርሳቤህ ሰሎሞንን ወለደ ። ኢሊያስ ሴቶቹ ከአረማውያን ወገን ቢሆኑ ነው ፣ እነዚህማ እሱ ዕብራዊ እሱዋ ዕብራዊት ሰለምን እንዲህ አለ ቢሉ ። ዳዊትማ ጉልማሳ አስ ገድሎ የጉልማሳ ሚስት ቀምቶ ማማውን ግርማውን ቢፈራ ኃጢአቱን ሳይገልጽበት ቀረ እንዳይሉት ሐዋርያ መምህር ወመገሥጽ ዘኢያደሉ ለገጽ እንደ ሆነ ለማጠየቅ ፣ እንድም በተነሳሕያን ፍርሃት አን ሉለባቸው ለማጠየቅ ፣ አዳምን ያህል ሰው በድሎ ንስሐ ቢገባ ተማረ ። ዳዊትን ያህል ሰው በድሎ ንስሐ ቢገባ ተማረ ። ጴጥሮስን ያህል ሰው ክዶ ንስሐ ቢገባ ተማረ እናንተም ንስሐ ብትገቡ ትድናላች ለ ማ ለ ት ፣ እ ን ድ ም በ ዓ ዊ በ ሕ ግ ይ መ ካሉና እናንተስ የሕግ አፍራሽ ልጆች አይደላች ሁምን ለማለት ። ክርስቶስ በዳዊት ከበረ ይላሉና ፤ ዳዊት በክርስቶስ ከበረ እንጂ እሱማ ጉልማሳ አስገ ድሎ የጉልማሳ ሚስት ቀምቶ አልነ በረም ለማለት ፣ ፯ ወሰሎሞንኒ ወለደ ሮብዓምሃ ፫ነገ ፣ ፲፩ ፣ ፵፫ ፣ ። ፲፬ ፣ ፴፩ ። ፲፭ ፣ ፳ ።

፯ ሰሎሞንም ሮብአምን ወለደ ወሮብዓምኒ ወለደ አብያሃ ሮብዓምም አብያን ወለደ ። ወአብያኒ ወለደ አሳፍሃ ። አብያም አሳፍን ወለደ ።

፰ ወአሳፍኒ ወለደ ኢዮሳፍጥሃ ።

፰ አሳፍም ኢዮሳፍጥን ወለደ ። ወኢዮሳፍጥኒ ወለደ ኢዮራምሃ ኢዮሳፍጥም ኢዮራምን ወለደ ወኢዮራምኒ ወለደ አካዝያስሃ ኢዮራምም አካዝያስን ወለደ ወአካዝያስኒ ወለደ ኢዮአስሃ ፣ አካዝያስም ኢዮአስን ወለደ ፤ ወኢዮአስኒ ወለደ አሜስያስሃ ኢዮአስም አሜስያስን ወለደ ሐተታ ፤ አካዝያስን ፣ ኢዮአስን አሜስያን የሚጽፍም የማይጽፍም ይገኛል ። የጸፈ እንደሆነ የተመቸ ። የተወ እ ን ደ ሆ ነ በሀገራቸው አንድ አ አንጂ ሁለት አ አይገኝምና አና አ አሳስቶት በሀገራቸውስ ስንኳን ሁለት አ አራት አ ይገኛል ብሎ ዝያና ዝያ አሳስቶስ ፤ እንድም መምለኪያን ጣዖት ናቸውና ሰማቸው በመጽሐፍ መጻፍ አይገባውም ብሎ ። ይህማ እንዳይሆን ጌታ ግብር ይጸየፋልን ብሎ ፤ ለቊጥር ይመቸኝ ብሎ ፤ ለቊጥርስ ይመቸኝ ቢል በኒህ ዕጣ ወጥቶባቸዋልን ቢሉ ። ግድፈተ ጸሐፊ ነው ።

ወአሜስያስኒ ወለደ አዝያንሃ ዘተሰምየ አዛርያስ ፤ አሜስያስም አዛርያስ የተባለ አዝያንን ወለደ ፤

ሕዝቡ በፍና ተማልቆ፤በማይገባ ልብሰ ተክህኖ ስብሶ ማዕጠንተ ወርቅ ይዞ ከቤተ እግዚአብሔር ገብቶ ቢያጥኑ አዛርያስ ይባሉ ብለውታልና ፤ በፍና ተማልቆ ስለተናኘሩ አዛርያስ የተባለ አለ ፤ አንድም አዛርያስ በሉኝ ያለ አዝያንን ወለደ ። የአዛርያስን ሥራ ልሥራ ማለት አዛርያስ በሉኝ ማለት ነውና ፤ በዘመኑ ሊቀ ካህናቱ አዛርያስ ይባላል በቀኙ ይቀመጣል ምነው ይሰዋል ፡ ወካህን ይነብር በየማኑ እንጂ ይላል ይለዋል ። ፍርዱን ይገሥበታል ምነው ይለዋል እምነ መንግሥት የዓቢ ክህነት እንጂ ይላል ይለዋል። ክሱ የሚበልጥ ልብስ ይለብሳል ፤ ምነው ይለዋል ፤ ካህናቲከ ይለብሱ ጽድቀ እንጂ ይላል ይለዋል ። ባባቴ ከቤተ መንግሥት ብወለድ በናቴ ከቤተ ክህነት እወለድ የለምን ብሎ ልብስ ተክህኖ ለብሶ ማዕጠንተ ወርቅ ይዞ ሊያጥን ሲገባ ሕዝቡ ተው አይገባም አይሆንም አሉት ። ንጉሥ ነውና ተጋፍቶ ገባ ፤ ሲያጥን ጢሰ ቅታሬው ቢነካው ከግንባሩ ለምፅ ወጣበት በሻሽ ቢሸፍነው ከሻሹ ላይ ወጣ ። እሥራኤል ለምፅ የያዘውን ስንኳን ሊያነግሡት ሊገናኙት አይወዱምና ወአውፅእዎ ለአዝያን ውስተ ቤተ ሐፍሶት እንዲል ። ቆላ አወጡት ወኢዮአታም ወልዱ የዓቅብ ቤተ መንግሥት ወይኲንን ሕዝበ ምድር እንዲል ልጁን ኢዮአታምን አንግሠዋል ይህንንስ ለምን ይሻዋል ቢሉ ፤ ሐተታ እሱ ካስተማሩት ትምህርት ከሠሩለት ሥራት ቢወጣ እንዲህ ያለ መከራ አገኘው ፤ እናንተም ካስ ተማርናችሁ ትምህርት ከሠራንላችሁ ሥራት ብት ወጡ እንዲህ ያለ መከራ ያገኛችኋል ለማለት ፤

፱ ወአዝያንኒ ወለደ ኢዮአታምሃ ፪ ነገ፡ ፳፮ ፡ ፳፫ ፡ ፳፯ ፡ ፱ ፡ ፳፰ ፡ ፳፯

፱ ሕዝያንም ኢዮአታምን ወለደ ። ወኢዮአታምኒ ወለደ አካዝሃ ። ። ኢዮአታምም አካዝን ወለደ ። ወአካዝኒ ወለደ ሕዝቅያስሃ አካዝም ሕዝቅያስን ወለደ ።

፲ ወሕዝቅያስኒ ወለደ ምናሴሃ ። ፪ ነገ፡ ፴፪ ፡ ፴፫፡፴፫ ፳ ፡ ፳፩ ።

፲ ሕዝቅያስም ምናሴን ወለደ ። ወምናሴኒ ወለደ አሞፅሃ ። ምናሴም አሞፅን ወለደ ። ወአሞፅኒ ወለደ ኢዮስያስሃ አሞፅን ኢዮስያስን ወለደ ።

፲፩ ወኢዮስያስኒ ወለደ ኢኮንያንሃ ወአኃዊሁ አመ ፍልሰተ ባቢሎን ፡ ነገ፡ ፴፮ ፡ ፩፡፱ ።

፲፩ የባቢሎን ሰዎች ወደ ኢየሩሳሌም በዘመቱ ጊዜ የኢየሩሳሌም ሰዎች ተማርከው ወደ ባቢሎን በወረዱ ጊዜ ኢዮስያስም ኢኮንያንን ወንድሞቹን ወለደ ሐተታ ወንጌላዊ ስቶን ዘንግቶ የልጅ ልጁን ልጁ ብሎ እኅቶቹን ወንድሞቹ ብሎ እንደነገሠ ጊዜ የተደረገውን ስልደቱ ሰጥቶ ተናገረ ቢሉ ፤ ስቶም ዘንግቶም አይደለ ልማድ ይዞ ነው እንጂ የልጅ ልጁን ልጁ አለ ልማድ ይዞ ፤ ያዕቆብ ከላባ ኮብልሎ ሚስቶቹን ልጆቹን ይዞ በመጣ ጊዜ ላባ ሦስት ቀን የሄደውን አንድ ቀን ገሥግሦ ደርሶ ፤ ለምንት ትሰርቀኒ ደቂቅየ ወአዋልድየ ከመ ዘበኲናት ፄወወ ወሚመ ኢይደልወኒኑ አበዓም ደቂቅየ ወአዋልድየ ብሎታል ። እኅቶቹንም ወንድሞቹ አለ ልማድ ይዞ የአብርሃም ቤተሰቦችና የሎጥ ቤተሰቦች በማር በውኃ ምክንያት ቢጣሉ ፡ ለምንት ንትጓመፅ እንዘ አኃው ንሕነ በበይናቲነ ለእመ አነ የማነ ሖር አንተ ፀጋመ፡ ወለእመ ፀጋም አነ ሖር አንተ የማነ ብሎታል እንደ ነገሠ የተደረገውን ስልደቱ ሰጥቶ ተናገረ ። ይህንም ልማድ ይዞ ነው ፡ ደቂቅከ ይነብሩ ፈላስያነ ብሔረ ነኪር ወይቀነይዎሙ ግብጽ ፬ ፲ ዓመተ እንዳለ ። በግብጽ የሚኖሩት ሁለት መቶ ዐሥራ አምስት ዘመን ሲሆን በከነዓንየሚኖሩትን ደርቦ ስደቱን ከሰመት ብሎ እንደተናገረ ። አሁንም ፄዋዌውን ከሰመት ብሎ እንደ ነገሠ ጊዜ የተደረገውን ስልደቱ ሰጥቶ ተናገረ ። ታሪክ ኢዮስያስ በነገሠ ባሥራ ሦስት ዓመት ኤልያቄም ኢኮንያንን ይወልዳል ። በዚህ ጊዜ ነቢዩ ኤርምያስ ይህ ልጅ በነገሠ ጊዜ ፄዋዌ ይደረጋል ብሎ ትንቢት ተናግሯል ፤ የኢዮስያስ መላ ዘመኑ መንግሥቱ ሠላሳ አንድ ነው ። ኢኮንያን በተወደ ባሥራ ስምንት ኢዮስያስ በነገሠ በሠላሳ አንድ ዓመት ፈርዖን ኒካው ዘመተ ኒካው ማለት እንካሳማለት ነው ። ስለ ምን ዘመተ ቢሉ ንጉሠ በብንግን ለመውጋት ። አንድም መንግሥት ለማዳረስ ፤ ኪመ ያብጽሕ እዴሁ ላዕለ ፈለገ አፍራጢን እንዲል ፤ ቀድሞ የሀገራችን ነገሥታት መንግሥት ለማዳረስ እዙሰም ይወጡ እንደነበረ ፡ መጥቶ ሰፈረ ። ንጉሠ እስራኤል ካንተ ፀብ የለኝምና መንገድ ስጠኝ አለው ። ለሕዝቡ ቢነግራቸው እኛስ ሀገራችንን የአሕዛብ መገሥገሻ አናደርጋትም አሉት ። አይሆንም በሌላ መንገድ ሂድ አለው እንግዲያውማ የመጣሁበትን ሳላደርግ የምመለስ ነኝ ብሎ ኃለኛ ንጉሥ ነውና ተጋፍቶ ሄደ ፤ ኢዮሲያስም ሰልፍ ቀየው ኢዮሲያስ በንፍጥ ተመቶ ወደቀ አሽከሮናቸውን ይዘው ወደ አምባ ተጠጉ እሱም ፀብ የለውምና አልፎ ሄደ አምባ ገብተው ኢዮስያስን ቀብረው ልጁን ዮአክስን አንግሠው ተቀመጡ ንጉሠ በብንግን ወግቶ ሦስት ወር ኑሮ ግብሩን ተገብሮ ወደ ኢየሩሳሌም ቢመለስ አገራቱን ጫብላ አገኛት የዚህች ሀገር ኃያላን እንደ ቀትር ንብ ይናደፉ ነበረ ወዴት ሄደዋል ብሎ ጠየቀ ፤ አንድም የቀሩት መጥን ሲያገቡልኝ እነዚህ የማያገቡልኝ በምን ምክንያት ነው ብሎ ጠየቀ ። አንድም የዚች አገር ንጉሥ ቲመቶ ነበር አሰን ሞተ ብሎ ጠየቀ ። እሱማሙቶ አምባ ገብተው እሱን ቀብረው ልጁን ዮአክስን አንግሠው ተቀምጠዋል ብለው ነገሩት ። በሀገራቸው ሥራት ፈሊጥ የለም የገደለ ያንግሥ የዘመተ ይመለስ አይሉም ብሎ አምባውን

ሰብሮ ዮአክስን አሥሮ ኤልያቄምን አንግሦላቸው ሄድዋል ኤልያቄም ማለት ቆመ ለነ እግዚአብሔር ማለት ነው ፤ ኢቆመ ለከሙ ሲል ኢዮአቄምብለሎ ታል ፤ ግብጽ ከሄደ በኋላ ሦስት ዓመት ይገብርለታል ወተቀንየ ኢዮአቄም ንጉሠ ይሁዳ ለንጉሠ ግብጽ ሠለስተ ዓመተ እንዲል ። በአራተኛው ዓመት ናቡከደነጾር ዳር ዳር መውጋት ጀመረ መን ገድ ተያዘብኝ ብሎ ግብር ነሣ ባምስተኛው ዓመት መጥቶ ገብር አለው ። ንጉሥ ፍርድ ልበስ ፈርኦን ኒካው አባቴን ገድሎ ወንድሜን አስሮ እኔን አንግሦ ግብሩን ትገብር ሄደ አንድ ባሪያ ለሁለት ጌታ መገ ዛት እንደምን ይሆንለታል አለው ፤ አሕዛብ ፍርድ ጠነቀቅን ባዮቶ ናቸውና የዚያን ያንካሳ መዳ ረሻ ሳላሳይህ የዕለት ራት የጣት ቀለበት ልትለኝ አይገባህም ብሎ ግብጽ ወርዶ ፈርኦን ኒካውን ገድሎ ሦስት ዓመት ኑሮ ባቢሎን ዘግብጽ አሰኝቷት ተመ ልስዋል ። ከተመለስም በኋላ ሦስት ዓመት ይገብር ብርለታልአሥር አንድ ዓመት ይሆናል ከዚህ በኋላ ሞት ቢያምረው በሰማይ የለ ዱር በእሥራኤል የለ ግብር ብሎ ግብር ነሣው ፤ እሱም ተክል ለማየት ወጥቶ ሳለ ከለዳውያን ገድለውታል ። አንድም በእደ እግዚአብሔር ታሞ ሙቷል ፤ ልጅን ኢኮንያን አነ ግሡ ኢኮንያን ሦስት ወር እንደ ነገሠ ናቡከደነጾር ተመልሶ መጣ ይተወኛል መስሎት ወባት ገባ ፤

እሱን አሰሮ ሕዝቡን ማርኮ ሲሄድ አንቱ ናታን ከመንገድ ቆይቶ ልጅ ሳለሁ የልጅ ልጅ አዋቂ ሳለሁ አላዋቂ ፤ ታላቀ ሳለሁ ታናሽ አንግሠውብኝ ነበር የዚህን ግፍ አይቶ እግዚአብሔር መንግሥትን ላንተ አሳልፎ ከሴጠህ ንጉሥ ፍርድ ልበስ አለው ምን ላድርግልህ አለው ፤ አንግሠኝ አለው፤ ሕዝቡን ማርኬ እወስዳቸዋለሁ በማን አነግሥሃለሁ አለው በሀገሬ እኔ አውቃለሁ ተክል በሚኰተኰቱት በገበ ራርት አንግሠኝ አለው፤ አንግሦት ሄዷል ስሙን ሴዴቅስያስ አለው ። ባተከደኝ፣ ማለት ነው ። እሱም እምባውን እያጸና ግብሩን እየሰደደ ስምንት ዓመት ኖረ ፤ በዘጠነኛው ዓመት እንደወንድሙ ሞት ቢያምረው በእሥራኤል የለ ግብር በሰማይ የለ ዱር ብሎ ግብር ነሣው ። አስቀድሞ ፀባኢተ ሞዓብን ፀባኢተ ሶርያን ስዶ አስከበበው ፤ ኋላም እሱ ፪ት ዓመት ከ፮ ወር ይከበዋል ፤ ወተገፍትዓት ሀገር ይላል የዘመነ ረኃብ ሰው ቀዩ ይጠቁራል ጥቁሩ ይነጣልና ። አንድም እኩሉ እንገብር እኩሉ አን ዋጋ በማለት ተለያዩ ። ናቡከደነጾር ሥራት ሠርቶ ላቸው ነበር ሰው የሞተባቸው እንደሆነ ፤ መቃብር አይከልከሉ እያወጡ በየርስታቸው ይቅበሩ ብሎ በዚያ ልማድ ዋይ ሸሸ ተበላሸ ብላችሁ ይዛችሁኝ ውጡ አላቸው ። ዋይ ሸሸ ተበላሸ እንያሉ ይዘውት ሲሄዱ ያ ምንድነው ብሎ ጠየቀ። በምን አውቆ ቢሉ

ሰው በዝቶ ነበርና ። አንድም ፍርድ ያደላባት ቤት ነግራበት የእሥራኤል ንጉሥ ሞቶ በሠራህላቸው ሥራት ሊቀብሩት ይወስዱታል አሉት ። የወዳጅን እንጂ አስከሬን አጥቦ ገንዞ መቅበር ይገባል ወደኔ አምጡት ብሎ አስመጥቶ መግነዙን ፈተው ቢያዩት ዓይኑቆስል ቆለል ሲል ተገኝቷል ወተናገሮ ፍትሐ እን ዲል ወቀሰው ። መርጬ ባነግሥህ ምነው ከዳኸኝ ። ከከዳኸኝስ በኋላ ወይ እችላለሁ ብለህ አትዋጋ ወይ አልችልም ብለህ አትገብር በዚያውስ ላይ እኔን ከዚህ እኑረህ ወዴት ልትሄድ ኑሯል ብሎ መኳንንቱን ፍረዱልኝ አላቸው ። እችላለሁ ብሎ አይዋጋ አልቻ ልም ብሎ አይገብር ሞት ይገባዋል አሉ ፍርድስ እላ ወቃችሁም ሞቴ ስብእሲ ዕረፍቱ ሞትማ ዕረፍት አይደለምን እኔ አውቃለሁ ብሎ ፯ ለመንግሥት የደረሱ ልጆች ነበሩት ከፊቱ በሠይፍ አስመታቸው፤ እሱንም ከፉ ባየበት ዓይኑ በጎ አይይበት ብሎ ሁለት ዓይኖቹን በፍላት አውጥቶ ትብትብ አሸክሞ ዱር ለዱር በፈረስ ጭራ እያስጎተተ ባቢሎን ይዞት ወር ዷዋል ከዚያም ባቈላ ሲፈጭ ከወፍጮ ስር ልቡ ፈርሶ ሞቱዋል ወይከውን መቃብረከ ታኅተ አግረ ማኅረፀ ያለው የነቢዩ ቃል ይደርስ ይፈጸም ዘንድ የዮአክስ ሦስት ወር የኢኮንያን ሦስት ወር ከመንፈቅ የሴዴቅያስ ዓሥርዓመትከመንፈቅአሥራአንድዓመት የኤልያቄም ዓሥራ አንድ ። የኢዮስያስ ዓሥራ ስም ንት ፤ አርባ ይሆናል ፤ ይኸ ሁሉ ዘመን እያለ ፄዋዌ ውን ከሰሙት ብሎ አንደ ነገሠ ጊዜ የተደረገውን ለልደቱ ሰጥቶ ተናገረ አንድም ከዚህ ሁሉ ሐተታ ለመዳን ዘአመ ፍልሰተ ባቢሎን የሚል ይገኛል እሥራኤል ተማርከው ባቢሎን በወረዱ ጊዜ የነገሠ ኢኮንያንን ወለደ ይህ አያሳስትም ። ፄዋዌ ሥጋው ለፄዋዌ ነፍሱ ምልክት እንደሆነ ሚጠተ ሥጋው ለሚጠተ ነፍስ ምልክት ነውና። እሥራኤል ተማር ርከው ባቢሎን መውረዳቸው ነፍሳት ገሃነም ለመውረዳቸው ምሳሌ ነውና እሥራ ኤል ከባቢሎን መውጣታቸው ነፍሳት ከሲኦል ከገሃነም ለመውጣቸው ምሳሌ ነውና ። ኤልያቄምን ዮሚጽፈውም የሚተወውም አለ ፡፡ የተወው እንደ ሆነ መጽሐፈ ኤርምያስን አቃጥሎ ነበርና በመጽ ሐፍ መጻፍ አይገባውም ብሎ ። ይኸማ እንዳይሆን ጌታ ግብር ይጸየፋል እንጂ ባሕርይ ይጸየፋልን ብሎ ለቍጥር ይመቸኛል ብሎ ያውስ ፤ ቢሆን

በሉ ዕጣ ወጥቶበታልን ብሎ ። ግድፈተ ጸሐፊ ነው ይህን ለምን ይሻዋል ቢሉ አባቸው ከሠ ሩላቸው ሥራት ካስተማሯቸው ትምህርት ቢወ ጡ እንዲህ ያለ መከራ አገኛቸው ። እናንተም ከሠራንላችሁ ሥራት ካስተማርናችሁ ትም ርት ብትወጡ እንዲህ ያለ መከራ ያገኛችኋል ለማለት ።

፲፪ ወእምድኅረ ፍልሰተ ባቢሎን ኢኮንያንኒ ወለደ ሰላትያልሃ ።

፲፪ የኢየሩሳሌም ሰዎች ተማርከው ባቢሎን ከወረዱ በኋላም ኢኮንያን ሰላትያልን ወለደ ፤ ሐተታ ምነዋ ኢየዓርግ ብእሲ እምውስተ ዘርዑ ዘይነብር ዲበ መንበሩ ይል የለምን ቢሉ፤ አይነግሥም አለ እንጂ አይወለድም አለ ፤ ያውስ ቢሆን አይነግሥም ያለው ሴዴቅያስ ኢኮንያንን ነው እንጂ ፤ ኤልያቄም ኢኮንያንን ነውን ፤

ወሰላትያልኒ ወለደ ዘሩባቤልሃ ሰላትያልም ዘሩባቤልን ወለደ

፲፫ ወዘሩባቤልኒ ወለደ አብዩድሃ

፲፫ ዘሩባቤልም አብዩድን ወለደ ።
ወአብዩድኒ ወለደ ኤልያቄምሃ አብዩድም ኤልያቄምን ወለደ ። ወኤልያቄምኒ ወለደ አዛርሃ። ኤልያቄምም አዛርን ወለደ ።

፲፬ ወአዛርኒ ወለደ ሳዶቅሃ ።

፲፬ አዛርም ሳዶቅን ወለደ ።
ወሳዶቅኒ ወለደ አኪንሃ ፤ ሳዶቅም አኪንን ወለደ ። ወአኪንኒ ወለደ ኤልዩድሃ ፤አኪንም ኤልዩድን ወለደ ፤

፲፭ ወኤልዩድኒ ወለደ አልዓዛርሃ

፲፭ ኤልዩድም አልዓዛርን ወለደ ወአልዓዛርኒ ወለደ ማትያንሃ አልዓዛርም ማትያንን ወለደ ወማትያንኒ ወለደ ያዕቆብሃ ማትያንም ያዕቆብን ወለደ።

፲፮ ወያዕቆብኒ ወለደ ዮሴፍሃ ፈኃሪሃ ለማርያም እንተ እምኔሃ ተወልደ እግዚእ ኢየሱስ ዘተብህለ ክርስቶስ ።

፲፯ ያዕቆብም ክርስቶስ የተባለ ኢየሱስ ከእሷ የተወለደ የእመቤታችን እጮኛ የሚሆን ፤ ዓቃቤሃ ተለአኪሃ አገልጋይዋ ጠባቂዋ የሚሆን ዮሴፍን ወለደ መገናኛው ጉንዱ አልዓዛር ነው አልአዛር ማትያንንና ቅስራን ይወልዳል ማትያን ያዕቆብን ያዕቆብ ዮሴፍን ይወልዳል ቅስራ ኢያቄምን ኢያቄም እመቤታችንን ፤ በሀገራቸው ሴትና ወንድ አቀላቅሎ መቍጠር የለምና ሥርዓት አፈረሰ ይሉኛል ብሎ በዮሴፍ እንጻር ቆጠረ እሷንም እንዳትቀር በቅጽል አመጣት፤ ሐተታ በ፫ ቤት እንድትታጭ ማድረጉ ስለ ምን ቢሉ በልማድ ፤ አዋልደ ሰለጳድ ከሙሴ ዘንድ ሄደው አባታችን የሞተ በበደሉ ነው እኛ ከነገር አልገባንምና ርስት አካፍለን ስሙን እናጸራው አሉት ፤ ወደ እግዚአብሔር ቢያመለክት ። ርቱዓ ይቤላ አዋልደ ሰለጳድ ሀቦን መክፈልቶን ማዕከለ አኃዊሆን አለው ፤ እሥራኤል ይኸነን ሰምተው ሴት የያዘችው ነገር ከሁሉ ይደርሳል ከእንግዲህ ወዲህ ርስት ከርስት ትውልድ ከትውልድ እንደተፋለሰ ዕወቅ አሉት ፤ ሁለተኛ አመለከተ ። አስተዋስቦን ዘእምቅሩቦን ባባታቸው ወገን በሦስት በሦቤት ቤት እየተጋቡ እንዲወርሱ አድርግ ብሎታልና በነዚያ ልማድ ፤ አንድም ፪ዋዌ ቢጸናባቸው ወንዱ ለሴቲቱ ሴቲቱ ለወንዱ የማያዝኑ ሁነዋል በተዘምዶተ ሥጋ ላይ የግቢ ተዘምዶ የተጨመረ እንደሆነ ጥሏት አይሄድም ያዝንላታል ብለው የሚያጋቧቸው ሁነዋልና በዚያ ልማድ በዚያስ ላይ እንድትታጭ ማድረጉ ስለ ምን ቢሉ ፤ ኃይል አርያማዊት ባሏት ነበርና ፤ ወንድ ከወንድ ተገኘ ባሉ ነበርና ኪመ በብሂሎቱ ፍሕርተ ብእሲ ያግሕድ ከመ እግዝእትነ ማርያም በአማን ብእሲት ይእቲ እንዲል ፤ አንድም ፅንስን ከአጋንንት ለማሳሳት ዐውቀው ቢሆን ብዙ ፅንስ ባበላሹ ነበርና ፤ አንድም መስተመይናን ዝሁላን አእምሮ አይሁድ ሰብሳብ ርኩስ፤ ይላሉና ። ንጹሕ እንደሆነ ለማጠየቅ ። አንድም በመከራዋ ጊዜ ሊከተላት ከርስት ገብቶ ሊቆጠርላት ከውግረት ሊያድናት ፤ ዮሴፍ ምክንያት ባይኖራት በድንጊያ ወግረው በገደሏት ነበርና ፤ ከፅዕለትም ሊያድናት ፤ ወይእንዛሁ ሰብዑ እንስት ለ፩ዱ ብእሲ ወይብላሁ አክለዚአነ ንሴሰይ ወልብሰ ዚአነ ንትኤረዝ ዳዕሙ ይሰመይ ሰምከ በላዕሌነ ወእኅድገነ ዘንተ ጽዕለተ እንዲል ፤ ይህንም ፪ ሊቃውንት አመሩ ፈቃደ ዮሴፍ ወሠለስቱ ሊቃውንት አመሩ ፈቃደ ሥላሴ ይላል ። ሁለቱ ሊቃውንት የተባሉ ዮሴፍ ለጊዜው አገባለሁ መስሎት ነበር ብለው የጻፉ ሳዊሮስ ዘአስሙናይን ያዕቆብ ዘሮሃ ናቸው ። ፫ቱ ሊቃውንት የተባሉ ሥላሴ ንጽሕናውን ባወቁ አስጠብቀውታል ብለው የጻፉ አትናቴዎስ ሐዋርያዊ ጎርጎርዮስ ዘኑሲስ ዮሐንስ አፈወርቅ ናቸው ዘተብህለ ክርስቶስ አለ ይህም ስም ብቻ የትስብእት ብቻ የመለኮት አይደለም ። ከሁለት አካል አንድ አካል ከሁለት ባሕርይ አንድ ባሕርይ ቢሆን የወጣለት ስም ነው እንጂ ወእነግር አነሂ ከመ ኢመፍትው አስምዮ ለቃለ እግዚአብሔር ክርስቶስ ዘእንበለ ትስብእት ፤ ወኢለትስብእት ዘእንበለ መለኮት ክርስቶስሃ ይሰመይ ወእምቅድመ ትሥጉት እልቦ ዘይሰምዮ በዝንቱ ስም ለቃለ እግዚአብሔር ክርስቶስ እንዲል ፤ በዝንቱ ስም ተሰምዩ ነቢያት ቅቡዓነ እሰመ ስመ ክርስቶስ ይትበሃል ሳዕለ ብዙኀ ጻታ ኪመ ነገሥተ እሥራኤል ወካህናቲሆሙ

ከመ አሮን ወዳዊት ወዘኃረየሂ ከመ ሥርዓተ
ቂሮስ ውእቱ ይላልሳ ቢሉ ፥ ይኸንም እንጂ ፥
ወተቀብዖሰ በመንፈስ ከመ ካህናቶ ሐዲስ
ው እ ቱ ወ ላ ዕ ለ ዘ ተ ወ ል ደ እ ም እ ግ
ዝእትነ ማርያም ይትብህል እንበይነ ተዋሕዶ
ዘኮነ ሊመለኮት በእንተ ዘተሠገወ እምድንግል
ሀየንተ ቅብዓተ ቅብዕ ባለው አፍርሶታል ፡፡
እንዲዐ ከሆነ ማን ሲያይ ተናግሮታል ቢሉ
አንዱን ሲያይ ፤ ገብርኤል ስሙ ዘአምኃ ለማ
ርያም ዘበትርጓሜሁ አምላክ ውእቱ እንዲል ፤
ኤልን ሲያይ ፤ ይህም አምላክ ሰው ቢሆን
የወጣለት ስም ነው ። ወዝ ስም ዘውእቱ ክር
ስቶስ ወፍካሬሁ ቅብዓት ምስለ አምጣነ ትስ
ብእቱ ረከቦ ለዋሕድ እንዲል ፤ ከበረ መባሉም
በሥጋ ነው ። ወቅብዓቱሰ ዘተወክፋ በትስብ
እቱ ይእቲ ወኢኮነ ቅብዓቱ አምሳለ ቅቡዓን
እስመ አለ ይትቀብዑ ይፈቅዱ ቀሪበ ኀቤሁ
ለከዊነ ወልድና ውእቱሰ አምላክ ውእቱ በጠ
ባይዒሁ ዘእንበለ ፈቂድ እንዲል ቦ አለ ይቤሉ
አምቅድመ ተዋሕዶ ወቦ አለ ይቤሉ እምድ
ኅረ ተዋሕዶ እንዲል ፤ ወገባሪሁሰ ለውእቱ
ሥጋ መንፈስ ቅዱስ እስመ ውእቱ ቀብዖ ወተ
ዋሕደ ቦቱ አምላክ ቃል ያለውን ይዘው ተቀ
ብቶ ተዋሀደ የሚሉ አሉ ፤ ተሠጊዎ ነሥአ
ቅብዓተ በዘተሰብአ ተቀብዓ ያለውን ይዘው
ሰው ሁኖ ተቀብቶ ተዋሕደ የሚሉ አሉ ። ነገር
ግን እንዲህ አይደለም ሲቀባም ሲዋሐድም
አንድ ጊዜ ነው ። ከመ ቅጽበተ ዓይን ፤ አለሰ
የአምኑ ርቱዓ ይሚህሩ ከመ ተቀበዓ ቃል በሥ
ጋሁ ወአምአመ ኮነ ቃል ሥጋ አሚሃ አስተር
አየ በመንፈስ ቅዱስ እንዲል ።

፲፯ ወኵሎንኬ ትውልድ እምአብርሃም እስከ
ዳዊት ፲ወ፬ቱ ፡

፲፯ ከአብርሃም እስከ ዳዊት ዐሥራ አራት
ትውልድ ነው ፤ ወእምዳዊት እስከ ፍልሰተ ባቢሎን
ትውልድ ፲ወ፬ቱ ። ከዳዊት እስከ ዬዋዬ ፲፬ ትው
ልድ ነው ። ወእምፍልሰተ ባቢሎን እስከ ክር
ስቶስ ትውልድ ፲ወ፬ቱ ።

ከዬዋዬ እስከ ክርስቶስ ዐሥራ አራት ትውልድ ነው ፤
ወኵሎንኬ ትውልድ እምአብርሃም እስከ ክርስቶስ
፵ወ፪ቱ ከአብርሃም እስከ ክርስቶስ መላው አንድ ሁኖ
ቢቈጠር አርባ ሁለት ነው ። ፲ወ፬ቱ ፲ ወ፬ቱ ፲ወ፬ቱ
ይላል ። አርባ ሁለት ይሆናል ። ዐሥራ አራት ዐሥራ
ሰባት አሥራ ሁለት ይላል አርባ ሦስት ይሆናል ።
ዐሥራ አራት ዐሥራ ሰባት ዐሥራ አራት ይላል አርባ
አምስት ይሆናል ፥ አርባ ሁለት ያለ እንደ ሆነ ሁለ
ቱን አግብቶ ሦስቱን ነገሥታት አውጥቶ ፥ አርባ
ሦስት ያለ እንደ ሆነ ከሦስቱ አንዱን አግብቶ ሁለ
ቱን አውጥቶ ። አርባ አራት ያለ እንደሆነ ከሁለቱ
ከአመቤታችንና ከኤልያቄም አንዱን አግብቶ አንዱን
አውጥቶ ፥ አርባ አምስት ያለ እንደሆነ ፥ መላውን
አግብቶ ፥ ከፍ ብሎ አርባ ስድስት ዝቅ ብሎ አርባ
አንድ ቢል ግድፈተ ጸሐፊ ነው ተርትሮ የቈጠ
ረውን ደምሮ ፥ ደምሮ የቈጠረውን ተርትሮ
ቈጠረ ደምሮ የቈጠረውን ተርትሮ ተርትሮ
የ ቈ ጠ ረ ው ን ፥ ደ ም ሮ ባ ይ ቈ ጥ ር
አይሁድ ወንጌላዊ ተርትሮ መቈጠር እንጂ መደ
መር መደመር እንጂ ተርትሮ መቁጠር አይሆንለ
ትም ብለው ደገኛዪቱን ሕገ ወንጌልን ከመቀበል
በተከለከሉ ነበርና ፥ አንድም ተርትሮ መቍጠር
የሦስትነት ደምሮ መቍጠር ያንድነት ምሳሌ ። አን
ድም ተርትሮ መቍጠር እንደ ሦስት ምስክር ደምሮ
መቍጠር ቃሉ አንድ የመሆኑ ምሳሌ ፥ ልማ በሥ
ሉስ ጥፉ በሥሉስ አንዱሉ ፥ አንድም በዳንኤል
ልማድ ፸ ሰንበታተ አድኅኖሙ ለሕዝብከ ያለውን
ተርትሮ የቆጠረውን ደምሮ ደምሮ የቆጠረውን
ተርትሮ እንደ ቈጠረ ፥ አንድም በሦስቱ ክፍለ ዘመን
የተቈጠረው ባንድ በጌታ እንደተፈጸመ ለማጠየቅ
በዘመነ አበው በዘርዕከ ይትባረኩ ኵሎሙ አሕዛበ
ምድር ተብሎ ፥ በዘመነ ነገሥት እስመ እምፍሬ ክር
ሥከ እነብር ዲበ መንበርከ በዘመነ ካህናት መቅ
ደስ ትትሐነጽ እስከ ክርስቶስ ንጉሥ ወእምዝ ትት
መዘበር ተብሎ የተነገረው ተስፋ ባንድ በጌታ እንደ
ተፈጸመ ለማጠየቅ ፥ አንድም ተርትሮ ቆጠረ ሥጋዊ
ምግብና ሲሰዋወጥ መጥቷል ፥ በዘመነ አበው ምክር
ተግሣፅ ሁኖዋል ያባት ለልጅ ያልፍ ነበር መጻሕ
ፍት አልተጻፉም ፥ በዘመነ መሳፍንት ፥ መጻሕፍት
ተጽፈዋል መስቀል መቁረጥ ሁነዋል ። በዘመነ
ካህናት እንደ ሁለቱም ሁኖዋል እንደ ዘመነ አበው
ምክር ተግሣፅ ሁኖዋል ። ያባት ለልጅ የማያልፍ
ሁኖዋል ። እንደ ዘመነ መሳፍንትም መስቀል መቍ
ረጥ ሁኖዋል መጻሕፍት ተጽፈዋል ። ደምሮ ቆጠረ
መንፈሳዊ ምግብና ምንም በካህናት በኤጲስ ቆጶሳት
እጅ ቢሆን አልተለወጠም አንድ ነው ለማለት ፤
አርባ ሁለት ባለው ለሰሎሞን ስድስት እርከን
ያላት አትሮንስ ነበረችው እሱ በስድስተኛዪቱ ሁኖ
ነገር ሲሰማ ሲፈርድ ይውል ነበር ስድስቱ እርከን
በሱባዔ ሲገቡት አርባ ሁለት ይሆካል ። ያርባ ሁለቱ
አበው ምግብና ሲፈጸም ጌታ ሰው የመሆኑ ምሳሌ ፥
ሰሎሞን የጌታ አትሮንስ የእመቤታችን ምሳሌ፥አርባ
ሦስት ባለው ለደብተራ አሪት አርባ ሦስት አእማድ
ነበሯት አርባ ሦስት አዕማደ ቅስብእት አበው ሲፈ
ጸሙ ጌታ ሰው ለመሆኑ ምሳሌ ። አርባ አራት ባለው
እሥራኤል ባአርባ አራተኛው ጉዞ ሰጢን ሰፍረው
ርስታቸውን አይተው አድረዋል ፥ እንደዚህ ምዕ
መናንም ካአርባአራተኛዪቱትውልድ ከእመቤታችን

ተወልዶ ርስታቸው ጌታን አይተዋልና አርባ አም ስት ሺው ባርባ አምስተኛ ገዛ እየርስታቸው ገብ ተዋል ፤ እንደዚህ ሁሉ ምእመናንም አርባ አምስ ተኛ ትውልድ የሚሆን ርስታቸው ጌታን ይወር ሳሉና ።

በእንተ ልደተ ክርስቶስ ።

፲፰ ወለእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ከመዝ ውእቱ ልደቱ ፤ የነትዕማርን የነራኬብን የነሩትን ሲናገር

፲፰ መጥቶ ነበርና ፤ የጌታችን የኢየሱስ ክርስ ቶስ ልደቱ እንዲህ ነው አለ፤ ከጥንት ሲነገር ሲያያዝ የመጣው ነው እንጂ ፤ እንደ እንግዳ ደራሽ እንደ ውኃ ፈሳሽ አይደለም ። ወሶበ ተፍኀረት ማንሻ ፤ አንድም ወለእግዚእነስ ይላል ፤ በዘር በሩካቤ የሚ ወለዱ የእበውን ልደት ሲናገር መጥቶ ነበርና ፤ የጌ ታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ግን ልደቱ እንዲህ ነው አለ ፤ እንበለ ዘር ነው ፤ ከመዝ ያለውን ያመጣዋል ፤ ወሶበ ተፍኀረት እሙ ማርያም ለዮሴፍ ፤ ሉቃ ፩፥፳፯ እናቱ እመቤታችን ለዮሴፍ በታጨች ጊዜ ።

ዘእንበለ ይትቃረቡ ተረክበት ጽንስተ እንዘባ ውስተ ማኅፀና እመንፈስ ቅዱስ ።

ዘእንበለ ይትቃረቡ ዘእንበለ ይትራከቡ ይላል ፤ እሱ ሴት እንደሆነች ሳያውቃት እሷ ወንድ እንደ ሆነ ሳታውቀው ዮሴፍ ጠባቂ ሳላት አጋዥ ሳትሻ አንድም ድንጋሌ ሥጋ ድንጋሌ ነፍስ ሳላት ፤ አን ድም ቧእምዘ ካላት ከባሕርይዋ በግብረ መንፈስ ቅዱስ ፀንሳ ተገኘች ወገባሪሁስ ለውእቱ ሥጋ መንፈስ ቅዱስ እስመ ውእቱ ቀብዖ ወተዋሐደ ቦቱ እምላክ ቃል እንዲል ይህ እም በሲሆን ነው ፤ እስመ እም ይትረኑም ለጎበ ብዙኀ ፍና እንዲል ስማያት ወም ምድር ተፈጥሩ እምእግዚአብሔር አዳም ወሔዋን ተፈጥሩ እምእግዚአብሔር እንዲል እመንፈስ ቅዱ ስም ቢል በመንፈስ ቅዱስ ተከፍሎ ኑሮበት አይደ ለም ፤ አነጻት ሲል ነው እንጂ ፤ ወእኮ ዘቦቱ ሥጋ ለመንፈስ ቅዱስ ፤ አላ መንፈስ ቅዱስ እንጽሐ ሥጋሃ ለማርያም ወረሰያ ድሎተ ለተወክፎ ቃለ እብ እንዲል ። አነፃትም ቢል ኑሮባት አነፃት ማለት አይደለም ከለከላት ሲል ነው እንጂ ። ውእ ቱስ ንጹሕ እምነ ፫ቱ ግብራት እለ ሥሩዓን በእጓለ እመሕያው ወእሙራን በሙ ዘውእቶሙ ሩካቤ ወዘ ርዕ ወስስሎተ ድንግልና እንዲል ከለከላትም ቢል ብታደርገው ዕዳ የሚሆንባት ሁና አይደለም አላደ ረገችውም ቢል ነው እንጂ ። ከዚያ ሁሉ ወኮነ ይስ ሐቅ ያፈቅሮ ለዔሳው እስመ ዘውእቱ ነዐወ ይሴሰይ ብሎ ወያዕቆብስ ንጹሕ እምዝንቱ ይላል ። አሁን በኤሳው አድኖ መብላት ዕዳ ሁናበትን ነው ፤ ያዕ ቆብን አላደረገውም ድልድል ቅምጥል ከቤት ዋይ ነው ሲል ነው እንጂ ። ልደቱን በዘር ያላደረገው እንበለ ዘር ያደረገው ስለምን ቢሉ ቀዳማዊ ልደቱን ለመግለጥ ። እምስተ ሽህ አምስት መቶ ዘመን ሲፈ ጸም ከእመ ቤታችን ያላባት መወለዱ ትድመ ዓለም ከአብ ያለእናት እንደተወለደ ያስረዳልና ፤ ልደት ቀዳማዊ ተዓውቀ በደኃራዊ ልደት እንዲል ። ዳግ መኛ በዘር በሩካቤስ ተወልዶ ቢሆን ዕሩቅ ብእሲ ባሉት ነበርና ፤ ሶበስ ተወልደ በሩካቤ ብእሲ ወብ እሲት ዘከማየ ብዙኃን እምተኃዘብዎ ወእምረሰይዎ ሐስተ እንዲል ። ያውስ ቢሆን ልደቱን ተፈትሖ ካላት ያላደረገው ተፈትሖ ከሌላት ያደረገው ስለምን ቢሉ ፤ ትንቢቱ ምሳሌው እንደተፈጸመ ለማጠየቅ ትንቢት ፤ ናሁ ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም አዳም ከንቱም ምድር ተገኝቷል ጌታም በንቱም ማኅፀን ለመገኘቱ ምሳሌ ነውና ። ሔዋን ከንቱም ገቦ ተገኝታለች ጌታም ከንቱም ማኅፀን ለመገኘቱ ምሳሌ ናትና ። ቤዛ ይስ ሐቅ በግዕ ከንቱም ጕንድ ተገኝቷል ። ቤዛ ዓለም ክርስቶስም በንቱም ማኅፀን ለመገኘቱ ምሳሌ ነውና ፤ ጽምዓ እሥራኤልን ያበረደ ውኃ ከንቱም ኰኵሕ ተገኝቷል ጽምዓ ነፍሳትን ያበረደ ማየ ሕይወት ጌታም በንቱም ማኅፀን ለመገኘቱ ምሳሌ ነውና ። ጽምዓ ሶምሶንን ያበረደ ውኃ ከንቱም መንሰከ አድግ ተገኝቷል ፤ ጽምዓ ነፍሳትን ያበረደ ማየ ሕይወት ጌታም በንቱም ማኅፀን ለመገኘቱ ምሳሌ ነውና ፤ ትንቢቱን ዐውቆ እናግሯል ። ምሳሌውንም እንጂ ዐውቆ አስመስሏል ፤ ፍጻሜው እንደምን ነው ቢሉ ከመ ትኩን መራሒተ ለሃይማኖት ዓባይ እንጂ ይላታል ። ድንግል ወእም ስቱባል መኖሯ ፤ እም ላክ ወሰብእ ሲባል ለመኖሩ ምሳሌ ነውና ስትወ ልደው ማኅተመ ድንግልናዋ አለመለወጡ ፤ ሰው ሲሆን ባሕርየ መለኮቱ ሳለመለወጡ ምሳሌ ናትና።

፲፱ ወዮሴፍስ ፈኀሪሃ እስመ ጻድቅ ውእቱ ኢፈቀደ ይክሥታ

፲፱ እጮኛዋ የሚሆን ዓቃቢሃ ተስአኪሃ ፤ እገል ጋይዋ ጠባቂዋ የሚሆን ዮሴፍ ግን ደግ ነውና ሲገ ልጣት ሊገልጥባት አልወደደም ።

ሕሳ መከረ ጽሚተ ይኅድጋ ። ትቷት ሊሄድ ወደደ እንጂ ፤ ሐተታ ፤ ይህን ደግነቱን ያስቀርበታልን በአሪት ታዞ የለምን ሚስቱን የጠረጠራት እንደሆነ ውኃ በመንቀል የገብስ ዶቄት አድርጐ ሚስቱን ይዞ ይሄዳል ከመድረኩ ስትደርስ ሊቃ ካህናቱ ከንን ብሽን ግለጭ ይላታል ይግለጥብኝ በይ ሲላት ነው። በኦሪቱ የሚደገም አለ ያንን ደግሞ ሕራረ ዕጣኑን ጨምሮ በጥብጦ ባልሽ የጠረጠረሽን አድርገሽው እንደሆነ ሥጋሽ ይበጥ ቁርበትሽ ይሳጥ አጥንትሽ ይርገፍ ፤ አላደረግሽው እንደሆነ በወንድ ልጅ ተበ ከሪ ብሎ ይሰጣታል ። እስዋም መርገሙ ይደረግ ብኝ በረከቱ ይሁንልኝ ብላ ትጠጣዋለች ፤ ይህ ደግ

ነቱን ያስቀርበታልን በአራቱ ታዞ የለም ቢሉ ዮሴፍ ጻድቀ ወንጌል ነው እንጂ መቼ ጻድቀ ኦሪት ነዋ ።

፲፰ ወእንዘ ዘንተ ይሔሊ ናሁ አስተርአዮ መልአክ እግዚአብሔር ለዮሴፍ በሕልም ።

ታሪክ፣እመቤታችን የብፅዓት ልጅ ናት ሦስት ዓመት ሲሆናት አባት እናቷ ወስደው ለካህናት ሰጡ፤ካህናትም ተቀብለው አክብረው ከቤተ መቅደስ ያኖሯታል ዐሥራ ሁለት ዓመት ትኖራለች ከዚያ፫ ከዚያ ፲፪ ዐሥራ አምስት ዓመት ይሆናል ። አይሁድ ለም ቀኝነት አያርፋምና ይሀች ብላቴና መጠነ አንስት አደረሰች ቤተ መቅደሳትንን ታሳድፍብናለች ትው ጣልን አሉት ፣ ዘካርያስ ሂዶ እንደምን ተሆኝ አባት ወደ እግዚአብሔር አመልክትልኝ አለችው ቢያመ ለክት ከነገደ ይሁዳ ሚስቶቻቸው የሞቱባቸውን በትር ሰብስበህ ከቤተ መቅደስ አግብተህ አውጣው ምልክት አሳይልሃለሁ አለው ። ቢሰበስብ ሽህ ዘጠኝ መቶ ሰማንያ አምስት ለሁለት ሽህ ዐሥራ አምስት የጎደለው ማለት ነው ያን አግብቶ ቢያወጣው ከዮ ሴፍ በትር ፣ አ ዮሴፍ ዕቀባ ለማርያም የሚል ተገኘ። ዕጣም ቢያወጡ ለሱ ወጣ ፤ ርግብም መጥታ በራሱ ላይ ዐረፈች ፣ እንዴ ሦስት ምስክር ያም ሆነ ያም ሆነ ከእግዚአብሔር አግኝተን የሰጠንህን ከእግዚ አብሔር አግኝተን እስክናሰናብትህ ወስደህ ጠብቅ አትንካ ብለው ሰጡት ። ይዟት ሄደ ጊዜው ዓፀባ ነበርና ንግድ ሂዶ ሦስት ወር ኑሮ ቢመለስ ዮሐንስ የሚባል ፈላስፋ ወዳጅ ነበረው ሊጠይቀው መጣ ተጨዋውተው ሲሄድ ሊሸኘው ወጣ ፤ ይህች ብላ ቴና ፀንሳለች ካንተን ነው ከሌላ አለው ። እኔስ እንኳን ነቢብ ገቢር ሐልዮም አላውቅባት አለው ። እንኪያስ ፀንሳለች ገብተህ ጠይቃት አለው ። በምን ዐውቆ ቢሉ ፈላስፋ ነውና በመልኳ ገብቶ አወሰተ እሥራኤል መኑ ቀረጸ አክናፈ ድንግልናኪ ወአመኀበ መኑ ፀነስኪ ብሎ ጠየቃት ። እመንፈስ ቅዱስ አለችው ፤ ነገሩ ቢረቅበተ ከደጁ ወድቆ የሚኖር ደረቅ ግንድ ነበርና ተክላ አለምልማ አሳይታዋለች ። በዚያውስ ላይ አዕዋፍን ከባሕርያ ቸው እንዲራቡ አዕዋምን እንዲያፈሩ የሚያደርግ ማን ይመስልሃል አለችው ነገሩን ተረዳው ። ከዚህ በኋላ ለበዓል የሚወጡበት ጊዜ ደረሰ ። ትቻተ ብወጣ ያደረገችውን ታስታውቅ ከዴረቷ ትታጠቅ እንዲሉ ያደረገውን ዐውቆ ትቷት መጣ ይሉኛል ይገባት ብወጣ ሴሰነች ብለው በደንጊያ ወግረው ይገሉብኛል እያለ ፤ ወወድቀ ዮሴፍ ውስተ ጽኑዕ መዋግደ ሕሊና ይላል ይህነን ቢያወጣ ሲያወርድ ። ከእግዚአብሔር የታዘዘ መልአክ ለዮሴፍ በሕልም ነገረው (ሐተታ) ህልም ከሦስት ወገን ነው ከሐሞት ከመልአክ ከሰይጣን የሚገኝ ነው ፤ ከሐሞት የሚ ገኝ በልቀም ደም ሳፍራ ሳውዳ የሚባሉ ሐሞታት

አሉ ። በልቀም አሳታዊ ፤ ደምማያዊ ፣ ሳፍራ ነፋ ሳዊ ፣ ሳውዳ መሬታዊ ነው ፣ እኒህ በሠለጠኑ ጊዜ በየጎብረቸው ሲያሳዩ ያድራሉ ፣ ከሰይጣን የሚገኝ እንደ ሄሮድስ በስደቷ ጊዜ ከዚህ ዋለች ከዚህ አደ ረች እያለ ይነግረው ነበር ፣ ከመልአክ የሚገኝ እንደ ዮሴፍ እንደ ፈርዖን እንደ ናቡከደነፆር ፣

እንዘ ይብል አ ዮሴፍ ወልደዳዊት ኢትፍራህ ነሚአታ ለማርያም ፍኀርትከ ፣

አ ቃለ አክብሮ ቃለ አንሥሮ ቃለ አራኅርሖ ይሆናል። ቃለ አንሥሮ ፣ ኦሐናንያ አኢብዳን ሰብአ ገላትያ ፣ ቃለ አክብሮ አ ጳውሎስ ምንተ ትቤ አ አኃውየ ፍቁ ራን ፣ ቃለ አራኅርሖ አድንግል አዘከሪ አዮሴፍ ያለው ይህ ነው ። የርኅሩኅ የዳዊት ልጅ ዮሴፍሆይአንትህ ናትና ራራላት ፣ እንድም የጥቡዕ የዳዊት ልጅ ዮሴፍ ሆይከካህናት እጅ እንደ ተቀበልህ ከእደ መንፈስ ቅዱስ መቀበልን አትፍራ ነሚአታ ባለው አብንት አዕርጎታ ኢውፅአታ ዓቂቦታ ተልእኮታ ይላል ። አስመ እም ፍሬ ከርሥከ አነብር ዲበመንበርከ ያለው ትንቢት እንደተፈጸመ ለማጠየቅ ዳዊትን አነሣው ።
እስመ ዘይትወለድ እምኔሃ እመንፈስ ቅዱስ ውእቱ፣ ከሱዋ የሚወለደው በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነውና ማቴዎስ እመንፈስ ቅዱስ ያለውን ሉቃስ መንፈስ እግዚአብሔር ቅዱስ ይመፅእ ላዕሌኪ ያለውን ፣ ኢሳይያስ መንፈስ እግዚአብሔር ዘላዕሌየ ዘበእን ቲአሁ ቀብዓኒ ያለውን ሊቁ ባቲመ ትርጓሜሃ ለቅ ብዓት ፣ እስመ መንፈስ ቅዱስ አንጽሐ ሥጋሁ ለአዳም ብሎ ወስዶታል ፣ ንጽሕን ክብር የሚል ወዴት አለ ቢሉ ። ወሠዓርኮ እምንጽሑ ይላል ።

፳፩ ወትወልድ ወልደ ፣

፳፩ ወንድ ልጅ ትወልዳለች ፣ ሉቃ ፡ ፩ ፡ ፴፩ ግብረ ሐዋ ፬፣ ፲፪ ።

ወትሰምዮ ስሞ ኢየሱስሃ ። ስሙንም ኢየሱስ ትለ ዋለች ። እስመ ውእቱ ያድኅኖሙ ለሕዝቡ እምኃ ጣውኢሆሙ ፣

ወገኖቹ እሥራኤልን በኃጢአት ከመጣባቸው ፍዳ ያድናቸዋልና ፣ ኢየሱስ ብሎ ንባቡን ፣ ያድኅኖሙ ብሎ ስሙን ከነትርጓሜው ተናገረ ። ኃይሉ ለስም ወፍካሬሁ አብጽሐ ቅዱስ መልአክ እንዲል ።

፳፪ ወዝንቱ ኵሉ ዘኮነ ከመ ይትፈጸም እም ኀበ እግዚአብሔር ፣

፳፫ በነቢይ እንዘ ይብል ፣ ናሁ ድንግል ትጸ ንስ ወትወልድ ወልደ ፣ ኢሳ ፯ ፣ ፲፬ ።
አጸፋውን ለወንጌላዊ የሰጡ እንደሆነ ፳፪ ፣ እመ ቤታችን በግብረ መንፈስ ቅዱስ ትፀንሳለች በግብረ መንፈስ ቅዱስ ትወልዳለች ብሎ መልአኩ ለዮሴፍ መንገሩ ፣ ፳፫ ነቢይ ድንግል ትፀን

፳፫ ወትወልድ ወልደ ብሎ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ፤ አጸፋውን ለመልአኩ የበጡ እንደሆነ እመቤታችን በድንግልና መጽነስዋ በድ ንግልና መውለድዋ እግዚአብሔር በነቢዩ አድሮ ነቢይ ከእግዚአብሔር አግኝተ ተገልጾለት ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ብሎ የተናገረው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ፤ ወይሰመይ ስሙ ዐማኑኤል ። ስሙም ዐማኑኤል ይባላል ። ዘበትር ርጓሜሁ እግዚአብሔር ምስሌነ ።

ዐማኑኤልም ማለት እግዚአብሔር ከሥጋችን ሥጋ ከነፍሳችን ነፍስ ነሥቶ ከኛ ጋራ አንድ ሆነ ማለት ነው ፤ ሐተታ ወንጌላዊ የሚጽፍላቸው በቋንቋቸው በዕብራይስጥ ነው ። መልአኩም ለዮሴፍ የሚነግረው በዕብራይስጥ ነው ። ምን ይተረጕማል ቢሉ ያበ ቅዱስ ቄርሎስ የንበጥርበን ነገር ሲያስፈርድ አንተ ነድረት ካልሀ ዐማኑኤል ያለውን ንባብ እግዚአ ብሔር ምስሌነ ብሎ የተረጐመ ወንጌላዊ አበላ ፤ ሕበወኬ ይመስይ ወንጌላዊ ዘይተረጉም በንቤሆሙ ብሎ ረትቶበታል ይተረጕምላትዋል ትርጓሜው ግን በቋንቋቸው ካህናቱ የሚያውቁት ሕዝቡ የማያው ውቁት እንደ ጥሬ ያለ አለና ያነን ማጽናት ማጕላት ነው መጽሐፍ በወ በዘ ያጕላል በወ ቢያጕላ ፍሥሐ ወኃሤት ፍቅር ወሰላም ፤ በዘ ሲያጕላ ምንት ብከ ዘኢነግእከ እምካልዕከ ወምንት ብከ ዘኢኮነ ውሁበ ለከ ይላል እንድም ዮሐንስ ወንጌላዊ የማቴዎስ ወንጌልን ለሰብአ ኢሳንሳን ተርጕሞላቸዋል ፤ በዚያ ጊዜ ዐማኑኤል ንባቡ ከእብራይስጥ እግዚአብ ሔር ምስሌነ ትርጓሜው ከኤሳንሳን መጥቶልናል፤ ዐማኑኤልን የመሰለ የኤሳንሳን ንባብ ሳይመጣልን ቀርቷል ። እንድም የሀገራችን መላሽ ዐማኑኤል ያለውን የዕብራይስጡን ቋንቋ ወደግእዝ ቢመልሱት እግዚአብሔር ምስሌነ ማለት ነው ፤ እግዚአብ ሔር ምስሌነ ማለትም ከሥጋችን ሥጋ ከነፍሳችን ነፍስ ነሥቶ ከኛ ጋራ አንድ አካል አንድ ባሕርይ ሆነ ማለት ነው ብሎ ተርጕሞታል ፤ ወተንሢአ

፳፬ ዮሴፍ እምንዋሙ ገብረ በከመ አዘዞ መል አከ እግዚአብሔር ።

፳፬ ዮሴፍ ከዕንቅልፉ ተነሥቶ መልአኩ ያዘ ዘውን እንዳዘዘው አደረገ ።

ወነሥአ ለማርያም ፍኅርቱ ፤ ይዘሃት ውጣ እንዳለው ይዟት ወጣ ፤ ጠብቅ እንዳለው ጠበቀ ተቀበል እን ዳለው ተቀበለ

፳፭ ወኢየአምራ እስከ አመ ወለደት ወልደ ዘበኩራ ።

፳፭ መጻሕፍት በዞር ያሉላት ልጅዋን እስከ ትወልድ ድረስ አላወቃትም ፤ አአመራ አዳም ለሔዋን አአመራ ሕልቃና ለሐና ብእሲቱ እንዲል የግብር ዕውቀት አላወቃትም ፤ ከወለደች በኋላስ ዐወቃት ማለት ነውን ቢሉ ፍጻሜ የሌለው እስከ ነው ኢተመይጠ ቋዕ እስከ አመ ነትገ ማየ አይኅ ኢወለደት ሜልኮል እስከ አመ ሞተት እንዲል ሜል ኮል ከሞተች በኋላ ወለደች ማለትን ነው ፍጻሜ የሌለው እስከ ነው ፤ እንድም ባንድ ኅብረ መልክእ አላወቃትም ሲል ነው ሥጋዌው በብዙ ኅብረት ትንቢት የተነገረለት በብዙ ኅብረ አምሳል የተመ መሰሉትን እሱን እንደፀነሰች ለማጠየቅ መልኳን ይለዋውጠው ነበርና ። ቦ ኢመ ታሕመስምል ወቦ አመ ትጸዓዱ እንዲህ ስንኳን የፀሐየ ጽድቅ ሰሌዳ ድንግልን ሙሴንስ እንኳ ኃላፊ ብርሃን ቢሳልበት እስራኤል ተገልበብ ለነ ብለውታል እንድም ኢያእ መረ ይላል ወልድ የተባለ እሱ ድንግል የተባለች ልርበዊ እንደ ሆነች አላወቀም አጸፋውን ለወንጌ ላዊ የሰጡ እንደሆነ ምነው መልአኩ ነግሮት የለ ምን ቢሉ ፤ ፩ ከሆነ ብሎ ፩ ዓይን እያስረግጥ ፤

፩ ምስክር ኢያስደነግጥ እንዲሉ ፤ አጸፋውን ለመልአኩ የሰጡ እንደሆነ ነቢዩ ነግሮት የለምን ቢሉ ድንግል አለ እንጂ እሷን አለው ወልድ አለው እንጂ እምላክን አለው ብሎ አምስት ነገር አይቶ ኢበኪረዳ ድረስ ኢያእመረ አላወቀም ። ምጽእተ ሰብእ ሰገል ዘምስለ አምኃ ፤ ሐረተ ኮከብ በካልእ ፍና ፤ ሥርቀተ ሰብሐተ እግዚእ ዓቢይ ቅዳሴ መላ እከት ፤ ፍርሃተ ኖሎት ይህን አይቶ እስኪረዳ ድረስ ዐላወቀም ። በኩራ በጥንት በበዓት በተቀድሶ ። ወጸውዐ ስሞ ኢየሱስሃ ።

እስከ አመ ወለደት ወእስከ አመ ጸውዐ መጻሕፍት በዞር ያሉላት ልጇዋን እስከትወልድ በሙንም ኢየ ሱስ ብሎ እስኪጸሩት ድረስ ኢያእመረ፤እንድም ዘበ ኩራ ወዘጸውዐ መጻሕፍት በዞር ያሉላት በሙንም ኢየሱስ ያሉት ልጇዋኒ እስከትወልድ ድረስ ኢያ እመረ ። ወአኮ በከመ ቃየን ዘእምእኩይ ወቀተሎ ለእኍሁ እንዲል ። ወዘቀተሎ ሲል ፤ በእንተ ምጽአተ ሰብአ ሰገል ።

ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወተወሊዶ እግዚእ ኢየሱስ በቤተ ልሔም ዘይሁዳ በመዋዕለ ሄሮድስ ንጉሥ ናሁ ሰብአ ሰገል መጽኡ እምብሔረ ጽባሕ ። ሉቃ ፪ ፥፯ ።

፩ ሄሮድስ ነግሦበት በነበረ ዘመን የይሁዳ ዕፃ በምትሆን በቤተ ልሔም ጌታችን ኢየሱስ ክር ስቶስ ተወልዶ ሳለ በተወለደ ጊዜ ከተወለደ በኋላ ። ሰብአ ጥበብ ሲል ነው ጥበብ ያላቸው ሰዎች ከወደ ምሥራቅ መጡ ገል ውስተ አፈ ንጉሥ እንዲል ። እንድም መሰግላን ይላል ጥበበኞች ሰዎች ማለት ነው ።

ሐተታ ፣ ቤተ ልሔምን እነሣ ወአንቲኒ ቤተልሔም ብሎ የሚያመጣ ነውና ሄሮድስን እነሣ ወአዘዘ ይቅትሉ ኵሎ ሕፃናተ ዘቤተልሔም ብሎ የሚያመጣ ነውና ፣ አንድም ቤተልሔምን እነሣ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፡ ትንቢት ወአንቲኒ ቤተልሔም ተብሎ ተነግሯል ምሳሌ ካሌብ ምድረ ርስትን ሰልሎ ሲመለስ ኬብሮንን አይቶ መጥቶ ኢያሱን ኬብሮንን ስጠኝ ቀድሞ ሙሴ ሰጥቶኝ ነበር ፡ ካሥራ ሁለቱ ጉበኞች አንዱ እኔ ነበርኩ ያን ጊዜ ፵ ዘመን ሁኜኝ ነበር ፤ ዛሬም ፹ ዘመን ይሆነኛል ካንተ ጋራ መውጣት መውረድ ይቻለኛል ገና ከጉልበት ነኝ አለው እሥራኤልን አስመክር ሰጠው እሱዋን እጅ አድርጎ እዙብ የምትባል አገባ ። ከጠላቶቹ ወገን ነበረችና በሱዋ ስም አልጠራትም ፣ ቀጥሎ ክብታ የምትባል አገባ በክብታ ክብታ ተብላለች ቀጥሎ ኤፍራታ የምትባል አገባ ፣ በኤፍራታ ኤፍራታ ተብላለች ። ከሱዋ ወንድ ልጅ ወለደ በዚያ ወራት እንጀራ አገባ አገባ ብሎት ነበርና ስሙንም ልሔም አለው ጎብስት ማለት ነው ። ወአምጽኡ ልሔሞሙ እንዲል ኅብስቶሙ ሲል በልሔም ቤተልሔም ተብ ላለች ክብታ ማለት ቤተ ስብሐት ማለት ነው ቤት የእመቤታችን ስብሐት የጌታችን ምሳሌ ኤፍራታ ማለት ጸዋሪተ ፍሬ ማለት ነው ፤ ጸዋሪት የእመ ቤታችን ፍሬ የጌታችን ምሳሌ ቤቀልሔም ማለት ቤተ ኅብስት ማለት ነው ቤት የእመቤታችን ልሔም የጌታችን ምሳሌ ።

ሄሮድስን አነሳ ዘመን ትውልድ የሚቆጠር በን ጉሥ ነውና ። ታሪክ እስክንድር የሚባል ንጉሥ ነበረ እስክንድርያ የምትባል ቤት አግብቶ አቶሮብ ሎስን ሕርቃሎስን ይወልዳል በሚሞትበት ጊዜ ለሚስቱ ታናሹን እንግሡሽ ታላቁን ካህን አድርገሽ ኑሪ አላት ፣ አድልቶ አይደለም ታናሹ ሕርቃሎስ ብልህ ነው ሰው ማሳደር ያውቃል ብሎ ነው እንጂ እንደ ነገራት አድርጋ ስትኖር ፣ ሄሮድስ ወደ ሐን ዶፌር የእስራኤልን መንግሥት በማናቸውም ምክ ንያት ይፈላለገው ነበርና ከታላቁ ከአትሮብሎስ ይልክበታል ፣ ታላቅ ባለህ ታናሽ አዋቂ ባለህ ላዋቂ ያንገሡብህ በምን ምክንያት ነው ፣ ጦርም እንሰህ እንደሆነ ከኔ ወሰደህ እሱን ገድለህ ንገሥ አለው እሱም እውነት መስሎት ጦር ተቀብሎ መጥቶ ወን ድሙን ገድሎ ነገሠ ፣ የሕርቃሎስ አርስጥእሎስ የሚ ባል ልጅ ነበረው በጥበብም ቢሉ ተዋግቶም ቢሉ ያጕቱን ጆሮውን ቈረጠው ። እሥራኤል አካሉ የጐደለ አያነግሡም ነበርና መንግሥት በመካከል ላለ እኅታቸው ማርያ ትባላለች እሱዋን አግብቶ ነገሠ ምንም እሱ በጥበብ በተንኮል የነገሡኩ ቢመ ስለው መንግሥት ከቤተ ይሁዳ አልመጣም ። ኢይ ጠፍዕ ምስፍና ወምልክና እምእባሉ ለይሁዳ እስከ አመ ይረክብ ዘጽንሐ ሎቱ ተብሎ የተነገረው ትንቢት እንደ ተፈጸመ ለማጠየቅ በላዩ ላይ ስማያዊ ንጉሥ ተወለደ ለማለት ሄሮድስን አነ ሣው ። እምብሔረ ጽባሕ እለ ብርሃን የሚገኝ ከም ሥራቅ ነው ። ብርሀት ሕግ ሠራሁላችሁ ሲል ፤ የምሥራቅ ወርቅ ጽሩይ ነው ፤ ጽሪት ሕግ ሠራሁ ላችሁ ሲል እነሀስ ምን ይዘው መጥተዋል ቢሉ ሠለ ስቱ መላእክት ሦስቱን ንዋያት ወርቅ ዕጣን ከርቤ አምጥተው ለአዳም ሰጡት ፡ አዳም ንሥኢ ሕዜኪ ብሎ ለሔዋን ሰጣት ። ከዚያ ሲወርድ ሲዋረድ ካባ ታቸው እጅ ገብቷል ዝረደሽት የሚባል ፈላስፋ አባት ነበራቸው ፣ በቀትር ጊዜ ከነቅዓ ማይ አጠገብ ሁና ፍልስፍና ሲመለከት ድንግል በሰሌዳ ኮከብ ተሥላ ሕፃን ታቅፋ አየ ፈጥኖ በሰሌዳ ብርት ቀርጾ አኖረው ፣ በሚሞቱበት ጊዜ እንዲህ ያለ ኮከብ ሲወጣ ባያችሁ ጊዜ ሰማያዊ ንጉሥ ይወለዳልና ወስዳችሁ ስጡ ብሏቸው ነበርና ያን ሰምተው ይዘው መጥተዋል ። አንድም ዘእምዘመዱ ለበለዓም እንጂ ይላቸዋል ፣ በለዓም ኮከብ ይሠርቅ እምያዕቆብ ያለውን ሰምተው ይዘው መጥተዋል ፣ አንድም ትሩ ፋን ባቢሎን ሳሉ ነገሥተ ተርሴስ ወደሰያት አምኃ ያበውኡ ነገሥተ ሳባ ወዓረብ ጋዳ ያመጽኡ እያሉ ሲጸልዩ ይሰሙ ነበርና ይህን ይዘው መጥተዋል ። አንድም ባርክ አቴና ወርዶ ዐሥራ ሦስት ያህል ልሳን ተምሯል ያን ጊዜ ዛሬ የሀገራችሁ ንጉሥ የሚ ገበረውን ወርቅ ኋላ በሀገራችን ከኛ ወገን ንጉሥ ተወልዶ ይገበረዋል ብሎ ነግሯቸው ነበርና ይህንን ይዘው መጥተዋል ። አንድም ዳንኤል መቅደስ ትት ሐነጽ እስከ ክርስቶስ ንጉሥ ወእምዝ ትትመዘበር ያለውን ሰምተው ይዘው መጥተዋል ፣ አንድም ዳንኤልን ምንም እሱን ባውነቱን ባይወዱት ነገ ሩን ይቀበሉት ነበርና ዛሬ የናንተ ሀገር ንጉሥ የሚ ገበረውን ኋላ ከኛ ወገን ንጉሥ ተወልዶ ይገበረዋል ብሎ ነግሯቸው ነበርና ይህኑ ሰምተው ይዘው መጥ ተዋል ለነዚህስ እንዲገለጽላቸው ያደረገ ስለምን ቢሉ ይሹት ነበርና ለፍቅሩ ይሳሱ ነበርና ፣ ከሕደት በዚህ ጸንቶ ነበርና ፣ ከሕደትም ወደጸናበት መሄድ ልማድ ነው አሁን በመዋዕለ ሰደቱ ከሕደት ወደ ጸናባቸው ወደ ግብጽ ሄደ ብሎ እንዲያመጣው በእሥ ራኤል ዘለፋ ለአሕዛብ ተስፋ ለመሆን እኛስ እንኳ ዐውቀን ስንመጣ እስካሁን ሳያውቁት ኑረው ብለው አንድም ከመ ይንግሥ ንዋየ አቡሁ እንጂ ይላል ያባቱን ገንዘብ ለመቀበል ፣ እሶር የአክዩ በዕብራው ያን ወዕብራውያን የአክዩ በእሦር እንዲል ነገ ሥተ ፋርስ ለጸብእ እንጂ ለፍቅር አይመጡም ነበ ርና በጌታ ልደት ፍቅር እንደ ተጀመረ ለማጠየቅ

፪ ወበጽሐ ውእተ ኢየሩሳሌም እንዘ ይብሉ
አይቴ ሀሎ ዘተወልደ ንጉሠ አይሁድ ።

፪ የተወለደው የአይሁድ ንጉሥ ወዴት አለ እያሉ ፤ ኢየሩሳሌም ደረሱ ። ሐቲታ ፤ ምነው ኮከቡ ይመራቸው አልነበረምን ቢሉ ከስው ሲደርሱ ይሰወራቸው ነበርና ፤ ከዚህም ስም ሳዕላዊ ስም ማእከላዊ ስም ታሕታዊ አለ ፤ ስም ሳእላዊ ስም ታሕታዊ አልገለጠላቸውም ፤ ስም ማእከላዊ ገለጸላቸው እንጂ ስለምን ቢሉ ስም ላዕላዊ ገልጾላቸው ፤ አይቴ ሀሎ አምላክ ዘተወልደ አይቴ ሀሎ ፈጣሪ ዘተወልደ ብለው ጠይቀው ቢሆን ፤ እኒህ ሞኞች ተላሎች ሰማይንና ምድር የማይችሉትን ማን ችሎት ተወለደ ይላሉ ባሏቸው ነበርና ። ይህንማ እንዳይሉ አሕዛብ አይደሉ እስራኤል አይደሉምን ቅንጊት የተቆጠረውን ቡባኤ ያውቁ የለም ቢሉ ፤ በዚያውስ ላይ እኛ ይልቅ እናውቀውምን ባሏቸው ነበርና ስም ታሕታዊ ገልጾላቸው ፤ አይቴ ሀሎ ሕፃን ዘተወልደ ብለው ጠይቀው ቢሆን ፤ እነዚህ ሞኞች ተላሎች በአዕላፈ እሥራኤል ከቱማ እልፍ ሙቶ እልፍ ቶወልዶ ያድራል ስንቱን እናውቅላቸዋለን ባሏቸው ነበርና ፤ ስም ማእከላዊ ገለጹላቸው እ[ሰ]ሙ ርኢነ ኮከበ ዚአሁ በምሥራቅ ወመጻእነ ከ[መ] ንሰግድ ሎቱ ።

በተፈጥሮ ገንዘቡ የሚሆን ፤ እንድም እምሳያው የሚሆን ኮከቡን አይተን ልንሰግድለት መጥተናልና ፤ ይኸስ በቁሙ ኮከብ ነውን መልአክን ቢሉ ፤ መልአክ ነው ፤ በምን ይታወቃል ቢሉ ፤ ኮከብ በሌሊት እንጂ በመዓልት አይታይም ፤ በመዓልት በመታየቱ ፤ ኮከብ ወደ ምዕራብ ይሄዳል እንጂ ወደ መስዕ አይሄድም ፤ ወደመስዕ በመሄዱ ፤ ኮከብ መጥቶ ይሄዳል እንጂ በቆመ ብእሲ ዘቅዝቆ አይሄድም ፤ በቆመ ብእሲ ዘቅዝቆ በመሄዱ ይኸስ በሌሊት የሚታየውን በመዓልት እንዲታይ ወደ ምዕራብ የሚሄደውን ወደ መስዕ እንዲሄድ መጥቶ የሚሄደውን በቆመ ብእሲ ዘቅዝቆ እንዲሄድ የሚያደርግ እሱ ነው ብሎ በቁሙ ኮከብ ነው ፤ ስለምን በኮከብ መራቸው ቢሉ በለመዱት ለመሳብ ኮከብ ያመልኩ ነበርና ፤ ከዚያ ሁሉ ግብጻውያን ላም ያመልኩ ነበር በለመዱት ለመሳብ ላም ሠዉልኝ እንዳላቸው ።

፫ ወሰሚዖ ሄሮድስ ንጉሥ ደንገፀ ወተሀውከ

፫ ንጉሥ ያሉትን ሰምቶ ሄሮድስ ደነገጸ አሀነ፤ ሐተታ ፤ ንጉሥማ ከሆነ ንጉሥ ሳይገድል ይነግሣል ብሎ ።

ወሆላ ኢየሩሳሌም ምስሌሁ ፤ ተሀውከት ያለበት ነው ። ከተማይቱ ከሱ ጋራ እንደ እሱ ተደረጸች ፤ የንጉሥ ሞት የፀሐይ እርበት የሁሉ ነውና እንድም ሞስቱ ነገሥታት ማንቱ ቢማር በዲዳስፋሜልኩ ይባላሉ እልፍ እልፍ ሠራዊት አስከትለው መጥተዋልና ይኸን በሰማ ጊዜ ደነገጠ አዘነ ሕዝቡም ደነገጡ አዘኑ ፤ ፪ዋዊ ተመሳልሶባቸው ነበርና ፤ ታምረ ኢየሱስ ምስት ይላል ፤ ትርጓሜ ወንጌል ፲፪ አለ ፤ አይጣላም ቢሉ አይጣላም ፤ ነገር እንደ ትርጓሜ ወንጌል ነው ፤ ፀሥራ ሁለት ሁነው ተነሥተዋል ፤ ፈለገ ኤፍራጥስ ሲደርሱ ንጉሠ ነገሥቱ ፍርዌዑር ይባላል ዘጠኙን ይዟቸው ተመልሷል በምን ምክንያት ቢሉ ከወደኋላትሁ ጦር ተነሣባቸው ብለዋቸው ። እንድም ስንቅ አልቆባቸው ፤ እንድም ኢየሩሳሌም ጠባብ ናት ለሰፈር አትበቃም ብለዋቸው ምሥጢሩ ግን ከበረከት ልደቱ እንዳላሳተፋቸው ያጠይቃል ። በደቂቀ ነቢያት ወይትነሥኡ ፲፻ቱ ኖሎት ወ፰ቱ ሠራዊት ይላልና ቢሉ ፤ ሰባቱ ንጉሠ ነገሥትነት የደረሱ ናቸው ፤ አምስቱ ንጉሠ ነገሥትነት ያልደረሱ ናቸውና እንደ አንድ ንጉሠ ነገሥት አድርጎ ላምኖሙ በማለት ተናገራቸው እንጂ ነገር እንደ ትርጓሜ ወንጌል ነው ።

፬ ወአስተጋብአሙ ለኵሎሙ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍተ ሕዝብ

፬ የሕዝቡን ጸሐፍትና ሊቃነ ካህናትን ሰበሰባቸው ፤ ሐተታ ፤ ሊቀ ካህናቱማ አንድ አይደለም ቢሉ ፤ ምስና ዱማ ሁነው ተሹመው ነበርና ፤ እንድም አንዱ ሹም እንዱ የሹም ሹር ነው ፤ ጸሐፍት የሚላቸው ወተሠይሞሙ ለለነገዶሙ እንዲል ካሥራ ሁለቱ ነገደ እሥራኤል ተወጽጽተው ርስት ከርስት ትውልድ ከትውልድ እንዳይፋለስ የሚጽፉ ናቸው ። ይልቁንም ክህነት ከቤተ ሌዊ መንግሥት ከቤተ ይሁዳ እንዳይወጣ የሚጽፉ ናቸው። እንድም ከነገደ ስምዖን ተወልደው ይኸን ሁሉ የሚጽፉ ናቸው ከእህ ወግ ታሪክ አይታጣምና ብሎ ሰበሰባቸው ።

ወይቤሎሙ በአይቴ ይትወለድ ክርስቶስ ።
ክርስቶስ ወዴት ይወለዳል ብሎ ጠየቃቸው ።

፭ ወይቤልዎ በቤተ ልሔም ዘይሁዳ ።

፭ እንደ ዛሬ ምቀኝነት አልሰፋም ነበርና ቀንተው ይመልሱለታል ። የይሁዳ ዕፃ በምትሆን በቤተ ልሔም ነው አሉት ።

እስመ ከማሁ ጽሑፍ በነቢይ ፤ እንዲህ ያለ ጽሑፍ አለና ነበርና ይላል ወንጌላዊ ፤ ከነዋዌው ጠቅሰው ወበአንቲአከሙ ይጸርፉ አሕዛብ ላዕለ ስመ እግዚአብሔር እንዲል ።

፮ ወአንቲኒ ቤተ ልሔም ምድረ ኤፍራታ ኢትቴሐቲ እምነገሥተ ይሁዳ ፤ ሚክ ፭ ፤ ፪ ዮሐ ፯፡፵፪ ፯ የይሁዳ ዕፃ የምትሆኝ አንቺም ቤተ ልሔም የይሁዳ ነገሥታት ከነገሡባቸው አህጉር ብትበልጭ እንጂ አታንሽም የሚል ጽሑፍ አለና ነበርና ይላል እስመ እምኔኪ ይወጽእ ንጉሥ ዘይርእዮሙ ለሕዝብየ እሥራኤል ።

ወገኖቼ እሥራኤል ዘሥጋን የሚጠብቃቸው ንጉሥ ባንቺ ይነግሣልና ። ታሪክ ነቢዩ ሚክያስ ነው ሴላውን ሲያስተምር ውሎ ወደ ማታ በቤተ ልሔም በኩል አልፎ ሲሄድ ተፈታ ምድረ በዳ ሆና ቋያ በቅሉባት አየ ። እንዲህ እንጂ እንደሆንሽ አትቀሪም ንጉሥ ይነግሥብሻል የነጋሪት ድምፅ ይሰማብሻል ድንኳን ይተከልብሻል እሥራኤል ደጅ ይጠኑብሻል አሕዛብ ይገብሩብሻል ብሎ ትንቢት ተናገረ ይህም አልቀረ ዘሩባቤል ነግሦባታል እሥራኤል ደጅ ጠንተውባታል የነጋሪት ድምፅ ተሰምቶባታል አሕዛብ ገብረውባታል ድንኳን ተተክሎባታል እንድም ወገኖቼ እሥራኤል ዘነፍስን የሚጠብቃቸው ንጉሥ ክርስቶስ ባንች ይወለዳልና ዘሩባቤል እንደ ነገሠ ጌታ ተወልዶባታል፤ ድንኳን እንደ ተተከለባት የብርሃን ድንኳን ተተክሎባታል ፣ ነጋሪት እንደ ተሰማባት ቅዳሴ መላእክት ተሰምቶታል ፣ እስራኤል ደጅ እንደ ጠኑ መቶው ነገደ መላእክት ደጅ ጠንተውባታል አሕዛብ እንደ ገበሩ ሰብአ ሰገል ገብረዋል ። አንድም አንቺ የኤፍራታ ልጅ እመቤታችን በይሁዳ ከነገሡ ነገሥታት ብትበልጭ እንጂ አታንሽም ፣ ወገኖቼ እሥራኤል ዘነፍስን የሚጠብቃቸው ንጉሥ ክርስቶስ ባንቺ ባሕርይ ይወለዳል፣ እምኔኪ ካንች ይወለዳልና።

፯ ወእምዝ ጸውዖሙ ሄሮድስ ለሰብአ ሰገል ጽሚተ ።

፯ ከዚህ በኋላ ሰብአ ሰገልን በቆይታ ጸራቸው ካህናትን ጠይቆ ባዳራሽ አውጥቶ ሰብአ ሰገልን በእልፍኝ ጠራቸው ፣ አሁን ከኛ ጠይቆ ይነግራቸዋል እንዳይሉት ፣ አንድም ካህናትን በእልፍኝ አስወጥቶ ሰብአ ሰገልን በአዳራሽ አስጠራቸው ፣ ይኸም ውዳሴ ከንቱ ሽቶ ነው ። እኛስ እንኳን አውቀን ስንመጣ እሱ ከዚህ ሁኖ እስከዛሬ ሳይሰማ ከዚህ ሁኖ እስከ ዛሬ ሳይሰማ ኑሯል ይሉኛል ብሎ ።

ወተጠየቀ እምኔሆሙ መዋዕሊሁ በዘአስተርአዮሙ ኮከብ። ኮከብ የታየበትን ቀን ጠየቃቸው ። አንድም ኮከቡ በታየበት ቀን የጌታን ዘመኑን ዐውቆ ተረዳው ፤ ይህን ኮከብ ካያችሁ ምን ያህል ዘመን ሁኖታል አላቸው ፣ ሁለት ዓመት ሁኖታል አሉት ፣ ለካ ያም ብላቴና ሁለት ዓመት ሁኖታል አለ !

፰ ወፈነዎሙ ኀበ ቤተልሔም

፰ ቤተልሔም ነው ብሎ ሰደዳቸው ።
ወይቤሎሙ ሐዊረክሙ ተስእሉ ጥዩቀ በእንተ ውእቱ ሕፃን ወእምከመ ረከብክምዎ ግብኡ ኀቤየ ወዜንውኒ ሄዳችሁ የብላቴናውን ነገር ጠይቃችሁ ድርሱን ያገኛችሁት እንደሆነ በኔ በኩል ተመልሳችሁ ንገሩኝ አላቸው ።

ከመ እምጻእ አነሂ ወእስግድ ሎቱ ።
እኔም መጥቼ መእሰግድሰት ዘንድ ፣ ለሄሮድሳውያን ጉሕሉት ልማዳቸው ነውና እሰግድ ሎቱ አለ እንጂ እቅትሎ ሲል ነው ሐተታ እንዲህማ ከማለት ተቀድሞ ሄዶ አይነግራቸውምን ቢሉ ካህናቱ ዘመዶቹ ናቸውና ልከው ያሸሹብኛል ብሎ ። ባንድ ሂዶ አይገድለውም ነበር ቢሉ ሰብአ ሰገል ይጋሳግሉኛል ብሎ ፣ አይሆንም ያልኋቸው እንደሆነ እልፍ እልፍ ሠራዊት አስከትለው መጥተዋል አግባ መልስ ብለው ይጣሉኛል ብሎ አንድም እኛ ብቻ መስሎን የሆነሩም ነገሥታት ያምኑበታልሳ ብለው የሰብአ ሰገል ሃይማኖታቸው እንዲጸናላቸው ፣ መንፈስ ቅዱስ አፉን ከፍቶ ፈቱን ጸፍቶ እናገረው ።

ወሰሚያሙ ሐሩ እምኀበ ንጉሥ ፤

ቤተልሔም ነው ያላቸውን ሰምተው ወተእዚዞሙ ይላል ፣ ወእምከመ ረከብክምዎ ግብኡ ኀቤየ ያላቸውን ሰምተው ንጉሥ ነውና ይበጅ ያድርግ ብለው ሄዱ ።

፱ ወናሁ ኮከብ ዘርእዩ በምሥራቅ ይመርሆሙ እስከ ሶበ አብጽሖሙ ቤተልሔም ።

፱ በምሥራቅ ያዩት ኮከብ ቤተልሔም እስኪያደርሳቸው ይመራቸው ነበር ።
ወቆመ መልዕልተ በዓት ኀበ ሀሎ ሕፃን ።
ባለበት ቦታ በሰው ቁመት ልክ ዘቅዝቆ ቆመ በጣት ጠቅሶ እንደ ማሳየት ።

፲ ወርእዮሙ ኮከበ ተፈሥሑ ዓቢየ ፍሥሐ ።

፲ ኮከቡን አይተው ፈጽመው ደስ አላቸው ፣ ስልማዱ ከሰው ሲደርሱ ይሰወራቸው ከሰው ሲለዩ ይመራቸው ነበር አሁን ሲገለጽላቸው እሱ እንጂ ቢሆን ነው ብለው ፣ አንድም ስንኳን ሁለት ዓመት ያሄዱለት ነገር ሁለት ሰዓት የሄዱለት ነገር ሲፈጸም ደስ ያሰኛልና ፤ አንድም እንዲህ መርቶ ከምን ያደርሰን ይሆን ፣ ከባሕር ያጠልቀን ከገደል ይጥለን ከጾር ያደርሰን ይሆን ብለው ነበርና ካሰቡት ቢያደርሳቸው ደስ አላቸው ፣ አንድም የሚቀድመው አለ ።

፲፩ ወበዊዖሙ ውስተ ቤት ረከብዎ ለሕፃን ምስለ ማርያም እሙ መዝ ፸፩፤ ፲

፲፩ ከቤት ገብተው ብላቴናውን ከናቱ ጋራ አይተው ፣ ከዚህ በኋላ ኮከቡን አይተው እምሳያውሁኖ ቢያገኙት ፈጽሞ ደስ አላቸው ። ቤት በዓት ጎል ይላል አብነት ፣ ቤት ቢል የሴፍ እንደ ዳስ አድርጎ ጥሎ ነበርና በዓት ያለ እንደሆነ ኢዮስያስ በጨውማሽጋ ግምብ አሠርቶ ነበርና ፣ ጨውን ሲልሱ እንስሳት እየጋጡ አጐድጉደውት ነበርና ፣ ጎል ያለ እንደሆነ የተመቸ የእንስሳት ማደሪ ሁኖ ነበርና ። ወወድቁ ወሰገዱ ሎቱ ።

ከፈረሰ ከሰረገላ ወርደው ሰገዱለት ፤ አንድም መላ ልሰው ሰገዱለት ፤ ሐተታ ፤ እንደ ስናሩ ንጉሥ ጃን ተክል ሲደርስ ይሰግዳል ፤ የታዘዘ ብላቴና መጥቶ ተንሥ ብለውሃል ይለዋል ፤ ዳግም አልፎ ይሰግዳል ተንሥ ብለውሃል ይለዋል እንዲህ እያለ ከዚያ ሲደ ርስ እጅ ነሥቶ ከዙፋኑ በቀኝ አብሮ ይቀመጥ ነበር ። ወአርኃው መዛግብቲሆሙ ፤ ሣጥናቸውን ከፈቱ ፤ አየራሳቸው ጭነዋል ያሉ እንደሆን የተመቸ ፤ አንድ ነው ያሉ እንደሆነ ስደፋ ብዙ ነውና ፤ እንዴ ሰደፍ ነፍጥ ፤ አንድም ፈትሑ ወአርኃው ይላል ሣጥና ቸውን ከፈቱ ኮረጆዋቸውን ፈቱ ።

ወአብዑ ሎቱ አምኃ ወርቀ ከርቤ ወስኂን ።

ወርቁን ዕጣኑን ከርቤውን ግብር አገቡለት ፤ ሐተታ ወርቅ አመጡለት ይህን የምንገብራቸው ነገሥታት ቀድሞም ፍጡራን ኋላም ኃላፍያን ናቸው አንተ ግን ቀድሞም ያልተፈጠርህ ነህ ኋላም የማታልፍ ነህ ሲሉ ፤ ዕጣን አመጡለት ይህን የምናጥናቸው ጣዖ ታት ቀድሞም ፍጡራን ኋላም ኃላፍያን ናቸው ። አንተ ግን ቀድሞም ያልተፈጠርህ ኋላም የማታልፍ ነህ ሲሉ ፤ ከርቤ አመጡለት ምንም ቀድሞ ያልተ ፈጠርህ ኋላም የማታልፍ ብትሆን በሰውነትህ መራራ ሞትን መቀበል አለብህ ሲሉ ፤ አንድም ወርቅ ጽሩይ ነው ፤ ጽሩየ ባሕርይ ነህ ሲሉ ፤ ዕጣን ምዑዝ ነው ፤ ምዑዝ ባሕርይ ነህ ሲሉ ፤ ከርቤ የተሰበረውን ይጠ ግናል የተለየውን አንድ ያደርጋል ፤ አንተም ከማ ኅበረ መላእክት የተለየ አዳምን አንድ ታደርገ ዋለህ ጽንዓ ነፍስ ሰጥተህ ታጸናዋለህ ሲሉ ፤ አን ድም ወርቅ ጽሩይ ነው ባንተ ያመኑ ምእመናን ጽሩ ያን ምግባር ወሃይማኖት ናቸው ሲሉ ፤ ዕጣን ምዑዝ ነው ፤ ባንተ ያመኑ ምእመናን ምዑዛን ምግባር ወሃይማኖት ናቸው ሲሉ ፤ ከርቤ አመጡለት በዕለተ ዓርብ ያቀምሱታልና ፤ አንድም ወርቅ የሰማዕታት ምሳሌ ነው ከመ ወርቅ በእሳት ፈተኖሙ ለሰማ ዓዕት እንዲል ዕጣን የባሕታውያን ፤ ከሩቅ እንዲ ሸት ባሕታውያንም በተስፋ ይኖራሉ ፤ ከርቤ የም አመናን በፍቅር አንድ ይሆናሉና ፤ ወርቅ አመጡ ለት ወርቅ የሃይማኖት ምሳሌ ወርቅ ጽሩይነ ቱም ግብዝነቱም የሚታወቅ በእሳት ሲፈተን ነው፤ የሃይማኖትም ጽሩይነቱና ግብዝነቱ የሚታወቅ መከራ ሲቀበሉበት ነውና ፤ ዕጣን የተስፋ ፤ ዕጣን ከሩቅ እንዲሸት ፤ ተስፋም ያልያዙትን እንደያዙት ያላዩ ትን እንዳዩት ታደርጋለችና ። አሚንሰ ትሬስዮ ለዘኢሀለወ ከመ ዘሀለወ እንዲል ፤ ከርቤ የፍቅር ያ አንድ እንዲያደርግ ፍቅርም አንድ ታደርጋለችና ሃይማኖት ፍቅር ተስፋ ገንዘቦችህ ናቸው ሲሉ ፤ ወርቅ ዕጣን ከርቤ ገበሩለት ፤ አንድም ወርቅ የመላ እከት ዕጣን የደቂቀ አዳም ከርቤ የካልዕ ፍጥረት፤ ከመ ለስሙ ለኢየሱስ ክርስቶስ ይስግድ ኵሉ ብርክ ዘውስተ ሰማይ ወዘውስተ ምድር ወዘታሕተ ምድር እንዲል ፤ መላእክት ደቂቀ አዳም ካልዕ ፍጥረት ገንዘቦችህ ናቸው ሲሉ ወርቅ ዕጣን ከርቤ አመጡ ለት ይህስ ከወዴት የመጣ ነው ቢሉ ሦስቱ መላእ ክት ቅዱስ ሚካኤል ቅዱስ ገብርኤል ቅዱስ ሩፋኤል ወርቅ ዕጣን ከርቤ አምጥተው ለአዳም ሰጡት ፤ አዳም ንሥኢ ሕጼኪ ብሎ ለሔዋን ሰጣት ሔዋን ለሴት ሰጠችው ከሴት ሲወርድ ሲዋረድ ከኖኅ ደር ሷል ። ኖኅ ከመርከብ ሲገባ ይዞት ገብቷል ሲወጣም ይዞት ወጥቷል በሚሞትበት ጊዜ ሴምን ልጄን ከወንድምህ ከካም ወገን ደግ ልጅ ይወለዳ ልና ካባት ከናቱ አስናብተህ ወርቁን ዕጣኑን ከር ቤውን አጽመ አበውን አስጠብቀው ሥራት ሥራ ብት ብሎታል ፤ ካባት ከናቱ አስናብቶ ወርቁን ዕጣ ኑን ከርቤውን አሸክሞ ሲሄድ ወንድሞቹ ያፌቱና ክፃ ተከተሉት እናንተ አልታዘዛችሁም የታዘዝን እኛ ነን ተመለሱ አላቸው ተመለሱ ፤ መልአክ ተገ ልጾ እየመራቸው ሄዱ ዱዳሌም ሲደርሱ ጐድጓዳ ቦታ አገኙ ዓጽመ አበውን ቀብሮ ሦስቱን ንዋያተ ሰጥቶ ሥራት ይሠራበታል ከቤት አትድረስ ዳባ ልበስ ሥጋ አትብላ ጠጅ አትጠጣ ራስክን አት ላጭ ጥፍርህን አትቁረጥ በሥንዴ በወይን አስታኵት ብሎ ፤ እንዲህ ሁኖ ሲኖር ፤ አብርሃም ላምበቱ ነገ ሥት ሰዶም ረድቶ አራቱን ነገሥት ኮሎዶጎሞርን ድል ነሥቶ ሲመለስ ጅስ ቢለው በመዋዕልየኑ ተፈነ ቃለከ ወሚመ ታርእየኒሁ ኪያሃ ዕለተ አው አልቦ አለው ፤ እሱንስ አታየውም ምሳሌውን ታያለ ህና ሑር ዕድዎ ለዮርዳኖስ የርዳኖስን ተሻግረህ ሂድ አለው ዮርዳኖስን ተሻግሮ ቢሄድ መልከ ጼዴቅ ኅብስተ በረከት ጽዋዓ አኰቴት ይዞ ተቀ ብሎታል ፤ መልከ ጼዴቅ የቀሳውስት አብርሃም የም እመናን ኅብስቱ የሥጋው ጽዋዕ የደሙ ዮርዳኖስ የጥምቀት ምሳሌ ፤ በዚህ ጊዜ መልከ ጼዴቀ ወር ቁን ዕጣኑን ከርቤውን ለአብርሃም ሰጠው ከአብር ሃም ለይስሐቅ ከይስሐቅ ለያዕቆብ ደርሶዋል ያዕ ቆብ ወደግብጽ ሲወርድ ይዞት ወርዷል ሲወጣም ይዞት ወጥቷል ፤ ከያዕቆብ ሲወርድ ሲዋረድ ከዕ ሤይ ደርሶዋል ፤ ከዕሴይ ለዳዊት ከዳዊት ለሰሎሞን ከሰሎሞን ለሮብዓም ደርሶዋል ፤ በሮብዓም ጊዜ መን ግሥት ከሁለት ተከፈለ ፤ ኢዮርብዓም ወልደ ናባጥ ባሥሩ ነገድ በሰማርያ ፤ ሮብዓም በሁለቱ ነገድ በኢየሩሳሌም ነገሡ ሁለቱ ቢጣሉ ሱስቀም ንጉሠ ግብጽ ለኢዮርብዓም ረዳት ሁኖ መጥቶ ሮብዓምን ወግቶ ግብጽ ይዞት ወርዷል ፤ ይህም ብቻ አይደለ ፤ ሰሎሞን ወደ ቤተ እግዚአብሔር ሲገባ ብላቴኖቹ ይዘው የሚከተሉት ሦስት መቶ የወርቅ ጋሻ ሦስት መቶ የወርቅ ጦር የወርቅ ሾተል አሠርቶ ነበር ይህን ሁሉ አውርዶታል ፤ ከግብጽ ባቢሎን እንደምን ይወርዳል ቢሉ ናቡከደነጾር

ፊርያን ኒካሁን ገድሎ ሦስት ዓመት ባቢሎን ዘግብጽ አለኝቶ ሲሄድ ከግብጽ ባቢሎን ይዞት ወርዷል ፤ ከዚያ አግኝተው ይዘው መጥተዋል ፤ ሲረዳውስ መጥቶ አይወስድበትም እሕዛብ የሰው ከብት ናቂ ዎች ናቸውና ብሎ ሮብዓምን ወጉኖ ለኢያርብዓም ሰጥቶት ይሄዳል ። ኢያርብዓም ከኢየሩሳሌም ሰግ ስጦ ይዞት ወርዷል ፤ ስልምናሶር ዐሥሩን ነገድ በማ ረከ ጊዜ ፋርስ ባቢሎን ይዞት ወርደዋል ከዚያ አግ ኝተው ይዘው መጥተዋል ። አንድም አሚሰያስ በሁለቱ ነገድ በኢየሩሳሌም የአስ ባሥሩ ነገድ በሰማርያ ነግሦ አሜስያስ ንጉሥ ኢዮምያስን ወግቶ ሲመለስ ኃይል ቢሰማው ነዓ ንትረዓይ ገጸ በገጽ ብሎ በዮአስ ላከበት ። እሱም እስመሁ ሞዕከሙ ለኤዶምያስ ተዘንገረ ልብከ ፤ ኢቃኒ ዘውስተ ዕፅ ለአከት ኀበ ዕፀወ ቄድሮስ እንዘ ትብል ሀቦ ወለ ተከ ለወልድየ ፤ ወመጽኡ ዓራዊተ ገዳም ወኬድዋ ለዓቃኒ ብሎ ገሥግሦ ሄዶ ገጠመው ድል አድርጎ ታል በአንቀጸኤፍሬም አራት መቶ ክንድ አደባባይ አለ በዚያ አስነትቶታል ንጉሠ እሥራኤል ኃያላን ነን ነገሥተ ይሁዳ ድኩማን ናቸው ሲል ፤ በዚህ ጊዜ ከኢየሩሳሌም ሰማርያ አውርዶታል ፤ ከሰማርያ ስልምናሶር ዓሥሩን ነገድ በማረከ ጊዜ ፋርስ አውር ዶታል ፤ ከዚያ አግኝተው ይዘው መጥተዋል ፤ ይህማ እንዳይሆን ዘእንበለ ያእምር ሕፃን ስምየ አቡሁ ወእሙ ይነሥኢ ኃይለ ደማስቆ ወምህርካ ሶርያ ይቅ ካሬል ይላልሳ ቢሉ ወርቁ እንጂ ብዙ ነው ከዚ ያም ከዚያም ደርሷል ፤ አንድም እግ በሁለቱ ነገድ ፤ በአስ በዓሥሩ ነገድ ነግሠው ሳሉ የአሳ ፤ ራማ የምትባል መውጫ መግቢያ ነበረችው ፤ ባእስ ሄዶ ቀጸረበት በዚህ አዝኖ ሳለ በዚህን ታዝናለህ ከወልደ አዴር ጋራ ሊወጋህ ተማምሎብሃል አሉት ኀድግእ ኪዳነ ዘተካየድከ ምስለ በአስ ብሎ ከቤተ እግዚአብሔር ዕቃቤት ከቤተ መንግሥት ዕቃቤት የተገኘውን ወርቅ ጨምሮ ለወልደ አዴር ወልደ ጤዲርማን ወልደ አዚን ወልደ አዛሄል ንጉሠ ሶርያ ይብድለታል በዚህ ጊዜ ሶርያ ይወርዳል ፤ አንድም ኢዮአስ በሁለቱ ነገድ ነግሦ ሳለ አዛሄል ሰባት ያህል አኀጉር ወግቶ መጥቶ ከዳር ሰፍሮ ገብር አለው ። አቱእ እግዚእየ ዘአጸርከኒ እፀውር ብሎ ከቤተ እግዚ አብሔር ዕቃቤት ከቤተ መንግሥት ዕቃቤት የተገ ኘውን ወርቅ ሰዶለታል ሶርያ ይወርዳል ፤ ከሶርያ ፋርስ ባቢሎን እንደምን ይወርዳል ቢሉ ቴልጌል ቴልፌልሶር በፋርስ ረዓሶን በሶርያ ፋቁሄ ወልደ ሮሜልዩ በሰማርያ አካዝ በኢየሩሳሌም ነግሠዋል በሶርያና በሰማርያ መካከል ራማት ዘገለዓድ የምት ባል አገር አለች የሶርያው ሲበረታ ወደሶርያ የሰማ ርያው ሲበረታ ወደ ሰማርያ የምትገዛ እንደ ዋግ ያለች ናት ዋግ የትግሬው ሲበረታ ወደ ትግሬ የበ ጌምድሩ ሲበረታ ወደ በጌምድር ትገዛ እንደ ነበረ በዚህ ጊዜ ፋቁሄ እጅ ነበረች ። እሱም ይህችን አገር ላንተ እስጥሃለሁ ላባቶቼ ሲገዙ የነበሩ ሁለቱ ነገድ አምፀውብኛልና እነዚያን አስገዛኝ ብሎ ክረ ዓሶን ላከበት በዚህ ተማምለው ሁለቱ አንድ ሁነው ወደ ኢየሩሳሌም ዘመቱ ። ወዕበ ስምዓ ዘንተ ዳዊት ደንገፀት ነፍሱ ወነፍሰ ኵሉ ሕዝቡ እንዲል ። አካዝ ይህን ሰምቶ ገብርከኒ ወወልድከኒ ፤ በግድ ባሪህ በፈቃድ ልጅህ ነኝና ፤ እርዳኝ ብሎ ከቴልጌልቴ ልፌልሶር ዘንድ ላከበት እሱም ከተት ሠራዊት ምታ ነጋሪት ብሎ ዘመተ ፤ ሶርያ ሲደርስ ይህች አገር የማናት ብሎ ጠየቀ የረአሶን አሉት ። እሱ ወዴት ሄዷል አለ አካዝን ሊወጋ ኢየሩሳሌም ሄዷል አሉት የአካዝን ብላቴና ጥሩ ብሎ አስጠርቶ ጌታህ እርዳኝ ብሎ የላከብኝ ወዴት ድረስ ነው አለው ። ኢየሩሳሌም ድረስ አለው ። ልጅ እንጂ ቢሆን የጦር መላ ባያውቅ ነው ብሎ ተኩሶ ዝረፍ አለ ፤ የቀጡን አወርድ ብላ የብብቷን ማለች እንዲሉ ፤ የሰው አገር እንወጋለን ብላችሁ አገራችሁ ተወጋ ላችሁ አሏቸው ፤ ተመልሰው ገጠሙት ረዓሶን በፃ ፍጥ ተመቶ ከዚያውሙቷል ፤ ፋቁሄ ተመቶ ከገፉ ይሞታል ፤ በዚህ ጊዜ ቴልጌቴልፌሶር ከሶርያ ፋርስ አውርዶታል ። ከዚያ አግኝተው ይዘው መጥተዋል እምጥተው ለእመቤታችን ሰጧት ፤ እመቤታችንም ተቀብላ ከፍላ ለነዳያን መጽውታለት ለቅዱስ ጴጥሮስ ሰጥታዋለች ቅዱስ ጴጥሮስም ከፍሎ ለነዳያን መጽ ውቶለት ለቀሌምንጦስ ሰጥቶታል ቀሌምንጦስ ከፍሎ ለነዳያን መጽውቶለት ከሰምንቱ መጻሕፍት ጋራ በአንቀጸ ሮም ቀብሮታል ፤ እነዚህስ ምን ጊዜ ቱን ሥተው ምን ጊዜ ደርሰዋል ቢሉ ለልደት ሁለት ዓመት ሲቀረው ተነሥተው የልደት ለት ደርሰዋል ይህ በምን ይታወቃል ቢሉ ኤጲፋንዮስ የም ተወልደ ይላልና ፤ ይህማ እንዳይሆን እመቤታችን ሰብአ ሰገልን ሸኝታ አልዋለችም አላደረችም ወደያው መንገድ ጀመረች ይላል በሰምንት ቀን ቤተ ግዝ ረት መግባት ባርባ ቀን ዕጉለ ርግብ ዘውገ ግዕነት ይዞ ቤተ መቅደስ መግባት ይቀር የለም ቢሉ አይ ቀርም ። ቄሣር በግብር ምክንያት አስጠርቶት ሮም ሁለት ዓመት ኑሮ ይመለሣል ከዚያ በኋላ ነገሩን ያነሳዋል አንድም መንፈስ ቅዱስ ሁለት ዓመት ነገሩን አዘንግቶት ከዚህ በኋላ ያነሣዋል ። አንድም የልደት ዕለት ተነሥተው በሁለት ዓመት ደርሰዋል ወሠሊጦሙ ግብሮሙ አተው ሀገሮሙ ናዝሬተ ይላል ፤ ወዴት አግኝተው ይሰጧታል ቢሉ በእድ ባረሊባኖስ ሳለች ባመት ባመት ለገቢረ በዓል ትወጣ ነበርና ከዚያ አግኝተው ይሰጧታል ፤ ኤጲፋንዮስ ዮም ተወልደ ይላል ዓ ቢሉ እንጂ ዛሬ ደብተራ ባመት ባመት ዮም ተወልደ እንዲል ።

ወርቅ ያመጣ የሴም ወገን ነው መንግሥት ከሴም ወገን ነውና ፤ ዕጣን ያመጣ የያፌት ወገን ነው ክህ ነት ከያፌት ወገን ይበዛሉና ፤ ከርቤ ያመጣ የካም ወገን ነው ፤ ምእመናን ከካም ወገን ይበዛሉና ፤ ወርቅ ያመጣ የሺያ ዓመት ነው ፤ መንግሥት ከዚህ በላይ በ፷ ዘመን ይገባል ለማለት ፤ ዕጣን ያመጣ ያርባ ዘመን ነው መንፈሳዊ ሹመት ከዚህ በላይ ባምሳ ዘመን ይገባል ለማለት ፤ ከርቤ ያመጣ የ፳ ዘመን ነው ከዚህ በላይ ሞት ያጠራጥራልና ፤ ለነዚህም ለሕፃኑ በአምሳለ ሕፃን ለወሬዛው በአምሳለ ወሬዛ፣ ለአረጋዊው በአምሳለ አረጋዊ ታይቷቸዋል ወጥ ቶው ሲሄዱ አንዱ መልካም ብላቴና አለ ፤ መልካም ጐልማሳ እንጂ ፤ መልካም አረጋዊ እንጂ ተባብለው ተመልሰው ቢገቡ በአምሳለ ሕፃን ለታየው በአም ሳለ ወሬዛ በአምሳለ ወሬዛ ለታየው በአምሳለ አረ ጋዊ በአምሳለ አረጋዊ ለታየው በአምሳለ ሕፃን ታይቷቸዋል ። ከዚህ በኋላ ወጥተው ነገር እንዳንተ መልካም ብላቴና አለው ፤ እንዳንተ መልካም ጐልማሳ እንጂ እንዳንተ መልካም አረጋዊ እንጂ ተባብለዋል። መልአኩ እንደሁላችሁም ነው አትጣሉ አላቸው ፤ ማየትንስ መስማት አያስረዳውም ብለው ተመል ሰው ቢገቡ በአምሳለ ሕፃን ለታየው በአምሳለ አረጋዊ በአምሳለ አረጋዊ ለታየው በአምሳለ ወሬዛ በአምሳለ ወሬዛ ለታየው በአምሳለ ሕፃን ታይቷቸው ለሁሉም ሦስት ሦስት መልክ ደርሷቸው ፍጹም አምላክነቱን በዚህ ተረድተው ሂደዋል ፤ እነዚህስ ክብር አላቸው ቢሉ የላቸውም ፤ ዕድማተ በለዓምን እ ብነ ሆሣዕናን እንዳናገረ የታምራት ነው ፤ ይህማ እንዳይሆን አመቦ ዘአከበረ ልደተ እግዚእ ይከውን ክብሩ ምስለ ሰብአ ሰገል ይላልና ብሎ ክብር ያላ ቸው ናቸው ይህም ሲታወቅ ወእስነቀቶሙ ኀብ ሰተ ስገም ይላል አመቤታችን ሐሪጸ ሰገም ስንቅ ሰጥታ ሰደደቻቸው እልፍ እልፍ ሠራዊት እየተመ ገበለት ባያልቅ አገራቸው ሲደርሱ ደግን ነገር ከከተማ ፤ ይዞ መግባት አይገባም ብለው ከከተማ በአፍአ ትተውት ገቡ ፤ ደርሳችሁ መጣችሁን አሏ ቸው ፤ አዎን አሉ ፤ ምን ምልክት አላችሁ አሏቸው፣ እነሱም ምልክታቸውን እንዲህ ብለው ተናገሩሁለት ዓመት የሄድነውን በ፱ ቀን ገባን እናቱ ስንቅ ሰጥ ታን ይህ ሁሉ ሠራዊት እየተመገበው ባያልቅ ከቡር ነገር ነውና ከከተማ ይዞ መግባት አይገባም ብለን በአፍአ ትተነው መጥተናል አሏቸው ።

እስኪ አሳዩን አላቸው ፤ ቢሄዱ ሲጤስ ሲነድ ተገኝቷል ። ከዚህ የተነሣ በእሳት እንጂ አምልኩ ሲለን ነው ብለው እሳት የሚያመልኩ ሁነዋል ። ናትናኤል ሀገረ ሰብከቱ ከዚያ ነውና ፤ ይኸስ የታ ምራት ነው ሰማዩን ምድሩን ባሕሩን የብሱን በፈ ጠረ በእግዚአብሔር እመኑ ብሎ አስተምሮ አሳምኖ አጥምቋቸዋልና ክብር ያላቸው ናቸው ፤

፲፪ ወነገሮሙ በሀልም ከመ ኢይግብኡ ኀበ ሄሮድስ ።

፲፪ በሄሮድስ በኩል እንዳይመለሱ በራእይ ነገራቸው ፤ ከነገ ከሠልስት ይመጣሉ ሲል አመቤ ታችን መንገድ እንድትገፉ ሃይማኖት እንዲሰፉ በመጡበት የተመለሱ እንደ ሆነ ሃይማኖት ይጸ ናል እንጂ ፤ አይሰፋም ባልመጡበት ቢመለሱ ግን ያልሰማው እየሰማ ይሰፋልና ፤ አንድ መንገድ እንዲቀርባቸው ሁለት ዓመት የመጡትን በ፱ ቀን ገቡ የሚል ነውና ።

ወእንተ ካልዕ ፍኖት ገብኡ ወአተው ብሔሮሙ በሌላ ጎዳና በሌላ ኃይለ ቃል በሌላ ሃይማኖት ወደ ሀገራቸው ተመልሰው ገቡ ። በሌላ ጎዳና ሁለት ዓመት የሄዱትን በ፱ ቀን ገብተዋል ፤ በሌላ ኃይለ ቃል አይቴ ሀሎ እያሉ መጥተው ነበር ። ረከብናሁ እያሉ ተመልሰዋል በሌላ ሃይማኖት ንጉሥ እያሉ መጥተው ነበር አምላክ እያሉ ተመልሰዋል ። በከመ ጐየ ውስተ ምድረ ግብጽ

፲፫ ወእምድኅረ ኃለፉ እሉ ናሁ መልአከ እግ ዚአብሔር አስተርአዮ በሕልም ለዮሴፍ ።

ወእንተ ካልዕፍኖት ገብኡወአተው ብሔሮሙ ብሎ ነበርና ፤

፲፫ ሰብአ ሰገል ከሄዱ በኋላ ከእግዚአብሔር የታዘዘ መልአክ ለዮሴፍ በሕልም ነገረው ፤ ሳሉ አለመንገሩ ከሄዱ በኋላ መንገሩ ስለምን ነው ቢሉ፣ ሰብአ ሰገል ሳሉ ነግሮት ቢሆን ሲሰደድ አይተው አምላክነቱን በተጠራጠሩ ነበርና ፤ አንድም ካልቀ ረስ ይዘነው እንሂድ ባሉ ነበርና ። ይዘውትም እንዳ ይሄዱ የጌታ ስደቱ ወደ ግብጽ ነው እንጂ ፤ ወደ ባቢሎን አይደለምና ። እንዘ ይብል ተንሥእ ወንሣእ ሕፃነ ወእሞ ወጕየይ ውስተ ምድረ ግብጽ ። ተነሥ ተህ እናቱን ብላቴናውን ይዘህ ወደ ግብጽ ሂድ ብሎ ነገረው ሐተታ ፤ ሕፃነ ወእሞ አለ ሕፃነ ብሎ እሞን ቢተው ብላቴናውን አለኝ እንጂ እናቱን አለኝ ባለ ነበርና እሞ ብሎ ሕፃነ ባይል እናቱን አለኝ እንጂ ብላቴናውን አለኝ ባለ ነበርና ሕፃነ ወእሞ አለ፤አንድም ሰይጣን የሆነ እንደሆነ አመልክቶ ይተ ዋል ለመልአክ ግን አካቶ መናገር ልማድ ነውና ሕፃነ ወእሞ አለ ። ወሀሉ ሀየ እስከ እመ እነግረከ ተመለስ ብየ እስክነግርህ ከዚያ ኑር አለው ። እስመ ሀለዎ ለሄሮድስ ይኅሥሦ ለሕፃን ከመ ይቅ ትሎ ። ሄሮድስ ብላቴናውን ሊገድለው ይሻው ዘንድ አለውና ።

፲፬ ወተንሥአ ነሥአ ሕፃነ ወእሞ በሌሊት ወሖረ ውስተ ብሔረ ግብጽ ።

፲፬ ተንሥአ ብላቴናውን እናቱን ይዞ በሌሊት ወደ ግብጽ ሄደ ኵብሳይ ለልማዱ መንገዱ ሌሊት ነውና አንድም ወዲያው እንደነገረው ሳያንተላክስ ሄደ ቢል ሖረ በሌሊት አለ ፤

፲፭ ወነበረ ህየ እስከ አመ ሞቱ ለሄሮድስ ። ሆሴዕ ፤ ፲፩ ፤ ፩ ።

፲፭ ሄሮድስ እስኪሞት ድረስ ፫ ዓመት ከመ ንፈት በግብጽ ኖረ ።

ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ እምኀበ እግዚአብሔር በነቢይ እንዘ ይብል እምግብጽ ጸዋዕክዎ ለወልድየ፡ እግዚአብሔር በነቢይ አድሮ ነቢይ ከእግዚአብሔር ተገልጾለት በነቢዩ ቃል ልጄን ከግብጽ ጠራሁት ተብሎ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ። ሐተታ ይህማ መውጣቱን ያስረዳል እንጂ መውረዱን ያስ ረዳልን ቢሉ ካልወረደ መውጣትን አለ አንድም እም ቅሉ ወደ ሲሆን ነው ፤ ተጸውዑ እምቴዎፍ ሎስ ጽውዓን እምሰማይ እንዲል ልጄን ወደ ግብጽ ጠራሁት ተብሎ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ወደ ግብጽ ያደረው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳ ሌው ሊደርስ ሊፈጸም ፤ ትንቢት ናሁ እወዲ እዴየ ውስተ ምድረ ግብጽ ፤ ወትክውን አሐቲ ሀገር ምሥ ዋዕ ለእግዚአብሔር ይላል ደብረ ቍስቋምም እስከ ንድርያም ቢሉ ፤ ወይወርድ እግዚእነ ውስተ ምድረ ግብጽ እንዘ ይጼዓን ዲበ ደመና ቀሊል ፤ እምግብጽ ጸዋዕክዎ ለወልድየ ተብሎ ተነግሯል ፤ ይህማ የተነ ገረ ለያዕቆብ አይደለም ቢል ለጊዜው ለያዕቆብ ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ ነውና ፤ ነቢየ ያነሥእ ለከሙ እምአኃዊከሙ ያለው ለኢያሱ ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ እንደሆነ ፤ምሳሌም አባቶቹ ወደ ግብጽ ተብ ደዋል ትንቢቱን አውቆ አናግሯል ። ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ አስመስሏል ፍጻሜው እንደምነው ቢሉ ግብጽ ታቀርበዋለችና ይሹታልና ለፍቅሩ ይሳ ሳሉና ፤ ክህደት በነዚህ ጸንቶ ነበርና ፤ ወደ ጸናበ ትም መሄድ ልማድ ነው ። አሁን በመዋዕለ ስብከቱ ደዌ ወደ ጸናባቸው ወደ ጌርጌሴኖን ሄደ ብሎ እንዲ ያመጣው ፤ አንድም ገዳማተ ግብጽን ለመባረክ ደጋጉ ገዳማት እንሲሐት እነ አስቄጥስ ከዚያ አሉና። አንድም መልኩን አይተው የሚያምኑ አሉና ። ወተ በሀሳ እዋልደ ቤሐት ንዑ ንርአዮ ለወልደ መንከራት እንዲል ፤ አንድም ኪዳነ መልከ ጼዴቅን ለመፈጸም ዘመዶቼን ማርልኝ ቢለው ልጄን በሥጋ ስድጂ እምርልሃለሁ ብሎት ነበርና ። አንድም ሃይማኖቶ ከሁሉ ሲጠፉ በግብጽ አይጠፋምና ፤ እስከ ምጽአት ድረስ ወልድ ዋህድ ስትል ትኖራለችና ፤ በዚያውስ ላይ መሰደዱ ስለምነው ፤ ቢሉ እንዳይሞት ጊዜው አልደረሰምና ከዚያ ሳለ ድኖም ቢሆን ምትሐት ነው ባሉ ነበርና ፤ አንድም አዳም ከዚህ ዓለም እፍአ ከምትሆን ገነት ተሰዶ ነበርና ለዚያ እንደ ካሰ ለማጠየቅ ፤ አንድም ለስማዕታት ስደትን ለመባረክ ሰማዕትነት ብቻ በእሳት በስለት አይደለም ። አገር ንም ጥሎ መሰደድ ሰማዕትነት ነውና ። አንድም ጕየተ ሕፃን አጕየየ ለዲያብሎስ እንዲል ። አጋ ንንትን ከሰው ልቡና አስወጥቶ ለመሰደድ ። በእንተ ሚጠት እምነ ግብጽ ።

፲፮ ወሶበ ርእየ ሄሮድስ ከመ ተሣለቁ ላዕሌሁ ሰብአ ሰገል ተምዐ ጥቀ ።

፲፮ ሄሮድስ እንደዘበቱበት ባየ ጊዜ ማለት ባንተ በኩል እንመለሳለን ብለው በሌላ ጎዳና እንደሄዱ በሰማ ጊዜ ፈጽሞ ተበሳጨ ፤ በማን ይበሳጫል ቢሉ ብስጩ ለልማዱ ባልጋው በመከዳው በቤተ ሰቡ የጨለማ ገልማጭ እንዲሉ ።
ወአዘዘ ሐራሁ ወፈነወ ይቅትሉ ኵሎ ሕፃናተ ዘቤተልሔም ወዘኵሉ አድያሚሃ ።
በቤተልሔም ባውራጃዋ ያሉ ሕፃናትን ሁሉ ግደሏ ብሎ አዝዞ ሰደደ ። ዘ፪ኤ ዓመት ፤ ወዘይንእስሂ እምኔሁ ።
ዓመት ከመንፈቅ ፤ ዓመት የሆነውንም ፤
በከመ ሐሳበ መዋዕል ዘተጠየቀ እምኀበ ሰብአ ሰገል፤ ከሰብአ ሰገል ጠይቆ በተረዳው ዘመን ልክ ፤

፲፯ አሜሃ ተፈጸመ ዘተብህለ በኤርምያስ ነቢይ እንዘ ይብል

፲፰ ቃል ተሰምዐ በራማ ።

ያን ጊዜ ኤርምያስ ቃል በራማ ተሰማ ብሎ የተና ገረው ትንቢት ደረሰ ተፈጸመ ይደርስ ይፈጸም ዘንድ አዘዘ ፤ ራማ በቁሙ ሰማይ አንድም ከፍ ባለ ቦታ ፤ አንድም በመላእክት ዘንድ ፤ አንድም በእግ ዚአብሔር ዘንድ፡ ብካይ፤የል ጆቻቸው ከናቶቻቸው ሲለዩዋቸው ።

ወስቆቃው ፤
የናቶቻቸው ፤
ወገዓር ፤

የልጆቹ ጠምዘው ሲያርዷቸው
ወሕማም ብዙኀ ይላል ፱ ወር ከምስት ቀን የፀነሰ ማሕፀን አይችልምና ፤

፲፰ ራሄል እንዘ ትበኪ በእንተ ውሉዳ ኤር ፴፩ ፤ ፲፭ ።

፲፰ ራሄል ለልጆችዋ ስታለቅስ ተሰማ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ አዘዘ ። አንድም ደረሰ ተፈ ጸመ ።

ሐተታ ልያን አሳነሣ ራሄል አለ ምነው ቢሉ የልያ ዕዳዋ ነው ጌታ ከሷ ወገን ተወልዷልና የራሄል ግን ያለዕዳዋ ነው ጌታ ከሷ ወገን አይወለድምና አንድም የልያ በርኅቀተ ሀገር

ቢበዛት ድንውሊታል የራሄል ግን በማነስ በቅርብ አልተወለታልና ። እንድም በራሄል ልያን መናገር ነው ፤ አንድም እናታችን ራሄል ኑራልን መከራች ንን አይታ አልቀሳልንብለው በላለቀሱ ፤ እንድም እንድናለን መስሏቸው ከመቃብረ ራሄል ገቡተ ዋል ከዚያ እየገቡ ፈጅተዋቸዋልና እንድም በራሄል ሁሉን መናገር ነው ይህማ እከፍሎ ውስተ ያዕቆብ ወእዘርዎ ውስተ እሥራኤል እንዲል ፤ ሁሉን በሚ ገናኝ በያዕቆብ ባልተናገረውም ነበር ቢሉ ፡ ወንድ ልጅ ለፈረስ ሴት ልጅ ለበርኖስ ከደረሱ በኋላ የሞቱ እንደሆነ ኃዘን ባባት ይጸናል በሕፃንነት የሞቱ እንደሆነ ግን ኃዘን በእናት ይጸናልና በሚጸናው ተና ገረ ። እንድም ግፍ ለግፍ ሲያነጻጽር የቀደመችቱ ራሄል የምትባል ቤት ባኗ ርቤልም ስምእንም ይባ ባል ባኗ ሙቶ በባኗ ሥፍራ ኖራ እርጉዊ ብልዋት ስትረግጥ መንታ ፀንሳ ኑራ ወጥተው ወጥተው ወደቁ ደንግጣ ቆመች የሰው ሥጋ ያጸናዋል እንጂ ምን ይለዋል እርጉዊ አሏት ኢሀሉኑ በዙ ሰሚይ አምላከ እሥራኤል ብላ ዕንባዋን በእጅዋ ተቀብላ ወደ ላይ ረጭተዋለች ፤ ሰማዕኩ ገዓሮሙ ለሕዝብየ ወወ ረድኩ ከመ አድኅኖሙ ያሰኘው ይህ ነው ። እንድም ራሄል መንግሥተ ሰማይ የሚገባባት አጥታ ታዝ ናለች ታለቅሳለች ።

ወዓበየት ተናዝዞ ወንጊፈ ላሀ ራሄል ልቅሶ መተ ውን መጽናናትን እምቢ አለች ፤ ግፉ ያሳዝናልና የጸር ሞት ነውና ኀዘን በየደጁ ሁኑአልና ።

እስመ ኢኮንዋ ውሉዳ ውሉደ ልጆቹአ ልጆች አል ሆኑአትምና ሙተዋልና ማለት ነው ። እንድም እስመ ኢኮኑ ውሉደ ፤ ልጆቹ አይደሉምና የተውሶ ናቸውና ።
ወኢሀለው ።

በሕይወተ ሥጋም የሉምና ፤ ሐተታ ፤ እነዚህንስ እንደምን አድርጎ ይሰበስባቸዋል ፤ቢሉ ቂማር ሕፃ ናትን ሰብስበሀ ልብስ ምግብ እየሰጠሀ በማር በወ ተት አሳድገሀ ለናት ለአባታቸው ርስት ጉልት እየ ሰጠሀ ጭፍራ ሥራልኝ ብሎኛል ብሎ ፀዋጅ ነገረ ፤ ያላት ልጅዋን የሌላት ልብስ ምግብ ልቀበልበት ብላ እየተዋሰች ይዛ ሄዳለች እንዲሀ አድርጎ ሰብ ስቦ ፈጅቷቸዋል ። ይሀስ ዕዳው ፤ በማን ይሆናል ቢሉ በሱ ፤ በዳዊት ምክንያት ፫፻ ፹፭ ሌዋውያን ቢያልቁ ፤ ፭ሳሙ ፳፪ ፤ ፲፰ በጴጥሮስ ምክንያት ፲፮ ሰዓራት ቢያልቁ ግብረ ሐዋ ፲፪፡ ፲፱ ።

ዕዳው በሳኦል በሄሮድስ ሆነ እንጂ በዳዊት በጴጥ ሮስ ሆነን አሊያስ ባያውቁ ነው እሱማ እያወቀ ቢሉ ያውቃልማ ካሉ ሁሉንም ያውቃል መጠቀ ማቸውንም ያውቃል ፤ ለነሀስ ክብር አላቸው ቢሉ የላቸውም ይኋል ፤ ይሀማ እንዳይሆን ስንክሳር ተጽ ፎላቸው ታቦት ተቀርጾላቸው አብያተ ክርስቲያና ናት ታንጾላቸው የለም ቢሉ ሳያውቁ በሠሩት ሥራ መጠቀም እንደሌለ ለማጠየቅ ነው እንጂ ክብር አላቸው

፲፱ ወመዊቶ ሄሮድስ ናሁ መልአከ እግዚአ ብሔር አስተርአዮ በሕልም ለዮሴፍ በብሔረ ግብጽ

፲፱ ሄሮድስ ከሞተ በኋላ በግብጽ ሳለ ከእግ ዚአብሔር የታዘዘ መልአክ ለዮሴፍ በህልም ነገረው

፳ እንዘ ይብል ተንሥእ ንሣእ ሕፃነ ወእሞ ወሑር ውስተ ምድረ እሥራኤል ።

፳ ተነሥተህ ብላቴናውን እናቱን ይዘሀ ወደ ምድረ እሥራኤል ተመለስ ብሎ ነገረው ።
እስመ ሞቱ እለ የኃሥሥዋ ለነፍሰ ዝ ሕፃን ።
የዚሀን ብላቴና ሰውነት ለጥፋት የሚሹዋት ሰዎች ሙተዋልና ፤ ኢትቅትል ነፍሰ እንዲል ፡ እንድም ነፍስ እንደነሣ ለማጠየቅ ለነፍሰ ዝ ሕፃን አለ ። ሐተታ ፡ ምነው የሞተ አንድ ሄሮድስ አይደለም ሞቱ ብሎ አበዛ ቢሉ ፡ የምክር ኃናቸው እሱ ነው እሱ ከሞተ ያነሡታልን ብሎ ፡ እንድም በሥልጣ ኅመት ከመንፈቅ ለንኳን በዓላውያን ከቀማ በምእ መናን ከተማሽ እንኳ ብዙ ሰዎች ይሞታሉና ፡ እሱ ንም የመሰሉ ሰዎች ሙተዋልና ሞቱ አለ ።

፳፩ ወተንሥአ ነሥአ ሕፃነ ወእሞ ወቦአ ውስተ ምድረ እሥራኤል

፳፩ ተነሥቶ ብላቴናውን እናቱን ይዞ ወደ ምድረ እሥራኤል ተመለሰ ።

፳፪ ወሰሚዖ ከመ አርኬላኦስ ነግሠ ለይሁዳ ህየንተ አቡሁ ሄሮድስ ፈርሀ ሐዊረ ህየ ።

፳፪ ባባቱ በሄሮድስ ፈንታ ይሁዳን ለመግ ዛት አርኬላኦስ እንደ ነገሠ ሰምቶ ወደ ኢየሩሳሌም መሄድ ፈራ ። ሐተታ የክፉ ልጅ ክፉ አባቱ ያባቱን ክፋት ይተውናል ብሎ ፡ እንድም ልጆቻቸው የሞ ቱባቸው የይሁዳ ሰዎች ልጆቻችን ያለቁ ባንተ ልጅ ምክንያት አይደለም ብለው ቢጣሉኝ ብሎ ደም ፈራ ፤ ወአስተርአዮ በሕልም ፡ በሕልም ነገረው ፡ ወተግኀሠ ውስተ ደወለ ገሊላ ገሊላ ገባ ተገኅሠ አጋእዝትየ እንዲል ።

፳፫ ወበጺሖ ኃደረ ውስተ ብሔር እንተ ስማ ናዝሬት ፤

፳፫ ገሊላ ደርሶ ናዝሬት ገብቶ ናዝሬት በም ትባል አገር ኖረ ፤ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ በነቢይ ከመ ናዝራዊ ይሰመይ ወልድየ ።
ልጄ እንደ ናዝራዊ እንደ ሶምሶን ይባላል ተብሎ በነቢይ ቃል የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ናዝ ሬት ገብቶ ኖረ ። ሐተታ እንዲህ የሚል ወዴት አለ ቢሉ በኄኖክ ጠፍቷል በኄኖክም እንደጠፋበት

ግዛጸ ሰሎሞን ታውቋል ። ይህስ እዝራ ነሥኦን ወኢ ስተጋብኦን ይለዋል ብሎ ተናግሮት ሳይጻፍ የቀረ ነው ። ተናግረውት የቀረውን ማምጣት ለሐዋርያት ልማድ ነው ። ተዓቀቡ በመዋዕለ አፅራር ያለውን በከመ ይቤ ኢዮብ እንዳሉ እንደ ናዝራዊ እንደ ሶምሶን ይባላል ተብሎ በነቢይ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ በናዝሬት ኖረ ፤ አንድም በአራቱ እስመ ናዝራዊ ሐዲስ ውእቱ ለእግዚአብሔር ያለውን እን ዲህ ስውጦ አንብበው ፤ ይህንማ የተናገረ መልአክ አይደለም ስለምን ነቢይ አለው ቢሉ ፤ መልአክ ይሰመይ በእንተ ተልእኮቱ ወሐዋርያ ይሰመይ በእ ንተ ሐዊሮቱ እንዲል ፤ ከዚያ በግብሩ መልአክ እንደ አለው ከዚህም በግብሩ ነቢይ አለው ። ያውስ ቢሆን ይህ የተነገረ ለሶምሶን አይደለምን ቢሉ ፤ ለጊዜው ስሶምሶን ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ ነውና ፤ እነ እከውኖ አባሁ ወውእቱ ይከውነኒ ወልድየ ያለው ለጊዜው ለሰሎሞን ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ እንደ ሆነ ያውስ ቢሆን በምን ይመስለዋልና እን ዲህ አለ ቢሉ ፤ ሶምሶን በተናቀች መንሰከ አድግ ጠላቶቹን እንዳጠፋ ጌታም አይሁድ አጋንንት መና ፍቃን በናቁት ሞቱ ሞትን አጥፍቷልና ። ሶምሶን በሕይወተ ሥጋ ሳለ ካጠፋቸው አሕዛብ በሞቱ ያጠፋቸው ይበዛሉና ፤ ጌታም በሕይወተ ሥጋ ሳለ ካጠፋቸው አጋንንት በሞቱ ያጠፋቸው ይበዛሉና ። አንድም ክመ ናዝራዊ ይሰመይ ብለህ ናዝሬት ማለት ፍልጠት ክፍለት ማለት ነው ። ልዩ ልዩ ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ ። ዘተብህለ በነቢ ቢይ ስሙ ለልዑል ቅዱሰ ቅዱሳን ወይትቀባዕ ቅዱሰ ቅዱሳን ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ አን ድም ናዝሬት ማለት ንሥርት ማለት ነው ፤ ይእተ አሚረ ይሰምያ ለናዝሬት በስመ ኃሣር እንዲል ። ልጁ ኀሡር ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ እልህን ሡር እንዲል በዓረብ ኀሡር ቢል ፤ አንድም ናዝሬት ማለት አጽቀ ጽጌ ማለት ነው ልጁ አጽ ቅያዊ ጽጌያዊ ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ ። እሴ እንደ ጉንድ ናሁ ምእመናንን እንደ አዕጹቅ እንደ ጽጌያት አድርጎ ያበዛኛልና ፤ ያው ግን በነ ቢይ ቃል ትወፅእ ፀትር እምሥርወ ዕሤይ ወየዓርግ ጽጌ እምጉንዱ ተብሎ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ።

በእንተ ስብከተ ዮሐንስ ።

ምዕራፍ ፫ ፤

፩ ወበውእቱ መዋዕል በጽሐ ዮሐንስ መጥምቅ እንዘ ይሰብክ በገዳመ ይሁዳ ዘዮርዳኖስ ፤

፩ ክመ ናዝራዊ ይሰመይ ወልድየ ብሎ ነበ ርና ናዝራዊ በተባለበት ወራት ፤ ቦአ ናዝሬተ ብሎ ነበርና ናዝሬት በገባበት ወራት ፤ ሃያ አምስቱን ዘመን አንድ ወገን አድርጎ ወበውእቱ መዋዕል አለ በዮሐንስ አርባውን ቀን እንዳንድ ቀን አድርጎ ወእመ ሳኒታ እንዳለ ። አንድም ወተወሊዶ ብሎ ነበርና ሥጋ በሆነበት ወራት ። አንድም ለዮሐንስ ሠላሳ ሲመላው ስጌታ መንፈቅ ሲቀረው በዚያ ወራት የዮርዳኖስ አውራጃ በምትሆን በይሁዳ ምድረ በዳ ዮሐንስ መጥምቅ ሲያስተምር ደረሰ ፤ በገዳም አለ ቦታው ነውና አንድም በገዳም ዕንጨት በባሕ ውኃ ቆጂ አይታጣምና ፤ አንድም በገዳም ጾር ይቀ ላል ለውጣንያን እብነት ለመሆን በገዳም ጾር ይጸናል ለፍጹማን አብነት ለመሆን ፤ አንድም ገዳም የአይ ሁድ ልቡና ነው ። በገዳም እፀል ቀከል እንደይገኝ በአይሁድም ልቡና ምግባር ሃይማኖት አይገኝምና እንድም ኢሳይያስ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ብሎ የተናገረልኝ እኔ ነኝ ሲል ።

፪ እንዘ ይብል ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ፤ ማር ፩ ፥ ፪ ፥ ሉቃ ፥ ፫ ፥ ፫ ።

፪ መንግሥተ ሰማያት በልጅነት ልጅነት በሃ ይማኖት ልትሰጥ ቀርባለችና እመኑ እያለ ሲያስተ ምር ደረሰ ።

፫ እስመ ዝንቱ ውእቱ ዘተብህለ በኢሳይያስ ነቢይ እንዘ ይብል ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ። ኢሳ ፥ ፵ ፥ ፫ ። ማር ፥ ፩ ፥ ፫ ። ሉቃ ፥ ፫ ፥ ፬ ።

፫ ፤ በገዳም የሚያስተምር ዐዋጅ ነጋሪ ተብሎ በኢሳይያስ ቃል የተነገረለት ይህ ዮሐንስ ነውና ቃለ ዐዐዋዲ ፤ እዕዋዲ ቃል ይላል ትምህርቱን ከዚ ያም ከዚያም የሚያደርስ ማለት ነው ቃል ዓዋዲ ይላል ። ይህንንም ቃል ዘይኬልህ በገዳም ብሎ ሊቁ ወስዶታል ።

ወይብል ጺሑአ ፍኖቶ ለእግዚአብሔር ፤ የእግዚአብሔርን መንገድ ጽረጉ ። ወርቱዓ ግበሩ መጽያሕቶ ።

ጽርጊያውን የቀና አድርጉ እያለ ሲያስተምር ደረሰ ሐተታ ፤ ንጉሥ በመጣ ጊዜ ተራራው ቆረብ ታው ተንዶ ጉድጓዳው መልቶ ሥሩ ተነቅሎ ደን ጊያው ተለቅሞ ለፈረስ ለሠረገላ እንዲመች ቀድ ልድሎ ይቆያልና ከዚያ ግሥ ተናገረው ። የእግዚ አብሔር ግደሪያ በውነታችሁን ከኃጢአት ከጣእት ንጹሕ አድርጉ ።

፬ ወልብሱ ለዮሐንስ ኮነ እምፀጉረ ገመል ፤ ዮሐንስማ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ ኪያ ሳንቃ ያልብሱኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደሆነ ፤ ይህ ለሥጋውያን ነው ። እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና

፬ ይህን አይሻም ፤ ዮሐንስስ የሚለብሰው የገመል ጠጕር ነበር ። ሐተታ የገመል ምን ጠጕር እሳትና ቢሉ ከጋማዋ ከጅራቷ ቢፈልጉ አይታጣም

ልብሱን ሲል ወምበዴ ይጣሳዋል ብላ እናቱ ያንን
አሥርታ አልብሳው ነበር ፤ አንድም ገመል በቀለኛ
ናት አጥብቆ የመታትን እስከ ፯ እስከ ፯ ዓመት አት
ዘንጋም ባጥብሳ ትረግጠዋለች ሥፍራ ሲመቻት ገደል
ገፍታ ትጥለዋለች ። እሱም ወይወድይዎሙ ውስተ
እቶነ እሳት የምትል ሕገ በቀል ወንጌልን አስተም
ራለሁ ሲል ። አንድም ገመል ሁለት ግብር አሳት ።
የሚበሳና የማይበሳ እንደ ሳምና እንደ በሬ ምንዛን
ታወጣለች እንደ ፈረስ እንደ በቅሎ ሰኮናዋ ጽፉቅ
ነው ። አስመ ገመል ጽፉቅ ሰኮናሁ ወያመሰኩዕ
እንዲል ። እሱም ሕገ አሕዛብ ወሕዝብ ወንጌልን
አስተምራለሁ ሲል ፤ አንድምገመሉ የሚባል ዕፅ
አለ ቆርጠው አድርቀው ከባሕር የጣሉት እንደ
ሆነ ጭረት ይወጣዋል ያንን ታትታ አልብሳዋለች
ለጊዜው ኑሮው በገዳም ነውና ልብሱን ሲል ወም
በዴ እንዳይጣሳው ነው ። ፍጻሜው ግን ለምእመናን
እብነት ለመሆን ተርታ ልብስ ለብሳችሁ እልባሌ
መስሳችሁ ኑሩ ለማለት ።

ወቅናቱ ዘአዲም ውስተ ሐቌሁ ዮሐንስማ እንዲህ
ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ የወርቅ ዝናር ያስ
ታጥቁኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደሆነ ። ይህ ለሥጋው
ያን ነው ። እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና ይኸን አይ
ሻም ። እሱስ ወገቡን የሚታጠቅበት ዓረብ ነበር ፤
ያ ከደመ ነፍስ የተለየ እንደሆነ ፤ እሱም ከሥጋዊ
ከደማዊ ግብር ልዩ ነኝ ሲል ፥ ይኸን አስቀድሞ
ከደመ ነፍስ ይለዩታል ከወጋ ይነክሩታል ኋላ
ጥጕሩን ይመልጡታል ያለፋታል ቀለም ያገቡታል ፤
ከደመ ነፍስ እንዲለዩት መክር አስተምሮ ከሥጋዊ
ከደማዊ ግብር ይለያቸዋል ፤ ከወጋ እንደ መንከር
ያጠምቃቸዋል ያስተምራቸዋል እንደ ማልፋት ምግ
ባር ሃይማኖት ያሠራቸዋል ቀለም እንደ ማግባት
ጸጋ ክብር ያሰጣቸዋል ዮሐንስ ግን እንዲህ ማድረጉ
ፍትወት እንስሳዊት ሠባሕርዩ እያለች በገቢር አን
ዳሳወረዳት ያጠይቃል ።

ወሲሳዩ አንበጣ ወመዓረ ገዳም ዮሐንስማ እንዲህ
ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ ጣቦ ጋቦዶሮ ስቅ
ስቆ ያብሉኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደ ሆነ ይህ ለሥጋ
ውያን ነው ፤ እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና ይህን አይ
ሻም ምግቡም አንበጣ የሚባል ቅጠል ደቂቦ ጨው
ነስንሶ ነበር ፤ አንድም አንበጣ በልሳነ እቴና ቀም
ሲስ ይለዋል በኛም ሰበቦት የጋጃ ማ ይባላል ።
ወመዓረ ገዳም አለ ። የማጓማር ይሏል ፤ አንድም
አንበጣ ይላል በቁሙ አንበጣውን ይበላው ነበር ፤
በዐረቡ እልጅራድ ይላል አንበጣ ሲል ፤ ሐተታ ፤
በዘመኑዋ እያሉ እንድታልፍ ለማጠየቅ አሪትን
አይጠብቋትም ነበር።በ፰ ቀን ግዘሩ የምትለውን
ኢያሱ በ፵ ዘመን ገዝሯል ። ሶምሶን ከአፈ አን
በሳ መዓር አግኝቶ ተመግቧል ከመንሰከ አድግ
ውጋ ጠጥቷል ። ኤልያስም በአፈ ቋዕ ሥጋ እየመ
ጣለት ይበላ ነበር ፤ ዮሐንስም በቁሙ አንበጣውን
ይበላው ነበር ። ወመዓረ ገዳም ባለው ወመዓረ
ጸደና ይላል ፤ የጣዝማ ማር ፤ ይህንም ሲቁ ጸንበጣ
ዘይቤ ልዕልና ስብከቱ ይእቲ ፤ መዓር ዘይቤ ጣዕመ
ስብከቱ ይእቲ ብሎ ተርጕሞታል ።

፭ ወየሐውሩ ኀቤሁ ኵሎሙ ሰብአ ይሁዳ ወኢ
የሩሳሌም ወኵሉ አድያሚሃ ለዮርዳኖስ ።
ማር ፩ ፤ ፭ ።

በኢየሩሳሌም በይሁዳ በዮርዳኖስ አውራጃ
ያሉ ሰዎች ሁሉ ከሱ ዘንድ እየሄዱ ፤

፮ ወያጠምቆሙ ለኵሎሙ በፈለገ ዮርዳኖስ
እንዘ ይትአመኑ ኃጣውኢሆሙ ።

፯ ኃጢአታቸውን እየነገሩት በዮርዳኖስ ያጠ
ቃቸው ነበር ። እገሌ ተጠመቅ በማየ ንስሐ ከመ
ትኩን ረድአ ለክርስቶስ እያለ ፤ ሐተታ ፤ ጥምቀት
ከሦስት ወገን ነው ። መዝገበ ውሉድ ፍቁራን የም
ትባል የጌታ ጥምቀት ፤ ጥምቀት ዮሐንስ ጥምቀተ
አይሁድ ፤ ጥምቀተ አይሁድና ጥምቀተ ዮሐንስማ
አንድ አይሆንም ሁሉም ልጅነት አያሰጥ ቢሉ አንድ
አይደለም ከሰውነታቸው ሰውነቱ እንዲበልጥ ፤
ከጥምቀታቸውም ጥምቀቱ ይበልጣል ። አንድም
፫ ወገን ነው ፩ቱ ምሳሌ ፩ቱ አማናዊ ፤ ምሳሌ አጥ
መቃ ለምድር በማየ አይህ ፤ ወለኵሉሙ አበዊነ
አጥመቆሙ ሙሴ በደመና ወበባሕር ፤ ወተጠምቃ
አገሪሆሙ ለካህናት ያለው ፤ ጥምቀተ ዮሐንስ ፤
ይህ ምሳሌ ነው ። አራቱ አማናዊ መዝገበ ውሉድ
ፍቁራን የምትባል የጌታ ጥምቀት እንብዓ ንስሐ፤
ደመ በማዕት ባሕረ እሳት ።

፰ ወሶበ ርእየ ብዙኀነ አሕዛብ እምፈሪሳው
ያን ወሰዱቃውያን እንዘ ይመጽኡ ውስተ ጥምቀቱ
ጽሚተ ። ሉቃ ፫ ፤ ፯ ።

፱ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ወገን ብዙ ሰዎች
ጻድቃን መስለው ኃጢአታቸውን ሰውረው አል
ባሌ መስለው ተርታ ልብስ ለብሰው የኦሪትን መፍ
ረሻ የወንጌልን መታነጫ እናያለን ብለው እሱ
ወደሚያጠምቅበት ሲመጡ ባየ ጊዜ ፤ ሐተታ ፤
እሥራኤል አይደለም ስለምን አሕዛብ አሳቸው ቢሉ
ስለብዛታቸው ፤ እንድም በጸያፍ የገባ ግብረ አሕ
ዛብ ይሠራሉና ፤ ባባታቸው በፋሬስ ፈሪሳውያን
በሳዶቅ ሰዱቃውያን ተብለዋል ባባትም ስም መጠራት
ልማድ ነው ። በዔቦር ዕብራውያን በይሁዳ አይሁድ
እንደ ተባሉ ።

ወይቤሎሙ አ ትውልደ አራዊተ ምድር መኑ አመ
ረከሙ ትጕየዩ እመቅሠፍት ወእመንሱት ዘይመ
ጽእ ።

እናንተ የፍኘት እባብ ልጆች በነፍስ በሥጋ ከሚመጣው መከራ ትድኑ ዘንድ ማን ነገራችሁ ። እመቅሠፍት ወእመንሡት ወእመዓት ዘይመጽእ ይላል ። በጥሞስ በሐሳዊ መሲሕ በምጽዓት ከሚመጣው መከራ ትድኑ ዘንድ ማን ነገራችሁ ። ሊማሩለት እንዳልመጡ ያውቅ ያለምን ቢሉ የማይጠቀም ከጉባዔው አይመጣምና እንድም የሹም ሰነፍ ባይለፈልፍ እንዲሉ ፤ ንግር ወኢታርምም ብሎታልና ። አባቶቻቸው ወደው ባወጡት ስም ትውልደ አራዊተ ምድር አላቸው ። ወንድማቸውን ዮሴፍን ሸጠው ዐልቂው እኩይ አርዌ በልዖ ብለው ነበርና ። ትውልደ አራዊተ ምድር ያላት እፍዌ ገሞራዊት ናት አፈ ማኅፀንዋ ጠባብ ነው ዘሩን ባፏ ትቀበለዋለች አባለ ዘሩን ቆርጣ ታስቀረዋለች ። በፅንስ ጊዜ አባት ይሞታል በሚወለዱበትም ጊዜ አፈ ማኅፀኑዋ ጠባብ ነውና ሥጋዋን በልተው ሆዷን ቀደው ይወጣሉ ፣ በዚህ ጊዜ እናት ትሞታለች እኒህም እንዳባት የሚሆኑዋቸውን ነቢያትን እንደ እናት የሚሆኑዋቸው ሐዋርያትን ገድለዋልና ። ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም እንተ ትቀትሎሙ ለነቢያት ወትዌግሮሙ ለሐዋርያት እለ ተፈነው ኀቤየ ብሎ እንዲያመጣው

፰ ግበሩኬ እንከ ፍሬ ሥርናየ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ።

፰ ከእንግዲህስ ወዲህ ለማመን የሚያበቃች ሁን ሥራ ሥሩ ።

፱ ወኢይምሰልክሙ ዘታመሥጡ በብሂለ ዘትብሉ አብ ብነ አብርሃም ፤ ዮሐ ፣ ፰ ፣ ፴፱ ።

፱ አብርሃምን ያህል አባት ሳለን ትውልደ አራዊተ ምድር ይለናል በማለት ትውልደ አራዊተ ምድር ከመባል የምትድኑ አይምሰላችሁ ፣ እንዲሉት ዐውቆ አመጣ እንዲሉትም ዐውቆ ማምጣት ልማድ ነው ። ብጹዓን ብጹዓን እያለ ሲያስተምር ሰምተው አሪትን ነቢያትን ሲያሳልፋቸው መጥቷል እንዲሉት ዐውቆ ኢይምሰልክሙ ዘመጻእኩ እስዓሮሙ ለኦሪት ወነቢያት ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ እፈጽሞሙ እንዳለ ። ወኢትሁቦ ለጻድቅከ ይርአይ ሙስና ቢላቸው ፤ ይህንማ ዳዊት የተናገረው ለራሱ አይደለም እንዲሉት ዐውቆ ታበውሁ ነሁ እ ሰብእ ንንግርክሙ ክሡተ በእንተ ዳዊት ርእሰ አበው ቀደምት ከመሂ ሞተ ወተቀብረ እንዳለ ከዚህም እንዲህ አለ ።

እብለክሙ ከመ ይክል እግዚአብሔር እምእላንቱ እዕባን እንሥእ ውሉድ ለአብርሃም ፣ እግዚአብሔር ለአብርሃም ከነዚህ ከአሕዛብ ልጅ ማሥነግት አቅሞ ውሉድ ይላል መተካት እንዲቻለው ይቻለዋል ብየ እነግራችኋለሁ ፣ እንሥእ ውሉድ እንሥእ ውሉደ ይላል ። እላንቱ እላቸው አሁን ያሉ በመካከል ነውና ኋላ ብሔረ ጊርጊሴን ገባ ብሎ እንዲያመጣቸው ፣ እዕባን አላቸው ደንጊያ ያመልካሉና ፣ እንድም ይቡስ ነው ይቡሳን አእምሮ ናቸውና ፣ ቆሪር ነው ፣ ቆሪራን አእምሮ ናቸውና ፣ ክቡድ ነው ክቡዳን አእምሮ ናቸውና ።

፲ እስመ ናሁ ተሠይመ ማሕጼ ውስተ ጉንደ ዕፀው ይንበር ፤

፲ ምሳር ዓፅቁን ከግንዱ ሊለይ ተቃቷልና ። ማለት ያናንተን ልጅነት ከአብርሃም አባትነት ሊለይ ሥልጣነ እግዚአብሔር ተቃጥቷልና ኢይምሰልክሙ በብሂለ ዘትብሉ ላለው ፤ ወንጌል ሕገ አሕዛብ ወሕዝብ ልና ተሠርቷልና ፣ እብለክሙ ከመ እግዚአብሔር ይክል እንሥእ ውሉድ ላለው ፣ መለኮት ከሥጋ ተዋሕዷልና ሙት አመረክሙ ላለው ክፉውን ሕሊና ከበጎ ሕሊና ሊለይ ሥልጣነ ክህነት ተቃጥቷልና ግበሩኬ እንከ ፍሬ ሠናየ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ላለው ፣

ኵሉኬ ዕፀ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይገዘምዎ ወውስተ እሳት ይወድይዎ ።

በጎ ፍሬ የማያፈራውን ዕፅ ሁሉ ይቆርጡታል በእሳት ያቃጥሉታል ፣ በኔ ትምህርት አምኖ በጎ ሥራ የማይሠራውን ሰው ሁሉ ነፍሱን ከሥጋው ይለዩታል ፀገሃነም ሥቃይ ያመጡበታል ።

፲፩ አንሰኬ አጠምቀክሙ በማይ ለንስሐ ፤ ማር ፩ ፰፣ ሉቃ ፫፣፲፯ ዮሐ ፩፣፳፮ ግብ ሐ፣፩፣፭። በዚህ ያልተያዘ በሉቃስ የተያያዘ ነው ባለጸጎች መጥተው ምንተ ንግበር እሉት ፣ ዘቦ ፪ኤ ከዳናት የሀብ ፩ደ ለዘአልቦቱ ወዘሂ ቦ እክል ከማሁ ደግበር አላቸው ፣ ኃጥአን መጸብሐን መጥተው ምንተ ንግበር እሉት ። አልቦ ፍድፋዴ ዘትገብሩ እምዘተአዘዝክሙ አላቸው እንበሳ ወደቅ የወርቅ ተኩስ የግምጃው መክንጃ የላሙን መንጃ እያሉ የሚወስዱት አላቸውና ፣ የደል ጭፍራ መጥተው ምንተ ንግበር እሉት ፤ ኢትግዓሉ ወኢትሂዱ መነሂ አላ ንበሩ በበሲሳይክሙ አላቸው ዮሐንስ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ክርስቶስ እንጂ ቢሆን ነው ብለዋል እኔስ ለጸጅ ቢረሉን

፲፩ ለልብስ ንሳን እንዲያጽቡለት ሰሱ ጥምቀት በሚያበቃ ጥምቀት አጠምቃችኋለሁ ሰሱ ተአምምኖ ጣውእ በሚያበቃ ተአምኖ ኃጣውእ አስተምራችኋለሁ እንጂ ክርስቶስ አይደለሁም ።

ወዘይመጽእ እምድኅሬየ ውእቱ ይጸንዕ እምኔየ ። ከኔ በኋላ የሚመጣው እሱ ከኔ አስቀድሞ የነበረው ነው አለ ። የባሕርይ አምላክ ነው ።

ዘኢይደልወኒ እጹር ዓሣዕኖ ። ጫማውን ልይዝ የማይገባኝ ። ሐተታ ፣ የንጉሥን የንግሥትን ጫማ ትበቃለህ ያሉት ሰው አይዝምና ።

እንደም ባሕርዩን ልመረምር ከማይቻለኝ ፤ አንድም ፡ እሱ ከሚያደርገው ከታምራቱ ከትሩፋቱ አንዱን ሳደርግ ከማይቻለኝ ፡ አንድም እግሩን መር ገምን ከምእመናን ለአንዱ አርቅለት ዘንድ ከማ ይቻለኝ ከኔ አስቀድሞ የነበረ ነው ።

ውእቱስ ያጠምቀክሙ በመንፈስ ቅዱስ ወበእሳት ፤ እሱ ግን በጀ ብትሉ በመንፈስ ቅዱስ በጀ ባትሉ በገሃነመ እሳት ያጠምቃችኋል ፤ ግነምቱ ምድር ይእቲ እንተ ኢትመልዕ ማየ እንዲል ፤አንድም በመ ንፈስ ቅዱስ እሳትነት ያጠምቃችኋል ። ሐተታ ፡ መንፈስ ቅዱስን እሳት አለው ፡ እሳት ምሉእ ነው፡ መንፈስ ቅዱስም ምሉእ ነውና ፤ እሳት በምልአት ባለበሳድ ካልመቱ አይገለጽም ። መንፈስ ቅዱ ስም ጽንቋ ሲያናግር ምሥጢር ሲያስተረጉም እንጅ ልድሮ ሳለ አይታወቅምና ፤ እሳት ከቡሳዱ ሲወጣ በመጠን ነው ኋላ በዕንጨት እያቀጣጠሉ ያስፋታል መንፈስ ቅዱስም በጥምቀት ሲሰጥ በመጠን ነው። ኋላ በሥራ ያስፋታልና እሳት ጣዕምን መዓዛን ያመ ጻል ፡ መንፈስ ቅዱስም ጣዕመ ጸጋን መዓዛ ጸጋን ያመጣልና፡እሳት በመጠን ቢሞቁት ሕይወት ይሆ ናል ። ከመጠን ወጥቶ የሞቁት እንደሆነ ግን ያቃ ጥላል ። መንፈስ ቅዱስም በሚገባ በተጻፈው የመረ መሩት እንደሆነ ሕይወት ይሆናል ፤ በማይገባ ከተ ጻፈው ወጥቶ የመረመሩት እንደሆነ ግን ይቀስፋልና እሳት በላኢ ለዓማፅያን ለእለ ይክህዱ ስሞ ወእሳት ማሕየዊ ለርቱዓን ልብ ለእለ ይገብሩ ፈቃዶ እን ዲል ፤ እሳት ያቀረቡለትን ሁሉ ያቃጥላል መንፈስ ቅዱስም ሕዝብ አሕዛብ የጸለዩትን ጸሎት ያቀረቡትን መሥዋዕት ይቀበላልና ፤ እሳት ወጋ ገደል ካልከለ ከለው ሁሉን ሳጥፋ ቢል ይቻለዋል ። መንፈስ ቅዱስም ቸርነቱ ካልከለከለው ሁሉን ሳጥፋ ቢል ይቻለዋልና እሳት ዱር ይገልጻል መንፈስ ቅዱስም ምሥጢር ይገልጻልና እሳት የበሳው መሬት ለእ ህል ለተክል ይመቻል ፡ መንፈስ ቅዱስም ያደረ በት ሰውነት ለገድል ለትሩፋት ይመቻልና እሳት ከዛንሳቸው ሳይለተፍ ሰባቱን መዓድናት ያጸራቸ ዋል መንፈስ ቅዱስም ከግብራቸው ሳይለተፍ ሁሉን ያነጻልና ይእቲ ታነጽሕ ወኢትረኩሕ እንዲል ፤ እሳት ካንዱ ፋና አምሳ ስልሳ ፋና ቢያበሩለት ተከ ፍሎ የለበትም ፤ መንፈስ ቅዱስም ተከፍሎ ሳይኖር በት እስከ ምጽአት ድረስ ሲሰጥ ይኖራልና ይእቲ ትሁብ ወኢትቀብል እንዲል በእሳት ቀድሞ ሰብአ ሰዶም ሰብአ ገሞራን ከእሥራኤል አንዱን ኀብር አጥፍቶበታል ለመዓት እንጅ ለምሕረት አልተፈ ጠረም እንዳይሉ ለምሕረትም እንደ ተፈጠረ ለማ ጠየቅ ። አንድም ሽክላ ሠሪ ሥርታ ለቅጨርስ ንቅ ያገኝበት እንደሆነ እንደ ገና መልሳ ከስክሳ በውኃ ለውሳ በእሳት ታድለዋለች ። ተሐድሶም በመን

ፈስ ቅዱስ ነውና ፤ ዛቲ እሳት እንተ ኮነ ይትማፀኑ አዳም እንበለ ይትዓዶ ትእዛዘ እግዚአብሔር ፈጣ ሬሁ ኮመ ነበረ ውቱቀ ኀቤተ ዋዕየ በልዓ እምዕፀ ዕልወት ተዓርቀ ወኢረከበ እስከነ መጽአ ለዳም ዳግማዊ ወአሰ/ሰ እኑመ እግዚ ወእመንፈስ እንዲል

፲፪ ዘመሥኢ ውስተ እዴሁ ዘቦቱ ያነጽሕ ዓውደ እክሉ ።

፲፪ ፍሬውን ከገለባ የሚለይበት መንሽ በጁ ተይዞ ያለ ።

ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ። ፍሬውን ከገለባው ለይቶ በሪቅ በጎታ በጎተራ የሚ ሰበስብበት ወኃሠርሰ ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍዕ። ገለባውን ግን በማይጠፋ እሳት የሚያቃጥል እሱ ያጠምቀክሙ በል ወደ ወርቅ ሂዶ ዘኢይጠፍዕ እለ ፤ አንድም ዘመሥኤ ብለህ መልስ ፡ ጣቱ ሦስት ነው ቢሉ የሦስትነት መያዣው ያንድነት ሁለት ነው ቢሉ ጌዕና ሕሩ የሚልበት ሥልጣን ገንዘቡ የሚሆን ።

ዘቦቱ ያነጽሕ ዓውደ እክሉ ዘውእቱ ፍጥረተ ሰብእ ብሎ ወስዶታል ሊቁ ፡ ጻድቃንን ከኃጥአን የሚ ለይበት ።

ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ፡ ጻድቃንን ከኃጥአን ለይቶ በመንግሥተ ሰማያት የሚያኖርበት ፡ መዛግብት ብሎ አበዛ በብዙ ወገን ትወረሳለችና ፡ እስመ ውስተ ቤተ አቡየ ብዙኀ ማኅደር ወምዕራፍ ቦቱ እንዲል ።

ወኃሠርሰ ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍዕ ፡ ኃጥአንን ከጻድቃን ለይቶ በገሃነም ሥቃይ የሚያመጣበት ሥልጣን ገንዘቡ የሚሆን ፡ አንድም ክፉውን ሐሊና ከበጎው ሐሊና የሚለይበት ሥልጣን ክህነት ገን ዘቡ የሚሆን ፡ ወሥርናዮስ በጎውን ሐሊና ከክፉ ሐሊና ለይቶ በመንፈስ ቅዱስ የሚያስጠብቅበት እሱ ፡ መዛግብት ብሎ አበዛ ስለ ሀብቱ ብዛት ወኃ ሠርሰ ፡ ክፉውን ሐሊና ከበጎ ሐሊና ለይቶ በቀኖና የሚያጠፋበት ሥልጣን ክህነት ገንዘቡ የሚሆን እሱ በመንፈስ ቅዱስ እሳትነት ያጠምቃችኋል

## በእንተ ጥምቀተ እግዚእ ኢየሱስ

፲፫ ወአሜሃ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ እምገ ሊላ ውስተ ዮርዳኖስ ከመ ይጠመቅ እምዮሐንስ

፲፬ ማር ፩፡፱ ። ለጌታ ሠላሳ ሲመላው ለዮሐ ንስ መንፈቅ ሲቀርፈው ያን ጊዜ ጌታ በዮሐንስ እጅ ይጠመቅ ዘንድ ከገሊላ ወደዮርዳኖስ መጣ ። አንድም ለሙ ሰብስቦ በማያጠምቅበት ጊዜ መጣ እብ በደመና ዝንጉቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመሰክር

መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ከራሱ ላይ ሲቀመጥ አንድነት ሦስትነት ይታወቃልና ፤ ያን ጊዜ ጌታ ከገሊላ ወደ ዮርዳኖስ መጣ አለ ። ሐተታ ምነው ባሪያ ወደ ጌታው ይሄዳል እንጅ ጌታ ወደ ባሪያ ይሄዳልን ፤ ባሪያ በጌታው እጅ ይጠመቃል እንጅ ጌታ በባሪያው እጅ ይጠመቃልን ቢሉ ጌታ መምጣቱ ለትሕትና ነው እንጅ ልልዕልና አይደለምና ፤ አንድም ለአብነትነት ጌታ ዮሐንስን መጥተህ አጥምቀኝ ብሎት ቢሆን ዛሬ ነገሥታት መኳንንት መጥታችሁ አጥምቁን ባሉ ነበርና ፤ ሂዳችሁ ተጠመቁ ለማለት አብነት ለመሆን ፤ ጥምቀቱን በዮርዳኖስ ያደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፤ ትንቢት ባሕርኒ ርእየት ወጎየት ወዮርዳኖስኒ ገብአ ድኅሬሁ ርእዩከ ማያት እግዚኦ ርእዩከ ማያት ወፈርሁ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም ዮርዳኖስ ከላይ ነቁ አንድ ነው ዝቅ ብሎ በደሴት ይከፈላል ከታች ወርዶ ይገናኛል ። ዮርዳኖስ ከላይ ነቁ አንድ እንደሆነ የሰው ሁሉ ነቁ አንድ አዳም ነው ። ዝቅ ብሎ በደሴት እንዲከፈል እስራኤል በግዝረት አሕዛብ በቍልፈት ተለያይተዋል ። ከታች ወርዶ በወደብ እንዲገናኝ ሕዝብና አሕዛብ በክርስቶስ በጥምቀት አንድ ሁነዋልና ፤ አንድም አብርሃም ሳምስቱ ነገሥተ ሰዶም ረድቶ አራቱን ነገሥተ ከሎዶጎሞርን ድል ነሥቶ ቢመለስ ደስ ቢለው በመዋዕልየኑ ትሬኑ ቃለከ ወሚሙ ታርእየኒዑ ከያዕለቱ አው እልቦ አለ ፤ እሱንስ እታየውም ምሳሌውን ታያለህና ሑር ዕድዎ ለዝንቱ ዮርዳኖስ ፤ ዮርዳኖስን ተሻግረህ ሂድ አለው ፤ ዮርዳኖስን ተሻግሮ ቢሄድ መልከ ጼዴቅ ኅብስተ በረከት ጽዋዓ አኰቴት ይዞ ተቀብሎታል አብርሃም የምእመናን ዮርዳኖስ የጥምቀት መልከ ጼዴቅ የቀሳውስት ኅብስተ በረከት ጽዋዓ አኰቴት የሥጋው የደሙ አንድም ኢዮብ ከዚህ ተጠምቆ ከደዌው ድኗል ፤ ኢዮብ የአዳም ከነሕፃናቱ ደዌ የመርገመ ሥጋ የመርገመ ነፍስ ዮርዳኖስ የጥምቀት ምሳሌ ፤ አንድም እሥራኤል ዮርዳኖስን ተሻግረው ምድረ ርስት ገብተዋል ፤ ምእመናንም አምነው ተጠምቀው ገነት መንግሥተ ሰማያት ገብተዋልና ፤ ኤልያስ ዮርዳኖስን ተሻግሮ ገነት አርጓል ምእመናንም አምነው ተጠምቀው ገነት መንግሥተ ሰማያት ለመግባታቸው ። አንድም የኤልሳዕ ደቀ መዛሙርት ጸበበነ ማኅደር ንዑ ንግዝም ዕፀ ወንሕንጽ ካልዓ ማኅደረ ብለው ሄዱ ፤ እሱም መምህረ ትሕትና ነውና አብሯቸው ሄደ ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ ሲቆርጥ ምሳሩ ከዛቢያው ወልቆ ከባሕር ገባበት ፤ ዝኒ ኀቡይ እግዚእየ ፤ ጌታዬ ጥንቱን የተውሶ ያውም ጠፋ ተጨርሶ አለው የገባበትን አሳየኝ አለው አሳየው ቅርፍተ ዕፅ ቀርፎ ጨምሮ ቢመታው መዝቀጥ የማይቻለው ቅርፍተ ዕፅ ዘቅጦ መዝቀጥ የሚገባውን ብረት ይዞት ወጥቷል ። እንደዚህም ሁሉ ሞት የማይገባው መለኮት ሙቶ ሞት የሚገባው አዳምን ለማዳኑ ምሳሌ ፤ ጥምቀቱንም ሽቶ አላደረገውም ። አኮ ፈቂዶ ለተጠምቆ አላ ከመ የሀበነ ሱታፌ ንጽሕ እንዲል በመጠመቁም ጸጋ ያገኘበት አይደለም ። አኮ ዘረከበ ጸጋ በተጠምቆቱ አላ ከመ ያብርህ መካናተ ወያነጽሕ ማያተ ለእለ ህለዎሙ ይጠመቁ ውስቴታ እንዲል ፤ ዮርዳኖስን ብርሀት ማሕፀን ለማድረግ ለጥምቀት ኃይል ለመስጠት ነው እንጂ አንድም ዮርዳኖስ በበጋ የማይጎድል በክረምት የማይተርፍ ማእከላዊ ውኃ ነው የጌታም ጥምቀቱ እኛም ከመጥቀም በላይ እሱን ከመጥቀም በታች ነውና ፤ ዳግመኛ በባሕረ ጥብርያዶስ ላይ የሚሄድ ውኃ ነው ዐባይ በጣና ላይ እንዲሄድ የጌታም ጥምቀት ከኛ ጥምቀት በላይ ነውና ፤ አንድም ብዙ ንዑሳን እንቅዕት ይገቡበታል እሱ ያበረታቸዋል እንጂ እነሱ አያበረቱትም ፤ የጌታም ጥምቀት ለኛ ጥምቀት ኃይል ጽንዕ ይሆናል እንጂ የኛ ጥምቀት ለጌታ ጥምቀት ኃይል ጽንዕ አይሆንምና ። አንድም ንዕማን ከዚህ ተጠምቆ ከደዌው ተፈውሷል ንዕማን የአዳም ከነሕፃናቱ ደዌ የመርገመ ሥጋ የመርገመ ነፍስ ዮርዳኖስ የጥምቀት ምሳሌ ፤ ኢዮብን ዕማን ጌታ የተጠመቁበት ወደቡ አንድ ነው ። ትንቢቱን ዐውቆ እናግሯል ምሳሌውንም እንጂ ዐውቆ አስመስሏል ። ምሥጢሩ እንደምነው ቢሉ ዲያብሎስ የጨለማ መጋረጃ ጋርዶ በአዳምና በሔዋን ሥቃይ አጸናባቸው ስመ ግብርናታችሁን ጽፋችሁ ብትሰጡኝ ባቀለልሁላችሁ ነበር አላቸው ። አዳም ገብሩ ለዲያብሎስ ሔዋን አመቱ ለዲያብሎስ ብለው ጽፈው ሰጡት መጽሐፈ የለም ይሁንብን ማለታቸውን መናገር ነው እንጂ እሱ በሁለት ዕብነ ሩካም ጽፎ አንዱን በዮርዳኖስ አንዱን በሲኦል ጥሎታል ፤ በዮርዳኖስ የጣለውን ሲጠመቅ እንደ ሰውነቱ ተረገጦ እንደ አምላክነቱ አቅልጦ አጥፍቶላቸዋል ። በሲኦል የጣለውን በዕለተ ዓርብ በአካለ ነፍስ ወርዶ ነፍሳትን ሲያወጣ አጥፍቶላቸው ወጥቷል ።

፲፬ ወዮሐንስሰ ዓበዮ እንዘ ይብል አንሰ እፈቅድ እምኀቤከ እጠመቅ ።

፲፬ ዮሐንስ ግን ባሪያ በጌታው እጅ ይጠመቃል እንጂ ጌታ በባሪያው እጅ ይጠመቃልን ብሎ አይሆንም አለው ።

ወአንተኑ ትመጽእ ኀቤየ ፤

ባሪያ ወደ ጌታው ይሄዳል እንጂ ጌታ ወደ ባሪያው ይሄዳልን አለው ፤ እናቱ ምንትኑ አነ ከመ ትምጽእ ኀቤየ እሙ ለእግዚእየ ብላ ነበርና ። ከዚያ አያይዞ እንዲህ አለ ።

፲፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ኅድግ ምዕረ ።

፲፭ ጌታ መለሰ አንድ ጊዜስ ተው አለው ። ሐተታ ፤ አንድ ጊዜ ቢጠመቅ ሁለተኛ ፤ በፈቃድ ቢጠመቅ በግድ ፤ በሰውነቱ ቢጠመቅ ባምላክነቱ መጠመቅ የለበትምና ።

እስመ ከመዝ ተድላ ውእቱ ለነ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና ፤ ሐተታ ፤ ራሱን ከዮሐንስ አግብቶ አን ተም መጥምቀ መለኮት ተብለህ ክብርህ ይነገራልና እኔም በባሪያው እጅ ተጠመቀ ተብሎ ትሕትናየ ይነገራልና ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሉ ጽድቀ። ትንቢተ ነቢያትን ልንፈጽም ይገባናልና ዮሐንስ እንዲያጠምቅ ጌታ እንዲጠመቅ ትንቢት ተነግሯልና አንድም እስመ ከመዝ ተድላ ለነ ፤ ራሱን ከምእ መናን አግብቶ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና ፤ እናንተም ብትጠመቁ ይወርድላችኋል ሲገለት ፤ ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሎ ጽድቀ ። ጽድቀ ተሰብእን ልን ፈጽም ይገባናልና ፤ አንድም ራሱን ከአብ ከመ ንፈስ ቅዱስ ጋራ አንድ አድርጎ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና አለ ። አብ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመ ስክር መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ከራሱ ላይ ሲቀመጥ አንድነት ሦስትነት ይገለጸልና ። ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሉ ጽድቀ ፤ በማኅፀን የጀመርነውን ቸርነት ልንፈጽም ይገባናልና ። ወእምዝ ኅደጎ ።

ከዚህ በኋላ ተወው ። ሐተታ ፤ እንዲያው አይተወ ውም ስመ አብ ብከ ወስመ ወልድ ሰሊከ ወስመ መንፈስ ቅዱስ ህልው ውስቴትከ ባዕደ አጠምቅ በስምከ ወበስመ መኑ አጠምቅ ኪ ያ ከ አለው ወልዱ ለቡሩክ ክግቴ ብርሃን ተግሣለነ ፤ አንተ ካህኑ ለዓለም በከመ ሢመቱ ለመልከ ጼዴቅ ብለህ አጥምቀኝ አለው ። ከዚህ በኋላ ተያይዘው ወደ ባሕር ወርደዋል ።

፲፮ ወተጠሚቆ እግዚእ ኢየሱስ ሶቤሃ ወፅአ እማይ ። ሉቃ ፤ ፫ ፤ ፳፩ ፤ ፳፪ ፤

፲፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከተጠመቀ በኋላ ከውኃው ወጣ ሐተታ ፤ ጥምቀቱን በውኃ ያደረገው በሌላ ያላደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፤ ትንቢት ወእነዝኃክሙ በማይ ንጹሕ ወትነጽሑ እምርኩሰክሙ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳ ሌም ለታውፅእ ባሕር ኵሎ ዘይትሐወስ ዘቦ መን ፈስ ሕይወት ባለ ጊዜ በልብ የሚሳቡ በእግር የሚ ያሽከረክሩ በክንፍ የሚበሩ በደመ ነፍስ ሕያዋን ሁነው የሚኖሩ ፍጥረታት ተገኝተዋል ፤ በረው በረው የሄዱ አሉ ከዚያውም የቀሩ አሉ ። በረው የሄዱ የኢጥሙቃን ከዚያው የቀሩ የጥሙቃን ምሳሌ ፤ ይህስ እንዳይሆን ወባረኮሙ ለክልኤሆሙ በአሐቲ በረከት ይላል ብሎ በልብ የሚሳቡ የሰብአ ዓለም በእግር የሚያሽከረክሩ ከትሩፋት ወደ ትሩፋት የሚሉ የባሕታውያን ፤ በክንፍ የሚበሩ ተመስጦ ያላቸው የበግዕታት ምሳሌ ትንቢቱን ዐውቆ እናገሯል ፤ ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ እስመሰሏል ፍጻሜው እንደምነው ቢሉ ውኃ በዙፋን ካለ ንጉሥ ባደባባይ እስካለ ጽኑስ ለሁሉ ርኩብ ነው ጥምቀት መሥራቱ ለሁሉ ነውና ፤ ውኃ ጽንፍ እስከ ጽንፍ ይፈሳል ። ጥምቀትም ጽንፍ እስከ ጽንፍ ይደረጋልና ። ውኅ ያነጻል ጥምቀትም ያነጻልና ፤ ውኅ ለወሰደው ፍለጋ የለውም በጥምቀትም የተሰረየ ኃጢአት በፍዳ አይ መረመርምና ፤ ውኅ መልክ ያሳያል መልክ ያለመ ልግል ፤ ጥምቀትም መልክአ ነፍስ ያሳያልና መልክአ ነፍስ ያስመልግልና ፤ በውሀ የታጠበ ልብስ ኃይል ጽንዕ ግዘፍ እየነሣ ይሄዳል ምእመናንም ተጠምቀው ገድል ትሩፋት እያከሉ ይሄዳሉና ፤ አንድም ሥጋዊ ተፍኅሮ የነርብቃ የነሲፓራ በውኃ ምክንያት ሁኑዋል መንፈሳዊ ተፍኅ ሮንም በውኃ ለማድረግ ፤ አንድም ሸክላ ሠሪ ሠርታ ስትጨርስ የነቃባት እንደሆነ እን ደገና ከስክሳ በውኃ ለውሳ ታድሰዋለች ። ተሐድሶም በጥምቀት ነውና ፤ አንድም በውኃ ቀድሞ ሰብአ ትካትን ኋላ ግብጻውያንን ካጠፋበት በኋላ ለመዓት እንጂ ለምሕረት አልተፈጠረም ብለውታል ፤ ለም ሕረትም እንደተፈጠረ ለማጠየቅ ። ሐተታ የወዲ ያኛው ቀስቱን እያጋለ መርዝ እየቀባ እያተባ ይመ ጣል ። የወዲህኛውም እግዚአብሔር ጥበቡን ገልጾ ለት ጀባውን ከውኃ ነክሮ ለጋሻው አልብሶ ይሄዳል መርዙን ጀባው ይጠርግለታል ፤ ግለቱን ውኃው ያቀዘቅዝለታል ስለቱን ጋሻው ይመልስለታል እንደ ዚህ ሁሉ ምእመናንም በጥምቀት ባገኙት ኃይል ድል ይነሳሉና ።

ወናሁ ተርኅወ ሎቱ ሰማይ ፤ ሰማይ ተከፈተለት ። ሐተታ ፤ በሰማይ መከፈት መዘጋት የለበትም ደጅ በተከፈተ ጊዜ የውስጡ እንዲታይ ያልተገለጸ ምስ ጢር ተገለጸለት ሲል ነው ። ወርእየ መንፈሰ እግ ዚአብሔር እንዘ ይወርድ ከመ ርግብ ወነበረ ላዕሌሁ። መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ በራሱ ላይ ሲቀመ ጥበት አየ ። ሐተታ ፤ መንፈስ ቅዱስን ርግብ አለው ርግብ ኃዳጊተ በቀል ናት ። መንፈስ ቅዱ ስም ኃዳጌ በቀል ነውና አንድም ርግብ በኖኅ ጊዜ ሐጸ ማየ አይኅንትኅ ማየ አይኅ ስትል ቈጽለ ዕፀ ዘይት ይዛ ተገኝታለች ፤ መንፈስ ቅዱስም ተሰፋ መስቀ ልን ያበሥራልና ፤ አንድም ርግብ ከንፏን ቢመቷት ዕንቍላሏን ቢሰብሩባት ቤቷን ካፈረሱባት አት ሄድም ። መንፈስ ቅዱስም ኃጢአት ቢሠሩ ፈጽ መው ካልካዱት አይለይምና ፤ ታሪክ ፤ አንድ ባሕ ታዊ እንዳየው ወለተ ካህነ ግፎርን አጊጣ አይቶ

በሐጸ ዝሙት ተንደፈ ። ሳማባሽ አላት ሳባቴ ንጉሬው እምቢ አይልህም አለችው ሂዶ ነገረው ። ፈጣሪዩን ልጠይቅ ብሎ ከጣዖቱ ዘንድ ገብቶ ልለጨው አል ስጠው ብሎ ጠየቀው ። ቆቡን ይቅደድ ፈጣሪውን ይካድ ይኸን ካላደረገ አትስጠው አለው ሂዶ ነገረው ። ቆቡን ቀደደ ፈጣሪውን ካደ ። በዚህ ጊዜ አድሮበት የነበረ መንፈስ ቅዱስ በነጭ ርግብ አምሳል ተለይቶት ሲሄድ አይቷል ። ያልኸኝን አደረግሁ ስጠኝ አለው ሁለተኛ ልጠይቅ ብሎ ገብቶ ቢጠይቀው ፤ ቆይ ፈጣሪውም ፈጽሞ አልራቀውም ባጠገብ ባጠገቡ ይጠብቀዋልና አትስጠው አለው ። አይሆንም አለው ፤ ለዚህን ብዩ ፈጣሪዩን ካድሁ ቆቤን ቀደድሁ ብሎ ንስሐ ቢገባ ተመልሶ በርግብ አምሳል ሲያድርበት አይቷል ። ጥምቀቱን በመዓልት ያላደረገው በሌሊት ያደረገው ስለምን ቢሉ ፤ በመዓልት አድርገት ቢሆን መንፈስ ቅዱስን በቁሙ ርግብ ነው ብለው በተጠራጠሩ ነበርና አሁንስ በቁሙ ርግብ አለመሆኑ መንፈስ ቅዱስ መሆኑ በምን ይታወቃል ቢሉ ፤ ጌታ የተጠመቀ ከሌሊቱ ባሥረኛው ሰዓት ነው በዚያን ጊዜ ተሐዋስያን ከየቦታቸው አይናወጡምና ፤ በቁሙ ርግብ አለመሆኑ መንፈስ ቅዱስ መሆኑ በዚህ ይታወቃል ፤ መንፈስ ቅዱስም መውረዱ ከውኃው ከወጣ ሆዮሐንስ ዘተለየ ነው ። ከወኃው ሳለ ወርዶ ቢሆን ስቀድሶተ ማያት የወረደ ነው ባሉ ነበረና ከዮሐንስ ጋራም ሳለ ቢሆን ስለ ክብረ ዮሐንስ የወረደ ነው ባሉ ነበርና ፤ ረቦ ወርዷል ያሉ እንደ ሆነ አብ ምሉእ ነው አንተም ምሉእ ነህ እኔም ምሉእ ነኝ ሲል ፤ አሰይፎ ወርዷል ያሉ እንደሆን የብሉይ መዋዕል የአብ ሕይወት ነኝ ፤ ብሉየ መዋዕል ያንተም ሕይወት ነኝ እኔም ብሉየ መዋዕል ሕይወት ነኝ ሲል ወርዶ ራሱን ቆንጠጥ አድርጎ ይዞታል አብ እጋዜ ዓለም ነው አንተም እጋዜ ዓለም ነህ እኔም እጋዜ ዓለም ነኝ ሲል ፤ መውረዱ ግን የማኅፀኑን ሊመግለጽ ነው ። አንድም ለአብነት እናንተም ብትጠመቁ እንዲህ ይወርድላችኋል ለማለት ወናሁ መጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ዘቦቱ ሠመርኩ ። ሉቃ ፱ ፴፮ ፤ ፪ ጴጥ ፩ ፲፯።

፲፯ ለተዋሕዶ የመረጥሁት በሱ ሀልው ሁኜ ልመለክበት የወደድሁት ልጅ ይህ ነው የሚል ቃል ከወደ ሰማይ ተሰማ ሐተታ ፤ በዚህ አድሮ ያለው ልጅ ነው አላሰም ፩ አካል ፩ ባሕርይ አድርጎ ይህ ልጅ ነው አለ እንጂ ፤ ኢይቤ ዘላዕለ ዝንቱ ወልድየ እላ ይቤ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ እንዲል። ወልድየም ማለቱ እንደ አምላክነቱ ነው እንጂ እንደ ሰውነቱ አይደለም ። ኢይቤ ዝንቱ ወልድየ ዘከመ ትስብእቱ አላ ይቤ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘከመ መለኮቱ እንዲል ።

በእንተ ተመክሮት ዘኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወእምዝ ወሰዶ መንፈስ ገዳመ ለእግዚእ ኢየሱስ ። ማር ፩ ፤ ፲፪ ሉቃ ፬ ፩ ፤ ከተጠመቀ በኋላ ፈቃዱ አንሣስቶ ወደ ገዳም ወሰደው ። ወሶበ ትሰምዕ እንዘ ይብሰክ መንፈስ ወሰዶ ገዳመ ኢትሐሊኬ ከመ ፍጡር ውእቱ ፤ አላ መንፈስሰ ምግባሩ ይእቲ እንዲል ፤ አንድም መንፈስ ቅዱስ የሚል አብነት ይገኛል ሰማዕታትን አንሣሥቶ ወደ ደም ጻድቃንን አንሣስቶ ወደ ገዳም እንዲወስድ ወሰደው ማለት አይደለም ፈቃዳቸው አንድ መሆኑን መናገር ነው ። ቀጠምቁም አልዋለም አላደረም ዕለቱን ገዳም ሄዷል ። እናንተም ተጠምቃችሁ አትዋሉ አትደሩ ዕለቱን ገዳም ሂዱ ለማለት አብነት ለመሆን ወደ ገዳም ሄደ አለ ። አዳም ከዚህ ዓለም አፍአ በምትሆን በገነት ድል ተነሥቶ ነበርና ፤ እሱም ከዚህ ዓለም አፍአ በምትሆን በገዳም በጦቱ አርጅስተ ኃጣውእ ድል ለመንሳት ። አንድም በገዳም ጸር ይቀላል ለወጣንያን አብነት ለመሆን አንድም በገዳም ጻር ይጸናል ለፍጹማን አብነት ለመሆን ። ከመ ይትመከር እምዲያብሎስ ከዲያብሎስ ይፈተን ዘንድ ፤ እፈተናለሁስ ብሎ ሂዶ ቢሆን ዕጻ በሆነበት ነበር ፤ ከሄደ ዘንድ ጸሩን እየቀሰመ ይሰብርበታል እንጂ ።

ይሆንም ጸር እማርበታለሁ ብሎ አላደረገውም ንግእ ፩ መዓዶ እምአፍአ ከመ ትኩን ፍቱነ ወስቡክ እንዲል መከራውንም ሽቶ አላመጣውም አኮ ፈቃዶ መከራሁ ለጸላኢ አላ ከመ ያብጥል ኃይሎ ለዘያሜክር በኃይሉ ለቃል ዘኮነ ፩ደ ምስለ ሥጋ እንዲል ። መከራውንም አንሣሥቶ አላመጣውም ኢሦክ እግዚእነ እሎንቱ ሕማማት ከመ ይባልዑ ዲቤሁ አላ በሁከቶሙ ማለት እንዲል ፤ መዋጋቱም በሰውነቱ ነው ፤ ኢሠርዓ እግዚእነ ቀትለ በመለኮቱ አላ በሥጋሁ ዘይትቄበል ሕማማተ እንዲል ። ድል መንሳቱም በሰውነቱ ነው እንጂ በአምላክነቱ አይደለም ። ወኢሞአ በኃይሉ መዋኢት እንዲል ፤ በአምላክነቱስ ድል ቢነሳው ባልተደነቀም ነበር ፤ ሶበሰ ሞአ እግዚእን በኃይሉ መዋኢት እምኢኮነ መንከረ ወእም አኮኑ ትኑፋት ዘወሰቱ ዘአሰበ ሕጻወዘ ኢውድሰት እኮ መንከር እመ ምእ ኃይል ለድኩም እንዲል ።

፪ ወጾመ ፵ መዓልተ ወ፵ ሌሊተ

፪ ፵ መዓልት ፵ ሌሊት ጾመ ። ሥራዔ ሕግ ነውና ጾምን መጀመሪያ ሕግ አደረገ ። አንድም ሥራውን በጾም ጀመረ ። ሐተታ ፤ መብል ስጋጣውእ መሠረት እንደ ሆኑ ፤ ጾምም ለምግባር ሰናያት መሠረት ናትና ፤ እማ ለጸሎት ወእኅታ ለአርምሞ

ምሞ ወነቅዓ ለእንብዕ ወጥንተ ዙሉ ገድል ሙናይት እንዲል ፡፡ ፵መዓልት ፵ ሌሊት መሆኑ ስለምን ቢሉ ቀድሞ አባቶቹ ነቢያት ፵ ፵ ጾመዋል ከዚያ ቢያተርፍ አተረፈ ቢያጐድል አጐደለ ብለው አይ ሁድ ደጊቱን ሕገ ወንጌልን ከመቀበል በተከለከሉ ነበርና ፡ ሙሴ በ፵ ዘመኑ ለዕብራዊ ረድቶ ግብጻዊን ገድሎ በኖጻ ቀብሮታል ፡፡ ሙሴ የወልደ እግዚአ ዚአብሔር ዕብራዊ የአዳም ግብጻዊ የዲያብሎስ ኖጻ የመስቀል ፡፡ እንድም የጅቶ አርአስተ ኃጣውእ ምሳሌ ፡ ሙሴ ፵ ጾም ሕገ ኦሪትን ሠርቷል እሱም ፵ ጾሞ ሕገ ወንጌልን የሚሠራ ነውና ሙሴ ፵ ዘመን በምድያም ኑሮ እሥራኤልን ከግብጽ አውጥቷ ቸዋል ፡፡ እሱም ፵ ጾሞ

ነፍሳትን የሚያወጣ ነውና ፡ እንድም የእሥራኤል ጉበኛች በ፵ ቀን ተመልሰዋል ፡፡ እሱም የመንግሥተ ሰማይ ጉበኛ ነውና እሥራኤል በገዳም ፵ ዘመን ኑረው ምድረ ርስት ገብተዋል ፡፡ እናንተም ፵ ብትጾሙ ጎሩት መንግሥተ ሰማያት ትገባላችሁ ለማለት ፡፡ ኤልያስ ፵ ጾሞ ገነት ገብቷል ፡፡ እናንተም ፵ ብት ጾሙ ገነት መንግሥተ ሰማያት ትገባላችሁ ለማለት ሕዝቅኤል በፀጋማይ ጐኑ ፵ ቀን ተኝቶ ስድስት መቶ ሙታን አስነሥቷል ፡፡ እናንተም ፵ብትጾሙ ትንሣኤ ዘለክብር ትነሣላችሁ ለማለት ፡ ዕዝራ ፵ ቀን ከም ግቡ ተከልክሎ መጻሕፍትን አጽፏል ፡፡ እንሰ በው እቶን መዋዕል ኢበላዕኩ እክለ ወኢሰተይኩ ማየ ፡፡ እሙንቱስ መዓልተ ይጽሕፉ ወሠርከ ይዴረሩ እን ዲል እነዚያ ቀን ሲጽፉ እየዋሉ ማታ ይመገባሉ ፡፡ እሱ ግን ቀን ሲያጽፈው የሚውለውን ሌሊት ሲያስ በሙያድር ነበር ፡፡ እናንተም ፵ ብትጾሙ ምሥጢር ይገለጥላችኋል ለማለት ፡ እነብ አካሉ የደገደገበት እንደሆነ ፵ ቀን ከምግብ ተከልክሎ ይሰነብታል ፡፡ በስቁረተ ዕፅ በስቁረተ እብንም ቢሉ አልፎ ሲሄድ ተግፎ ይወድቅበታል ይታደሳል ፡፡ እናንተም አርባ ብትጾሙ ተሐድሶተ ነፍስ ታገኛላችሁ ለማለት ፡፡ ምሳሌውን አውቆ አስመስሏል ፍጻሜው እንደም ነው ቢሉ አዳም በ፵ ቀን ያገኘውን ልጅነት አስ ወስዶ ነበርና ለሱ እንደካሰ ለማጠየቅ ፡ እንድም በ፵ቀን ተሰእሎተ መልክእ ለተፈጸመለት ሰው ሁሉ ሊክስ እንደመጣ ለማጠየቅ ፡፡ ሳ፬ቱ ባሕርያት ዐሥር ዐሥሩን ለመካስ ፡፡ አምስቱኛ ባሕርየ ነፍስን የጨመሩ እንደሆነ ስምንት ስምንቱን ሊክስ እንደመጣ ለማጠየቅ ፡፡ ከዚህም ተራብ አልሳሳም ተዋጋ ድል አልተነሣም ወሶበ ጾመ እግዚእ ፵መዓልተ ወ፵ሌሊተ ከሠተ ከመ ኢሐመ ሥጋሁ እምረኃብ ወጽምዕ በኃ ይል ዘይደሉ ለመለኮት እንዲል ፤ ከዚህም ሥራውን ሠርቶ ሥሩ አለ እንጂ ፡፡ ባልዋጁበት ጣት የዘንዶ ጉድጓድ ይለኩበት እንዲሉ ሳይሠሩ እኛን ሥሩ አላ ለንም ወሐርገ እግዚእ ለጌሰ ግብሩት እንዲል ፫

ጊበሩት የተባሉ ጥምቀት ፡ ተአምኖ ኃጣውእ ከዊነ ሰማዕት ተባሕትዎ ምንዝትስና ፡፡ ጥምቀት በእደ ዮሐ ንስ መጠመቅ ተአምኖ ኃጣውእ ከተአማንያን ኃጣ ውእ ጋራ አንድ ሁኖ መቆጠር ከዊነ ሰማዕት አንሰ በእንተ ዝንቱ ተወለድኩ ወእንበይነ ዝንቱ መጻእኩ ውስተ ዓለም ከመ እኩን ሰማ ዕተ በጽድቅ ብሎ ከጲላጦስ ፊት ቁሞ መመስ ከር ተባሕትዎ ፵ ቀን ከምግብ ተከልክሎ በገዳም መኖር ፡ ምንኵስና በድንግልና መኖር ነው ፡፡ ረቂቅ ዘእምረቂቅ እንደሆነ ለማጠየቅ በኑቱም ድንግልና ተፀንሰ በኑቱም ድንግልና ተወለደ ፡፡ ዘኢይርኅብ እም ዘኢይርኅብ እንደሆነ ለማጠየቅ ፵ መዓልት ፵ሌሊት ጾመ ዘኢይትገሠሥ እምዘኢይትገሠሥ እንደሆነ ለማጠየቅ በባሕር ላይ ሄደ ፡፡ ብርሃን ዘእምብርሃን እንደሆነ ለማጠየቅ ብርሃን መለኮቱን በደብረ ታቦር ገለጸ ሕይወት ዘእምሕይወት እንደሆነ ለማጠየቅ ያራት ቀን ሬሳ አልዓዛርን አነሣ ፡፡ ወእምዝ ርኅበ ፡ ከዚህ በኋላ ተራበ ፡፡ ሐተታ ረኃቡም የፈቃድ ረኃብ ነው እንደ እኛ እንደኛ ረኃብ አይደለም እኛ ብንበላው ቁንጣን ብንተወው ስልት ቀጠና ይሆንብናል ፤ ረኀበ እግዚእነሰ አኮ ከመ ረኃበ ዚአነ አላ ገጸ ረኃቡ ፍሉጥ እምኔነ ለነሰ በግብር ይመውአነ ወሎቱሰ በፈቃዱ እንዲል ፤ አንድ ጊዜ ርኅበ አንድ ጊዜ ኢርኅበ ይላል እንደምነው ቢሉ ፡ ከ፪ት አካል ፩ አካል ከሁለት ባሕርይ ፩ባሕርይ እንደሆነ ለማጠየቅ ፡፡ በእንተ ምንት ርኅበ እግዚእነ ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ ያጠይቅ ከመ ውእቱ እም ፪ ህላዌያት እንዲል ፡፡ መራቡም ለአጽድቆተ ትስብእት ለካሣ ነው ፡፡

፫ ወቀርበ ዘያሜክሮ ፡፡

፫ የሚፈታተነው ዲያብሎስ ቀረበ ሐተታ እንዲያው አይቀርበውም ርኅብኩ የሚል ድምፅ ሰ ምቶት ፍሬ ዕፅ ሲሻ አይቶት ፡ መልኩን አጠውልጎ ታይቶት እሱም እንዲያው አይቀርብም በአምሳለ ሠዓሊ በአምሳለ ሐራሲ በቀዳዳ ሽልቻ ትኩስ ዳቦ የያዘ መስሎ ሁለት ደንጊያ ይዞ ይቀርባል አንዱን ሳተ አንዱን ለኔ ዳቦ አድርገህ እንብላ እለዋለሁ ደንጊያውንማ ዳቦ ከማድረግ የያዝኸውን እንበላም ያለኝ እንደሆነ አዳምን አባቱን በመብል ምክንያት ድል እንደነሣሁት እሱንም በመብል ምክንያት ድል እነሣዋለሁ ብሎ ፡

ወይቤሎ እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ በል ከመ እላ እዕባን ኅብስተ ይኩና ፡

፬የርዳኖስ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመሰክርለት ሰምቶ ነበርና የእግዚአብሔርስ ልጅ ከሆንክ እኒህ ደንጊያዎች ኅብስት ይሁኑ ቁዕህ እዘዝ አለው ፡፡ ቢያደርገው የሰይጣን ተአዛዚ ብየ ዕዳ እልበታለሁ

ባያደርገው ደካማ አሰኘዋለሁ ። ቢያደርገው ሌላ ጾር እሻለታለሁ ባያደርገው ድካሙን አይቼ እቀርበ ለሁ ብሎ ፤ ደንጊያውን ኅብስት አድርግ ማለቱ ምን ልማድ ይዞ ነው ቢሉ በዮሴፍ ልማድ ፤ ዮሴፍን እባቱ የሱን ስንቅ ሉብቻ አሲዞ ለወንድሞችህ ስንቃቸውን ሰጥተህ ወንድሞችህን ጠይቀህ ና ብሎ ላከው ። ያሉ በትን እጥቶ ሲፈልግ የሱ ስንቅ እለቀበት ከዚያ እን ዳይበጣ አባቱ ያላዘዘው ነው ። ረኃብ ጸንቶበት ሳለ መልአክ ያጣትህን ፈጣሪ ደንጊያውን ዳቦ አድርግ ልኝ አትለውም አለው ። ወደ እግዚአብሔር ቢያ መለከት ደንጊያው ዳቦ ሁኖለት ተመግቧልና እን ዲህ አለ ።

፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ጌታም መለሰ ። ወይቤሎ ጽሑፍ ከመ አኮ በኅብስት ከመ ዘየሐዩ ሰብእ ። ዘዳ ፰ ፫ ሉቃ ፬፥፬ ።

፬ ሰው የሚድነው በኅብስት ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ።

አላ በኵሉ ቃል ዘይወፅእ እምአፉሁ ለእግዚአብሔር እግዚአብሔር ዳን ያለው ይድናል ሙት ያለው ይሞ ታል እንጂ ፤ አንድም ሰው የሚያድን ገበሬ በጻረበት በኅብስት ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ፤ እግዚአብሔር ምግብ ይሁን ያለውም ምግብ ይሆናል እንጂ እስራ ኤል ፵ ዘመን በትርሀ አልወደቀ ሜማህ አልወለቀ ልብስህ አላለቀ እንዲሉ ከውቅያኖስ በደመና አይ በት ተቋጥሮ በነፋስ ወደልጋዝ ተጭኖ መጠኑ ድን ብላል እህሉ መልኩ በረድ መስሉ ወእንዘ የኃድግ ህቦ ይላል የውርጭ ገበታ ሲነጸፍ እየዘነመላቸው አርባ ዘመን ተመግበዋልና ፤ አንድም ሰው የሚድን ገበሬ በጻረበት ቢጋረበት በእንጀራ ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ፤ በዓቂበ ሕግም በትምህርትም ነው እንጂ ሐተታ ። የሰው ባሕርዩ ባሕርይ እንስሳዊ ባሕርይ መልአካዊ ነው ባሕርይ እንስሳዊ ምግብ ሲያጣ ይጎ ዳል ፤ ባሕርይ መልአካዊ ትምህርት ሲያጣ ይጎዳልና እእምር ከመ በእማን ቢያይ ቃለ እግዚአብሔር ሲቢተ ልብ ቃላቲሁ ለእግዚአብሔር ወእምጽእ ረ ኃ በ እ ክ ል ወጽምዓ ማ ይ ለ ብ ሐ ር ረኃብስ እምስሚዓ ቃለ እግዚአብሔር እንዲል ። አንድም ወልደ እግዚአብሔርስ ከሆንህ ይህ እንደ ድንጊያ ፈዞ ያለ ሰውነትህ ኅብስተ ሕይወት ኅብስተ መድኃኒት ይሁን ብለህ እዘዝ ሲያሰኘው ነው ። ጌታም ሰው የሚያድን በዕሩቅ ብእሲ ሥጋ እንዳይ ደለ ተጽፏል ። አካላዊ ቃል በተዋሐደው ሥጋ ነው እንጂ አለው ፭ ወእምዝ ነሥአ ወወሰዶ ውስተ ቅድስት ሀገር ።

፭ ከዚህ በኋላ ወደ ቅድስት ሀገር ወደ ኢየሩሳሌም ወሰደው ሐተታ እሱስ አይወስደውም ፈቃዱን ዐውቆ ስለሄደለት ክህናትን ድል ነሥቼበት በማላውቅ በገዳም ቢሆን ነው እንጂ ፡ ክህናትን ድል በምነሳ በት በቤተ መቅደስ ቢሆን መች ድል ይነሳኝ ነበር ብሏል ፈቃዱን አይቶ ስለሄደለት ነሥአ ወሰዶ አዕ ረጎ ይላል ወዓቀሞ ውስተ ተድባበ ቤተ መቅደስ ። ተድባብ ማዕዘንት ርእስ ይላል አብነት ፤ ተድባብ ያለ እንደሆነ ከዝንቦው ማዕዘንት ያለ እንደሆነ ከም ሕዋሩ ርእስ ያለ እንደሆነ ከጉልላቱ አቆመው ። ከዚ ህም በአምሳለ ሊቀ ካህናት እምዋ ጠምጥሞ መነሳ ንስ ይዞ ይታየዋል ።

፮ ወይቤሎ እመሰ አማን ወልደ እግዚአብሔር አንተ ቅንጽ እምዝየ ወተወረው ታሕተ ።

፮ መዝ ፡ ፺፩ ።
በእውነት ወልደ እግዚአብሔር ከሆንህ ከዚህ ዘለህ ወደታች ውረድ አለው ፤ ሐተታ ቢሰበር ዐርፈዋለሁ ባይሰበር ምትሐት አሰኘዋለሁ ቢያደርገው ሌላ ጾር እሻለታለሁ ባያደርገው ደካማ አሰኘዋለሁ ቢያደር ገው የሰይጣን ተአዛዚ ብየ ዕዳ እልበታለሁ ባያደ ርገው ድካሙን አይቼ እቀርበዋለሁ ብሎ ነው ። እስመ ጽሑፍ ከመ ለመላእክቲሁ ይኤዝዞሙ በእን ቲአከ ከመ ይዕቀቡከ በኵሉ ፍናዊከ በመንገድህ ሁሉ ይጠብቁህ ዘንድ መላእክትን ሰላንተ እንዲያዛ ቸው ተጽፏልና ፤ ወበእደዊሆሙ ያነሥኡከ ከመ ኢትትዐቀፍ በእብን እግርከ እግረከ ይላል ፤ እግርህ እንዳይሰናከል፤በእጆቻቸውም ያነሡሃል የሚል ጽሑፍ አለና ፡ ጌታ ከላይ ጠቅሶበት ነበርና ፤ እሱም ፈን ታውን ይንጐዳጐዳል ።

፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ካዕበ ጽሑፍ ኢታመክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ።
፯ ፡ ዘዳ ፡ ፮ ፡ ፲፮ ።

ዳግመኛ ፈጣሪህን እግዚአብሔርን አትፈታተነው የሚል ጽሑፍ አለ አለው ፤ እንዲህ የሚል ከምን አለ ቢሉ እንደ ጊዜ ገድሉ ጠቀሰ ። እሥራኤል በገ ዳም ሳሉ ሙሴ ካሥራሁለቱ ነገድ አውጣጥቶ ኢያሱና ካሌብን ምድረ ርስትን ሰልላችሁኑ ብሎ ሰደዷ ቸው ። እሳቸውም ሰልለው ሲመለሱ ከወይኑ ዘለላ ከሰንደሌው ዛላ በባጢ ቀፎ ይዘው መጡ ። እንደምን ሁናችሁ መጣችሁ ሀገሪቱስ እንደምን ያለች ናት ብለው ጠየቋቸው ። ሀገሪቱስ መልካም ናት እንደዚህ ያለ ታፈራለች ፤ ባሕቱ ርኢነ ደቂቀ ለኤናቅኑኖሙ ከመ እርዝ ወጽንየሙ ከመ እውልዕ ንሕነሰ ኮነ ከመ አናብጥ በቅድሜሆሙ ምድርኒ ትረድእሙ ወተዓቅቦሙ ብለው ፲ሩ እስገርመው እስፈርተው ተናገሩ ካሌብና ኢያሱ በፈቃደ እግዚአብሔር እንገባታለን አሉ ፲ሩ ካገባንስ አሁን ያገባን ሙሴ ተነሣ ታቦተ ጽዮንንም እንሣ እንሂድ አሉት ፤ ሙሴ ታቦተ ጽዮንም አሁን አትነሣ እናንተም እግዚአብ ሔር ፈጣሪያችሁን አትፈታተኑት አላቸው ። አይሆ ንም ብለው ሄዱ ። በወሰን ያሉ አሕዛብ ገጥመው

ድል አደረጓቸው ፤ በዚህ ጊዜ ከባሕር ጠልቀው ። ከገደል ወድቀው አልቀዋል ፤

ከዚህም ጌታ እንደ ጊዜ ገድሉ ጠቀሰው ።

፰ ወእምዝ ነሥኦ ዲያብሎስ ወአዕረጎ ውስተ ደብር ነዋኅ ጥቀ

፰ ከዚህ በኋላ ወደ ረጅም ተራራ አወጣው ሐተታ ነገሥታትን ድል በማልነሣበት በቤተ መቅደስ ቢሆን ድል ነሣኝ እንጅ ፣ ነገሥታት ድል በምነሣበት በተራራ ቢሆን መቸ ድል ይነሣኝ ነበር ብኋል ፈቃዱን ዐውቆ ስለሄደለት አዕረጎ አለ ።

ወአርአዮ መንግሥታተ ኵሉ ዓለም ፣ ወኵሎ ክብሮ ፣ ጠጠሩን ወርቅ ብር ፣ ቅጠሉን ግምጃ አስመስሎ አሳየው እንድም መንግሥታተ ኵሉ ዓለም ። ግዛቱን ሁሉ አሳየው ወኵሎ ክብሮ እንስሳትን አራዊትን ፈረስ በቅሎ ሠራዊት አስመስሎ አሳየው ፣ እሱስ ያይለታል ቢሉ ስለመሰለው ነው እንጅ አያይለትም ድል መንሳቱ በምን ይታወቃል ቢሉ ባለመጽነኑ ።

፱ ወይቤሎ ዘንተ ኵሎ እሁበከ እምከመ ሰገድከ ሊተ ወአማኅከኒ ፣ ደፋር ነውና ብትሰግድልኝ እጅ ብትነሳኝ ይህን ሁሉ እሰጥሃለሁ አለው ።

፲ ወእምዝ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር እምድኅሬየ ሰይጣን ።

፲ ዘዳግም ፮ ፲፫ ፣ ከዚህ በኋላ ከኋላየ ወግድ እሰው ራስ አይቶ የሚመጣ ጠላት ከፉ ነውና ጽኑ ባላጋራዬ ሲል ነው ። ወዓቀመ አዶርሃ ሰይጣነ ላዕለ ሰሎሞን እንዲል ። እንድም እምድኅሬየ ይላል አብነት ከኔ በኋላ ከሚነሱ ከምእመናን ወግድላቸው አለው ። እንዲህ ባለው ጊዜ እንደጢስ ተኖ እንደ ትቢያ በኖ ጠፍቷል ። ሐተታ እስካሁን ሑር እያለው አሁን ሑር ማለቱ ስለምን ቢሉ ። በቀዳሚ ጊዜ ጉየይ ወበካልዕ ጊዜ ጉየይ ወበሣልስ ተንሥእ ወተቃተል እንዲል ፣ አብነት ለመሆን በሦስተኛው ድል ንሱ ለማለት ንጉሥ በመንግሥቱ ጉልማሳ በሚስቱ እንዲቀና ፣ ጌታም ስአምልኮቱ ቀናዒ ነውና ፣ እስመ አነ አምላክ ቀናዒ ዘእፈዲ ኃጢአተ አብ ላዕለ ውሉድ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትውልድ ለእለ ይጸልዑኒ ። ወለአለሰ ያፈቅሩኒ እገብር ምሕረተ እስከ ፲ቱ፻ ትውልድ እንዲል ።

ጽሑፍ ለእግዚአብሔር አምላክከ ትሰግድ ወኪያሁ ባሕቲቶ ታምልክ ፣ ለፈጣሪህ ለእግዚአብሔር ትሰግድ ዘንድ እሱንም ብቻ ታመልክ ዘንድ ተጽፏል አለው። ሑር እምድኅሬየ ባለው ጊዜ እንደጢስ ተኖ እንደ ትቢያ በኖ ጠፋ አላለምን ለማን ይጠቅሰዋል ቢሉ ሰይጣንና ውሻ ምልልስ ወዳጅ ነውና ተመልሶ ያሰማዋል ። እንድም እንደ አምላክነቱ እጽንቶት ሰምቶ ይሄዳል ። እንድም ወጺጋሁ ታሰምዖ

እንዲል ካለበት ሁኖ እንዲሰማው አድርጎታል ። እንድም ከሐተታ ለመዳን ጥቅሱ ይቀድማል ።

፲፩ ወእምዝ ኀደጎ ዲያብሎስ ።

፲፩ ከዚህ በኋላ ተወው እስከ ጊዜሁ ብሎ በሉቃስ ያቀናዋል ። በዕለተ ዓርብ በአይሁድ ሥጋው ሁኖ እስኪያስቀስው ድረስ አይመለስበትም ። ከዚህም በጎ ልጅ ተወልዶ ለአዳምና ለሔዋን በሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል ነሣላቸው ። አሁን ዛሬ ደም ያለበት ሰው ጌሻ አስነሥቶ አምባውን ሰብሮ ደመኛውን ገድሎ ደሙን መልሶ ሲሄድ የቀሩት ከዛፍ ከገደል ተጠግተው የሆነስ ሆነ አንተ ማነህ እንወቅህ ባሉት ጊዜ የዘመዶቼን የእገሌ የእገሌ ደም የማይቀርብኝ እኔ እገሌ ነኝ ብሎ እንዲል ፣ ጌታም የአባቴ የአዳም የእናቴ የሔዋን ደም የማይቀርብኝ ሲል በሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል ነሣላቸው ፣ ሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ስስዕ ትዕቢት ፍቅረ ንዋይ ናቸው ። በስት ያልሰጡትን መሻት ነው ። ትዕቢት እምሳክ እሆናለሁ ማለት ነው ። ፍቅረ ንዋይ በቃኝ አለማለት ነው ። በዚህ ሁሉ ድል ነሥቶታል ። ዛቲ ስፍጠት አንተ ረስየቶ ለአዳም ይትመየጥ ውስተ መሬት ወሶበ በጽሐ ኀበ አምላኪየ ወኀቤ ሲሳይ ለኵሉ ገብአ ሰይጣን ተኃፈሮ ወተመዊአ

እንዲል ፣ እንድም ድል መንሳቱ ለአዳምና ለሔዋን ብቻ አይደለም ለሁሉም ድል ነሥቶላቸዋል የመነኮሳትም ጾራቸው ስስት ነው በሹት ጊዜ እያገኙትምና በትኅርምት ኑዋሪዎች ናቸው በቦታቸው በገዳም በስስት ቢመጣበት በትዕግሥት ድል ነሥቶላቸዋል የካህናት ጾራቸው ትዕቢት ነው አእምሯችን ረቂቅ ማዕርጋችን ምጡቅ እያሉ ይታበያሉ ። በቦታቸውም በቤተ መቅደስ በትዕቢት ቢመጣበት በትሕትና ድል ነሥቶላቸዋል ። የነገሥታት ጾራቸው ፍቅረ ንዋይ ነው ቤታቸውን ከፍ ካለ ቦታ ሠርተው ያለፈ ያገደመውን የወጣ የወረደውን እያዩ የዚህ ሁሉ እንጅ ኑሮው በኛ ነው እያሉ ገንዘብ ይሰበስባሉ ቦታቸው በተራራ ነው ። በተራራ በፍቅረ ንዋይ ቢመጣበት በጸሊዓ ንዋይ ድል ነሥቶላቸዋል ፣ ከዚህ በኋላ ኃጢአት ከሥሩ እንደተነቀለ ዛፍ ሁናለች ከሥሩ የተነቀለ ዛፍ እንዳይለመልም እንዳያብብ እንዳያፈራ ኃጢአትም በፍዳ የማታሲዝ ሆናለች ። ዛሬ የተያዙ አሉሳ ቢሉ እሊህማ ዐዋጅ አፍራሾች ናቸው ። ንጉሥ ይዘምታል ድል ነሥቶ ሲመለስ ከመንገድ የወጣህ ወታደር ብሎ ዐዋጅ ይነግራል በደለኛ ወታደር ገንዘብ ሲዘርፍ ከመንደር ገብቶ ቢሞት ንጉሥ ድል አልነሣም ይባላልን ? እኒህስ ዐዋጅ አፍራሾች ናቸው ።

ወናሁ መጽኡ መላእክት ይትለአከዎ ።

አርባ ቀን በትህርምት ኖሯልና መላእክት ኅብስት ሰማያዊ ጽዋዕ ሰማያዊ ይዘው መጡ እንድም ድል

ነሥቷልና ለከ ኃይል ለከ ጽንዕ እያሉ እያመሰገኑ ቀረቡ ። እንደ ዓቢይ ንጉሥ እንደ ንዑስ ንጉሥ ተሰ ልፈው ስንብተዋል ። ከዚህ በኋላ ሠራዊታችን ለምን ያልቃል አንድ ላንድ እንገናኝ ብለው ተገናኙ ። ዓቢይ ንጉሥ ንዑስ ንጉሥን ገደለው ። የዓቢይ ንጉሥ ሠራ ዊት ደስ ብሏቸው እየዘፈኑ ቀርበዋል ።የንዑስ ንጉሥ ሠራዊት እያዘኑ እየፈሩ ሸሽተዋል ። እኒህም ድል ነሥቶላቸዋልና ፣ መጡ አለ ። ድል ከነሣ በኋላ መምጣታቸውስ ስለምን ቢሉ አስቀድመው መጥ ተው ቢሆን መላእክትን ይዞ ድልነሣኝ እንጂ ብቻ ውንማ ቢሆን መች ድል ይነሣኝ ነበር ባለ ነበርና እንዲህ እንዳይል ። አንድም እናንተም ድል ብትነሱ ይገለጽላችኋል ለማለት ። አንዳንድ ባሕታዊ ሰይ ጣን መጥቶ ንጉሥ ይጠራሃል አለው ። አልብየ ንጉሥ ዘእንበለ እግዚእየ ኢየሱስ ክርስቶስ አለው ፣ ይህ ደፋር በዓለም እያለ ንጉሥ የለም ይላል ብሎ በያዘው በሎታ ቀጥቅጦት ሄዷል ። ከዚህ በኋላ መልአከ ዑቃ ቢው ተገለጸለት ማነህ አለው እኔ መልአከ ዑቃቢህ ነኝ አለው ። እንኪያ እስካሁን ወዴት ኖረሃል አለው አሁንም ድል ብትነሣ ነው እንጂ ድል ባትነሳ አልገለጽልህም ነበር ብሎታል ።
ዘከመ ነበረ እግዚእ ኢየሱስ በቅፍርናሆም ።

፲፪ ወሰሚዖ እግዚእየ ኢየሱስ ከመ አኀዝዎ ለዮሐንስ ተማኅው ውስተ ገሊላ ። ማር ፩፥፲፬ ።

፲፪ ከመ አኃዝዎ ከመ ተማኅሠ ይላል ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዮሐንስን እንዳጋዙት ዮሐንስ እን ደተጋዘ በሰማ ጊዜ ገሊላ ገባ መከራ በመጣባችሁ ጊዜ ሽሹ ለማለት አብነት ለመሆን ።

፲፫ ወኃደጋ ለናዝሬት ወመጺአ ኀደረ ቅፍርና ሆም እንተ መንገለ ባሕር ።

፲፫ ናዝሬትን ትቶ በባሕር አጠገብ ባለች በቅ ፍርናሆም ሲያስተምር ኖረ ። ውስተ አድባረ ዛብሎን ወንፍታሌም ። የዛብሎን የንፍታሌም ዕፃ በምትሆን

፲፬ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ በኢሳይያስ ነቢይ
፲፬ በነቢዩ በኢሳይያስ ቃል የተነገረው ትን ቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ኖረ ።

፲፭ እንዘ ይብል ምድረ ዛብሎን ወምድረ ንፍ ታሌም ። ኢሳ ፱፥፩ ።
፲፭ በዛብሎን በንፍታሌም ዕፃ ያሉ ፍኖተ ባሕር ። በባሕር አጠገብ ያሉ ጺራልዩ ወጺራልያስ ። ጠጠር ገጠር ።
ማዕዶተ ሐይቀ ዮርዳኖስ ። በዮርዳኖስ ወደብ ማዶ በእንጻረ ሊባኖስ ያሉ ፣ ገሊላ ዘአሕዛብ የአሕዛብ ክፍል ዕፃ በምትሆን በገሊላ ያሉ ሐተታ ዘሕዝብ አለና ከዚያ ሲለይ ዘአሕዛብ አለ ፡ ሰሎሞን ቤተ መቅ ደስን በሠራ ጊዜ ወአርድኦ ኪራም በዕፀወ ቄድሮስ ወጳውቄና እንዲል ፡ ጥድ ዘግባ እየጠረበ አግዞታል

ሃያ ያህል ቀላል ቀላል አህጉር ሰጠው እስመ ኢዓደ ማሁ ይላል ደስ ባያሰኙት ወዳጄ በኔና ባንተ ዘንድ ይህ ምን ቁም ነገር ነው አለው ። የመልክተኛ ማደ ሪያ ይሁንህ ብዩ ነው አለው ከዚህ በኋላ አሕዛብ እንደ ባለጉልት እሥራኤል እንደ ባለርስት ሁነው የሚኖሩ ሁነዋልና ገሊላ ዘአሕዛብ አለ ፤ አንድም ፈርዖን አሕዛብን ወግቶ ለልጁ ለሰሎሞን ሚስት ሰጥቷት ነበርና ገሊላ ዘአሕዛብ አለ ።

፲፮ ሕዝብ ዘይነብር ውስተ ጽልመት ርእየ ብርሃነ ዓቢየ ፤

፲፮ በጨለማ ላሉ ሕዝብ ታላቅ ብርሃን ወጣላ ቸው ። ወለእለሂ ይነብሩ ውስተ ጽልመት ወጽላሎተ ሞት ብርሃን ሠረቀ ሎሙ በጨለማ በሞት ጥላ ለሚ ኖሩ ብርሃን ወጣላቸው ብሎ ኢሳይያስ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ በቅፍርናሆም ኖረ ። አንድም በድንቁርና በቀቢጸ ተስፋ ለነበሩ ሰዎች ዕውቀት ተሰጣቸው ፣ አንድ ገጽ በማለት ሞትን በመምሰል ሞት ባመጣው ምስል ለሚኖሩ ሰዎች ክርስቶስ ተወ ለደላቸው ወንጌል ተጻፈላቸው ።

አንድም በሞተ ሥጋ በሞተ ነፍስ ለነበሩ ልጅነት ተሰጣቸው ። በኃጢአት በክህደት ለነበሩ ሃይማኖት ተገለጸላቸው ። ሐተታ ኃጢአትን ጽልመት ክህደ ትን ጽላሎተ ሞት አለው በጨለማ ላይ የዛፍ የገደል ጥላ የተጨመረ እንደሆነ ጨለማው እንዲጠና በኃ ጢአትም ላይ ክህደት የተጨመረ እንደሆነ ፍዳው ይጸናልና ፤

፲፯ ወእምአሜሃ አኀዘ እግዚእ ኢየሱስ ይስብክ ወይብል ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ። ማር ፩፥፲፬ ።

፲፯ ዮሐንስ ከተጋዘበት ቀን ጀምሮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ደጊቶ በልጅነት ልጅነት በሃይማ ኖት ልትሰጥ ቀርባለችና እመኑ እያለ ያስተምር ጀመረ ዮሐንስ ከተጋዘ በኋላ ማስተማሩ ስለምን ቢሉ መምር ሳለ በመምር ላይ እናስተምራለን አት በሉ ለማለት ። አንድም መምሩ አንድ ዮሐንስ ነበረ ያውም ተመተረ እንዳይሉ ትምህርቱንም አሰወጠ ውም የስንቱን ይስሟል እንዳይሉ ፣ አንድም ዮሐንስ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ብሎ ያስተማረልኝ እኔ ነኝ ሲል ነው ፡ ነያ ይሰምያ መንግሥተ ሰማያት ለእ ስተርእዮቱ ማእከለ ፍቁራኒሁ እንዲል ።
በእንተ ቀዳማውያን ሐዋርያት

፲፰ ወእንዘ ያንሶሱ መንገለ ባሕረ ገሊላ ርእየ ፪ተ አኃወ ። ማር ፩፥፲፮ ።

፲፰ በገሊላ ባሕር ማዶ ሲመላለስ ሁለት ወን ድማማቾች አገኘ ። ስምአንሃ ፡ ዘተሰምየ ጴጥሮስ ። ጴጥሮስ የተባለ ስምኦንን ። ወእንድርያስሃ እኅዋሁ

ወንድሙን እንድርያስን እንዘ ይወድዩ መርበብቶሙ ውስተ ባሕር ፤ መረባቸውን ከባሕር ሲጥሉ እስመ መሠግራን እሙንቱ ዓሣ ወጋሮች ነበሩና ።

፲፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ንዑ ትልውኒ ድኅሬየ ።

፲፱ ለጊዜው በእግር ተከተሉኝ ፍጻሜው በግብር ምስሉኝ አላቸው ወእሬስየክሙ መሠግራነ ሰብእ ሰውን እንደ ዓሣ ወንጌልን እንደ መረብ ይህን ዓለም እንደ ባሕር አድርጋችሁ እንድታስቀምሩ አደርጋችኋለሁ አላቸው ።

፳ ወበጊዜሃ ኀደጉ መሠግሪሆሙ ወተሰውዎ

፳ ያን ጊዜ ፈጥነው መርከባቸውን መረባቸውን ትተው ተከተሉት ለጊዜው በእግር ተከተሉት ፍጻሜው በግብር መሰሉት ።

፳፩ ወተዓዲዎ ሕቀ እምህየ ርእየ ካልዓነ ፪ተ አኃወ ።

፳፩ ከዚያ ጥቂት እልፍ ብሎ ሁለት ወንድማማች አገኘ ፤ ያዕቆብሃ ወልደ ዘብዴዎስ ወዮሐንስሃ እኁዋሁ ፤ የዘብዴዎስ ልጅ ያዕቆብን ወንድሙ ዮሐንስን ፤ ውስተ ሐመር ምስለ ዘብዴዎስ አቡሆሙ ፤ ከአባታቸው ከዘብዴዎስ ጋራ እንዘ ይሠርዑ ወያስተሣንዩ መሣግሪሆሙ ።

መረባቸውን ያደፈውን ሲያጥቡ የተቀረጠውን ሲቀጥሉ ፡ ወጸውዖሙ ። ለጊዜው በእግር ተከተሉኝ ፍጻሜው በግብር ምስሉኝ አላቸው ።

፳፪ ወበጊዜሃ ኀደጉ ሐመሮሙ ወዘብዴዎስሃ አባሆሙ ወተለውዎ ።

፳፪ ያን ጊዜ ፈጥነው መረባቸውን መርከባቸውን ዘብዴዎስ አባታቸውን ትተው ተከተሉት ፤ ሐተታ ፡ አክብር አባከ ወእመከ ይል የለም ቢሉ ። ይህን ቃሉ ካልተማሩ አያውቁትምና ። አንድም ክአክብሮተ አብ ወእም አክብሮተ እግዚአብሔር እንዲበልጥ ለማጠየቅ ። አባትን የሚረዳው ልጅ የሚረዳበት ገንዘብ ያለ እንደሆነ ትቶ መሄድ ይገባል ። የሚረዳው ልጅ የሚረዳበት ገንዘብ የሌለው እንደሆነ ትቶ መሄድ አይገባም እሱን ግን ምስለ አሳቡ ብሎ በማርቆስ ያቀናዋል ገንዘብ ያለው ነው ።
በእንተ ቀዳማዊ ስብከቱ ወመንክራቲሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፫ ወአንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ኵሉ ገሊላ እንዘ ይሜህር በምኵራባቲሆሙ ።

፳፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በምኵራብ ገብቶ ሲያስተምር በገሊላ ሲመላለስ ኖረ ።
ወይሰብክ ወንጌለ መንግሥት ፡ ጌትነቱን የምትናገር ወንጌልን እያስተማረ ኖረ ። ሐተታ ፡ ወልደ ፡ እግዚአብሔር እንደነገሠ ዲያብሎስ እንደተሻረ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ እንደጠፉ ትናገራለችና ወንጌለ መንግሥት ይላታል ወይፌውስ ኵሎ ድውያነ ወኵሎ ሕሙማነ ዘውስተ ሕዝብ ለዚህም ምልክት በሕዝቡ ዘንድ ያሉ ድውያንን ሁሉ ይፈውስ ነበረ ።

፳፬ ወወፅአ ስሙዓተ ነገሩ ውስተ ኵሉ ሶርያ

፳፬ የተአምራቱ ዜና በሶርያ በ፬ቱ መዓዝን ትነገረ ።

ወአምጽኡ ኀቤሁ ኵሎ ድውያነ ወኵሎ ሕሙማነ ዘለለዚአሁ ሕማሞሙ ።
ደዌያቸው ልዩ ልዩ የሚሆን ድውያንን ወደሱ ይዘውመጡ ወጺዑራነ፤ ወእለሂ ቦሙ አጋንንት ።
የተጨነቁትን ። አጋንንት ያደሩባቸውን ። ወወርኃውያነ ፤ ሠርቀ ወርኅ እያየ የሚጥላቸውን ፡ ጨረቃ አንጂ ባታመልኩ ነው ለሚሉት ፤ አንድም ምልአተ ወርኅ ሲሆን ደም ይመላል ብርድ ብርድ ይላል ደዌ ይቀሰቅሳልና ።
ወእለሂ ነገርጋር ።

ድልስጣ የሚባል ጋኔን አለ አንድ እግሩን ወደ ላይ አንድ እግሩን ወደታች አድርጎ ሲታያቸው ይጥላቸዋልና ።
ወመፃጉዓነ ።
የጸናባቸውን ።
ወአሕየዎሙ ፤
እነዚህን ሁሉ አዳናቸው ፤

፳፭ ወተለውዎ ብዙኃን አሕዛብ እምገሊላ ወእምዓሥርቱ አህጉር ወእምኢየሩሳሌም ወእምይሁዳ ወእማዕዶተ ዮርዳኖስ ። ማር ፫ ፡ ፯ ፡ ሉቃ ፡ ፯ ፡ ፲፯ ።

፳፭ ካሥር አህጉር ከብዙ መንደር ተወጣጥተው አምስት ገባያ ያህል ሰዎች ተከተሉት ፡ ላንድ ሽማግሌ ዐሥር ልጆች ነበሩት እኒህ እየራሳቸው እንድ አንድ አገር አቅንተው ይኖሩ ነበርና ፡ አንድም ጲላጦስ ለቀረጥ ይመቸኝ ብሎ አንዱን ከተማ ካሥር ከፍሎታል ፡ ከዚህ ተወጻጽተው ተከትለውታል እነዚህም ስለ አምስት ነገር ይከተሉታል ፡ አንዱ ገባያ መልኩን እናያለን ብለው ፡ አንዱ ገበያ ኅብስት አበርክቶ ያበላናል ብለው ፡ አንዱ ገባያ ትምርቱን እንሰማለን ብለው ፡ አንዱ ገባያ ከደዌያችን ይፈውሰናል ብለው ፤ አንዱ ገባያ የአሪትን መፍረሻ የወንጌልን መታነጫ እናያለን ብለው ነው ። ለኒህም ትንቢት ተነግሮላቸዋል ተነግሮባቸዋል ። መልኩን እናያለን ላሉት ይሜኒ ላህዩ እምውሉደ ዕጓለ እመሕያው ተብሎ ፤ ኅብስት አበርክቶ ይመግበናል ላሉት ወኢያንጥእሙ እምዘፈቀዱ ተብሎ ፡ ያስተምረናል ላሉት ጥዑም ለጉርዔየ ነቢብከ ተብሎ ። ከደዌያችን ይፈውሰናል ላሉት ነሥአ ደዌነ ወጾረሕማመነ ተብሎ

የእሪትን መፍረሻ የወንጌልን መኃንሜ እናያለን ባሉት ቅንዓት እንዘሙ ለሕዝብ አብዳን ተብሎ ተነግሮባቸዋል ። እኒህንም ባምስት ነገር ይፈውሳቸዋል በሐልዮ በነቢብ በገቢረ በዘፈረ ልብስ በወራቀ ምራቅ ገቢር ክሁሉ ይገባል ።

በእንተ ብፁዓን ።

ምዕራፍ ፣ ፭ ።

፩ ወርእየ ብዙኃነ አሕዛበ ዓርገ ውስተ ደብር ወነበረ ።

፩ ወሶበ ርእየ ይላል ፣ ብዙ ሰዎችን ባየ ጊዜ ከተራራ ላይ ወጥቶ ተቀመጠ ። ሐተታ ፣ ምነው አሕዛብ አላቸው እስራኤል አይደሉም ቢሉ ብዛታቸውን ቢያይ ፣ አንድም ግብረ አሕዛብን ይሠራሉና መሾምና የገዛ ሰው ሲሰለጥ ከመርከብ ከተራራ ሁኖ ማስተማር ልማድ ነው ። መምህር ከፍ ካለ ቦታ ሰማዕያን ዝቅ ካለ ቦታ የሆኑ እንደሆነ ትምህርት ለሰማዕያን ይረዳልና ፣ ወይረድ ከመ ጠል ነቢብየ እንዲል ። አንድም በደብረ ሲና ሕገ ኦሪትን የሠራሁ እኔ ነኝ ሲል ። አንድም ልዑል ባሕርይ ነኝ ሲል ። አንድም የምሠራላችሁ ሕግ ልዕልት ናት ። እናንተም ሉዓላውያን ናችሁ ሲል ።

ወቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ። ደቀ መዛሙርቱ ወደሱ ቀረቡ ። የቀረበ ግን የራቀውም ርቆ የቀረበውም ቀርቦ ይሰማል እነዚህ ግን መደበኞች ናቸውና ትምህርት የሚቀርብ በኒህ ነውና፣ አንድም ለጉባኤውም ፍሬ አለውና ፤ ጥንተ ቀራቢች ናቸውና ቀረቡ ።

፪ ወከሠተ አፉሁ ።

፪ ነገር ጀመረ ፤ ወከሠተ አፉሁ ኢዮብ ወረገመ ለዕለት እንተ ባቲ ተወልደ ። ወከሠተ አፉሁ ጴጥሮስ ወአኀዘ ይንግሮሙ እምጥንቱ እስከ ተፍጻሜቱ ። ወከሠተ አፉሁ ፊልጶስ ወአኀዘ ይንግሮሙ በውእቱ መጽሐፍ እንዲል ።
ወመሀሮሙ እንዘ ይብል ።

እንዲህ ብሎ አስተማራቸው ፤ ሐተታ እስከ አሁን ያምስት ገብያ ሰው ይከተለው ነበር ከእንግዲህ ወዲህ በብፁዓን ዓዋጅ ይለያቸዋል ። ንጉሥ መንግሥቱ እስኪደላደልለት ድረስ ሌባ ወምበዴ ይከተለዋል ። መንግሥቱ ግን ከተደላደለ በኋላ ሌባ ወንበዴ ተለይ ብሎ ዓዋጅ እንዲነግር ፣ በብፁዓን ዓዋጅ ይለያቸዋል

፫ ብፁዓን ነዳያን በመንፈስ ። ሉቃ ፮ ፣ ፳ ።
ብፁዓን አለ ያነድዩ ርእሶሙ ይላል ።

፫ አውቀው ከብዕል ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፣ ብዕል እንጂ የእግዚአብሔር የባሕርይ ገንዘቡ ነው ለኛስ ባሕርይ የሚስማማው ንጹሕ ነው ብለው ብዕሉም እንደ ኢዮብ እንደ አብርሃም ነው አንድም ከጥበብ ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ጥበብ እንጂ የእግዚአብሔር ገንዘብ ነው ለኛስ ባሕርይ የሚስማማው ድንቁርና ነው ብለው ጥበቡም እንደ ሲራክ እንደ ሰሎሞን ነው ። አንድም ከአእምሮ ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው መኳንንት ተሰሎንቄ አፈወርቅን እንደጠየቀው ፣ ቅዱሳን ከበቁ በኋላ ከአእምሮ ነዳያን ነን ማለታቸው እንደምነው አለው ፣ አንተ በሀገርህ እንደምን ትኖራለህ አለው ፣ ከሁሉ በላይ ነኝ አለው ። እልፍ ብለህ በቂሳርያስ አለው የምበልጣቸውም አሉ ፣ የሚተካከሉኝም አሉ አለው ። እልፍ ብለህባ ቁስጥንጥንያ አለው የሚበልጡኝም አሉ የምተካከላቸውም አሉ አለው ። ዝቅ እያለ ሄደ ። እልፍ ብለህ በአንጾኪያስ አለው ። ከዚያስ እንዳልሁም እንደ ሌላሁም የሚያውቀኝ የለም አለው ። ቅዱሳንም ከአእምሮ ነዳያን ነን ማለታቸው በበላያቸው ያለውን አያዩ ነው ብሎታል ። አንድም በመማር በማርሰተማር በምናኔ በንስሐ በሃይማኖት ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው እስመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት ።

መንግሥተ ሰማያት የሳቸው ናትና ማለት መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ፣

፬ ብፁዓን እለ ይላሀው ይእዜ ።

፬ መዝ ፴፯፣፲፩ ዛሬ የሚያዝኑ የሚያለቅሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ሐተታ ፣ የሚገባ ኃዘን የማይገባ ኃዘን አለ ። የማይገባ ኃዘን እናት አባት ሞተብኝ እኅት ወንድም ዘመድ የለኝ ርስት ጉልት ሄደብኝ ብሎ ማዘን አይገባም ። እንዳባት እንደናት ሥላሴ እንደ ወንድም እንደ እኅት መላእክት አሉና እንደ ርስት እንደ ጉልት የማታልፍ ርስት ጉልት መንግሥተ ሰማይ አለችና ፣ የሚገባ ኃዘን የራሱን ኃጢአት አስቦ የባልንጀራውን ኃጢአት አይቶ ግፍዓ ሰማዕታትን ሞተ ወልደ እግዚአብሔርን አስቦ ማዘን ይገባል ። የራስን ኃጢአት እያሰቡ ማዘን እንደ አዳም እንደ ቅዱስ ጴጥሮስ እንደ ዳዊት ነው ፣ መልካቸው ሳይለወጥ ሳይሰቀቁ ዕንባቸው እንደ ሰንውኃ ይወርድ ነበር ። የባልደራውን ኃጢአት እያሰቡ ማዘን እንደ ሳሙኤል ነው እስከ ማዕዜኑ ትላህዎ ሳሙኤል ለሳኦል እስመ አነ መነንክዎ ወገደፍክዎ ። ወሶበ ርእያ ለሀገር በከየ ላዕሌሃ ወሶበ ርእየ ለዘያገብእ ተሀውከ በመንፈሱ እንዲል ፣ ግፍዓ ሰማዕታትን አስቦ ማዘን እንደ እስጢፋኖስ ። ወለእስጢፋኖስስ ነሥዕዎ ዕደው ጻድቃን ወቀበርዎ ወለሀውዎ ዓቢየ ላሐ እንዲል ። ሞተ ወልደ እግዚአብሔርን አስቦ ማሀን እንደ ዮሐንስ ነው የዕለተ ዓርብ መከራውን እያሰበ ፭ ዘመን ቈጽረ ገጽ ሁኖ ኑሯል ። አንድም ዛሬ በንስሐ የሚያለቅሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ አሙንቱ ይትፌሥሑ ፤ የኃዘን አጸፋው ደስታ ነውና ይትፌሣሑ አለ እንጂ መንግሥተ ሰማይን ይወርሳሉና ሲል ነው ።

፭ ብፁዓን የዋሀን ፤

፭ ኢሳ ፲፩፥፪ ኃደግያን በቀል የሆኑ ከየውሃት ጠባይዓዊ የደረሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። አንድም ሰውነታችንን መክረን አስተምረን ማኖር እንደምን ይቻለናል ብለው በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን የሚኖሩ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው እስመ እሙንቱ ይወርስዋ ለምድር ።

ምድር መንግሥተ ሰማይን ይወርሳሉና ። ሐተታ ምድር አሳት ይህ አልፎ በዚህ የምትተካ ስለሆነች ምድራውያን ጻድቃን የሚወርሷት ስለሆነ ። በምድር በሥሩት ሥራ የምትወረስ ስለሆነች ፣ በምድር ተድላ ሥጋ እንዲፈጸም ። በመንግሥተ ሰማይም ተድላ ነፍስ ይፈጸማልና ፣ ወሥርዓተ እግዚእነስ አሰፈወነ በብሂሎቱ ብፁዓን የዋሀን እስመ እሙንቱ ይወርስዋ ለምድር ከመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት እን ዲል ።

፮ ብፁዓን እለ ይርኅቡ ወይጸምዑ በእንተ ጽድቅ ።

፮ አብዝተንማ ከተመገብን ሰውነታችንን ወስኖ ገቶ ማኖር እንደምን ይቻለናል ብለው ከሚበሉት ከሚጠጡት ከፍለው የሚራቡ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ ዘሯ ዘያነዲ ርእሶ እምነ መባልዕት ብዙኃት ውእቱ ይክል አኒዞተ ሥጋሁ እንዲል ፤ አንድም ጨርሰንማከተመገብነ መንግሥተ ሰማያትን በምን እንዋጃታለን ብለው ከፍለው ለነዳያን ሰጥተው የሚራቡ የሚጸሙ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ አን ድም ከመብልዓ ኃጢአት የሚራቡ ከስቴ ኃጢአት የሚጸሙ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ አንድም ሰፍ ቅሩ የሚሳሱ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ጽምዓት ነፍስየ ለከ እንዲል ፤ አንድም በመማር በማስተማር በሃይማኖት በምናኔ በንስሐ የሚራቡ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ እሙንቱ ይጸግቡ ። የረኃብ አጸፋው ጽጋብ ነውና ይጸግቡ አለ እንጂ መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ሲል ነው ይጸምዑ ባለው ፀጻፋ ይረውዩ የሚል ይገኛል ።

፯ ብፁዓን መሀርያን ፤

፯ ለሰው የሚያዝኑ የሚራሩ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ሐተታ ምሕረት ሥጋዊ ምሕረት መንፈሳዊ ምሕረት ነፍሳዊ አለ ምሕረት ሥጋዊ ቀዶ ማል በሰ ቆርሶ ማጉረስ ቢበድሉ ማሩኝታ ቢበደሉ ይቅርታ ነው ምሕረት መንፈሳዊ፥ ከፉው ምግባር በጐ ምግባር መስሎት ይዞ ሲኖር መክሮ አስተምሮ ክፉውን ምግባር አስትቶ በጐውን ምግባር ማሠራት ነው ምሕረት ነፍሳዊ ከፉው ሃይማኖት በጐ ሃይማኖት መስሎት ይዞት ሲኖር ከፉውን ሃይማኖት አስትቶ በጎውን ሃይማኖት ማስያዝ ነው ፤ አንድም ምሕረት ሥጋዊ አይለወጥም ምሕረት መንፈሳዊ ከፉውን ሃይማኖት ከፉውን ምግባር በጎ ምግባር ሃይማኖት መስሎት ይዞት ሲኖር መክሮ አስተምሮ ከፉውን ሃይማኖት አስትቶ በጎውን ማስያዝ ከፉውን ምግባር አስትቶ በጎውን ማሠራት ነው ። ምሕረት ነፍሳዊ መጥዎተ ርእስ ነው ። ታሪክ እንደ አንጢሳርዮስ እንደ እሁ ቅዱስ ይህ አንጢሳርዮስ ባለጸጋ ነው ንፉግ ነው ፤ ነዳያን ሲያልፍ አይተው ይህ ጽኑ ጨካኝ ባለጸጋ ለሰው አያዝንም አሉ አንዱ እኔ ፪፫ ሰጥቶኝ በልቼ ብመጣስ ባትመጣስ ተወ ራርደው ሂዷል ምግቡን አቅርቦ እጁን ታጥቦ በሚመገብበት ጊዜ ስመ እግዚአብሔር ጠራበት እንዳ ይሰጠው ተርቧል እንዳይነሣው ስመ እግዚአብሔር ጠራበት ተናዶ ዳቦውን ወርውሮ ግንባሩን ገመሰው ደሙን አብሶ ዳቦውን ጎርሶ ለምልክት ጥቂት ይዞ ሄደ ። በዚህ ሌሊት ራእይ ያያል ነፍሱ ከሥጋው ተለይታ መላእክተ ጽልመት እያዳፉት ይዘዋት ሲሄዱ መላእክተ ብርሃን ሲከተሏት እናንተ ከዚህ ምን አላችሁ ሲሏቸው ምነው ትላንት ለድኃ ሰጥቶ የለም ይሏቸዋል መታው እንጂ መቼ ሰጠው አላ ቸው ይመበክር ተባብለው መጥተው መበከር አሉት አ ባዕል ትማልም ዘአጽገብከኒ አምጽኡከኑ ዝየ ወኢተዓውቀኒ ደም እምጽንዓ ረኃብ ብሎ መስክሮ ሲያስለቅቃት መላእክተ ብርሃን እጅ ሲያደርጓት አየ ፡ ሲነጋ በዚህ ዓለም ሳሉ በገንዘብ ቢያውቁበት እንዲህ ያለ ጥቅም አለን ብሎ ነዳያንን ሰብስቦ ያለ ገንዘቡን ጨርሶ መጽውቶ ሲሄድ ነዳያን ከመንገድ አገኙት ገንዘብ ትሰጣለህ ቢሉን መጥተን ነበር አሉት ቀደም ብላችሁ መጥታችሁ ቢሆን ከፍየ እሰጣችሁ ነበረ አሁንማ ጨርሻለሁ አላቸው፤እንደምን አንሁን አሉትእኔን ሸጣችሁ ተካፈሉ አላቸው ለ፴ ወቄት ሸጠ ውታል ፤ ከተሸጠበት አገር ከብት ያውላል ማታ የሚያልበው ደም ይሆናል በዚህ ሰው እጅ ለመረዳት አልበቃችሁም ለማለት ሲያርስ ውሎ ማታ ማሩን አለምልሞ ውኃውን አፍልቆ ይመግባቸዋል በዚህ ዕጹብ ዕጹብ ሲሉ ከተወለደ ጀምሮ ተናግሮ የማያ ውቅ ድዳ ሰምቶ የማያውቅ ደንቆሮ ነበር አፍ ቢለው ድዳው ተናግሯል ደንቆሮው ሰምቷል በዚህ ዕጹብ ዕጹብ ሲሉ ተሰውሯል ።

እኑ ቅዱስ በአሕዛብና በክርስቲያን መካከል ባለች በወሰን አገር ኤጲስቆጶስነት ተሹሞ ይኖራል። አሕዛብ ክርስቲያንን እየማረኩ ሲወስዱ ገንዘብ

እየሰጠ ይመልሳቸዋል እንዲት ድኃ ልጁዋ ተማረ ከባት መዋታ ገንዘብ ሰጠኝ አለችው ገንዘቤን ጨርሻለሁ እኔን ተከተሽ ልጅሽን መልሺ አላት ። እሱን ተከታ ልጁዋን መልሳለች ከሄደበት አገር የንጉሡ ልጅ ሞተችበት ኃዘን እንደጸናበት አይቶ ልጅህን ባነሣልህ ምን ባደረግህልኝ አለው የመንግሥቴንም እኩሌታ ቢሆን እሰጥሃለሁ አለው ይህነንስ አልሻም ከኔም አስቀድሞ ከኔም በኋላ የተማረኩትን ክርስቲያን ትሰጠኝ እንደሆነ ላሥነ ሳልህ አለው ፤ ይሁንልህ አለው እሥነ ሥ ቶሉት ከሱም አስቀድሞ ከሱም በኋላ የተማረኩትን ክርስቲያን ይዞ ወጥቷል ፤ በዚህም ጌታን መስሎ ታል ጌታ እሱ ሰው ሳይሆን ከሱ አስቀድሞ የነበ ሩትን ሰው ከሆነም በኋላ ቢኦል የወረዱትን ፩ድ ቀን በዕለተ ዓርብ ይዞ ለመውጣቱ ምሳሌ አንድም በንስሐ ለሰው የሚያዝኑ ቀሳውስት ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ ሎሙኒ ይምህርዎሙ ፤

ለሳቸውም ሥላሴ ያዝኑላቸዋል ይራሩላቸዋልና ።

፰ ብፁዓን ንጹሓን ልብ ፤ መዝ፡ ፳፫ ፤ ፬ ።

፰ ከንጹሐን ልቡና የደረሱ አንድም በንስሐ ከኃጢአት ንጹሐን የሆኑ ፣ አንድም ከቂም ከበቀል ንጹሐን የሆኑ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ እስመ ዘያነብር ቂመ ውስተ ልቡ ኢውክፍት ጸሎቱ ቅድመ እግዚአብሔር ጸሎቱ ለመስተቀይም ከመ ዘርዕ ዘወድቀ ማእከለ አሰዋክ እንዲል ።
እስመ እሙንቱ ይሬእይዎ ለእግዚአብሔር ።
ሰውነታቸው ጸርቶላቸው እግዚአብሔርን ያዩታልና እስመ በእንጽሖ መንፈስ ርእይዎ ነቢያት ለእግዚአ ብሔር ወተናጸሩ ገጸ በገጽ እንዲል ። እስካሁን ይሬእይዎ አላለ አሁን ይሬእይዎ አለ ምነው ቢሉ በኒህ ማየት የሁሉን መናገር ነው ።

፱ ብፁዓን ገባርያነ ሰላም ።

፱ አብነት እለ ይገብሩ ሰላመ ይላል ፤ አቀበ ቱን ወጥተው ቍልቍለቱን ወርደው ሰውን ከሰው ጋራ የሚያስታርቁ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ እንደ መልከ ጼዴቅ እንደ ሊቀ ሀገር የመልከ ጼዴቅ በጳው ሎስ ታውቋል፤ሊቀ ሀገር ሦስት ልጆች ነበሩት።አንተ ይህን ሥራ አንተ ይህንሥራብሎ አዝዞ እሱማን ከማን ተጣልቷል እያለ እየዞረ ሲያስታርቅ ይውል ነበር ። አንድም ሰው ሰርቆ ቀምቶ ከፈጣሪው ጋራ የሚጣላ የሚበላው የሚለብሰው እንጂ ቢያጣ ነው ብለው የሚበላውን የሚለብሰውን ሰጥተው ከእግዚአብሔር ጋራ የሚያስታርቁ ባለጠጎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው አንድም ሰውን በንስሐ ከእግዚአብሔር ጋራ የሚ ያስታርቁ ቀሳውስት ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። እስመ እሙንቱ ውሉደ እግዚአብሔር ይሰመዩ ፣

የእግዚአብሔር ልጆች ይባላሉና እስካሁን ውሉደ እግዚእብሔር አላለም አሁን እንዲህ ማለቱ ስለምን ቢሉ በመሰሉት ጌታ በመስቀል ተሰቅሎ ወደ መቃ ብር ወርዶ ሰውን ከእግዚአብሔር እንዳስታረቀ እሳቸውም አቀበቱን ወጥተው ቍልቍለቱን ወር ደው በማስታረቃቸው ይመስሉታልና በኒህ መም ሰል የሁሉንም መምሰል መናገር ነው ።

፲ ብፁዓን እለ ይሰደዱ በእንተ ጽድቅ። ፩፡ጴጥ፡ ፪ ፡ ፳
፫ ፡ ፲፬ ፬ ፡ ፲፬

፲ በመማር በማስተማር በምናኔ በንስሐ በሃይማኖት አገራቸውን ጥለው የሚሰደዱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። እስመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት

መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ፡ በመጀመሪያ ተናግሯት ውስጥ ለውስጥ ሲናገራት መጥቶ ነበርና በ፰ኛው አነሣት በመጀመሪያ ማንሣቱ ለአዳም እንደ ተሰጠች ለማጠየቅ በ፰ኛው ማንሣቱ በ፰ኛው ሽህ ለሁሉ እንድትሰጥ ለማጠየቅ ።

፲፩ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይሰድዱክሙ ።

፲፩ ከሀገራችሁ አስወጥተው ቢሰዷችሁ ንዑ ዳን ክቡራን ናችሁ ወይዘነጕጕክሙ ።
ዓብዳን ዝንጉዓን ጊጉያን ርጉማን ስሑታን ቢሏችሁ ወይነቡ ኵሎ እኩየ ላዕሌክሙ እንዘ ይሔስው በእ ንቲአየ ።
በኔ ስም ስላመናችሁ በኔ ስም ስለተጠራችሁ በኔ ስም ስላስተማራችሁ ፣ በሐሰት ክፉውን ነገር ቢናገ ሩባችሁ ።

፲፪ ተፈሥሑ ወተሐሠዩ ።

፲፪ ፈጽሞ ደስ ይበላችሁ ።

እስመ ብዙኅ እሤትክሙ በሰማያት ።
ዋጋችሁ በኔ ዘንድ ፍጹም ነውና ካሥሩ ቃላት እነጸ ጽሮ ዐሥሩን ብፁዓን ተናገረ ዐሥረኛውን በዮሐንስ ያመጣዋል ። ሙሴ ዘጠኙን ቃላት በአሪት ዘፀአት ተናግሮ ዐሥረኛውን በአሪት ዘሌዋውያን እንዳመ ጣው ።
እስመ ከማሁ ሰደድዎሙ ለነቢያት እለ እምቅድሜ ክሙ ።
ከናንተ አስቀድሞ የነበሩ ነቢያትን ከሀገራቸው አስ ወጥተው ይሰዷቸው ነበርና ፤ ይሰድዱክሙ ላለው አንድም መከራስ እንቀበል ብንል ማን አብነት ይሆነናል ትሉኝ እንደሆነ ከናንተ አስቀድሞ የነበሩ ነቢያትንም እንጂ ነቢያትንም እኮን ከሀገራቸው አስወጥተው ይሰዷቸው ነበር ፣ እኒያ አብነት ይሁኗ ዋችሁ ።
በእንተ ሐዲስ ኪዳን ተአርዮታ ምሰለ ብሊት ፣
፲፫ አንትሙ ውእቱ ጼው ለምድር ማር ፱ ፵፱
ሉቃ ፲፬ ፣ ፴፬ ።

፲፫ በዚያውም ላይ የሰው አብነቱ እናንተ ናችሁ ወእመሰ ጼው ለሐሐ በምንት እንከ ይቄሰምዎ ።

ጨው ጣዕም ባይኖረው በምን ያጣፍጡታል ፣ ራሱን አንድም አፍርጁን ሽንኩርቱን በምን ያጣፍጡታል ፤ ኢልቦኬ እንከ ዘይበቍዕ ።

የሚረባው የሚጠቅመው የለም ለአፍርጁ ለሽን ኩርቱ ፣ አንድም ለራሱ የሚያገኘው ረብሕ ጥቅም የለውም ።

ዘእንበለ ዘይገድፍዎ አፍአ ።
አፍአ አውጥተው ይጥሉታል ወይከይድዎ ሰብእ በእ ገሪሆሙ ሰዎች በእግራቸው ይጠቀጥቁታል እንጂ ፤ ሐተታ ቢከቡት ይናዳል ቢንተራሱት ራስ ይመል ጣል ከተከል ቦታ ቢያደርጉት ተክል ያደርቃል ብለው አንድም አንትሙ ውእቱ ጼው ለምድር የሰው አብነት እናንት ናችሁ ፣ እናንተ አብነት ካልሆናችሁ ማን አብነት ይሆንላችኋል ፣ አንድም ለሕዝቡ እናንተ አብነት ካልሆናችኋቸው ማን አብነት ይሆና ቸዋል ። ለሕዝቡ የምትረቧቸው የምትጠቅሟቸው የለም ። አንድም ለራሳችሁ የምታገኙት ረብሕ ጥቅም የለም ። ዘእንበለ ዘይገድፍዎ አፍአ ፣ ሕዝቡ ከልቡ ናቸው በአፍአ ያወጥዋችኋል ፣ ወይከይድዎ ። በልቡናቸው ይነቅፉችኋል እንጂ ። አንድም ሥላሴ ከመንግሥተ ሰማይ አፍአ ወደምትሆን ወደ ገሃነም ያወጧችኋል እንጂ ፤ ወይከይድዎ ፣ አጋንንትም መከራ ያጸኑባችኋል እንጂ ። በማደሪያቸው ሰብእ አላቸው ። አንድም በቱሙ ሰዎች ይጠቀጥቋችኋል ቅዱስ ጊዮርጊስ እንዳስነሣው ፍቁራ እስንሥቶ ወዴት ነበርህ ቢለው ከኤጲስ ቆጶሳችሁ ላይ ነበርሁ ብሏል

፲፬ አንትሙ ውእቱ ብርሃኑ ለዓለም ።

፲፬ አብነትነታቸው በብዙ ወገን ነውና ደገ መው ፤ የሰው አብነቱ እናንተ ናችሁ ።
ኢትክል ተከብቶ ሀገር እንተ ተሐንጸት መልዕልተ ደብር ፣ ከተራራ ላይ የተሠራች መንደር መሰወር አይቻላትም ።

፲፭ ወኢየኀትው ማኅቶተ ከመ ያንብርዋ ታሕተ ከፈር ። ማር ፬ ፣ ፳፩ ፣ ሉቃ ፣ ፰ ፣ ፲፮ ።

፲፭ አንቅብ ቅርጫት ሊደፉባት መቅረዝ የሚ ያበራ የለም ። አላ ያነብርዋ ዲበ ተቅዋማ ወታበርህ ለኵሉ እለ ውስተ ቤት ከመቅረዝ ላይ አኑረዋት ከቤት ላሉ ሁሉ ታበራ ዘንድ ነው እንጂ ።

፲፮ ከማሁ ይብራህ ብርሃንክሙ በቅድመ ሰብእ ። ፩ጴጥ ፣ ፪ ፣ ፲፪ ።

፲፮ እንዲህም ሁሉ ሥራችሁ በሰው ፊት ይሁን ከመ ይርአዩ ምግባሪክሙ ሠናየ ወይሰብሕዎ ለአቡ ክሙ ዘበሰማያት ።

በጐ ሥራችሁን አይተው ሰማያዊ አባታችሁን ያመ ሰግኑት ዘንድ እንዲህ ያሉ የትሩፋት አበጋዝ ያለነ ማልን ብለው ፣ ሐተታ ፣ ምነው በሚያመጣው ጸሊ. በኀቡእ ይል የለም ቢሉ አብነት የሚሆኑበትን ተገ ልጸው ይሠሩታል አብነት የማይሆኑበትን ተሰውረው ይሠሩታልና እንዲህ አለ ፤ አንድም በተራራ ላይ የታነጸች መንደር ልሰወር ብትል መሰወር እንዳይ ቻላት የተራራው ከፍታ እንዲገልጸት ። በመቅረዝ ላይ ያለች ፋና ልሰወር ብትል መሰወር እንዳይቻላት የመቅረዙ ከፍታ እንዲገልጻት ፤ እናንተም ሥራውን አብዝታችሁ ሥሩት ግድ በተአምራት ይገልጻችኋል ሲል ነው ። ደብር ተቅዋም አንድ ወገን ሀገር ማኅ ቶት አንድ ወገን ፣ ደብር ተቅዋም ሥጋ ሀገር ማኅቶት ነፍስ ፣ ከሥጋ ጋራ የተዋሐደች ነፍስ ሥራ ሠርታ ልትገለጽ ነው እንጂ ፣ ተሰውራ ልትቀር አይደለም አንድም ደብር ተቅዋም ሰውነት ሀገር ማኅቶት አእ ምሮ ጠባይዕ በሰውነት ያለ አእምሮ ጠባይዕ ሥራ ሠርቶ ሊገለጽ ነው እንጂ ተሰውሮ ሊቀር አይደለም አንድም ደብር ተቅዋም ሥጋ ሀገር ማኅቶት መለኮት ከሥጋ ጋራ የተዋሐደ መለኮት አስተምሮ ታምራት አድርጐ አምላክነቱን ሊገልጽ ነው እንጂ ፣ ተሰ ውሮ ሊቀር አይደለም ። አንድም ደብር ተቅዋም መስ ቀል ሀገር ማኅቶት ጌታ በመስቀል የተሰቀለ ጌታ ሙቶ ተነሥቶ አምላክነቱን ሊገልጽ ነው እንጂ ሙቶ ሊቀር አይደለም ፣ አንድም ደብር ተቅዋም አሪት ሀገር ማኅቶት ወንጌል በኦሪት ላይ የተሠራች ወንጌል ባደባባይ ተገልጻ ልትነገር ነው እንጂ ። ተሰውራ ልትቀር አይደለም ። አንድም ደብር ተቅ ዋም ሕዝቡ ሀገር ማኅቶት ኢጲስ ቆጶስ በሕዝቡ ላይ የተሾመ ኤጲስ ቆጶስ ካደባባይ ወጥቶ ጉባኤ ሰርቶ ሕዝቡን ሊያስተምር ነው እንጂ ፣ ባዳራሽ ገብቶ እልፍኝ ተከቶ ተሰውሮ ቢባላ ሲጠጣ ሊውል አይ ደለም

፲፯ ኢይምሰልክሙ ዘመጻእኩ እሥዓሮሙ ለኦሪት ወለነቢያት ፣ ብፁዓን ብፁዓን እያለ ሲያስ ተምር ሰምተው ኦሪትን ነቢያትን እንጂ ሊያሳልፋ ቸው መጥቷል እንዲሉት ዐውቆ አመጣ ። እንዲሉ ትም ዐውቆ ማምጣት ልማድ ነው ። ትውልደ አራ ዊተ ምድር ቢላቸው አብርሃምን ያህል አባት ሳለን ትውልደ አራዊተ ምድር ይለናል እንዲሉት ዐውቆ ኢይምሰልክሙ ዘታመስጡ በብሂለ አብ ብነ አብ ርሃም እንዳለ ፣ ወኢትሁቡ ለጻድቅከ ይርአይ ሙስና ሙስና ቢላቸው ይህንማ ዳዊት ለራሱ የተናገረው አይደለም እንዲሉት ዐውቆ ታበውሑነሁ እሰብእ ንንግርክሙ ከሡተ በእንተ ዳዊት ርእሰ አበው ከመሂ ሞተ ወተቀብረ ወኀቤነ ሀሎ መቃብሪሁ እስከ ዮም እንዳለ ፣ ከዚህም እንዲህ አለ ፤

፲፯ አሪትን ነቢያትን ላሳልፋቸው የመጣሁ አይምሰላችሁ ኢመጻኩ ይላል ፣ ላሳልፋቸው አል መጣሁም ።

ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ እፈጽሞሙ ።
ፍጹማን ላደርጋቸው ነው እንጂ ፤ ኢትቅትልን በኢታምዕዐ ኢትፍቱን በዘርእያ ላጸናቸው ነው እንጂ ወፈጸሙ ሕገርትዕ በሕን ትሩፋት እንዲል ።

፲፰ አማን አማን እብለከሙ እስከ አመ የሐልፍ ሰማይ ወምድር የውጣ እንተ አሐቲ ኅርመታ ወአ ሐቲ ቅርጺታ ኢተሐልፍ እምኦሪት ወእምነቢያት እስከ ሶበ ኵሉ ይትገበር ወይከውን ። ሉቃ፡፲፮፡፲፯ ።

፲፰ ሰማይ ምድር አስኪያልፍ ይህ ሁሉ እስኪ ሆን ይህ ሁሉ እስኪደረግ ድረስ ሥርዓቷ ጽፈቷ አን ዲት የምትሆን ኢትፍቱስ እንኳ ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ አታልፍም ብየ እንዳታልፍ በውነት እነግ ራችኋለሁ የድ ለአሌፍ ዐሥረኛ እንደ ሆነ ኢትፍ ቱም ለኢታምልክ ዐሥረኛ ናትና ። አንድም አሰራ ረዟ አቀራረጹዋ አንድ የምትሆን ዐሥርቱ ቃላት ሁሉ ሲያልፍ ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ እንዳታልፍ አታልፍም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ፣ በሀገራ ቸው ፲ቱ ሲሉ የውጣ ይላሉ አንዲት ጭራ ናት ዕዝል ቅጽል የላትም ። በኛም ፲ አንዲት ጭራ ናት ዕዝል ቅጥል የላትም ። አንድም ለኛ ፊደል ዐሥረኛው ተ ነው፡መስቀላዊት ሕገ ክርስቶስ ወንጌል ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ ወደሰው ልቡና አትገባም ብየ እነግራችኋለሁ ። ወኀለፈት ሰንበት እንዲል ፣ አብራ ትነገራለች እንጂ ማለት ነው ፤ ውኅጣ የሚል አብ ነት ይገኛል ። የውጣ ማለት ነው ። በዳር ሮ ሎ ብሎ ይገኛል ፡ ሮ ቢል ከመንግሥተ ሮም የምትበልጥ ሎ ቢል ልዕልት የምትሆን ወንጌል ከኦሪት ከነቢ ያት ተለይታ ወደሰው ልቡና አትገባም ብየ እን ዳትገባ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፲፱ ዘኬ ፈትሐ አሐተ እምእላ ትእዛዛት እንተ ተሐጽጽ ወይሜህር ከመዝ ለሰብእ ሕጹጸ ይከውን በመንግሥተ ሰማያት ። ያዕ፡ ፪ ፡ ፲ ።

፲፱ ካ፲ቱ ቃላት አንዲቱ ታናሽ ናት ብሎ ለራሱ የሚሠራ ለሌላው የሚያስተምር ውፁእ ሲል ነው ከመንግሥተ ሰማያት የወጣ ይሆናል ፡ መኑ አብእ ለዘ እግዚአብሔር አሕጻጾ ወሐጺ መንፈቅ ወየሐጽጾሙ እመንግሥተ አቡሁ እንዲል ፤ ወዘሰ ይገብር ወይሜህር ከመዝ ለሰብእ ውእቱ ዐቢየ ይከ ውን በመንግሥተ ሰማያት፡ከዐሥርቱ ቃላት አንዲቱ ደግ ናት ብሎ ለራሱ የሚሠራ ለሌላው የሚያስተ ምር ግን ለመንግሥተ ሰማያት ባለቤት ይሆናል ። አንድም ይከውን ሕጹጸ ፣ እንደ ጨረቃ እንደ ንኡስ ኮከብ ይሆናል ፤ ይከውን ዐቢየ እንደ ፀሐይ እንደ ዐቢይ ኮከብ ይሆናል ።

፳ ናሁ እብለከሙ ከመ ለእመ ኢፈድፈደ ጽድ ቂከሙ እምጸሐፍት ወፈሪሳውያን ኢትበውኡ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ። ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፴፱ ።

፳ ብቁሙ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ናቸው ብሎ ፣ ሥራችሁ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ሥራ ካልበለጠ ኢያፈድፈድከሙ ጽዲቀ እብዝታችሁ ሥራ ካልሠ ራችሁ መንግሥተ ሰማያት አትገቡም ብየ እንዳት ገቡ በውነት እነግራችኋለሁ ። እኒያም አልገቡ እና ንተም አትገቡ ማለት ነው ። አንድም ደጋጎች አለ አብርሃም አለ ሙሴ አለ ዳዊት ናቸው ብሎ ሊቁ ወስዶታል ብሎ በሥራ መበላለጥ ከሌለ በክብርም መበላለጥ የለም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ። ሥራው ምንድ ነው ቢሉ አፍቅሮ ጸላዕት ተዐፍዖ መል ታሕት መንኖ ጥሪት ነው ። ይህንማ እነሱስ አድር ገውት የለም ለአመ ርኢከ እድግ ፀላዒከ ዘኃየሎ ጾሩ ኢትትኃደዎ እላ እስተልፅል ምስሌሁ እንዲል ዘፀ ፳፫፡፭ ፣ አድርገውት የለም ቢሉ መጥዎተ ርእስ ነው ይህንስ አድርገውት የሰም ሙሴ እምትጥሰዮሙ ለእሉ ሕዝብከ ጠስየኒ እመጽሐፈ ሕይወትከ ብሏል ዘፀ ፴፪፡፲፩ ፣ ዳዊትሰ ምንተ ገብሩ እሉ አባግዕ እንዘ ኖላዊሆሙ አነ ዘአበስኩ ፤ ዳዕሙ ለትረድ እዴከ ላዕሌየ ወላዕለ ቤተ አቡየ ብሎ የለም ቢሉ ፣ እኒያ ለዘመዶቻቸው ነው ፤ እናንተ ግን ለሁሉ አድርጉት ሲል እኒያ አስበውት ቀርቷል እናንተ ግን አድርጉት ሲል ነው ፣ ዳግመኛ ሕግ ሁኖ ስላልተጻፈ ተጽፎ የለም ቢሉ ገብሩ ተብሎ ተጽፏል እንጂ ግብሩ ተብሎ ተጽፏልን ፤ በሥራም ካልተበላለጣችሁ ማለቱስ እንደ ምነው ቢሉ ለእኒያ አብነት አልነበራቸውም ለኒህ ግን አብነት ጌታ አላቸውና ፣ እኒያ በልጅነት አልታደሱም እኒህ ግን በልጅነት ታድሰዋልና ። ለኒያ አጋዥ አልነበራቸውም ለኒህ ግን አጋዥ ሥላሴ መላእክት መጻሕፍት መምራን አሏቸውና ።

፳፩ ሰማዕከሙ ዘተብህለ ለቀደምትከሙ ኢት ቅትል ነፍሰ ።

፳፩ ሰቀደሙ ሰዎች ነፍስ አትግደል የተባ ለውን ዘጸ ፳፡፲፫ ዘከመ ተብህለ ሎሙ እንደተባለላቸው ዘይቤልዎሙ ያሏቸውን ዘከመ ይቤልዎሙ እንዳሏቸው ሰምታች ኋል ።
ወዘሰ ቀተለ ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ።
ነፍስ የገደለ ኃጥአ ተብሎ ይፈረድበታል
የተባለውን ሰምታችኋል ።

፳፪ ወአንሰ እብለከሙ ኵሉ ዘያምዕዕ እኁዋሁ በከንቱ ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ።

፳፪ እኔ ግን ወንድሙን በከንቱ ያሳዘነ ሁሉ ኃጥአ ተብሎ ይፈረድበታል ብየ እነግራ ችኋለሁ ፤ ሐተታ ኦሪትንስ ወንጌልንስ የሠራ እሱ አይደለም እኔ ግን

ግሰቱ ሰለምን ቢሉ ጌታ ሁን እንዳሻህ ሁን እንዲሉ ይህስ በጌታ የለበትም ብሎ አሪትን በሙሴ በኢያሱ አድሮ ሠርቷታል ወንጌልን ግን እሱ ሰው ሁኖ ሠርቷታልና ፤ አንድም ለቀደሙ ሰዎች እንዲህ ብየ ነበር ዛሬ ግን እንዲህ እልሁ ። አንድም እሚሄኒ የምኒ ያን ጊዜ እንዲህ ብየ ነበር ዛሬም እንዲህ እልኩ ። በከንቱ እለ ፀ መዓት ዘበርትዕ እንዲል ፤ የሚገባ ቁጣ አለና ሕፃናት ያል ተማሩትን እንዲማሩ የተማሩትን እንዳይገድፉ መናፍቃን እንዳይሠለጥኑ ሃይማኖት እንዳይጠፉ ከሀደት እንዳይሰፋ ፥ አንድም በከንቱ ያለውን መፍ ቀርያን መዓት የጨመሩትን ነው በሐጌ መጽሐፍ ፪ ፳ ፥ ዝወርቅ ወዝ ብሩር ዘዚአየ ባለው መፍቀርያን ብሩር ወለዘፈቀድኩ እሁቦ ባለው እንደጨመሩበት ወዘሂ ይቤሎ ኀሡር ዘጸርቅ ረስሐ ።

ወንድሙን ጨርቅ ለባሽ እባተ ታናሽ ብሎ የሰደበ በደለ ፤
ወይትኴነን በዐውድ
በዐደባባይ ይፈረድበታል ።
ወዘሂ ይቤሎ ለእኁኁ ዓብድ ረስሐ ውእቱ ።
ወንድሙን ዲዳ ደንቆሮ ያለው እሱ በደለ ።
ወይትኴነን በእሳተ ገሃነም ።

በእሳተ ገሃነም ይፈረድበታል ሐተታ ወንድሙን ጨርቅ ለባሽ አባተ ታናሽ ቢለው ባደባባይ ፤ ድዳ ደንቆሮ ቢለው በገሃነም ይፈረድበታል አለ ምነው ቢሉ ፥ ከተፈጥሮተ ሥጋ ተፈጥሮተ ነፍስ እንዲበልጥ ከስድቡም ስድቧ ይበልጣልና ፥ ከፍዳውም ፍዳውን አበለጠ ፤ አንድም በዓውድ ገሃነም በገሃነም ዓውድ ያሉነው።በአክብርዎ ፍርህዎ በፍርህዎ አክብርዎ እን ዳለ ። ይህንም ሊቁ ዘሰ ፀረፈ ሳዕለ ሰብእ ጸረፈኬ ላዕለ እግዚአብሔር ብሎ ወስዶታል ። መጽሐፉን አይቶ መንቀፍ ጸሐፊውን ሕንጻውን አይቶ መንቀፍ ሐናጺውን መንቀፍ እንደሆነ ፍጥረቱንም አይቶ መንቀፍ እግዚአብሔርን መንቀፍ ነውና ።

፳፫ ወእምከመኬ ታብውእ መባእከ ውስተ ምሥ ዋዕ ወበህየ ተዘከርከ ከመ ቦ እኁከ ዘተኃየሰከ ።

፳፫ መባህን ለቤተ እግዚአብሔር በምትሰጥ በት ጊዜ አንተ ወንድምህን የነቀፍህበት ፥ ዘተኃየ ሰከ እሱ አንተን የነቀፈበት ነገር እንዳለ ብታስብ ።

፳፬ ኅድግ ህየ መባአከ ቅድመ ምሥዋዕ ።

፳፬ መባውን ከደጅ ሰሳም አኑረህ ወሑር ቅድመ ተኳነን ምስለ እኁከ ።

እስቀድመህ ከወንድምህ ተወቃቅሰህ ታረቅ ።
ወእምዝ ገቢአከ አብእ መባእከ፣ ከዚህ በኋላ ተመል ሰህ መባህን ስጥ ። ሰጥቶ ቢሄድ መባው እንኳን የገ ባልኝ እንጂ ብሎ ዕርቁ በቀረ ነበርና ፤ ይዞ ወደ ቤቱ ተመልሶ ቢሆን ዕርቁም መባውም በቀረ ነበርና ልብ እንዲቀረው ከእዳሪ እኑራሰሁ ብሎ ፈጥኖ ታርቆ እንዲመለስ እንዲህ አለ አንድም ወእምከመኬ ብለህ መልስ ጸሎት በምትጸልይበት ጊዜ የነቀፈህ ወንድ ምህ የነቀፍከው ወንድምህ እንዳለ ብታስብ ጸሎቱን ትተህ ሂድ አስቀድመህ ከወንድምህ ተወቃቅሰህ ታረቅ ከዚህ በኋላ ተመልሰህ ጸሎትህን ጸልይ ። በቂም በበቀል ሁኖ የጸለዩት አይረባም አይጠቅም ምና እስመ ዘያነብር ቂመ ውስተ ልቡ ኢውከፍት ጸሎቱ ቅድመ እግዚአብሔር ጸሎቱ ለመስተቀይም ከመ ዘርዕ ዘወድቀ ማእከለ አሰዋክ እንዲል ።

፳፭ ኩን ጠቢበ ለዕድውከ ፍጡነ እንዘ ሀሎከ ምስሌሁ ውስተ ፍኖት ።

፳፭ በመንገድ ከሱ ጋራ ሳለህ በባላጋራህ ፈጥ ነህ ዕወቅበት ታረቅ በፍኖት ብሎ በሉቃስ ያቀና ዋል ።

ከመ ኢይመጡከ ዕድውከ ለመኰንን
ባላጋራህ ለዳኛ አሳልፎ እንዳይሰጥህ ።
ወመኰንን ይሜጥወከ ለወዓሊሁ ።
ዳኛውም አሳልፎ ለሎሌው ይሰጥሃል ።
ወወእሊሁ ይሞቅሐከ ።
ሎሌውም ያግዝሃል ።

፳፮ አማን እብለከ ከመ ኢትወፅእ እምህየ እስከ ሶበ ትሜልጥ ደኃሪተ ገመስ ዘላዕሌከ ።

፳፮ ሌላው ገንዘብህስ ይቅርና ሰንኪቶ የምት ባል ቀለበትህን እስክመስጠት ደርሰህ ፤ አንድም ገመሰ ደኃሪት ይላል ፤ የታናሽ ጣትህን ቀለበት እስከ መስጠት ደርሰህ ከግዞት ቤት አትወጣም ብየ እንዳ ትወጣ በውነት እነግርሃለሁ ። አንድም ኩን ጠቢበ ብለህ መልስ በዚህ ዓለም ሳለህ በባለጋራህ በዲያብ ሎስ ዕወቅበት ። ይህን ዓለም ፍኖት አለው በመን ገድ አንዱ ሲያልፍ አንዱ ሲተርፍ እንደሆነ በዚህም ዓለም አንዱ ሲያልፍ አንዱ ሲተርፍ ነውና ። ባለ ጋራህ ዲያብሎስ ለጌታ አሳልፎ እንዳይሰጥህ ። ጌታም አሳልፎ ለዲያብሎስ ይሰጥሃል ። ዲያብሎስ ያግዝሃል ። ወዓሊሁ አለ የግድ ነው የፈቃድ አይደ ለም ። ሥራ ሠርተህ ያገኘኸው ጸጋ ክብር ይቅርና ባርባቀን ያገኘኸውን ልጅነት እስከ ማጣት ደርሰህ ከገሃነም አትወጣም ብየ እንዳትወጣ በውነት እነግ ርሃለሁ ። አንድም ፥ በዚህ ዓለም ሳለህ በባለጋ ራህ በፈቃደ ሥጋህ ፈጥነህ ዕወቅበት ። ባላጋራህ ፈቃደ ሥጋ አስፈርዶ ለጌታ እንዳይሰጥህ ። ጌታም አሳልፎ ለዲያብሎስ ይሰጥሃል ፤ ዲያብሎስ ያግዝሃል እማን እብለከ ። በነቢብ በገቢር በሠራኸው ኃጢ አት ቀርቶ በሐልዮ በሠራኸው ኃጢአት ተፈርዶብህ ከገሃነመ እሳት አትወጣም ብየ እንዳትወጣ በውነት እነግርሃለሁ ። ከሐልዮ ኃጢአት የሚነጻ አለን ቢሉ

የሚየሲዝ ሐልዮ የሚያሲዝ ሐልዮ አለ ። የሚያሲዝ ሐልዮ አሰርቃለሁ እቀማለሁ ብሎ ሂዶ ሰው ነቅቶ በት ውሻ ጩሆበት አጥር ጠንቶበት ቢመለስ ያሲዛል ፤ የማያሲዝ ሐልዮ አሰርቃለሁ እቀማለሁ ብሎ ይሄዳል ከመንገድ ሲደርስ ፈጣሪየ ቢፈርድብኝስ ብሎ የተመለሰ እንደሆነ ይህ አያሲዝም ። አንድም ሁሉም ያሲዛል ስዚህ ቅሉ ጥቂት ቀኖና ያሻዋል በሰይጣን ጻር ተወግቷልና ፣ ሁለት ሰዎች ከሰልፍ ይገባሉ ሁለቱ ሁሉ ተወግተው ይመለሳሉ አንዱ ይሞታል አንዱ ይድናል ከዳነው ላይ እትራት ይጠፋልን ፤ ይህም በአቡነ እንጦንስ ታውቋል በሚሞቱ በት ጊዜ መላእክተ ጽልመት ቀረቡ መላእክተ ብርሃን መጥተው ከዚህ ሰው ምን አላችሁ አሏቸው ፤ ምነው ያስ የሐልዮው አሏቸው ከቆብ በኋላ ነው ከቆብ በፊት አሏቸው ከቆብ በፊት ነው እንጂ ከቆብ በኋላማ በእንጦንስ ምን ተገኝቶበት አሉ ። ያማ በቆብ ታርቆበት የለም ወግዱ ብለዋቸዋል ።

፳፯ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኢትዘምው ። ዘፀ ፳ ፡ ፲፬ ።

፳፯ ለቀደሙት ሰዎች አትስሰኑ የተባለውን ሰምታችኋል ።

፳፰ ወአንሰ እብለክሙ ዙሉ ዘርእያ ለብእሲት ወፈተዋ ወድአ ዘመወ ባቲ በልቡ ።

፳፰ እኔ ግን ሴትን ያየ ሁሉ ፈጽሞ በደለ ብየ እነግራችኋለሁ ርእይን መከልከሉ ነው ቢሉ አዎን አርቆ ማጠር ነው ፤ አንድም ፈተዋ ያለውን ይሻል አይቶ ባገኘኋት ቢል ።

፳፱ እመኒ ዓይንከ ዘየማን ታስሕተከ ምልሐ ወግድፉ እምላዕሌከ ማር ፱ ፡ ፵፯ ፤ ማቴ ፲፰ ፡ ፱ ።

፳፱ ቀኝ ዓይንህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆን ብህ ካንተ አውጥተህ ጣላት ።

እስመ ይኄይሰከ ነቋረከ ትባእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት እምትባእ ውስተ እሳተ ገሃነም ምስለ ክልኤ ሆን አዕይንቲከ ፣ ዛሬ ሁለት ዓይን ኑሮህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ በዚህ ዓለም ሳለህ ከሁለት ዓይንህ አንዱ ጠፍቶ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን ስምአን ሰፉዩ እሣዕን ፤ አንዲት ሴት ወይዘሮ መጥታ ጫማ ስፋልኝ አለችው ሰፍቶ ሰጣት እየተመላለሰች አስችገረችው ጫማውን ነው ሰፍቸ ስጥቸሻለሁ ምን ያመሳልስሻል አላት ፣ ይህ ሁሉ ምክንያት ነው አንተን ብወድህ ነው አለችው በምን ነገር አላት ፣ መልክ መልካም ነህና አለችው ምኔ መልካም ነው ቢላት ሁለንተናህ መልካም ነው ይልቁንም በዓይንህ ይጸናብኛል አለችው ትወጅዋለሽ አላት አዎን አለችው ። ይህማ ምን ቁም ነገር አለው ውጎ አይደለም ብሎ በያዘው መንጉል አውጥቶ ሰጧታል።

፴ ወእመኒ እዴከ ዘየማን ታስሕተከ ምትሩ ወግድፉ እምላዕሌከ ።

፴ ቀኝ እጅህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆንብህ ቁርጠህ ጣላት ። እስመ ይኄይሰከ ይታጎጐል አሐዱ እምአባልከ እምዙሉ ሥጋከ ይትወደይ ውስተ እሳተ ገሃነም ።

በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ሳይጐል ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ጎድሎ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ። ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ። ከዚያው ግን አባስ ካህን ሮሜ አትናቴዎስ ሊቀ ጳጳሳት ዘሀገረ እንጾኪያ ፤ አባስ ካህን ሮሜ በተአምረ ማርያም ታውቋል አትናቴዎስ ሊቀ ጳጳሳት ዘአንጾኪያ ቀድሞ አረማዊ ነበረ ኋላ አምኖ ተጠምቆ ተምሮ ተሾሟል በሀገራቸው የተሾመው ፯ ቀን ቀድሶ ያቈርባል በዚያ ልማድ በመስቀል እየባረከ ሲዞር ቀድሞ በአረማዊነት ሳለ በግብር የምታውቀው ሴት መለያ ይሁነኝ ብላ እጁን ነከሰችው ጦር ተነሣበት ከዚህ ሁሉ ያደረሰችኝ ይህች እጅ አይደለችም ብሎ ከዕቃ ቤት ገብቶ እጁን ቆርጦ ጣላት ፣ አባታችን ገብተህ ቀድስልን አሉት አይቻለኝም አላቸው ። ሁለተኛ ገብተህ ቀድስ አሉት አይቻለኝም አላቸው ፣ ይህ ሰው ወደ ቀደሞ ግብሩ ተመለሰን ብለዋል ወደ እመቤታችን አመለከተ እድ ብርሀት ቀጠለችለት ገብቶ ሲቀድስ የእጁ ብርሃን እየበዘበዘ የማያሳያቸው ሆነ ወጥተው አባታችን ነገሩ ምንድነው ግለጥልን አሉት ምንጣፉን ግለጡት አላቸው ቢገልጡት ወድቃ አገኙዋት ይህች የኔ እጅ ናት ይህች እመቤታችን የሰጠችኝ ናት ብሏቸዋል ።

ወእመኒ እግርከ ዘየማን ታስሕተከ ምትራ ወግድፉ እምላዕሌከ ።

ቀኝ እግርህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆንብህ ቆርጠህ ጣላት ፤ እስመ ይኄይሰከ ይትጎጐል ፩ዱ እምአባልከ እምዙሉ ሥጋከ ይትወደይ ውስተ እሳተ ገሃነም በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ሳይጎድል ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ፤በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ጐድሎ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ። ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን አባ መርትያኖስ፡በዓቱ ከመንደር አጠገብ ነው ከበረሃ ውሎ ወደማታ ሲመለስ ዘማት ተሰብስበው እይተው ይህ መነኮስ ኃያል ጽኑዕ ነው የሚያስተው የለም አሉ ፤ አንዲቱ እኔ ባስተውስ ባታስችውስ ተባብለው ተወራርደዋል ፤ አሁን በጊዜ የሄድኩ እንደሆነ አይቀበለኝም ብላ ሲመሽ ሒዳ እጅ ጸፋች ፤ ወጥቶ ማነሽ አላት ከሩቅ አገር የመጣሁ የእግዚአብሔር እንግዳ ነኝ የምጠጋበት አጥቸ አውሬ ይጣላኛል ወምበዴ ይቀጠቅጠኛል ብየ ቁሚያለሁ አለችው አሱም በስጋበት ጻር ይነሣብኛል አይሆንም ብላት

ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክሙኒ ያለው ይፈርስብኛል እያለ ያወጣ ያወርድ ጀመረ ። ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክሙኒ ያለውስ ቢፈርስብኝ ሰፋን እታገሠዋለሁ ብሎ እሳቱን እንድዶላት እሱ አልፍ ብሎ ጸሎቱን ያዘ እቢያም የምትቀባውን ትቀባ የምታጤሰውን ታጤስ ጀመር ። መዓዛው ቢያስቸግረው እግሩን ከእሳቱ ማገዶው የአቧን መዓዛ እስኪያጠፋው እስኪለውጠው ፤ ምትሩ ያለው ለዚህ ይመቻል ፣ እቢያም እባቴ እሳበጀሁም ብላ ንስሐ ገብታለች አንድም ገልጣ እንተኛ አለችው ኢንተኛማ ካልሽ ከእሳቱ ላይ አንተኛ እላት ይህማ ይፈጀን የሰም አለችው የዚህን ዓለም እሳት ያልቻልነው የወዲያኛውንማ ዓለም እሳት እንደምን እንችለዋለን አላት አባቴ እላበጀሁም ማረኝ ብላ ንስሐ ገብታለች እሱም አመንዝቢቱ በእቱን ለቆላትጊዷል አንድም ዓይን የተባለች ሚስት ናት። ከዓይን የሚሰወር እንደሌለ ከሚስትም የሚሰወር የለምና ፣ ሚስትህ ያልሆነ ሥራ ላሠራህ ብትል ፈቃዷን አፍርስባት ዛሬ በዚህ ዓለም የሚስትህን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ በዚህ ዓለም የሚስትህን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፣ እጅ የተባሉ ልጆች ናቸው ወድቆ ይነሡ በእጅ ዜግቶ ይከብሩ በልጅ እንዲሉ ። ልጆችህ ያልሆነ ሥራ እና ሠራህ ቢሉ ፈቃዳቸውን አፍርስባቸው ፣ በዚህ ዓለም የልጆችህን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ፤ በዚህ ዓለም የልጆችህን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና እግር የተባሉ ቤተሰብእ ናቸው ቤተሰቦችህ ምክንያተ ስሕተት ሁነው ያልሆነ ሥራ እናሠራህ ቢሉ ፈቃዳቸውን አፍርስባቸው ፣ በዚህ ዓለም የእሳቸውን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም እሳት ከምትገባ ፣ በዚህ ዓለም ፈቃዳቸውን አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ አንድም አንዳይንህ እንደ እጅህ እንደ እግርህ የምትወደው ወዳጅህ ያልሆነ ሥራ አሠራሃለሁ ቢልህ ፈቃዱን አፍርስበት በዚህ ዓለም የሱን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ ። በዚህ ዓለም የሱን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ አንድም ምድራውያን ነገሥታት ዓይን በፍላት እጅ እግር በሰለት ፣ እንዲቀጹ ሌዋውያን ካህናት ዓይንን በእንቃዕድዎ እጅን በሰፊህ ፤ እግርን በቀዊም ፣ ሠርተው ቀጽተው እንዲኖሩ ፤ አንተም ዓይንህን በእንቃዕድዎ እጅህን በሰፊህ እግርህን በቀዊም ሥራ ቅጻ ።

፴፩ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ዙሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ይጽሐፍ ላቲ መጽሐፈ ሕዳጋታሃ ወየሀባ ። ዘዳ ፳፬፥ ፩ ማቴ ፲፱፥፯፥፱ ማር ፲፬፥፲፪ ሉቃ ፲፯ ፣ ፲፰ ፣ ፩ ቆሮ ፯ ፣ ፲ ።

፴፩ ከናንት አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች ሚስቱን የሚፈታ ሰው ሁሉ የምትፈታበትን ነውር የሚናገር ደብዳቤ ጽፎ ሰጥቶ ይፍታት የተባለላቸውን ሰምታችኋል ፣ እንዳለፈው በል ።

፴፪ አንሰኬ እብለክሙ ኪሙ ዙሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ በላዕሌሁ ለሊሁ ረሰያ ዘማ

፴፪ እኔ ግን ሳትሰስንበት ሰነፈች ደረቀች ብሎ ሚስቱን የፈታ ሰው ሁሉ ዘማ አሰኛት ብየ እነግራችኋለሁ ።

ወዘሂ አውሰበ ኅድግተ ዘመወ በነውር የተፈታችውን ያገባ በደለ ፣ በምን ያውቀዋል ቢሉ አበውን ዕጨጌ ይፍቱኝ ባለማለቷ ፣ ኋላ እንደምን ትሁን ቢሉ የፍርድ መጽሐፍ በጉጉዓ ብሎ ወስዶታል ። ንስሐ መግባቷን መምህረ ንስሐዋ ጉረቤቶቿ መስክረውላት ታግባ ብዓል ። አንድም ሰማዕክሙ ብሰሀ መልስ ። አሪትን የሚተው ሰው ሁሉ ወንጌልን ተክቶ ይተው የወንጌልን ሥራ ላይሠራ ግን አሪትን የተወ ሰው ወንጌልን ኃላፊት ሕግ አደረጋት ። ከተዋትም በኋላ ወደ አሪት ቢመለስ በደለ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል አንድም መልስ ይህን ዓለም የሚተው ሰው ሁሉ መንግሥተ ሰማያትን ተክቶ ይተው ። የምናኔ ሥራ ይሥራ ። ወአንሰ እብለክሙ ፤ የምናኔ ሥራ ሳይሠራ ይህን ዓለም ተውሁ የሚል ሰው ግን መንግሥተ ሰማያትን ኃላፊት ርስት አደረጋት ። ከመነነም በኋላ ወደኋላም ቢመለስ በደለ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል።

፴፫ መከዕበ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምት በሙ ኢትምሐሉ በሐሰት ፣ ወባሕቱ አግብኡ መሐላክሙ ለእግዚአብሔር ። ዘሌዋ ፲፱፥፲፪ ዘፀ ፳፥፯ ዘዳ ፳፫፥፳፩ ያዕ ፭፥፲፪፣

፴፫ ለቀደሙ ሰዎች በእውነት እንጂ በሐሰት በስመ እግዚአብሔር እንጂ በስመ ጣዖት ዳኛ ፈርዶባችሁ ባለጋራ አውርዶላችሁ እንጂ ዳኛ ሳይፈርድባችሁ ባለጋራ ሳያወርድላችሁ አትማሉ ያሏቸውን ሰምታችኋል ።

፴፬ ወአንሰ እብለክሙ ኢትምሐሉ ግሙራ ።

፴፬ እኔ ግን ፈጽማችሁ አትማሉ እላችኋለሁ ኢበሰማይ ።
በሰማይም ሁኖ ከሰማይ የመጣ መቅሠፍት አይላተን ሰማይ ተንዶ ይጫነን እያሉ ይምላሉና ፣ እስመ መንበሩ ለእግዚአብሔር ውእቱ ።
የእግዚአብሔር ዙፋኑ ነውና ።
ወኢበምድር ።

በምድርም ሁኖ ምድር ይክዳን ምድር ተከፍቶ ይዋጠን እያሉ ይምላሉና ።
እስመ መከየደ እገሪሁ ይእቲ ፣
መመላለሻው ናትና ።

ግሣጼ ሰሎሞን ታውቋል ። ይህስ እዝራ ነሥኦን ወኢ ስተጋብኦን ይለዋል ብሎ ተናግሮት ሳይጻፍ የቀረ ነው ። ተናግረውት የቅረውን ማምጣት ለሐዋርያት ልማድ ነው ። ተዓቀቡ በመዋዕለ አፅራር ያለውን በከመ ይቤ ኢዮብ እንዳሉ እንደ ናዝራዊ እንደ ሶምሶን ይባላል ተብሎ በነቢይ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ በናዝሬት ኖረ ፣ አንድም በአራቱ እስመ ናዝራዊ ሐዲስ ውእቱ ለእግዚአብሔር ያለውን አን ዲህ ለውጦ አንፅበው ፣ ይህንግ የተናገረ መልአክ አይደለም ሰለምን ነቢይ አለው ቢሉ ፣ መልአክ ይሰመይ በእንተ ተልእኮቱ ወሐዋርያ ይሰመይ በእ ንተ ሐዊሮቱ እንዲል ፣ ከዚያ በግብሩ መልአክ እንደ አለው ከዚህም በግብሩ ነቢይ አለው ። ያውስ ቢሆን ይህ የተነገረ ለሶምሶን አይደለምን ቢሉ ፣ ለጊዜው ለሶምሶን ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ ነውና ፣ አነ እከውኖ አባሁ ወውእቱ ይከውነኒ ወልድየ ያለው ለጊዜው ለሰሎሞን ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ እንደ ሆነ ያውስ ቢሆን በምን ይመስለዋልና አን ዲህ አለ ቢሉ ፣ ሶምሶን በተናቀች መንሰከ አድግ ጠላቶቹን እንዳጠፋ ጌታም አይሁድ አጋንንት መና ፍቃን በናቁት ሞቱ ሞትን አጥፍቷልና ። ሶምሶን በሕይወተ ሥጋ ሳለ ካጠፋቸው አሕዛብ በሞቱ ያጠፋቸው ይበዛሉና ፣ ጌታም በሕይወተ ሥጋ ሳለ ካጠፋቸው አጋንንት በሞቱ ያጠፋቸው ይበዛሉና ። አንድም ከመ ናዝራዊ ይሰመይ ብለህ ናዝሬት ማለት ፍልጠት ክፍለት ማለት ነው ። ልጁ ልዩ ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ ። ዘተብህለ በነቢ ቢይ ስሙ ለልዑል ቅዱስ ቅዱሳን ወይትቀባዕ ቅዱስ ቅዱሳን ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ አን ድም ናዝሬት ማለት ኀሥርት ማለት ነው ፣ ይእተ አሚረ ይሰምያ ለናዝሬት በስመ ኃማር እንዲል ። ልጁ ኀሡር ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ እልህን ሡር እንዲል በዓረብ ኀሡር ቢል ፣ አንድም ናዝሬት ማለት አጽቀ ጽጌ ማለት ነው ልጁ አጽ ቅያዊ ጽጌያዊ ይባል ዘንድ ናዝሬት ገብቶ ኖረ ። እሱ እኁዱ ጕንድ ኖሁ ምእመናንን እንደ አዕጹቅ እንደ ጽጌያት አድርጎ ያስገኛልና ፣ ያው ግን በነ ቢይ ቃል ትወፅእ በትር እምሥርወ ዕሤይ ወየዓርግ ጽጌ እምጕንዱ ተብሎ የተነገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ።

በእንተ ስብከተ ዮሐንስ ።

ምዕራፍ ፫ ፡

፩ ወበውእቱ መዋዕል በጽሐ ዮሐንስ መጥምቅ እንዘ ይሰብክ በገዳመ ይሁዳ ዘዮርዳኖስ ፣

፩ ከመ ናዝራዊ ይሰመይ ወልድየ ብሎ ነበ ርና ናዝራዊ በተባለበት ወራት ፣ ቦአ ናዝሬት ብሎ ነበርና ናዝሬት በገባበት ወራት ፣ ሃያ አምስቱን ዘመን እንድ ወዓን አድርጎ ወበውእቱ መዋዕል አለ ወዮሐንስ አርባውን ቀን እንዳንድ ቀን አድርጎ ወእመ ሳኒታ እንዳለ ። አንድም ወተወልደ ብሎ ነበርና ሥጋ በሆነበት ወራት ። አንድም ለዮሐንስ ሠላሳ ሲመላው ለጌታ መንፈቅ ሲቀረው በዚያ ወራት የዮርዳኖስ አውራጃ በምትሆን በይሁዳ ምድረ በዳ ዮሐንስ መጥምቅ ሲያስተምር ደረሰ ፣ በገዳም አለ ቤታው ነውና አንድም በገዳም ዕንጨት በዓቴ ውኃ ቀጂ አይታጣምና ፣ አንድም በገዳም ጾር ይቀ ላል ለወጣንያን አብነት ለመሆን በገዳም ጾር ይጸናል ለፍጹማን አብነት ለመሆን ፤ አንድም ገዳም የአይ ሁድ ልቡና ነው ። በገዳም እፀል ተክል እንዳይገኝ በአይሁድም ልቡና ምግባር ሃይማኖት አይገኝምና እንድም ኢሳይያስ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ብሎ የተናገረልኝ እኔ ነኝ ሲል ።

፪ እንዘ ይብል ነስሑ እስመ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ፣ ማር ፩ ፡ ፪ ፣ ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፫ ።

፪ መንግሥተ ሰማያት በልጅነት ልጅነት በሃ ይማኖት ልትሰጥ ቀርባለችና እመኑ እያለ ሲያስተ ምር ደረሰ ።

፫ እስመ ዝንቱ ውእቱ ዘተብህለ በኢሳይያስ ነቢይ እንዘ ይብል ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ። ኢሳ ፡ ፵ ፡ ፫ ። ማር ፡ ፩ ፡ ፫ ። ሉቃ ፡ ፫ ፤ ፬ ።

፫ ፤ በገዳም የሚያስተምር ዐዋጅ ነጋሪ ተብሎ በኢሳይያስ ቃል የተነገረለት ይህ ዮሐንስ ነውና ቃለ ዐዐዋዲ ፣ አዕዋዴ ቃል ይላል ትምህርቱን ከዚ ያም ከዚያም የሚያደርስ ማለት ነው ቃል ዓዋዲ ይላል ። ይህንንም ቃል ዘይኬልሀ በገዳም ብሎ ሊቁ ወስዶታል ።

ወይብል ጺሑ ፍኖቶ ለእግዚአብሔር ፤ የእግዚአብሔርን መንገድ ጽረጉ ። ወርቱዕ ግበሩ መጸያሕቶ ።

ጽርጊያውን የቀና አድርጉ እያለ ሲያስተምር ደረሰ ሐተታ ፤ ንጉሥ በመጣ ጊዜ ተራራው ድረብ ታው ተንዶ ጕድጓዳው መልቶ ሥሩ ተነቅሎ ደን ጊያው ተሰቅጦ ለፈረስ ለሠረገላ እንዲመች ተደ ልድሎ ይቆያልና በዚያ ግሥ ተናገረው ። የእግዚ አብሔር ማደሪያ ሰውነታችሁን ከኃጢአት ከጣእት ንጹሕ አድርጉ ።

፬ ወልብሱ ለዮሐንስ ኮነ እምፀጕረ ገመል ፤ ዮሐንስማ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ ካፓ ሳንቃ ያልብሱኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደሆነ ፣ ይህ ለሥጋውያን ነው ። እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና

፬ ይህን አይሻም ፤ ዮሐንስስ የሚለብሰው የገመል ጠጕር ነበር ። ሐተታ የገመል ምን ጠጕር አላትና ቢሉ ከጋማዋ ከጅራቷ ቢፈልጉ አይታጣም

ልብሱን ሲል ወምበዴ ይጣሳዋል ብላ እናቱ ያንን አሥርታ አልብሳው ነበር ፣ አንድም ገመል በቀለኛ ናት አጥብቆ የመታትን እስከ ፯ እስከ ፯ ዓመት አት ዘነጋም ባጥብላ ትረግጠዋለች ሥፍራ ሲመቻት ገደል ገፍታ ትጥለዋለች ። እሱም ወይወድይዎሙ ውስተ እቶነ እሳት የምትል ሕገ በቀል ወንጌልን አስተም ራለሁ ሲል ። አንድም ገመል ሁለት ግብር አላት ። የሚበላና የማይበላ እንደ ላምና እንደ በሬ ምንዛሪ ታወጣለች እንደ ፈረስ እንደ በቅሎ ለኮናዋ ጽፋቅ ነው ። እስመ ገመል ጽፋቅ ለኮናሁ ወያመስኩዕ እንዲል ። እሱም ሕገ አሕዛብ ወሕዝብ ወንጌልን አስተምራለሁ ሲል ፣ አንድምገመሎ የሚባል ዕፅ አለ ቆርጠው አድርቀው ከባሕር የጣሉት እንደ ሆነ ጭረት ይወጣዋል ያንን ታትታ አልብሳዋለች ለጊዜው ኑሮው በገዳም ነውና ልብሱን ሲል ወም በዴ እንዳይጣሳው ነው ። ፍጻሜው ግን ለምእመናን አብነት ለመሆን ተርታ ልብስ ለብሳችሁ አልባሌ መስላችሁ ኑሩ ለማለት ።

ወቅናቱ ዘአዲም ውስተ ሐቌሁ ዮሐንስማ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ የወርቅ ዝናር ያስ ታጥቁኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደሆነ ። ይህ ለሥጋው ያን ነው ። እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና ይኸን አይ ሻም ። እሱስ ወገቡን የሚታጠቅበት ዓረብ ነበር ፣ ያ ከደመ ነፍስ የተለየ እንደሆነ ፣ እሱም ከሥጋዊ ከደማዊ ግብር ልዩ ነኝ ሲል ፣ ይኸን አስቀድሞ ከደመ ነፍስ ይለዩታል ከወኃ ይነከሩታል ኋላ ጢጉሩን ይመልጡታል ያስፉታል ቀለም ያገቡታል ፣ ከደመ ነፍስ እንዲለዩት መክር አስተምሮ ከሥጋዊ ከደማዊ ግብር ይለያቸዋል ፣ ከውኃ እንደ መንከር ያጠምቃቸዋል ያስተምራቸዋል እንደ ማልፋት ምግ ባር ሃይማኖት ያሠራቸዋል ቀለም እንደ ማግባት ጸጋ ክብር ያሰጣቸዋል ዮሐንስ ግን እንዲህ ማድረጉ ፍትወት እንስሳዊት ሠባሕርዩ እያለች በገቢር እን ዳላወረዳት ያጠይቃል ።

ወሲሳዩ አንበጣ ወመዓረ ገዳም ዮሐንስማ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ነገሥታት እንጂ ጣዐ ጋዐዶሮ ስቅ ስቆ ያብሉኝ ብሎ ነው ትሉኝ እንደ ሆነ ይህ ለሥጋ ውያን ነው ፣ እሱ ግን መንፈሳዊ ነውና ይህን አይ ሻም ምግቡም አንበጣ የሚባል ቅጠል ደቂቦ ጨው ነስንሶ ነበር ፣ አንድም አንበጣ በልሳነ አቴና ቀም ሲስ ይለዋል በኛም ሰበቦት የጋጃ ማ ይባላል ። ወመዓረ ገዳም አለ ። የማንግር ይሏል ፣ አንድም አንበጣ ይላል በቁሙ አንበጣውን ይበላው ነበር ፤ በዐረቡ እልጅራድ ይላል አንበጣ ሲል ፣ ሐተታ ፣ በዘመኑዋ እያሉ እንድታልፍ ለማጠየቅ አሪትን አይጠብቋትም ነበር።በ፫ ቀን ግዘሩ የምትለውን ኢያሱ በ፵ ዘመን ገዝሯል ። ሶምሶን ከአፈ አን በሳ መዓር አግኝቶ ተመግቧል ከመንስከ አድግ ውኃ ጠጥቷል ። ኤልያስም በአፈ ቋዕ ሥጋ እየመ ጣለት ይበላ ነበር ፣ ዮሐንስም በቁሙ አንበጣውን ይበላው ነበር ። ወመዓረ ገዳም ባለው ወመዓረ ጸደና ይላል ፣ የጣዝማ ማር ፣ ይህንም ሊቁ ጸንበጣ ዘይቤ ልዕልና ስብከቱ ይእቲ ፣ መዓር ዘይቤ ጣዕመ ስብከቱ ይእቲ ብሎ ተርጕሞታል ።

፭ ወየሐውሩ ኀቤሁ ኵሎሙ ሰብእ ይሁዳ ወኢ የሩሳሌም ወኵሉ እድያሚሃ ለዮርዳኖስ ።
ማር ፩ ፣ ፭ ።

በኢየሩሳሌም በይሁዳ በዮርዳኖስ አውራጃ ያሉ ሰዎች ሁሉ ከሱ ዘንድ እየሄዱ ፣

፮ ወያጠምቆሙ ለኵሎሙ በፈለገ ዮርዳኖስ እንዘ ይትአመኑ ኃጣውኢሆሙ ።

፮ ኃጢአታቸውን እየነገሩት በዮርዳኖስ ያጠ ቃቸው ነበር ። እገሌ ተጠመቅ በማየ ንስሐ ከመ ትኩን ረድአ ለክርስቶስ እያለ ፤ ሐተታ ፣ ጥምቀት ከሦስት ወገን ነው ። መዝገበ ውሉድ ፍቁራን የም ትባል የጌታ ጥምቀት ፣ ጥምቀት ዮሐንስ ጥምቀተ አይሁድ ፣ ጥምቀተ አይሁድና ጥምቀተ ዮሐንስማ አንድ አይሆኑም ሁሉም ልጅነት አያስጥ ቢሉ አንድ አይደለም ከሰውነታቸው ሰውነቱ እንዲበልጥ ፣ ከጥምቀታቸውም ጥምቀቱ ይበልጣል ። አንድም ፫ ወገን ነው ፩ቱ ምሳሌ ፩ቱ አማናዊ ፣ ምሳሌ አጥ መቃ ለምድር በማየ አይህ ፣ ወለኵሎሙ አበዊነ አጥመቆሙ ሙሴ በደመና ወበባሕር ፣ ወተጠምቃ እገሪሆሙ ለካህናት ያለው ፤ ጥምቀተ ዮሐንስ ፤ ይህ ምሳሌ ነው ። አራቱ አማናዊ መዝገበ ውሉድ ፍቁራን የምትባል የጌታ ጥምቀት አንብዓ ንስሐ፣ ደመ ሰማዕት ባሕረ እሳት ።

፯ ወሶበ ርእየ ብዙኀነ እሕዛበ እምፈሪሳው ያን ወሰዱቃውያን እንዘ ይመጽኡ ውስተ ጥምቀቱ ጽሚተ ። ሉቃ ፫ ፣ ፯ ።

፯ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ወገን ብዙ ሰዎች ጻድቃን መስለው ኃጢአታቸውን ሰውረው አል ባሌ መስለው ተርታ ልብስ ለብሰው የኦሪትን መፍ ረሻ የወንጌልን መታነሚ እናያለን ብለው እሱ ወደሚያጠምቅበት ሲመጡ ባየ ጊዜ ፣ ሐተታ ፣ እሥራኤል አይደለም ስለምን እሕዛብ አላቸው ቢሉ ስለብዛታቸው ፣ አንድም በጺያፍ የገባ ግብረ አሕ ዛብ ይሠራሉና ፣ ባባታቸው በፋሬስ ፈረሳውያን በሳዶቅ ሰዱቃውያን ተብለዋል ባባትም ስም መጠራት ልማድ ነው ። በዔቦር ዕብራውያን በይሁዳ አይሁድ እንደ ተባሉ ።

ወይቤሎሙ እ ትውልደ አራዊተ ምድር መኑ አመ ረከሙ ትጕየዩ እመቅሠፍት ወእመንሱት ዘይመ ጽእ ።

እናንተ የፍኝት እባብ ልጆች በነፍስ በሥጋ ከሚመጣው መከራ ትድኑ ዘንድ ማን ነገራችሁ ። እመ ቅሠፍት ወእመንሱት ወእመዓት ዘይመጽእ ይላል ። በጥፆስ በሐሳዌ መሢሕ በምጽዓት ከሚመጣው መከራ ትድኑ ዘንድ ማን ነገራችሁ ። ሊማሩለት እንዳልመጡ ያውቃ የለምን ቢሉ የማይጠቀም ከጉባዔው አይመጣምና እንድም የሹም ስንፍ ባይለፈልፍ እንዲሉ ፤ ንግር ወኢታርምም ብሎታልና ። አባቶቻቸው ወደው ባወጡት ስም ትውልደ አራዊተ ምድር አላቸው ። ወንድማቸውን የቤፍን ሽጠው በልተው እኩይ አርዌ በልዖ ብለው ነበርና ። ትውልደ አራዊተ ምድር ያላት አርዌ ገሞራዊት ናት አፈ ማኅፀኑዋ ጠባብ ነው ዘሩን ባፏ ትቀበለዋለች አፃለ ዘሩን ቆርጣ ታስቀረዋለች ። በፅንስ ጊዜ አባት ይሞታል በሚወለዱበትም ጊዜ አፈ ማኅፀኑዋ ጠባብ ነውና ሥጋዋን በልተው ሆዷን ቀደው ይወጣሉ ፣ በዚህ ጊዜ እናት ትሞታለች እኒህም እንዳባት የሚሆኑዋቸውን ነቢያትን እንደ እናት የሚሆኑዋቸው ሐዋርያትን ገድለዋልና ። ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም እንተ ትቀትሎሙ ለነቢያት ወትዌግሮሙ ለሐዋርያት እለ ተፈነው ኀቤየ ብሎ እንዲያመጣው

፰ ግበሩኬ እንከ ፍሬ ሥርናየ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ።

፰ ከእንግዲህስ ወዲህ ለማመን የሚያበቃች ሁን ሥራ ሥሩ ።

፱ ወኢይምሰልክሙ ዘታመሥጠሩ በብሂለ ዘትብሉ አብ ብነ አብርሃም ፤ ዮሐ ፡ ፰ ፣ ፴፱ ።

፱ አብርሃምን ያህል አባት ሳለን ትውልደ አራዊት ምድር ይለናል በማለት ትውልደ አራዊተ ምድር ከመባል የምትድኑ አይምስላችሁ ፣ እንዲሉት ዐውቆ አመጣ ኸንዲሉትም ዐውቆ ማምጣት ልማድ ነው ። ብጹዓን ብጹዓን እያለ ሲያስተምር ሰምተው አሪትን ነቢያትን ሲያሳልፋቸው መጥቷል እንዲሉት ዐውቆ ኢይምሰልክሙ ዘመጻእኩ እስዓሮሙ ለኦሪት ወነቢያት ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ እፈጽሞሙ እንዳለ ። ወኢትሁብ ለጻድቅከ ይርአይ ሙስና ቢላቸው ፣ ይህንማ ዳዊት የተናገረው ስራሱ አይደለም እንዲሉት ዐውቆ ታበውሁ ነሁ እ ስብእ ንንግርክሙ ክሡተ በእንተ ዳዊት ርእስ አበው ቀደምት ከመሂ ሞተ ወተቀብረ እንዳለ ከዚህም እንዲህ አለ ።

እብለክሙ ከመ ይክል እግዚአብሔር እምእላንቱ እዕባን አንሥአ ውሉድ ለአብርሃም ፣ እግዚአብሔር ለአብርሃም ከነዚህ ከአሕዛብ ልጅ ማሥነሣት አቅሞ ውሉድ ይላል መተካት እንዲቻለው ይቻለዋል ብየ እነግራችኋለሁ ፣ አንሥአ ውሉድ አንሥአ ውሉደ ይላል ። እላንቱ አላቸው አሁን ያሉ በመካከል ነውና ኋላ ብሔረ ጌርጌሴን ገባ ብሎ እንዲያመጣቸው ፣ እዕባን አላቸው ደንጊያ ያመልኩሉና ፤ አንድም ይቡስ ነው ይቡሳን አእምሮ ናቸውና ፣ ቆሪር ነው ፣ ቆሪራን አእምሮ ናቸውና ፣ ክቡድ ነው ክቡዳን አእምሮ ናቸውና ።

፲ እስመ ናሁ ተሠይመ ማሕጼ ውስተ ጕንደ ዕፀው ይጓበር ፤

፲ ምሳር ዓፅቁን ከግንዱ ሊለይ ተቃቷልና ፣ ማለት የናንተን ልጅነት ከአብርሃም አባትነት ሊለይ ሥልጣነ እግዚአብሔር ተቃጥቷልና ኢይምሰልክሙ በብሂለ ዘትብሉ ላለው ፤ ወንጌል ሕገ አሕዛብ ወሕዝብ ሁና ተሠርታለችና ፣ እብለክሙ ከመ እግዚአብሔር ይክል አንሥአ ውሉድ ላለው ፣ መስኮት ከሥጋ ተዋሕዷልና መኑ አመረክሙ ላለው ከፉውን ሕሊና ከበጎ ሕሊና ሊለይ ሥልጣን ከህነት ተቃጥቷልና ግበሩኬ እንከ ፍሬ ሠናየ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ላለው ፣

ዙሉኬ ዕፅ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይገዘምዎ ወውስተ እሳት ይወድይዎ ።

በጎ ፍሬ የማያፈራውን ዕፅ ሁሉ ይቆርጡታል በእሳት ያቃጥሉታል ፣ በኔ ትምህርት አምኖ በጎ ሥራ የማይሠራውን ሰው ሁሉ ነፍሱን ከሥጋው ይለዩታል በገሃነም ሥቃይ ያመጡበታል ።

፲፮ እንስኬ አጠምቀክሙ በማይ ለንስሐ ፤ ማር ፩ ፰፣ ሉቃ ፫፣፲፯ ዮሐ ፩፣፳፮ ግብ ሐ ፩፣፭። በዚህ ያልተደ ያዘ ቢሉታብ የቴያያዘ ነው ባለጸጎች መጥተው ምንተ ንግበር አሉት ፣ ዘቦ ፪ኤ ክዳናት የሀብ ፩ደ ለዘአልቦቱ ወዘሂ ቦ እክል ከማሁ ይግበር አላቸው ፣ ኃጥአን መጸብሐን መጥተው ምንተ ንግበር አሉት ። አልቦ ፍድፋዴ ዘትገብሩ እምዘተአዘዝክሙ አላቸው አንበሳ ወደቅ የወርቅ ተኩስ የግምጃው መክንጃ የላሙን መንጃ እያሉ የሚወስዱት አላቸውና ፣ የደል ጭፍራ መጥተው ምንተ ንግበር አሉት ፤ ኢትግፍዑ ወኢትሂዱ መነሂ አላ ንበሩ በበሲሳይክሙ አላቸው ዮሐንስ እንዲህ ብሎ ማስተማሩ ክርስቶስ እንጂ ቢሆን ነው ብለዋል እኔስ ለጸጅ ቢረሱን

፲፮ ስልብዉ ገላን እንዲያጸፁለት ስሉ ጥምቀት በሚያበቃ ጥምቀት አጠምቃችኋለሁ ስሉ ተአምምኖ ጣውእ በሚያበቃ ተእምኖ ኃጣውእ እስተምራችኋለሁ እንጂ ክርስቶስ አይደለሁም ።

ወዘይመጽእ እምድኅሬየ ውእቱ ይጸንዕ እምኔየ ። ከኔ በኋላ የሚመጣው እሱ ከኔ አስቀድሞ የነበረው ነው አለ ። የባሕርይ አምላክ ነው ።

ዘኢይደልወኒ እጹር ዓሣዕኖ ። ጫማውን ልይዝ የማይገባኝ ። ሐተታ ፤ የንጉሥን የንግሥትን ጫማ ትቢቃለህ ያላሉት ሰው አይዝምና ።

እንደም ዓሕርዩን ልመረምር ከማይቻለኝ ፤ እንድም ፣ እሱ ከሚያደርገው ከታምራቱ ከትሩፋቱ አንዱን ሳደርግ ከማይቻለኝ ፣ እንድም አግዕነ መርገምን ከምእመናን ለአንዱ አርቅለት ዘንድ ከማይቻለኝ ከኔ አስቀድሞ የነበረ ነው ።

ውእቱስ ያጠምቀክሙ በመንፈስ ቅዱስ ወበእሳት ፤ እሱ ግን በጀ ብትሉ በመንፈስ ቅዱስ በጀ ባትሉ በገሃነመ እሳት ያጠምቃችኋል ፤ ሞገሥ ምድር ይእቲ አንተ ኢትመልዕ ማየ እንዲል ፤ አንድም በመንፈስ ቅዱስ እሳትነት ያጠምቃችኋል ። ሐተታ ፣ መንፈስ ቅዱስን እሳት አለው ፣ እሳት ምሉእ ነው፣ መንፈስ ቅዱስም ምሉእ ነውና ፣ እሳት በምልአት ሳለበሳድ ካልመቱ አይገለጽም ። መንፈስ ቅዱስም ቋንቋ ሲያናግር ምሥጢር ሲያስተረጉም እንጅ አድሮ ሳለ አይታወቅምና ፣ እሳት ከቡላዱ ሲወጣ በመጠን ነው ኋላ በዕንጨት እያቀጣጠሉ ያሰፉታል መንፈስ ቅዱስም በጥምቀት ሲሰጥ በመጠን ነው። ኋላ በሥራ ያሰፉታልና እሳት ጣዕምን መዓዛን ያመጸል ፣ መንፈስ ቅዱስም ጣዕመ ጸጋን መዓዛ ጸጋን ያመጣልና፣እሳት በመጠን ቢሞቁት ሕይወት ይሆናል ። ከመጠን ወጥቶ የሞቁት እንደሆነ ግን ያቃጥላል ። መንፈስ ቅዱስም በሚገባ በተጻፈው የመረመሩት እንደሆነ ሕይወት ይሆናል ፤ በማይገባ ከተጻፈው ወጥቶ የመረመሩት እንደሆነ ግን ይቀስፋልና እሳት በሳኢ ለዓማፅያን ለእለ ይክህዱ ስሞ ወእሳት ማሕየዊ ለርቱዓነ ልብ ለእለ ይገብሩ ፈቃዶ እንዲል ፤ እሳት ያቀረቡለትን ሁሉ ያቃጥላል መንፈስ ቅዱስም ሕዝብ አሕዛብ የጸለዩትን ጸሎት ያቀረቡትን መሥዋዕት ይቀበላልና ፣ እሳት ወኃ ገደል ካልከለከለው ሁሉን ሳጥፋ ቢል ይቻለዋል ። መንፈስ ቅዱስም ቸርነቱ ካልከለከለው ሁሉን ሳጥፋ ቢል ይቻለዋልና እሳት ዱር ይገልጻል መንፈስ ቅዱስም ምሥጢር ይገልጻልና እሳት የበላው መሬት ለእህል ለተክል ይመቻል ፣ መንፈስ ቅዱስም ያደረበት ሰውነት ለገድል ለትሩፋት ይመቻልና እሳት ከዛገባቸው ሳይሳተፍ ሰባቱን መዓድናት ያጸራቸዋል መንፈስ ቅዱስም ከግብራቸው ሳይሳተፍ ሁሉን ያነጻልና ይእቲ ታነጽሕ ወኢትረስሕ እንዲል ፤ እሳት ከንዱ ፋና አምሳ ስልሳ ፋና ቢያበሩለት ተከፍሎ የለበትም ፤ መንፈስ ቅዱስም ተከፍሎ ሳይኖርበት እስከ ምጽአት ድረስ ሲሰጥ ይኖራልና ይእቲ ትሁብ ወኢትቀብል እንዲል በእሳት ቀድሞ ሰብአ ሰዶም ሰብአ ገሞራን ከእሥራኤል አንዱን ኅብር አጥፍቶበታል ለመዓት እንጅ ለምሕረት አልተፈጠረም እንዳይሉ ለምሕረትም እንደ ተፈጠረ ለማጠየቅ ። እንድም ሽክላ ሠሪ ሠርታ ለቅጠርስ ንቅ ያገኘችበት እንደሆነ እንደ ገና መልሳ ከስክሳ በውኃ ሰውሳ በእሳት ታድሰዋለች ። ተሐድሶም በመንፈስ ቅዱስ ነውና ፤ ዛቲ እሳት እንተ ኮነ ይትዓፀፉ አዳም እንበለ ይትዓዶ ትእዛዘ እግዚአብሔር ፈጣሪሁ እመ ነበረ ውስተ ገነት ምስለ በልዓ እምዕፀ ዕልወት ተዓርቀ ወኢረከበ እስከነ መጽአ አዳም ዳግማዊ ወአል/ሁ እኑመ እማይ ወእመንፈስ እንዲል

፲፪ ዘመሥኢ ውስተ እዴሁ ዘቦቱ ያነጽሕ ዓውደ እክሉ ።

፲፪ ፍሬውን ከገለባ የሚለይበት መንሽ በጁ ተይዞ ያለ ።

ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ። ፍሬውን ከገለባው ለይቶ በሬቅ በጎታ በጎተራ የሚሰበስብበት ወኃሠርስ ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍዕ። ገለባውን ግን በማይጠፋ እሳት የሚያቃጥል እሱ ያጠምቀክሙ በል ወደ ወርቅ ሂዶ ዘኢይጠፍዕ አለ ፤ እንድም ዘመሥኤ ብለሀ መልስ ፣ ጣቱ ምስት ነው ቢሉ የምስትነት መያዣው ያንድነት ሁለት ነው ቢሉ ንዑና ሐሩ የሚልበት ሥልጣን ገንዘቡ የሚሆን ።

ዘቦቱ ያነጽሕ ዓውደ እክሉ ሀውኢቱ ፍጥረተ ሰብእ ብሎ ወስዶታል ሊቁ ፣ ጻድቃንን ከኃጥአን የሚለይበት ።

ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ፣ ጻድቃንን ከኃጥአን ለይቶ በመንግሥተ ሰማያት የሚያኖርበት ፣ መዛግብት ብሎ አበዛ በብዙ ወገን ትወረሳለችና ፣ እስመ ውስተ ቤተ አቡየ ብዙኅ ማኅደር ወምዕራፍ ቦቱ እንዲል ።

ወኃሠርሰ ያውዒ በእሳት ዘኢይጠፍዕ ፣ ኃጥአንን ከጻድቃን ለይቶ በገሃነም ሥቃይ የሚያመጣበት ሥልጣን ገንዘቡ የሚሆን ፣ እንድም ክፉውን ሕሊና ከበጎው ሕሊና የሚለይበት ሥልጣን ክህነት ገንዘቡ የሚሆን ፣ ወሥርናዮስ በጎውን ሕሊና ከክፉ ሕሊና ለይቶ በመንፈስ ቅዱስ የሚያስጠብቅበት እሱ ፣ መዛግብት ብሎ አበዛ ስለ ሀብቱ ብዛት ወኃሠርስ ፣ ክፉውን ሕሊና ከበጎ ሕሊና ለይቶ በቀኖና የሚያጠፋበት ሥልጣን ክህነት ገንዘቡ የሚሆን እሱ በመንፈስ ቅዱስ እሳትነት ያጠምቃችኋል

## በእንተ ጥምቀተ እግዚእ ኢየሱስ

፲፫ ወአሜሃ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ እምገሊላ ውስተ ዮርዳኖስ ከመ ይጠመቅ እምዮሐንስ

፲፫ ማር ፩፥፱ ፡ ለጌታ ሠላሳ ሲመላው ለዮሐንስ መንፈቅ ሲቀርፈው ያን ጊዜ ጌታ በዮሐንስ እጅ ይጠመቅ ዘንድ ከገሊላ ወደዮርዳኖስ መጣ ። እንድም ሰው ሰብሰቦ በማያጠምቅበት ጊዜ መጣ አብ በደመና ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመሰክር

መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ከራሱ ላይ ሲቀመጥ አንድነት ሦስትነት ይታወቃልና ፤ ያን ጊዜ ጌታ ከገሊላ ወደ ዮርዳኖስ መጣ አለ ። ሐተታ ምነው ባሪያ ወደ ጌታው ይሄዳል እንጅ ጌታ ወደ ባሪያ ይሄዳልን ፣ ባሪያ በጌታው እጅ ይጠመቃል እንጅ ጌታ በባሪያው እጅ ይጠመቃልን ቢሉ ጌታ መምጣቱ ለትሕትና ነው እንጅ ለልዕልና አይደለምና ፤ አንድም ለአብነትነት ጌታ ዮሐንስን መጥተህ አጥምቀኝ ብሎት ቢሆን ዛሬ ነገሥታት መኳንንት መጥታችሁ አጥምቁን ባሉ ነበርና ፤ ሄዳችሁ ተጠመቁ ለማለት አብነት ስለሆነ ፤ ጥምቀቱን በዮርዳኖስ ያደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፤ ትንቢት ባሕርኒ ርእየት ወጎየት ወዮርዳኖስኒ ገብአ ድኅሬሁ ርእዩከ ማያት እግዚኦ ርእዩከ ማያት ወፈርሁ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም ዮርዳኖስ ከላይ ነቁ አንድ ነው ዝቅ ብሎ በደቤት ይከፈላል ከታች ወርዶ ይገናኛል ። ዮርዳኖስ ከላይ ነቁ አንድ እንደሆነ የሰው ሁሉ ነቁ አንድ አዳም ነው ። ዝቅ ብሎ በደቤት እንዲከፈል እስራኤል በግዝረት አሕዛብ በቍልፈት ተለያይተዋል ። ከታች ወርዶ በወደብ እንዲገናኝ ሕዝብና አሕዛብ በክርስቶስ በጥምቀት አንድ ሁነዋልና ፤ አንድም አብርሃም ላምስቱ ነገሥተ ሰዶም ረድቶ አራቱን ነገሥት ኮሎዶጎምርን ድል ነሥቶ ቢመለስ ደስ ቢለው በመዋዕለየ ትሬኑ ቃለከ መሚሙ ታርእየኒው ኪያሃ ዕለተ አው አልቦ አለ ፤ እሱንስ አታየውም ምሳሌውን ታያለህና ሑር ዕድዎ ለዝንቱ ዮርዳኖስ ፤ ዮርዳኖስን ተሻግረህ ሂድ አለው ፤ ዮርዳኖስን ተሻግሮ ቢሄድ መልከ ጼዴቅ ኅብስተ በረከት ጽዋዓ አኰቴት ይዞ ተቀብሎታል አብርሃም የምእመናን ዮርዳኖስ የጥምቀት መልከ ጼዴቅ የቀሳውስት ኅብስተ በረከት ጽዋዓ አኰቴት የሥጋው የደሙ አንድም ኢዮብ ከዚህ ተጠምቆ ከደዌው ድኑዋል ፤ ኢዮብ የአዳም ከነሕፃናቱ ደዌ የመርገመ ሥጋ የመርገመ ነፍስ ዮርዳኖስ የጥምቀት ምሳሌ ፤ አንድም እሥራኤል ዮርዳኖስን ተሻግረው ምድረ ርስት ገብተዋል ፤ ምእመናንም አምነው ተጠምቀው ገነት መንግሥተ ሰማያት ገብተዋልና ፤ ኤልያስ ዮርዳኖስን ተሻግሮ ገነት አርጓል ምእመናንም አምነው ተጠምቀው ገነት መንግሥተ ሰማያት ለመግባታቸው ። አንድም የኤልሳዕ ደቀ መዛሙርት ጸበበነ ማኅደር ንዑ ንግዝም ዕፀ ወንሕንጽ ካልዓ ማኅደረ ብለው ሄዱ ፤ እሱም መምህረ ትሕትና ነውና አብሯቸው ሄደ ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ ሲቆርጥ ምሳሩ ከዛቢያው ወልቆ ከባሕር ገባበት ፤ ዝኒ ኀዑይ እግዚእየ ፤ ጌታዬ ጥንቱን የተውሶ ያውም ጠፋ ተጨርሶ አለው የገባበትን አሳየኝ አለው አሳየው ቅርፍቶ ዕፅ ቀርፎ አመሳቅሎ ቢመታው መዝቀጥ የማይቻለው ቅርፍቶ ዕፅ ዘቅጦ መዝቀጥ የሚገባውን ብረት ይዞት ወጥቷል። እንደዚህም ሁሉ ሞት የማይገባው መለኮት ሙቶ ሞት የሚገባው አዳምን ለማዳኑ ምሳሌ ፤ ጥምቀቱንም ሽቶ አላደረገውም ። አኮ ፈቂዶ ለተጠምቆ እላ ከመ የሀበነ ሱታፌ ንጽሕ እንዲል በመጠመቁም ጸጋ ያገኘበት አይደለም ። አኮ ዘረከበ ጸጋ በተጠምቆቱ እላ ከመ ያብርህ መካናተ ወያነጺል ማያተ ለእለ ሀለዎሙ ይጠመቁ ውስቴታ እንዲል ፤ ዮርዳኖስን ብርሀት ማሕፀን ለማድረግ ለጥምቀት ኃይል ለመስጠት ነው እንጂ አንድም ዮርዳኖስ በበጋ የማይጎድል በክረምት የማይተርፍ ማእከላዊ ውኃ ነው የጌታም ጥምቀት እኛም ከመጥቀም በላይ እሱን ከመጥቀም በታች ነውና ፤ ዳግመኛ በባሕረ ጥብርያዶስ ላይ የሚሄድ ውኀ ነው ዐባይ በጣና ላይ እንዲሄድ የጌታም ጥምቀት ከኛ ጥምቀት በላይ ነውና ፤ አንድም ብዙ ንዑሳን አንቀዕት ይገቡበታል እሱ ያበረታቸዋል እንጂ እነሱ አያበረቱትም ፤ የጌታም ጥምቀት ለኛ ጥምቀት ኃይል ጽንዕ ይሆናል እንጂ የኛ ጥምቀት ለጌታ ጥምቀት ኃይል ጽንዕ አይሆንምና ። አንድም ንዕማን ከዚህ ተጠምቆ ከደዌው ተፈውሷል ንዕማን የአዳም ከነሕፃናቱ ደዌ የመርገመ ሥጋ የመርገመ ነፍስ ዮርዳኖስ የጥምቀት ምሳሌ ፤ ኢዮብን ዕማን ጌታ የተጠመቁበት ወደቡ አንድ ነው ። ትንቢቱን ዐውቆ እናግሯል ምሳሌውንም እንጂ ፀውቀ አስመስሏል ። ምሥጢሩ እንደምነው ቢሉ ዲያብሎስ የጨለማ መጋረጃ ጋርዶ በአዳምና በሔዋን ሥቃይ አጸናባቸው ስመ ግብርናታችሁን ጽፋችሁ ብትሰጡኝ ባቀለልሁላችሁ ነበር አላቸው ። አዳም ገብሩ ለዲያብሎስ ሔዋን አመቱ ለዲያብሎስ ብለው ጽፈው ሰጡት መጽሐፈ የለም ይሁንብን ማለታቸውን መናገር ነው እንጂ እሱ በሁለት ዕብነ ሩካም ጽፎ አንዱን በዮርዳኖስ አንዱን በሲኦል ጥሎታል፤ በዮርዳኖስ የጣለውን ሲጠመቅ እንደ ሰውነቱ ተረግጦ እንደ አምላክነቱ አቅልጦ አጥፍቶላቸዋል ። በሲኦል የጣለውን በዕለተ ዓርብ በአካለ ነፍስ ወርዶ ነፍሳትን ሲያወጣ አጥፍቶላቸው ወጥቷል ።

፲፬ ወዮሐንስሰ ዓበዮ እንዘ ይብል አንሰ እፈቅድ እምኀቤከ እጠመቅ ።

፲፬ ዮሐንስ ግን ባሪያ በጌታው እጅ ይጠመቃል እንጂ ጌታ በባሪያው እጅ ይጠመቃልን ብሎ አይሆንም አለው ።

ወአንተኑ ትመጽእ ኀቤየ ፤

ባሪያ ወደ ጌታው ይሄዳል እንጂ ጌታ ወደ ባሪያው ይሄዳልን አለው ፤ እናቱ ምንትኑ አነ ከመ ትምጽእ ኀቤየ እሙ ለእግዚእየ ብላ ነበርና ። ከዚያ አያይዞ እንዲህ አለ ።

፲፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ኅድግ ምዕረ ።

፲፭ ጌታ መለሰ አንድ ጊዜስ ተው አለው ። ሐተታ ፡ አንድ ጊዜ ቢጠመቅ ሁለተኛ ፡ በፈቃድ ቢጠመቅ በግድ ፡ በስውነቱ ቢጠመቅ ባምላክነቱ መጠመቅ የለበትምና ።

እስመ ከመዝ ተድላ ውእቱ ለነ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና ፤ ሐተታ ፡ ራሱን ከዮሐንስ አግብቶ አንተም መጥምቀ መለኮት ተብለህ ክብርህ ይነገራልና እኔም በባሪያው እጅ ተጠመቀ ተብሎ ትሕትናየ ይነገራልና ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሉ ጽድቀ። ትንቢተ ነቢያትን ልንፈጽም ይገባናልና ዮሐንስ እንዲያጠምቅ ጌታ እንዲጠመቅ ትንቢት ተነግሯልና አንድም እስመ ከመዝ ተድላ ለነ ፤ ራሱን ከምእመናን አግብቶ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና ፤ እናንተም ብትጠመቁ ይወርድላችኋል ለማለት ፡ ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሉ ጽድቀ ። ጽድቀ ተሰብእን ልንፈጽም ይገባናልና ፡ አንድም ራሱን ከአብ ከመ ንፈስ ቅዱስ ጋራ አንድ አድርጎ ይህ ለኛ ተድላችን ነውና አለ ። አብ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመ ሰክር መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ከራሱ ላይ ሲቀመጥ አንድነት ሦስትነት ይገለጸልና ። ወይደልወነ ከመ ንፈጽም ኵሉ ጽድቀ ፡ በማኅፀን የጀመርነውን ቸርነት ልንፈጽም ይገባናልና ። ወእምዝ ኀደጎ ።

ከዚህ በኋላ ተወው ። ሐተታ ፡ እንዲያው አይተወውም ስመ አብ ብከ ወስመ ወልድ ለሊከ ወስመ መንፈስ ቅዱስ ሀልው ውስቴትከ ባዕደ አጠምቅ ብስምከ ወበስመ መኑ አጠምቅ ኪ ያ ከ አለው ወልዱ ለቡሩክ ከማቴ ብርሃን ተማሃለነ ፡ አንተ ካህኑ ለዓለም በከመ ሢመቱ ለመልከ ጼዴቅ ብለህ አጥምቀኝ አለው ። ከዚህ በኋላ ተያይዘው ወደ ባሕር ወርደዋል ።

፲፮ ወተጠሚቆ እግዚእ ኢየሱስ ሶቤሃ ወፅአ እማይ ። ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፳፩ ፡ ፳፪ ፡

፲፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከተጠመቀ በኋላ ከውኃው ወጣ ሐተታ ፡ ጥምቀቱን በውኃ ያደረገው በሌላ ያላደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሲፈጸም ፡ ትንቢት ወእነዝኃከሙ በማይ ንጹሕ ወትነጽሑ እምርኵስክሙ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም ለታውፅእ ባሕር ኵሎ ዘይትሐወስ ዘቦ መንፈስ ሕይወት ባለ ጊዜ በልብ የሚሳቡ በእግር የሚያሽከረክሩ በክንፍ የሚበሩ በደመ ነፍስ ሕያዋን ሁነው የሚኖሩ ፍጥረታት ተገኝተዋል ፡ በረው በረው የሄዱ አሉ ከዚያውም የቀሩ አሉ ። በረው የሄዱ የኢጥሙቃን ከዚያው የቀሩ የጥሙቃን ምሳሌ ፡ ይህስ እንዳይሆን ወባረኮሙ ለክልኤሆሙ በአሐቲ

በረከት ይላል ብሎ በልብ የሚሳቡ የሰብእ ዓለም በእግር የሚያሽከረክሩ ከትሩፋት ወደ ትሩፋት የሚሉ የባሕታውያን ፡ በክንፍ የሚበሩ ተመስጦ ያላቸው የሰማዕታት ምሳሌ ትንቢቱን ዐውቆ እናግሯል ፡ ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ አስመስሏል ፍጻሜው እንደምነው ቢሉ ውኃ በዙፋን ካለ ንጉሥ ባደባባይ እስካለ ጽኑስ ለሁሉ ርኩብ ነው ጥምቀት መሠራቱ ለሁሉ ነውና ፡ ውኃ ጽንፍ እስከ ጽንፍ ይፈሳል ። ጥምቀትም ጽንፍ እስከ ጽንፍ ይደረጋልና ። ውኀ ያነጻል ጥምቀትም ያነጻልና ፡ ውኀ ለወሰደው ፍለጋ የለውም በጥምቀትም የተሰረየ ኃጢአት በፍዳ አይ መረመርምና ፡ ውኀ መልክ ያሳያል መልክ ያለመ ልማል ፡ ጥምቀትም መልክአ ነፍስ ያሳያልና መልክአ ነፍስ ያለመልማልና ፡ በውሀ የታጠበ ልብስ ኃይል ጽንዕ ግዘፍ እየነሣ ይሄዳል ምእመናንም ተጠምቀው ገድል ትሩፋት እያከሉ ይሄዳሉና ፡ አንድም ሥጋዊ ተፍኀር የነርብቃ የነሲፓራ በውኃ ምክንያት ሁኖዋል መንፈሳዊ ተፍኀ ርንም በውኃ ለማድረግ ፡ አንድም ሽከላ ሠሪ ሠርታ ስትጨርስ የነቃባት እንደሆነ አን ደገና ከስክሳ በውኃ ለውሳ ታድስዋለች ። ተሐድሶም በጥምቀት ነውና ፡ አንድም በውኃ ቀድሞ ሰብአ ትካትን ኋላ ግብጻውያንን ካጠፋበት በኋላ ለመዓት እንጂ ለምሕረት አልተፈጠረም ብለውታል ፡ ለም ሕረትም እንደተፈጠረ ለማጠየቅ ። ሐተታ የወዲ ያኛው ቀስቱን እያጋለ መርዝ እየቀባ እያተባ ይመ ጣል ። የወዲህኛውም እግዚአብሔር ጥበቡን ገልጾ ለት ጀባውን ከውኃ ነክሮ ለጋሻው አልብሶ ይሄዳል መርዙን ጀባው ይጠርግለታል ፡ ግለቱን ውኃው ያቀዘቅዝለታል ስለቱን ጋሻው ይመልስለታል እንደ ዚህ ሁሉ ምእመናንም በጥምቀት ባገኙት ኃይል ድል ይነሳሉና ።

ወናሁ ተርኅወ ሎቱ ሰማይ ፡ ሰማይ ተከፈተለት ። ሐተታ ፡ በሰማይ መክፈት መዘጋት የለበትም ደጅ በተከፈተ ጊዜ የውስጡ እንዲታይ ያልተገለጸ ምስ ጢር ተገለጸለት ሲል ነው ። ወርእየ መንፈስ እግ ዚአብሔር እንዘ ይወርድ ከመ ርግብ ወነበረ ላዕሌሁ። መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ በራሱ ላይ ሲቀመ ጥበት አየ ። ሐተታ ፡ መንፈስ ቅዱስን ርግብ አለው ርግብ ኃዳጊተ በቀል ናት ። መንፈስ ቅዱ ስም ኃዳጌ በቀል ነውና አንድም ርግብ በኖኅ ጊዜ ሐጸ ማየ አይኅንነትን ማየ አይኅ ስትል ቈጽለ ዕፀ ዘይት ይዛ ተገኝታለች ፡ መንፈስ ቅዱስም ተስፋ መስቀ ልን ያበሥራልና ፤ አንድም ርግብ ከንፏን ቢመቷት ዕንቍላሏን ቢሰብሩባት ቤቷን ካፈረሱባት አት ሄድም ። መንፈስ ቅዱስም ኃጢአት ቢሠሩ ፈጽ መው ካልካዱት አይለይምና ፤ ታሪክ ፡ አንድ ባሕ ታዊ እንዳየው ወሉታ ካህን ግልፎን አጊጣ አይቶ

ቢሖጸ ዝሙት ተነደፈ ። ሳማባሽ አላት ሳባቴ ንጉ ረው እምቢ አይልህም አለችው ሂዶ ነገረው ። ፈጣሪ ዩን ልጠይቅ ብሎ ከጣዖቱ ዘንድ ገብቶ ልስጠው አል ስጠው ብሎ ጠየቀው ። ቆቡን ይቅደድ ፈጣሪውን ይካድ ይኸን ካላደረገ አትስጠው አለው ሂዶ ነገረው። ቆቡን ቀደደ ፈጣሪውን ካደ ፤ በዚህ ጊዜ አድሮ በት የነበረ መንፈስ ቅዱስ በንጭ ርግብ አምሳል ተለይቶት ሲሄድ አይቷል ። ያልኸኝን አደረግሁ ስጠኝ አለው ሁለተኛ ልጠይቅ ብሎ ገብቶ ቢጠይቀው ፤ ቆቤ ፈጣሪውም ፈጽሞ አልራቀውም ባጠገቡ ዓጠገቡ ጽጠብቀዋልና ኣትስጠው አለው ። አይሆንም አለው ፤ ለዚህን ብዬ ፈጣሪዬን ካድሁ ቆቤን ቀደድሁ ብሎ ንስሐ ቢገባ ተመልሶ በር ግብ አምሳል ሲያድርበት አይቷል ። ጥምቀቱን በመዓልት ያላደረገው በሌሊት ያደረገው ስለምን ቢሉ ፤ በመዓልት አድርጎት ቢሆን መንፈስ ቅዱስን በቁሙ ርግብ ነው ብለው በተጠራጠሩ ነበርና አሁንስ በቁሙ ርግብ አለመሆኑ መንፈስ ቅዱስ መሆኑ በምን ይታወቃል ቢሉ ፤ ጌታ የተጠመቀ ከሌሊቱ ባሥረኛው ሰዓት ነው በዚያን ጊዜ ተሐዋስያን ከየቦታቸው አይናወጡምና ፤ በቁሙ ርግብ አለመሆኑ መንፈስ ቅዱስ መሆኑ በዚህ ይታወቃል፤ መንፈስ ቅዱስም መውረዱ ከውኃው ከወጣ ከዮሐንስ ከተለየ ነው ። ከወኃው ሳለ ወርዶ ቢሆን ለቀድሶተ ማያት የወረደ ነው ባሉ ነበረና ከዮሐንስ ጋራም ሳለ ቢሆን ስለ ክብረ ዮሐንስ የወረደ ነው ባሉ ነበርና ፤ ረቦ ወርዷል ያሉ እንደ ሆነ አብ ምሉእ ነው አንተም ምሉእ ነህ እኔም ምሉእ ነኝ ሲል ፤ አሰይፎ ወርዷል ያሉ እንደሆነ የብሉይ መዋዕል የአብ ሕይወት ነኝ ዩብሉየ መዋዕል ያንተም ሕይወት ነኝ እኔም ብሉየ መዋዕል ሕይወት ነኝ ሲል ወርዶ ራሱን ቆንጠጥ አድርጎ ይዞታል አብ አኃዜ ዓለም ነው አንተም አኃዜ ዓለም ነህ እኔም አኃዜ ዓለም ነኝ ሲል ፤ መውረዱ ግን የማኅፀኑን ለመግለጽ ነው ። እንድም ለአብነት እናንተም ብትጠመቁ እንዲህ ይወርድላችኋል ለማለት ወናሁ መጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ዘቦቱ ሠመርኩ ። ሉቃ ፱ ፴፭ ፤ ፪ ጴጥ ፩ ፲፯።

፲፯ ለተዋሕዶ የመረጥሁት በሱ ህልው ሁኜ ልመለክበት የወደድሁት ልጄ ይህ ነው የሚል ቃል ከወደ ሰማይ ተሰማ ሐተታ ፤ በዚህ አድሮ ያለው ልጄ ነው እሳስም ፩ አካል ፩ ባሕርይ አድርጎ ይህ ልጄ ነው አለ እንጂ ፤ ኢይቤ ዘላዕለ ዝንቱ ወልድየ እላ ይቤ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ እንዲል። ወልድየም ማለቱ እንደ እምላክነቱ ነው እንጂ እንደ ሰውነቱ አይደለም ። ኢይቤ ዝንቱ ወልድየ ዘከመ ትስብእቱ አላ ይቤ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘከመ መለኮቱ እንዲል ።

በእንተ ተመክሮት ዘኢየሱስ ።

## ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወእምዝ ወሰዶ መንፈስ ገዳመ ለእግዚእ ኢየሱስ ። ማር ፩ ፤ ፲፪ ሉቃ ፬ ፩ ፤ ከተጠመቀ በኋላ ፈቃዱ አነሣስቶ ወደ ገዳም ወሰደው ። ወሰበ ትሰምዕ እንዘ ይብለከ መንፈስ ወሰዶ ገዳመ ኢተሐሊኬ ከመ ፍጡር ውእቱ ፤ አላ መንፈስሰ ሥምረቱ ይእቲ እንዲል ፤ እንድም መንፈስ ቅዱስ የሚል አብነት ይገኛል ሰማዕታትን አነሣሥቶ ወደ ደም ጻድቃንን አነሣስቶ ወደ ገዳም እንዲወስድ ወሰደው ማለት አይደለም ፈቃዳቸው አንድ መሆኑን መናገር ነው ። ቁጥምቆም አልዋለም አላደረም ዕለቱን ገዳም ሄዷል ። እናንተም ተጠምቃችሁ አትዋሉ አትደሩ ዕለቱን ገዳም ሂዱ ለማለት አብነት ለመሆን ወደ ገዳም ሄደ አለ ። አዳም ከዚህ ዓለም አፍአ በምትሆን በገነት ድል ተነሥቶ ነበርና ፤ እሱም ከዚህ ዓለም አፍአ በምትሆን በገዳም ቢቱ አርጅስተ ኃጣውእ ድል ስመንሳት ። አንድም በገዳም ጾር ይቀላል ለወጣንያን አብነት ለመሆን አንድም በገዳም ጾር ይጸናል ለፍጹማን አብነት ለመሆን ። ከመ ይትመከር እምዲያብሎስ ከዲያብሎስ ይፈተን ዘንድ ፤ እፈተናለሁብ ብሎ ሄዶ ቢሆን ዕዳ በሆነበት ነበር ፤ ከሄደ ዘንድ ጾሩን እየቀለመ ይሰብርበታል እንጂ ።

ይህንም ጾር እማርበታለሁ ብሎ አላደረገውም ንግእ ፩ መዓዴ እምአፍአ ከመ ትኩን ፍቱን ወስዑክ እንዲል መከራውንም ሽቶ አላመጣውም እኮ ፈቂዶ መከራሁ ለጸላኢ አላ ከመ ያብጥል ኃይሎ ለዘያሜክዩ በኃይሉ ለቃል ዘኮነ ፩ደ ምስለ ሥጋ እንዲል ። መከራውንም አነሣሥቶ አላመጣውም ኢዘኮ እግዚአን እሎንቱ ሕማማቲ ከመ ይሳልቁ ዲቤሁ አላ በሁከቶሙ ማዕኑ እንዲል ፤ መዋጋቱም በሰውነቱ ነው ፤ ኢሥርዓ እግዚእነ ቀትለ በመለኮቱ አላ በሥጋው ዘይትቄየሮ ሕማማተ እንዲል ። ድል መንሳቱም በሰውነቱ ነው እንጂ በእምላክነቱ አይደለም። ወኢሞአ በኃይሉ መዋኢት እንዲል፤ በእምላክነቱስ ድል ቢነሳው ባልተደነቀም ነበር ፤ ሶበሰ ሞአ እግዚእነ በኃይሉ መዋኢት እምኢኮነ መንክረ ወእም ኢኮኑቲ ትሩፋት ዘውስቴቱ ዘኢሰብእ ሕጉ ወዘ ኢውድሰት እኮ መንከር እመ ሞአ ኃይል ለድኩም እንዲል ።

፪ ወጾመ ፵ መዓልተ ወ፵ ሌሊተ

፪ ፵ መዓልት ፵ ሌሊት ጾመ ። ሠራዔ ሕግ ነውና ጾምን መጀመሪያ ሕግ አደረገ ። እንድም ሥራውን በጾም ጀመረ ። ሐተታ ፤ መብል ለኃጣውእ መሠረት እንደ ሆነ ፤ ጾምም ለምግባር ለትሩፋት መሠረት ናትና ፤ እማ ለጸሎት ወእኀታ ለአር

ምሞ ወነቅዓ ለአንብዕ ወኖንተ ዙሉ ገድል ሥናይት እንዲል ። ፵መዓልት ፵ ሌሊት መሆኑ ስለምን ቢሉ ቀድሞ አባቶቹ ነቢያት ፵ ፵ ጾመዋል ከዚያ ቢያተርፍ አተረፈ ቢያጐድል አጐደለ ብለው አይ ሁድ ደጊቱን ሕገ ወንጌልን ከመቀበል በተከለከሉ ነበርና ፤ ሙሴ በ፵ ዘመኑ ለዕብራዊ ረድቶ ግብጻዊን ገድሎ በኖጻ ቀብሮታል ። ሙሴ የወልደ እግዚአ ዚአብሔር ዕብራዊ የአዳም ግብጻዊ የዲያብሎስ ኖጻ የመስቀል ። አንድም የ፫ቱ ሕርእስተ ኃጣውእ ምሳሌ ፤ ሙሴ ፵ ጾም ሕገ ኦሪትን ሠርቷል እሱም ፵ ጾሞ ሕገ ወንጌልን የሚሠራ ነውና ሙሴ ፵ ዘመን በምድያም ኑሮ እሥራኤልን ከግብጽ አውጥቷ ቸዋል ። እሱም ፵ ጾሞ

ነፍሳትን የሚያወጣ ነውና ፥ አንድም የእሥራኤል ጉበኞች በ፵ ቀን ተመልሰዋል ። እሱም የመንግሥተ ሰማይ ጉበኛ ነውና እሥራኤል በገዳም ፵ ዘመን ኑረው ምድረ ርስት ገብተዋል ። እናንተም ፵ ብትጾሙ ገነት መንግሥተ ሰማያት ትገባላችሁ ለማለት ። ኤልያስ ፵ ጾሞ ገነት ገብቷል ። እናንተም ፵ ብት ጾሙ ገነት መንግሥተ ሰማያት ትገባላችሁ ለማለት ሕዝቅኤል በፀጋማይ ጐኑ ፵ ቀን ተኝቶ ስድስት መቶ ሙታን አስነሥቷል ። እናንተም ፵ብትጾሙ ትንሣኤ ዘለክብር ትነሣላችሁ ለማለት ፤ ዕዝራ ፵ ቀን ከም ግቡ ተከልክሎ መጻሕፍትን አጽፏል ። እንበ በው እቶን መዋዕል ኢበላዕኩ እከለ ወኢሰተይኩ ማየ ። እሙንቱሰ መዓልተ ይጽሕፉ ወሠርከ ይዱረሩ እን ዲል እነዚያ ቀን ሲጽፉ እየዋሉ ማታ ይመገባሉ ። እሱ ግን ቀን ሲያጽፈው የሚውለውን ሌሊት ሲያስ ቦው ያድር ነበር ። እናንተም ፵ ብትጾሙ ምሥጢር ይገለጥላችኋል ለማለት ፤ እ፻ብ አካሉ የደገደገበት እንደሆነ ፵ ቀን ከምግብ ተከልክሎ ይሰነብታል ። በስቁረተ ዕፅ በስቁረተ እብንም ቢሉ እልፎ ቢሄድ ተግፎ ይወድቅለታል ይታደሳል ። እናንተም አርባ ብትጾሙ ተሐድሶተ ነፍስ ታገኛላችሁ ለማለት ። ምሳሌውን አውቆ አስመስሏል ፍጻሜው እንደም ነው ቢሉ አዳም በ፵ ቀን ያገኘውን ልጅነት አስ ወስዶ ነበርና ለሱ እንደካሰ ለማጠየቅ ፤ አንድም በ፵ቀን ተሰእሎተ መልክእ ለተፈጸመለት ሰው ሁሉ ሊክስ እንደመጣ ለማጠየቅ ። ፬ቱ ባሕርያት ፀሥር ዐሥሩን ለመካስ ። አምስተኛ ባሕርዩ ነፍስን የጨ መሩ እንደሆነ ስምንት ስምንቱን ሊክስ እንደመጣ ለማጠየቅ ። ከዚህም ተራብ አልሳሳም ተዋጋ ድል አልተነሣም ወሶበ ጾመ እግዚእ ፵መዓልተ ወ፵ሌሊተ ከሠተ ከመ ኢሐመ ሥጋሁ እምረኃብ ወጽምዕ በኃ ይል ዘይደሉ ለመለኮት እንዲል ፤ ከዚህም ሥራውን ሠርቶ ሥሩ እለ እንጂ ። ባልዋጁበት ጣት የዘንዶ ጉድጓድ ይለኩበት እንዲሉ ሳይሠሩ እኛን ሥሩ እላ ለንም ወሐርን እግበእ ለጌሰ ግብራት እንዲል ፰

ጌብሩት የተባሉ ጥምቀት ፤ ተአምኖ ኃጣውእ ከዊነ ሰማዕት ተባሕትዎ ምንኵስና ። ጥምቀት በእደ ዮሐ ንስ መጠመቅ ተአምኖ ኃጣውእ ከተአማንያን ኃጣ ውእ ጋራ አንድ ሁኖ መቆጠር ከዊነ ሰማዕት አንበ በእንተ ዝንቱ ተወለድኩ ወእንበይነ ዝንቱ መጻእኩ ውስተ ዓለም ከመ እኩን ሰማ ዕተ በጽድቅ ብሎ ከጲላጦስ ፊት ቁሞ መመስ ከር ተባሕትዎ ፵ ቀን ዘምግብ ተከልክሎ በገዳም መኖር ፤ ምንኵስና በድንግልና መኖር ነው ። ረቂቅ ዘእምረቂቅ እንደሆነ ለማጠየቅ በኀቱም ድንግልና ተፀንሰ በኀቱም ድንግልና ተወለደ ። ዘኢይርኅብ እም ዘኢይርኅብ እንደሆነ ለማጠየቅ ፵ መዓልት ፵ሌሊት ጾመ ዘኢይትገሠሥ እምዘኢይትገሠሥ እንደሆነ ለማጠየቅ በባሕር ላይ ሄደ ። ብርሃን ዘእምብርሃን እንደሆነ ለማጠየቅ ብርሃነ መለኮቱን በደብረ ታቦር ገለጸ ሕይወት ዘእምሕይወት እንደሆነ ለማጠየቅ ያራት ቀን ሬሳ አልዓዛርን አነሣ ። ወእምዝ ርኅበ ፤ ከዚህ በኋላ ተራብ ። ሐተታ ረኃቡም የፈቃድ ረኃብ ነው እጂ እንደኛ ረኃብ አይደለም እኛ ብንበላው ቁንጣን ብንተወው ስልት ቀጠና ይሆንብናል ፤ ረኀበ እግዚእነሰ አኮ ከመ ረኃበ ዚአነ አላ ገጸ ረኃቡ ፍሉጥ እምኔነ ለነሰ በግብር ይመውአነ ወሎቱሰ በፈቃዱ እንዲል ፤ አንድ ጊዜ ርኅበ አንድ ጊዜ ኢርኅበ ይላል እንደምነው ቢሉ ፤ ከ፪ት አካል ፩ አካል ከሁለት ባሕርይ ፩ባሕርይ እንደሆነ ለማጠየቅ ። በእንተ ምንት ርኅበ እግዚእነ ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ ያጠይቅ ከመ ውእቱ እም ፪ ህላዌያት እንዲል ። መራቡም ለአጽድቆተ ትስብእት ለካሣ ነው ።

፫ ወቀርበ ዘያሜክሮ ።

፫ የሚፈታተነው ዲያብሎስ ቀረበ ሐተታ እንዲያው አይቀርበውም ርኅብኩ የሚል ድምፅ ሰሰ ምቶት ፍሬ ዕፅ ሲሻ አይቶት ፤ መልኩን አጠውልጎ ታይቶት እሱም እንዲያው አይቀርብም በአምሳለ ሠዓሊ በአምሳለ ሐራሲ በቀዳዳ ሽልቻ ትኩስ ዳቦ የያዘ መስሎ ሁለት ደንጊያ ይዞ ይቀርባል አንዱን ባተ አንዱን ለኔ ዳቦ አድርገህ እንብላ እለዋለሁ ደንጊያውንማ ዳቦ ከማድረግ የያዝኸውን እንበላም ያለኝ እንደሆነ አዳምን አባቱን በመብል ምክንያት ድል እንደነሣሁት እሱንም በመብል ምክንያት ድል እነሣዋለሁ ብሎ ፤

ወይቤሎ እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ በል ከመ እላ እዕባን ኅብስተ ይኩና ፤

በዮርዳኖስ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመሰክርለት ሰምቶ ነበርና የእግዚአብሔርስ ልጅ ከሆንክ እኒህ ደንጊያዎች ኅብስት ይሁኑ ፀልይ እዘዝ አለው ። ቢያደርገው የሰይጣን ተአዛዚ ብየ ዕዳ እልበታለሁ

ባያደርገው ደካማ እሰኝዋለሁ ። ቢያደርገው ሌላ ጾር እሻሊታለሁ ባያደርገው ድካሙን አይቼ እቀርባለሁ ብሎ ፣ ደንጊያውን ኅብስት እድርግ ማለቱ ምን ልማድ ይዞ ነው ቢሉ በዮሴፍ ልማድ ፣ ዮሴፍን አባቱ የሱን ስንቅ ለብቻ አሲዞ ለወንድሞችህ ስንቃቸውን ሰጥተህ ወንድሞችህን ጠይቀህ ና ብሎ ላከው ። ያሉበትን አጥቶ ሲፈልግ የሱ ስንቅ አለቀበት ከዚያ እንዳይበላ አባቱ ያላዘዘው ነው ። ረኃብ ጸንቶበት ሳለ መልእከ ያባትህን ፈጣሪ ደንጊያውን ዳቦ እድርግልኝ እትለውም አለው ። ወደ እግዚአብሔር ቢያመለከት ደንጊያው ዳቦ ሁኖለት ተመግቧልና እንዲህ አለ ።

፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ጌታም መለሰ ። ወይቤሎ ጽሑፍ ከመ እኮ በኅብስት ከመ ዘየሐዩ ሰብእ ። ዘዳ ፰ ፫ ሉቃ ፬፡፬ ።

፬ ሰው የሚድነው በኅብስት ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ።

አላ በኵሉ ቃል ዘይወፅእ እምእፉሁ ለእግዚአብሔር እግዚአብሔር ዳን ያለው ይድናል ሙት ያለው ይሞታል እንጂ ፣ እንድም ሰው የሚያድን ገበሬ በጻረበት በኅብስት ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ፤ እግዚአብሔር ምግብ ይሁን ያለውም ምግብ ይሆናል እንጂ እስራኤል ፵ ዘመን በትርህ አልወደቀ ጫማህ አልወለቀ ልብስህ አላለቀ እንዲሉ ከመትያናስ በደመና አይበት ተጋርደ በትርህ ወይልጋዝ ተጨና መጠኑ ድንብላል አህሉ መልኩ በረድ መሰሉ ወእንዘ የኃድግ ሀበ ይላል የውርጭ ገበታ ሲነጸፍ እየዘነመላቸው እርባ ዘመን ተመግበዋልና ፣ እንድም ሰው የሚድን ገበሬ በጻረበት በጋረበት በእንጀራ ብቻ እንዳይደለ ተጽፏል ፤ በዓቂበ ሕግም በትምህርትም ነው እንጂ ሐተታ ። የሰው ባሕርዩ ባሕርይ እንስሳዊ ባሕርይ መልእካዊ ነው ባሕርይ እንስሳዊ ምግብ ሲያጣ ይጎዳል ፣ ባሕርይ መልእካዊ ትምህርት ሲያጣ ይጎዳልና አእምር ከመ በእማን ሲያይ ቃለ እግዚአብሔር ሲሲተ ልብ ቃላቲሁ ለእግዚአብሔር ወእምጽእ ረ ኃ በ እ ክ ል ወጽምዓ ማ ይ ለ ብ ሔ ር ረኃብሰ እምሰሚዓ ቃለ እግዚአብሔር እንዲል ። እንድም ወልደ እግዚአብሔርሰ ከሆንህ ይህ እንደ ድንጊያ ፊዞ ያለ ሰውነትህ ኅብስተ ሕይወት ኅብስተ መድኃኒት ይሁን ብለህ እዘዝ ሲያሰኘው ነው ። ጌታም ሰው የሚያድን በዕሩቅ ብእሲ ሥጋ እንዳይደለ ተጽፏል ። እካላዊ ቃል በተዋሐደው ሥጋ ነው እንጂ አለው ፭ ወእምዝ ነሥእ ወወሰዶ ውስተ ቅድስት ሀገር ።

፭ ከዚህ በኋላ ወደ ቅድስት ሀገር ወደ ኢየሩሳሌም ወሰደው ሐተታ እሱስ እይወሰደውም ፈቃዱን ዐውቆ ስለሄደለት ካህናትን ድል ነሥቶበት በማላውቅ በገዳም ቢሆን ነው እንጂ ፣ ካህናትን ድል በምነሳበት በቤተ መቅደስ ቢሆን መች ድል ይነሳኝ ነበር ብሏል ፈቃዱን አይቶ ስለሄደለት ነሥአ ወሰዶ እዕረገ ይላል ወዓቀሞ ውስተ ተድባበ ቤተ መቅደስ ። ተድባብ ማዕዘንት ርእስ ይላል እብነት ፣ ተድባብ ያለ እንደሆነ ከዝንቦው ማዕዘንት ያለ እንደሆነ ከምሕዋሩ ርእስ ያለ እንደሆነ ከጉልላቱ አቆመው ። ከዚህም በእምሳለ ሊቀ ካህናት እምሞ ጠምጥሞ መነሳንስ ይዞ ይታየዋል ።

፮ ወይቤሎ እመሰ አማን ወልደ እግዚአብሔር አንተ ቅንጽ እምዝየ ወተወረው ታሕተ ።

፮ መዝ ፣ ፺፩ ።

በእውነት ወልደ እግዚአብሔር ከሆንህ ከዚህ ዘለህ ወደታች ውረድ አለው ፣ ሐተታ ቢሰበር ዐርፈዋለሁ ባይሰበር ምትሐት እሰኘዋለሁ ቢያደርገው ሌላ ጾር እሻሊታለሁ ባያደርገው ደካማ እሰኘዋለሁ ቢያደርገው የሰይጣን ተእዛዚ ብየ ዕዳ እልበታለሁ ባያደርገው ድካሙን አይቼ እቀርበዋለሁ ብሎ ነው ። እስመ ጽሑፍ ከመ ለመላእከቲሁ ይኤዝዞሙ በእንቲአከ ከመ ይዕቀቡከ በኵሉ ፍናዊከ በመንገድህ ሁሉ ይጠብቁህ ዘንድ መላእከትን ሰላንተ እንዲያዛቸው ተጽፏልና ፤ ወበእደዊሆሙ ያነሥኡከ ከመ ኢትትዐቀፍ በእብን እግርከ እግረከ ይላል ፤ እግርህ እንዳይሰናከል፤በእጆቻቸውም ያነሡሃል የሚል ጽሑፍ አለና ፣ ጌታ ከላይ ጠቅሶበት ነበርና ፣ እሱም ፈንታውን ይንጉዳጉዳል ።

፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ካዕበ ጽሑፍ ኢታመክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ።

፯ ፣ ዘዳ ፣ ፲ ፣ ፲፮ ።

ዳግመኛ ፈጣሪህን እግዚአብሔርን አትፈታተነው የሚል ጽሑፍ አለ አለው ፤ እንዲህ የሚል ከምን አለ ቢሉ እንደ ጊዜ ገድሉ ጠቀሰ ። እሥራኤል በገዳም ሳሉ ሙሴ ካሥራሁለቱ ነገድ አውጣጥቶ ኢያሱና ካሌብን ምድረ ርስትን ሰልላችሁን ብሎ ሰደዳቸው ። እሳቸውም ሰልለው ሲመለሱ ከወይኑ ዘለላ ከሰንዴው ዛላ በባጢ ቀፎ ይዘው መጡ ። እንደምን ሁናችሁ መጣችሁ ሀገሪቱስ እንደምን ያለች ናት ብለው ጠየቋቸው ። ሀገሪቱስ መልካም ናት እንደዚህ ያለ ታፈራለች ፤ ባሕቱ ርኢነ ደቂቀ ሰኤናቅንኖሙ ከመ እርዝ ወጽንንሆሙ ከመ አውልዕ ንሕነሰ ኮነ ከመ እናብጥ በቅድሚሆሙ ምድርኒ ትረድኦሙ ወተዓቅቦሙ ብለው ፲ሩ እስገርመው አስፈርተው ተናገሩ ካሌብና ኢያሱ በፈቃደ እግዚአብሔር እንገባታለን አሉ ፲ሩ ካገባንስ አሁን ያግባን ሙሴ ተነሣ ታቦተ ጽዮንንም እንሣ እንሂድ አሉት ፣ ሙሴ ታቦተ ጽዮንም አሁን አትነሣ እናንተም እግዚአብሔር ፈጣሪያችሁን አትፈታተኑት አላቸው ። አይሆንም ብለው ሄዱ ። በወሰን ያሉ እሕዛብ ገጥመው

ድል አደረጓቸው ፤ በዚህ ጊዜ ከባሕር ጠልቀው ። ከገደል ወድቀው አልቀዋል ፤

ከዚህም ጌታ አንደ ጊዜ ገድሉ ጠቀሰው ።

፰ ወአምዝ ነሥአ ዲያብሎስ ወአዕረጎ ውስተ ደብር ነዋን ጥቀ

፰ ከዚህ በኋላ ወደ ረጅም ተራራ አወጣው ሐተታ ነገሥታትን ድል በማልነሣበት በቤተ መቅደስ ቢሆን ድል ነሣኝ እንጅ ፣ ነገሥታት ድል በምነሣበት በተራራ ቢሆን መቸ ድል ይነሣኝ ነበር ብኋል ፈቃዱን ዐውቆ ስለሄደለት አዕረጎ አለ ።

ወአርአዮ መንግሥታተ ኵሉ ዓለም ፣ ወኵሎ ክብሮ ፣ ጠጠሩን ወርቅ ብር ፣ ቅጠሉን ግምጃ አስመስሎ አሳየው አንድም መንግሥታተ ኵሉ ዓለም ። ግዛቱን ሁሉ አሳየው ወኵሎ ክብሮ እንስሳትን አራዊትን ፈረስ በቅሎ ሠራዊት አስመስሎ አሳየው ፣ እሱስ ያይለታል ቢሉ ስለመሰለው ነው እንጅ አያይለትም ድል መንሳቱ በምን ይታወቃል ቢሉ ባለመጽነኑ ።

፱ ወይቤሎ ዘንተ ኵሎ እሁበከ እምከመ ሰገድከ ሊተ ወአማኅከኒ ፣ ደፋር ነውና ብትሰግድልኝ እጅ ብትነሳኝ ይህን ሁሉ እሰጥሃለሁ አለው ።

፲ ወእምዝ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር እምድኅሬየ ሰይጣን ።

፲ ዘዳግም ፮ ፲፫ ፣ ከዚህ በኋላ ከኋላየ ወግድ እለው ራስ አይቶ የሚመጣ ጠላት ክፉ ነውና ጽኑ ባሳጋራዬ ሲል ነው ። ወዓቀመ አዴርሃ ሰይጣነ ሳዕለ ሰሎሞን እንዲል ። አንድም እምዘድኅሬየ ይላል አብነት ከኔ በኋላ ከሚነሱ ክምእመናን ወግድላቸው አለው ። እንዲህ ባለው ጊዜ እንደጢስ ተኖ እንደ ትቢያ በኖ ጠፍቱአል ። ሐተታ እስካሁን ሑር አላለው አሁን ሑር ማለቱ ስለምን ቢሉ ። በቀዳሚ ጊዜ ጉየይ ወበካልዕ ጊዜ ጉየይ ወበሣልሰ ተንሥእ ወተቃተል እንዲል ፣ አብነት ለመሆን በሦስተኛው ድል ንሱ ለማለት ንጉሥ በመንግሥቱ ጉልማሳ በሚበቱ እንዲቀና ፣ ጌታም ለአምልኮቱ ቀናዒ ነውና ፣ እስመ አነ እምላከ ቀናዒ ዘአፈዲ ኃጢአተ አብ ላዕለ ውሉድ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትውልድ ለእለ ይጸልዑኒ ። ወለአሰሰ ያፈቅሩኒ አገብር ምሕረተ እስከ ፲ቱ፻ ትውልድ እንዲል ።

ጽሑፍ ለእግዚአብሔር አምላክከ ትሰግድ ወኪያሁ ባሕቲቶ ታምልክ ፣ ለፈጣሪህ ለእግዚአብሔር ትሰግድ ዘንድ እሱንም ብቻ ታመልክ ዘንድ ተጽፏል አለው። ሑር እምድኅሬየ ባለው ጊዜ እንደጢስ ተኖ እንደ ትቢያ በኖ ጠፋ አላለምን ሰማን ይጠቅሰዋል ቢሉ ሰይጣንና ውሻ ምልልሰ ወዳጅ ነውና ተመልሶ ያሰማዋል ። አንድም እንደ አምላክነቱ አጽንቶት ሰምቶ ይሄዳል ። አንድም ወጺጋሁ ታሰምዖ

እንዲል ካሰበት ሁኖ እንዲሰማው አድርጎታል ። አንድም ከሐተታ ለመዳን ጥቅሱ ይቀድማል ።

፲፩ ወእምዝ ኀደጎ ዲያብሎስ ።

፲፩ ከዚህ በኋላ ተወው እስከ ጊዜሁ ብሎ በሉቃስ ያቀናዋል ። በዕለተ ዓርብ በአይሁድ ሥጋውሁኖ እስኪያሰቅለው ድረስ አይመለሰበትም ። ከዚህም በኃ ልጅ ተወልዶ ለአዳምና ለሔዋን በሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል ነሣሳቸው ። አሁን ዛሬ ደም ያለበት ሰው ጌሻ አስነሥቶ አምባውን ሰብሮ ደመኛውን ገድሎ ደሙን መልሶ ቢሄድ የቀሩት ከዛፍ ከገደል ተጣግተው የሆነስ ሆነ አንተ ማነህ እንወቅህ ባሉት ጊዜ የዘመዶቼን የአገሌ የአገሌ ደም የማይቀርብኝ እኔ አገሌ ነኝ ብሎ እንዲል ፣ ጌታም የአባቴ የአዳም የእናቴ የሔዋን ደም የማይቀርብኝ ሲል በሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል ነሣሳቸው ፣ ሦስቱ አርእስተ ኃጣውእ ስስት ትዕቢት ፍቅረ ንዋይ ናቸው ። ስስት ያልሰጡትን መሻት ነው ። ትዕቢት እምሳክ እሆናለሁ ማለት ነው ። ፍቅረ ንዋይ በቃኝ አለማለት ነው ። በዚህ ሁሉ ድል ነሥቶታል ። ዞቲ ስፍጠት አንተ ረሰየቶ ለአዳም ይትመየጥ ውስተ መሬት ወሶበ በጽሐ ኀበ እምላኪየ ወኀቤ ሲሳይ ለኵሉ ገብአ ሰይጣን ተኃፊሮ ወተመዊኦ

እንዲል ፡ አንድም ድል መንሳቱ ስአዳምና ስሔዋን ብቻ አይደለም ለሁሉም ድል ነሥቶላቸዋል የመነኰሳትም ጾራቸው ስስት ነው በሹት ጊዜ አያገኙትምና በትኀርምት ኑዋሪዎች ናቸው በቦታቸው በገዳም በስስት ቢመጣበት በትዕግሥት ድል ነሥቶላቸዋል የካህናት ጾራቸው ትዕቢት ነው እእምሯችን ረቂቅ ማዕርጋችን ምጡቅ እያሉ ይታበያሉ ። በቦታቸውም በቤተ መቅደስ በትዕቢት ቢመጣበት በትሕትና ድል ነሥቶላቸዋል ። የነገሥታት ጾራቸው ፍቅረ ንዋይ ነው ቤታቸውን ከፍ ካለ ቦታ ሠርተው ያለፈ ያገደመውን የወጣ የወረደውን እያዩ የዚህ ሁሉ እንጅ ኑሮው በኛ ነው እያሉ ገንዘብ ይሰበስባሉ ቦታቸው በተራራ ነው ። በተራራ በፍቅረ ንዋይ ቢመጣበት በጸሊዓ ንዋይ ድል ነሥቶላቸዋል ፣ ከዚህ በኋላ ኃጢአት ክሥሩ እንደተነቀለ ዛፍ ሁናለች ክሥሩ የተነቀለ ዛፍ እንዳይለመልም እንዳያብብ እንዳያፈራ ኃጢአትም በፍዳ የማታሲዝ ሆናለች ። ዛሬ የተያዙ አሉሳ ቢሉ አሊህማ ዐዋጅ አፍራሾች ናቸው ። ንጉሥ ይዘምታል ድል ነሥቶ ሲመለስ ከመንገድ የወጣህ ወታደር ብሎ ዐዋጅ ይነግራል በደለኛ ወታደር ገንዘብ ሲዘርፍ ከመንደር ገብቶ ቢሞት ንጉሥ ድል አልነሣም ይባላልን ? እኒህስ ዐዋጅ አፍራሾች ናቸው ።

ወናሁ መጽኡ መላእክት ይትለአክዎ ።

አርባ ቀን በትህርምት ኖሯልና መላእክት ኅብስት ሰማያዊ ጽዋዕ ሰማያዊ ይዘው መጡ አንድም ድል

ወንድሙን እንድርያስን እንዘ ይወድዩ መርበብቶሙ ውስተ ባሕር ፤ መረባቸውን ከባሕር ሲጥሉ አስመ መሠግራን እሙንቱ ዓሣ ወጋሮች ነበሩና ።

፲፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ንዑ ትልውኒ ድኅሬየ ።

፲፱ ለጊዜው በእግር ተከተሉኝ ፍጻሜው በግብር ምሰሉኝ አላቸው ወእሬስየክሙ መሠግራነ ሰብእ ሰውን እንደ ዓሣ ወንጌልን እንደ መረብ ይህን ዓለም እንደ ባሕር አድርጋችሁ እንድታስተምሩ አደርጋችኋለሁ አላቸው ።

፳ ወበጊዜሃ ኀደጉ መሠግሪሆሙ ወተለውዎ

፳ ያን ጊዜ ፈጥነው መርከባቸውን መረባቸውን ትተው ተከተሉት ለጊዜው በእግር ተከተሉት ፍጻሜው በግብር መሰሉት ።

፳፩ ወተዓዲዎ ሕቀ እምህየ ርእየ ካልዓነ ፪ተ አኃወ ።

፳፩ ከዚያ ጥቂት እልፍ ብሎ ሁለት ወንድማማች አገኘ ፤ ያዕቆብሃ ወልደ ዘብዴዎስ ወዮሐንስሃ እኅዋሁ ፤ የዘብዴዎስ ልጅ ያዕቆብን ወንድሙ ዮሐንስን ፤ ውስተ ሐመር ምስለ ዘብዴዎስ አቡሆሙ ፤ ከአባታቸው ከዘብዴዎስ ጋራ እንዘ ይሠርዑ ወያስተሣንዩ መሣግሪሆሙ ።

መረባቸውን ያደፈውን ሲያጥቡ የተቆረጠውን ሲቀጥሉ ፡ ወጸውዖሙ ። ለጊዜው በእግር ተከተሉኝ ፍጻሜው በግብር ምሰሉኝ አላቸው ።

፳፪ ወበጊዜሃ ኀደጉ ሐመሮሙ ወዘብዴዎስሃ አባሆሙ ወተለውዎ ።

፳፪ ያን ጊዜ ፈጥነው መረባቸውን መርከባቸውን ዘብዴዎስ አባታቸውን ትተው ተከተሉት ፤ ሐተታ ፡ አክብር አባከ ወእመከ ይል የለም ቢሉ ። ይህን ቃሉ ካልተማሩ አያውቁትምና ። አንድም ከአክብሮተ አብ ወእም አክብሮተ እግዚአብሔር እንዲበልጥ ለማጠየቅ ። አባትን የሚረዳው ልጅ የሚረዳበት ገንዘብ ያለ እንደሆነ ትቶ መሄድ ይገባል ። የሚረዳው ልጅ የሚረዳበት ገንዘብ የሌለው እንደሆነ ትቶ መሄድ አይገባም እሱን ግን ምስለ አሳቡ ብሎ በማርቆስ ያቀናዋል ገንዘብ ያለው ነው ። በእንተ ቀዳማዊ ስብከቱ ወመንክራቲሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፫ ወአንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ኵሉ ገሊላ እንዘ ይሜህር በምኵራባቲሆሙ ።

፳፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በምኵራብ ገብቶ ሲያስተምር በገሊላ ሲመላለስ ኖረ ።
ወይሰብክ ወንጌለ መንግሥት ፡ ጌትነቱን የምትናገር ወንጌልን እያስተማረ ኖረ ። ሐተታ ፡ ወልደ ፡ እግዚአብሔር እንደነገሠ ዲያብሎስ እንደተሻረ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ እንደጠፋ ትናገራለችና ወንጌለመንግሥት ይላታል ወይፌውስ ኵሎ ደዌያነ ወኵሎ ሕሙማነ ዘውስተ ሕዝብ ለዚህም ምልክት በሕዝቡ ዘንድ ያሉ ድውያንን ሁሉ ይፈውስ ነበረ ።

፳፬ ወወፅአ ስሙዓተ ነገሩ ውስተ ኵሉ ሶርያ

፳፬ የተአምራቱ ዜና በሶርያ በ፬ቱ መዓዝን ትነገረ ።

ወአምጽኡ ኀቤሁ ኵሎ ድውያነ ወኵሎ ሕሙማነ ዘሰሰዚአሁ ሕማሞሙ ።
ደዌያቸው ልዩ ልዩ የሚሆን ድውያንን ወደሱ ይዘውመጡ ወጺዑራነ፤ ወእለሂ ቦሙ አጋንንት ።
የተጨነቁትን ። አጋንንት ያደሩባቸውን ። ወወርኃውያነ ፤ ሠርቀ ወርኅ እያየ የሚጥላቸውን ፡ ጨረቃ እንጂ ባታመልኩ ነው ስሚሉት ፤ እንድም ምልአተ ወርኅ ሲሆን ደም ይመላል ብርድ ብርድ ይላል ደዌ ይቀሰቅሳልና ።
ወእለሂ ነገርጋር ።

ድልስጣ የሚባል ጋኔን አለ አንድ እግሩን ወደ ላይ አንድ እግሩን ወደታች አድርጎ ሲታያቸው ይጥላቸዋልና ።
ወመፃጉዓነ ።
የጸናባቸውን ።
ወአሕየዎሙ ፤
እነዚህን ሁሉ አዳናቸው ፤

፳፭ ወተለውዎ ብዙኃን አሕዛብ እምገሊላ ወእምዓሥርቱ አህጉር ወእምኢየሩሳሌም ወእምይሁዳ ወእማዕዶተ ዮርዳኖስ ። ማር ፫ ፡ ፯ ፡ ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፲፯ ።

፳፭ ካሥር አህጉር ከብዙ መንደር ተወጣጥተው አምስት ገባያ ያህል ሰዎች ተከተሉት ፣ ላንድ ሽማግሌ ዐሥር ልጆች ነበሩት እኒህ እየራሳቸው እንድ አንድ አገር አቅንተው ይኖሩ ነበርና ፡ እንድም ጺላጦስ ለቀረጥ ይመችኝ ብሎ እንዱን ከተማ ካሥር ከፍሎታል ፣ ከዚህ ተወጻጽተው ተከትለውታል እነዚህም ስለ አምስት ነገር ይከተሉታል ፡ አንዱ ገባያ መልኩን እናያለን ብለው ፡ አንዱ ገበያ ኅብስት አበርክቶ ያበላናል ብለው ፣ አንዱ ገባያ ትምርቱን እንሰማለን ብለው ፣ አንዱ ገባያ ከደዌያችን ይፈውሰናል ብለው ፤ አንዱ ገባያ የአሪትን መፍረሻ የወንጌልን መታነጫ እናያለን ብለው ነው ። ለነዚህም ትንቢት ተነግሮላቸዋል ተነግሮባቸዋል ። መልኩን እናያለን ላሉት ይሜኒ ላህዩ እምውሉደ ዕጓለ እመሕያው ተብሎ ፤ ኅብስት አበርክቶ ይመግበናል ላሉት ወኢያንጥእሙ እምዘፈቀዱ ተብሎ ፡ ያስተምረናል ላሉት ጥዑም ለጉርዔየ ነቢብከ ተብሎ ። ከደዌያችን ይፈውሰናል ላሉት ነሥአ ደዌነ ወጾረ ሕማመነ ተብሎ

የእሪትን መፍረሻ የወንጌልን መታነጫ እናያለን ባሉት ቅንዓት አንሥዑ ለሕዝብ አብዳን ተብሎ ተነገርባቸዋል ። እኒህንም ባምስት ነገር ይፈውሳ ቸዋል በሐልዮ በነቢብ በገቢር በዘፈረ ልብስ በወ ራቅ ምራቅ ነቢር ከሁሉ ይገባል ።

## ወእንተ ብፁዓን ።

### ምዕራፍ ፡ ፭ ።

፩ ወርእዮ ብዙኃነ አሕዛበ ዓርገ ውስተ ደብር ወነበረ ።

፩ ወሶበ ርእየ ይላል ፡ ብዙ ሰዎችን ባየ ጊዜ ከተራራ ላይ ወጥቶ ተቀመጠ ። ሐተታ ፡ ምነው አሕዛብ አላቸው እስራኤል አይደሉም ቢሉ ብዛታ ቸውን ሲያይ ፡ አንድም ግብረ አሕዛብን ይሠራሉና ፀጸያፍ የገባ ሰው ሲበዛ ከመርከብ ከተራራ ሁኖ ማስ ተማር ልማድ ነው ። መምህር ከፍ ካለ ቦታ ሰማዕያን ዝቅ ካለ ቦታ የሆኑ እንደሆነ ትምህርት ለሰማዕያን ይረዳልና ፡ ወይረድ ከመ ጠል ነቢብየ እንዲል ። አንድም በደብረ ሲና ሕገ ኦሪትን የሠራሁ እኔ ነኝ ሲል ። አንድም ልዑለ ባሕርይ ነኝ ሲል ። አንድም የሠራሁላችሁ ሕግ ልዕልት ናት ። እናንተም ሉዓላ ውያን ናችሁ ሲል ።

ወቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ። ደቀ መዛሙርቱ ወደሱ ቀረቡ ። የቀረው ግን የራቀውም ርቆ የቀረበ ውም ቀርቦ ይሰማል እኒህ ግን መደበኞች ናቸውና ትምህርት የሚቀር በኒህ ነውና፣ አንድም ለጉባኤው ሥፍራ አለውና ፤ ጥንተ ቀራቦች ናቸውና ቀረቡ ።

፪ ወከሠተ አፉሁ ።

፪ ነገር ጀመረ ፤ ወከሠተ አፉሁ ኢዮብ ወረ ገማ ለዕለት እንተ ባቲ ተወልደ ። ወከሠተ አፉሁ ጴጥሮስ ወአኀዘ ይንግሮሙ እምቀንቱ እስከ ተፍጻ ሜቱ ። ወከሠተ አፉሁ ፊልጶስ ወአኀዘ ይንግሮሙ በውእቱ መጽሐፍ እንዲል ።
ወመሀሮሙ እንዘ ይብል ።

እንዲህ ብሎ አስተማራቸው ፤ ሐተታ እስከ አሁን ያምስት ገብያ ሰው ይከተለው ነበር ከእንግዲህ ወዲህ በብፁዓን ዓዋጅ ይለያቸዋል ። ንጉሥ መንግሥቱ እስኪደላደልለት ድረስ ሌባ ወምበዴ ይከተለዋል ። መንግሥቱ ግን ከተደላደለ በኋላ ሌባ ወንበዴ ተለይ ብሎ ዓዋጅ እንዲነግር ፡ በብፁዓን ዓዋጅ ይለያቸዋል

፫ ብፁዓን ነዳያን በመንፈስ ። ሉቃ ፮ ፡ ፳ ። ብፁዓን እለ ያነድዩ ርእሶሙ ይላል ።

፫ አውቀው ከብዕል ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፣ ብዕል እንጂ የእግዚአብሔር የባሕ ርይ ገንዘቡ ነው ልኛስ ባሕርይ የሚስማማው ንዴት ነው ብለው ብዕሉም እንደ ኢዮብ እንደ አብርሃም ነው አንድም ከጥበብ ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡ ራን ናቸው ጥበብ እንጂ የእግዚአብሔር ገንዘብ ነው ለኛስ ባሕርይ የሚስማማው ድንቁርና ነው ብለው ጥበቡም እንደ ሲራክ እንደ ሰሎሞን ነው ። አንድም ከአእምሮ ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው መኰንኑ ተሰሎንቄ አፈወርቅን እንደጠየቀው ፡ ቅዱ ሳን ከበቁ በኋላ ከአእምሮ ነዳያን ነን ማለታቸው እንደምንነው አለው ፡ አንተ በሀገርህ እንደምን ትኖ ራለህ አለው ፡ ከሁሉ በላይ ነኝ አለው ። እልፍ ብለህ በቂሳርያስ አለው የምበልጣቸውም አሉ፣ የሚተካከሉ ኝም አሉ አለው ። እልፍ ብለህ ባ ቁስጥንጥንያ አለው የሚበልጡኝም አሉ የምተካከላቸውም አሉ አለው ። ዝቅ እያለ ሂደ ። እልፍ ብለህ በአንጾኪያ አለው ። ከዚያስ እንዳለሁም እንደ ሌላሁም የሚያውቀኝ የለም አለው ። ቅዱሳንም ከአእምሮ ነዳያን ነን ማለ ታቸው በበላያቸው ያለውን እያዩ ነው ብሎታል ። አንድም በመማር በማርስተማር በምናኔ በንስሐ በሃ ይማኖት ነዳያን ነን የሚሉ ንዑዳን ክቡራን ናቸው እስመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት ።

መንግሥተ ሰማያት የሳቸው ናትና ማለት መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ፡

፬ ብፁዓን እለ ይላህዉ ይእዜ ።

፬ መዝ ፻፳፭፡፮ ዛሬ የሚያዝኑ የሚያለቅሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ሐተታ ፡ የሚገባ ኀዘን የማይገባ ኀዘን አለ ። የማይገባ ኀዘን እናት አባት ሞተብኝ እኅት ወንድም ዘመድ የለኝ ርስት ጉልት ሂደብኝ ብሎ ማዘን አይገባም ። እንዳባት እንደናት ሥላሴ እንደ ወንድም እንደ እኅት መላእክት አሉና እንደ ርስት እንደ ጉልት የማታልፍ ርስት ጉልት መንግሥተ ሰማይ አለችና ፡ የሚገባ ኀዘን የራሱን ኃጢአት አስቦ የባልንጀራውን ኃጢአት አይቶ ግፍዓ ሰማዕታትን ሞተ ወልደ እግዚአብሔርን አስቦ ማዘን ይገባል ። የራስን ኃጢአት እያሰቡ ማዘን እንደ አዳም እንደ ቅዱስ ጴጥሮስ እንደ ዳዊት ነው ፡ መል ካቸው ሳይለወጥ ሳይሰቀቁ ዕንባቸው እንደ ሰንሠጋ ይወርድ ነበር ። የባልጀራውን ኃጢአት እያሰቡ ማዘን እንደ ሳሙኤል ነው እስከ ማዕዜኑ ትላሀዎ ሳሙ ኤል ለሳኦል እስመ አነ መነንክዎ ወገደፍክዎ ። ወሶበ ርእያ ለሀገር በከየ ላዕሌሃ ወሶበ ርእዮ ለዘያገ ብእ ተሀውከ በመንፈሱ እንዲል ፡ ግፍዓ ሰማዕታትን አስቦ ማዘን እንደ እስጢፋኖስ ። ወሰእስጢፋኖስሰ ነሥእዎ ዕደው ጻድቃን ወቀበርዎ ወሰሀውዎ ዓቢየ ላሐ እንዲል ። ሞተ ወልደ እግዚአብሔርን አስቦ ማዘን እንደ ዮሐንስ ነው የዕለተ ዓርብ መከራውን እያሰበ ፸ ዘመን ቁጹረ ገጽ ሁኖ ኖሯል ። አንድም ዛሬ በንስሐ የሚያለቅሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ እሙንቱ ይትፌሥሑ ፤ የኃዘን አጸፋው ደስታ ነውና ይትፌሣሑ አለ እንጂ መንግሥተ ሰማይን ይወርሳሉና ሲል ነው ።

፭ ብፁዓን የዋሀን ፡

፭ ኢሳ ፲፩፥፪ ኃደግያን በቀል የሆኑ ከየውሃት ጠባይዓዊ የደረሱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። አንድም ሰውነታችንን መክረን አስተምረን ማኖር እንደምን ይቻለናል ብለው በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን የሚኖሩ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው እስመ እሙንቱ ይወርስዋ ለምድር ።

ምድር መንግሥተ ሰማይን ይወርሳሉና ። ሐተታ ምድር አላት ይህ አልፎ በዚህ የምትተካ ስለሆነች ምድራውያን ጻድቃን የሚወርሷት ስለሆነ ። በምድር በሠናት ሥራ የምትወረስ ስለሆነች ፤ በምድር ተድላ ሥጋ እንዲፈጸም ። በመንግሥተ ሰማይም ተድላ ነፍስ ይፈጸማልና ፤ ወሥርዓተ እግዚአነሰ እሰፈወነ በብሂሎቱ ብፁዓን የዋሀን እስመ እሙንቱ ይወርስዋ ለምድር ከመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት አንጺል ።

፯ ብፁዓን እለ ይርኅቡ ወይጸምዑ በእንተ ጽድቅ ።

፯ እብዝተንማ ከተመገብን ሰውነታችንን ወስኖ ገቶ ማኖር እንደምን ይቻለናል ብለው ከሚበሉት ከሚጠጡት ከፍለው የሚራቡ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ ሁሉ ዘያነዲ ርእሶ እምነ መብልዕት ብዙኃት ውእቱ ይክል እኂዞተ ሥጋሁ እንዲል ፤ አንድም ጨርሰንማከተመገብነ መንግሥተ ሰማያትን በምን እንዋጃታለን ብለው ከፍለው ለነዳያን ሰጥተው የሚራቡ የሚጸሙ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ አንድም ከመብልዓ ኃጢአት የሚራቡ ከስቴ ኃጢአት የሚጸሙ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ አንድም ለፍቅሩ የሚሳሱ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ጽምዓት ነፍስየ ለከ እንዲል ፤ አንድም በመማር በማስተማር በሃይማኖት በምግኔ በንስሕ የሚራቡ ሰዎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ እሙንቱ ይጸግቡ ። የረኃብ አጸፋው ጽጋብ ነውና ይጸግቡ አሉ እንጂ መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ሲል ነው ይጸምዑ ባለው ዐጸፋ ይረውዩ የሚል ይገኛል ።

፰ ብፁዓን መሀርያን ፤

፰ ለሰው የሚያዝኑ የሚራሩ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። ሐተታ ምሕረት ሥጋዊ ምሕረት መንፈሳዊ ምሕረት ነፍሳዊ እለ ምሕረት ሥጋዊ ቀዶ ማል በስ ቆርሶ ማጉረስ ቢበድሉ ማሩኝታ ቢበደሉ ይቅርታ ነው ምሕረት መንፈሳዊ፤ ክፉው ምግባር በጐ ምግባር መስሎት ይዞ ሲኖር መክሮ አስተምሮ ክፉውን ምግባር አስትቶ በጐውን ምግባር ማሠራት ነው ምሕረት ነፍሳዊ ክፉው ሃይማኖት በጐ ሃይማኖት መስሎት ይዞት ሲኖር ክፉውን ሃይማኖት አስትቶ በጎውን ሃይማኖት ማስያዝ ነው ፤ አንድም ምሕረት ሥጋዊ አይሰወጥም ምሕረት መንፈሳዊ ክፉውን ሃይማኖት ክፉውን ምግባር በጎ ምግባር ሃይማኖት መስሎት ይዞት ሲኖር መክሮ አስተምሮ ክፉውን ሃይማኖት አስትቶ በጎውን ማስያዝ ክፉውን ምግባር አስትቶ በጎውን ማሠራት ነው ። ምሕረት ነፍሳዊ መጥዎተ ርእስ ነው ። ታሪክ እንደ አንጢላርዮስ እንደ እሁ ቅዱስ ይህ አንጢላርዮስ ባለጸጋ ነው ንፉግ ነው ፤ ነዳያን ሲያልፍ አይተው ይህ ጽኑ ጨካኝ ባለጸጋ ለሰው አያዝንም አሉ አንዱ እኔ ፤፫ ሰጥቶኝ በልቼ ብመጣስ ባትመጣስ ተወራርዶ ሂዷል ምግቡን አቅርቦ እጁን ታጥቦ በሚመገብበት ጊዜ ስመ እግዚአብሔር ጠራበት አንዳ ይሰጠው ተርቧል እንዳይነግው ስመ እግዚአብሔር ጠራበት ተናዶ ዳቦውን ወርውሮ ግንባሩን ገመሰው ደሙን አብሶ ዳቦውን ጎርሶ ለምልክት ጥቂት ይዞ ሄደ ። በዚህ ሌሊት ራእይ ያያል ነፍሱ ከሥጋው ተለይታ መላእክተ ጽልመት እያዳፉት ይዘዋት ሲሄዱ መላእክተ ብርሃን ሲከተሏት እናንተ ከዚህ ምን አላችሁ ሲሏቸው ምነው ትላንት ለድሃ ሰጥቶ የለም ይሏቸዋል መታው እንጂ መቼ ሰጠው አላቸው ይመስክር ተባብለው መጥተው መስክር አሉት እ ባዕል ትማልም ዘአጽገብከኒ እምጽኡከኑ ዝየ ወኢተዓውቀኒ ደም እምጽንዓ ረኃብ ብሎ መስክር ሲያስለቅቃት መላእክተ ብርሃን እጅ ሲያደርጓት አየ ፤ ሲነጋ በዚህ ዓለም ሳሉ በገንዘብ ቢያውቁበት እንዲህ ያለ ጥቅም አለን ብሎ ነዳያንን ሰብስቦ ያለ ገንዘቡን ጨርሶ መጽውቶ ሲሄድ ነዳያን ከመንገድ አገኙት ገንዘብ ትሰጣለህ ቢሉን መጥተን ነበር አሉት ቀድም ብላችሁ መጥታችሁ ቢሆን ከፍየ እሰጣችሁ ነበረ አሁንማ ጨርሻለሁ አላቸው፤ እንደምን እንሁን እሉትእኔን ሸጣችሁ ተካፈሉ አላቸው ለ፴ ወቂት ሸጠውታል ፤ ከተሸጠበት አገር ከብት ያውላል ማታ የሚያልበው ደም ይሆናል በዚህ ሰው እጅ ለመረዳት አልበቃችሁም ለማለት ሲያርስ ውሎ ማታ ሣሩን እለምልሞ ውኃውን አፍልቆ ይመግባቸዋል በዚህ ዕጹብ ዕጹብ ሲሉ ከተወለደ ጀምሮ ተናግሮ የማያውቅ ድዳ ሰምቶ የማያውቅ ደንቆሮ ነበር እፍ ቢለው ድዳው ተናግሯል ደንቆሮው ሰምቷል በዚህ ዕጹብ ዕጹብ ሲሉ ተሰውሯል ።

እኑ ቅዱስ በአሕዛብና በክርስቲያን መካከል ባለች በወሰን አገር ኤጲስቆጶስነት ተሹሞ ይኖራል። አሕዛብ ክርስቲያንን እየማረኩ ሲወስዱ ገንዘብ

እየሰጠ ይመልሳቸዋል እንዲት ድኃ ልጁዋ ተማሬ ከባት መዋታ ገንዘብ ስጠኝ አለችው ገንዘቤን ጨርሻለሁ እኔን ተከተሽ ልጅሽን መልሺ አላት ። እሱን ተከታ ልጁዋን መልሳለች ከሄደበት አገር የንጉሡ ልጅ ሞተችበት ኃዘን እንደጸናበት አይቶ ልጅህን ባነሣልህ ምን ባደረግህልኝ አለው የመንግሥቴንም እኩሌታ቉ ቢሆን እሰጥሃለሁ አለው ይህንንስ አልሻም ከኔም አስቀድሞ ከኔም በኋላ የተማረኩትን ክርስቲያን ትሰጠኝ እንደሆነ ሳሥን ላልህ አለው ፤ ይሁንልህ አለው እሥን ሥ ቶቶት ከሱም አስቀድሞ ከሱም በኋላ የተማረኩትን ክርስቲያን ይዞ ወጥቷል ፤ በዚህም ጌታን መስሎ ታል ጌታ እሱ ሰው ሳይሆን ከሱ አስቀድሞ የነበ ሩትን ሰው ከሆነም በኋላ ቢአል የወረዱትን ፭ድ ቀን በዕለተ ዓርብ ይዞ ስመውጣቱ ምሳሌ እንድም በንስሐ ለሰው የሚያዝኑ ቀሳውስት ንዑዳን ክቡራን ናቸው ።

እስመ ሎሙ ይምህርዎሙ ፤

ለሳቸውም ሥላሴ ያዝኑላቸዋል ይራሩላቸዋልና ።

፰ ብፁዓን ንጹሐን ልብ ፤ መዝ፡ ፳፫ ፤ ፬ ።

፰ ከንጹሐን ልቡና የደረሱ እንድም በንስሐ ከኃጢአት ንጹሐን የሆኑ ፥ አንድም ከቂም ከበቀል ንጹሐን የሆኑ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ እስመ ዘያነብር ቂመ ውስተ ልቡ ኢመክፍት ጸሎቱ ቅድመ እግዚአብሔር ጸሎቱ ለመስተቀይም ከመ ዘርዕ ዘወድቀ ማእከለ አሰዋክ እንዲል ።
እስመ እሙንቱ ይሬእይዎ ለእግዚአብሔር ።
ሰውነታቸው ጸርቶላቸው እግዚአብሔርን ያዩታልና እስመ በአንጽሖ መንፈስ ርእይዎ ነቢያት ለእግዚአ ብሔር ወተናጸሩ ገጸ በገጽ እንዲል ። እስካሁን ይሬእይዎ እላለ አሁን ይሬእይዎ አለ ምነው ቢሉ በኒህ ማየት የሁሉን መናገር ነው ።

፱ ብፁዓን ገባርያነ ሰላም ።

፱ እብነት አለ ይገብሩ ሰላመ ይላል ፤ እቀበ ቱን ወጥተው ቍልቍለቱን ወርደው ሰውን ከሰው ጋራ የሚያስታርቁ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ፤ እንደ መልከ ጼዴቅ እንደ ሊቀ ሀገር የመልከ ጼዴቅ በጳው ሎስ ታውቋል፤ሊቀ ሀገር ሦስት ልጆች ነበሩት።አንተ ይህን ሥራ አንተ ይህን ሥራ ብሎ እዝዞ እሱማን ከማን ተጣልቷል እያለ እየዞረ ሲያስታርቅ ይውል ነበር ። እንድም ሰው ሰርቆ ቀምቶ ከፈጣሪው ጋራ የሚጣላ የሚበላው የሚለብሰው እንጂ ቢያጣ ነው ብለው የሚበላውን የሚለብሰውን ሰጥተው ከእግዚአብሔር ጋራ የሚያስታርቁ ባለጠጎች ንዑዳን ክቡራን ናቸው እንድም ሰውን በንስሐ ከእግዚአብሔር ጋራ የሚ ያስታርቁ ቀሳውስት ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። እስመ እሙንቱ ውሉደ እግዚአብሔር ይሰመዩ ፥

የእግዚአብሔር ልጆች ይባላሉና እስካሁን ውሉደ እግዚአብሔር እሳለም አሁን እንዲህ ማለቱ ስለምን ቢሉ በመስሉት ጌታ በመስቀል ተሰቅሎ ወደ መቃ ብር ወርዶ ሰውን ከእግዚአብሔር እንዳስታረቀ እሳቸውም እቀበቱን ወጥተው ቍልቍለቱን ወር ደው በማስታረቃቸው ይመስሉታልና በኒህ መም ሰል የሁሉንም መምሰል መናገር ነው ።

፲ ብፁዓን እለ ይሰደዱ በእንተ ጽድቅ። ፩፡ጴጥ፡ ፪ ፡ ፳ ፫ ፡ ፲፬ ፬ ፡ ፲፬

፲ በመማር በማስተማር በምናኔ በንስሐ በሃይማኖት እገራቸውን ጥለው የሚሰደዱ ንዑዳን ክቡራን ናቸው ። እስመ ሎሙ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት

መንግሥተ ሰማያትን ይወርሳሉና ፡ በመጀመሪያ ተናግሯት ውስጥ ለውስጥ ቢናገራት መጥቶ ነበርና በ፰ኛው እንሣት በመጀመሪያ ማንሣቱ ለአዳም እንደ ተሰጠች ለማጠየቅ በ፰ኛው ማንሣቱ በ፰ኛው ሽህ ለሁሉ እንድትሰጥ ለማጠየቅ ።

፲፩ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይሰድዱክሙ ።

፲፩ ከሀገራችሁ አስወጥተው ቢሰዷችሁ ንዑ ዳን ክቡራን ናችሁ ወይዘነጕጕክሙ ።
ዓብዳን ዝንጉዓን ጊጉያን ርጉማን ሰሑታን ቢሏችሁ ወይነቡ ኵሎ እኩየ ላዕሌክሙ እንዘ ይሔስው በእ ንቲአየ ።
በኔ ስም ስላመናችሁ በኔ ስም ስለተጠራችሁ በኔ ስም ስላስተማራችሁ ፡ በሐሰት ክፉውን ነገር ቢናገ ሩባችሁ ።

፲፪ ተፈሥሑ ወተኀሠዩ ።

፲፪ ፈጽሞ ደስ ይበላችሁ ።

እስመ ብዙኅ እሤትክሙ በሰማያት ።
ዋጋችሁ በኔ ዘንድ ፍጹም ነውና ካሥሩ ቃላት እንጸ ጽሮ ዐሥሩን ብፁዓን ተናገረ ዐሥረኛውን በዮሐንስ ያመጣዋል ። ሙሴ ዘጠኙን ቃላት በአሪት ዘፀአት ተናግሮ ዐሥረኛውን በአሪት ዘሌዋውያን እንዳመ ጣው ።
እስመ ከማሁ ሰደድዎሙ ለነቢያት እለ እምቅድሜ ክሙ ።
ከናንተ አስቀድሞ የነበሩ ነቢያትን ከሀገራቸው እስ ወጥተው ይሰዷቸው ነበርና ፤ ይሰድዱክሙ ሻለው እንድም መከራስ እንቀበል ብንል ማን እብነት ይሆነናል ትሉኝ እንደሆነ ከናንተ አስቀድሞ የነበሩ ነቢያትንም እንጂ ነቢያትንም አኮን ከሀገራቸው እስወጥተው ይሰዷቸው ነበር ፥ እኒያ እብነት ይሁኗ ዋችሁ ።
በእንተ ሐዲስ ኪዳን ተአርዮታ ምስለ ብሉይ ፥
፲፫ አንትሙ ውእቱ ጼው ለምድር ማር ፱ ፶ ሉቃ ፲፬ ፡ ፴፬ ።

፲፫ በዚያውም ላይ የሰው አብነቱ እናንተ ናችሁ ወእመሰ ጼው ለስሐ በምንት እንከ ይቄሰምዎ ።

ጨው ጣዕም ባይኖረው በምን ያጣፍጡታል ፣ ራሱን እንድም አፍርጁን ሽንኩርቱን በምን ያጣፍጡታል ፤ አልቦኬ እንከ ዘይበቍዕ ።

የሚረባው የሚጠቅመው የለም ለአፍርጁ ለሽን ኩርቱ ፣ እንድም ለራሱ የሚያገኘው ረብሕ ጥቅም የለውም ።

ዘእንበለ ዘይገድፍዎ አፍአ ።
አፍአ አውጥተው ይጥሉታል ወይከይድዎ ሰብእ በእ ገሪሆሙ ሰዎች በእግራቸው ይጠቀጥቁታል እንጂ ፤ ሐተታ ቢከቡት ይናዳል ቢንተራሱት ራስ ይመል ጣል ከተክል ቦታ ቢያደርጉት ተክል ያደርቃል ብለው እንድም አንትሙ ውእቱ ጼው ለም ድር የሰው አብነት እናንተ ናችሁ ፡ እናንተ አብነት ካልሆናችሁ ማን አብነት ይሆንላችኋል ፣ እንድም ለሕዝቡ እናንተ አብነት ካልሆናችኋቸው ማን አብነት ይሆና ቸዋል ። ለሕዝቡ የምትረቧቸው የምትጠቅሟቸው የለም ። እንድም ለራሳችሁ የምታገኙት ረብሕ ጥቅም የለም ። ዘእንበለ ዘይገድፍዎ አፍአ ፥ ሕዝቡ ከልቡ ናቸው በአፍአ ያወጥዋችኋል ፣ ወይከይድዎ ። በልቡናቸው ይንቅፋችኋል እንጂ ። እንድም ሥላሴ ከመንግሥተ ሰማይ አፍአ ወደምትሆን ወደ ገሃነም ያወጧችኋል እንጂ ፤ ወይከይድዎ ፥ አጋንንትም መከራ ያጸኑባችኋል እንጂ ። በማደሪያቸው ሰብእ አላቸው ። እንድም በቁሙ ሰዎች ይጠቀጥቋችኋል ቅዱስ ጊዮርጊስ እንዳስነሣው ፍቁራ እስነሥቶ ወደ፡ት ነበርሀ ቢለው ከኤጲስ ቆጶሳችሁ ላይ ነበርሁ ብሏል

፲፬ አንትሙ ውእቱ ብርሃኑ ለዓለም ።

፲፬ አብነትነታቸው በብዙ ወገን ነውና ደገ መው ፤ የሰው አብነቱ እናንተ ናችሁ ።
ኢትክል ተከብቶ ሀገር እንተ ተሐንጸት መልዕልተ ደብር ፣ ከተራራ ላይ የተሠራች መንደር መሰወር አይቻላትም ።

፲፭ ወኢየኃትው ማኅቶተ ከመ ያንብርዋ ታሕተ ቀፈር ። ማር ፬ ፥ ፳፩ ፥ ሉቃ ፡ ፰ ፥ ፲፮ ።

፲፭ እንቅብ ቅርጫት ሊደፉባት መቅረዝ የሚ ያበራ የለም ። እላ ያነብርዋ ዲበ ተቅዋማ ወታበርህ ለኵሉ እለ ውስተ ቤት ከመቅረዝ ላይ አኑረዋት ከቤት ላሉ ሁሉ ታበራ ዘንድ ነው እንጂ ።

፲፮ ከማሁ ይብራህ ብርሃንክሙ በቅድመ ሰብእ ። ፩፥ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲፪ ።

፲፮ እንዲህም ሁሉ ሥራችሁ በሰው ፊት ይሁን ከመ ይርአዩ ምግባሪክሙ ሠናየ ወይሰብሕዎ ለአቡ ክሙ ዘበሰማያት ።

በጐ ሥራችሁን አይተው ሰማያዊ አባታችሁን ያመ ሰግኑት ዘንድ እንዲህ ያሉ የትሩፋት አበጋዝ ያልነ ማልን ብለው ፥ ሐተታ ፥ ምነው በሚያመጣው ጸሊ በኀቡእ ይል የለም ቢሉ አብነት የሚሆኑበትን ተገ ልጸው ይሠሩታል አብነት የማይሆኑበትን ተሰውረው ይሠሩታልና እንዲህ አለ ፤ እንድም በተራራ ላይ የታነጸች መንደር ልሰወር ብትል መሰወር እንዳይ ቻላት የተራራው ክፍታ እንዲገልጻት ። በመቅረዝ ላይ ያለች ፋና ልሰወር ብትል መሰወር እንዳይቻላት የመቅረዙ ክፍታ እንዲገልጻት ፤ እናንተም ሥራውን አብዝታችሁ ሥሩት ግድ በተአምራት ይገልጻችኋል ሲል ነው ። ደብር ተቅዋም አንድ ወገን ሀገር ማኅ ቶት አንድ ወገን ፣ ደብር ተቅዋም ሥጋ ሀገር ማኅቶት ነፍስ ፣ ከሥጋ ጋራ የተዋሐደች ነፍስ ሥራ ሠርታ ልትገለጽ ነው እንጂ ፣ ተሰውራ ልትቀር አይደለም እንድም ደብር ተቅዋም ሰውነት ሀገር ማኅቶት አእ ምሮ ጠባይዕ በሰውነት ያለ አእምሮ ጠባይዕ ሥራ ሠርቶ ሊገለጽ ነው እንጂ ተሰውሮ ሊቀር አይደለም እንድም ደብር ተቅዋም ሥጋ ሀገር ማኅቶት መለኮት ከሥጋ ጋራ የተዋሐደ መለኮት አስተምሮ ታምራት አድርጐ አምላክነቱን ሊገልጽ ነው እንጂ ፣ ተሰ ውሮ ሊቀር አይደለም ። እንድም ደብር ተቅዋም መስ ቀል ሀገር ማኅቶት ጌታ በመስቀል የተሰቀለ ጌታ ሙቶ ተነሥቶ አምላክነቱን ሊገልጽ ነው እንጂ ሙቶ ሊቀር አይደለም ፣ እንድም ደብር ተቅዋም አሪት ሀገር ማኅቶት ወንጌል በኦሪት ላይ የተሠራች ወንጌል ባደባባይ ተገልጻ ልትነገር ነው እንጂ ። ተሰውራ ልትቀር አይደለም ። እንድም ደብር ተቅ ቀም ሕዝቡ ሀገር ማኅቶት ኤጲስ ቆጶስ በሕዝቡ ላይ የተሾመ ኤጲስ ቆጶስ ካደባባይ ወጥቶ ጉባኤ ሰርቶ ሕዝቡን ሊያስተምር ነው እንጂ ፣ ባዳራሽ ገብቶ አልፍኝ ተከቶ ተሰውሮ ሲባላ ሲጠጣ ሊውል አይ ደለም

፲፯ ኢይምሰልክሙ ዘመጻእኩ እሥዓሮሙ ለአሪት ወለነቢያት ፣ ብፁዓን ብፁዓን እያለ ሲያስ ተምር ሰምተው አሪትን ነቢያትን እንጂ ሊያሳልፋ ቸው መጥቷል እንዲሉት ዐውቆ አመጣ ። እንዲሉ ትም ዐውቆ ማምጣት ልማድ ነው ። ትውልደ አራ ዊተ ምድር ቢላቸው አብርሃምን ያሀል አባት ሳለን ትውልደ አራዊተ ምድር ይለናል እንዲሉት ዐውቆ ኢይምሰልክሙ ዘታመስጡ በብሂለ አብ ብነ አብ ርሃም እንዳለ ፣ ወኢትሁብ ለጻድቅ ይርአይ ሙስና ሙስና ቢላቸው ይህንማ ዳዊት ለራሱ የተናገረው አይደለም እንዲሉት ዐውቆ ታበውሑነሁ እ.ሰብእ ንንግርከሙ ክሡተ በእንተ ዳዊት ርእሰ አበው ከመሂ ሞተ ወተቀብረ ወኀቤነ ሀሎ መቃብሪሁ እስከ ዮም እንዳለ ፣ ከዚህም እንዲህ አለ ፤

፲፯ ኦሪትን ነቢያትን ላሳልፋቸው የመጣሁ አይምሰላችሁ ኢመጻኩ ይላል ፤ ላሳልፋቸው አል መጣሁም ።

ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ እፈጽሞሙ ።
ፍጹማን ላደርጋቸው ነው እንጂ ፤ ኢትቅትልን በኢታምዕዕ ኢትፍቱን በሀርእያ ላጸናቸው ነው እንጂ ወፈጸመ ሕገርትዕ በሕገ ትሩፋት እንዲል ።

፲፰ አማን አማን እብለከሙ እስከ አመ የሐልፍ ሰማይ ወምድር የውጣ እንተ አሐቲ ኀርመታ ወአ ሐቲ ቅርጸታ ኢተሐልፍ እምኦሪት ወእምነቢያት እስከ ሶበ ኵሉ ይትገበር ወይከውን ። ሉቃ፤፲፮፤፲፯ ።

፲፰ ሰማይ ምድር እስኪያልፍ ይህ ሁሉ እስኪ ሆን ይህ ሁሉ እስኪደረግ ድረስ ሥርዓቷ ጽፈቷ አን ዲት የምትሆን ኢትፍቱስ እንኳ ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ አታልፍም ብየ እንዳታልፍ በውነት እነግ ራችኋለሁ ዮድ ለአሌፍ ዐሥረኛ እንደ ሆነ ኢትፍ ቱም ለኢታምልክ ዐሥረኛ ናትና ። አንድም አሰራ ረሂ አቀራረጹዋ እንድ የምትሆን ዐሥርቱ ቃላት ሁሉ ሲያልፍ ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ እንዳታልፍ አታልፍም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ፤ በሀገራ ቸው ፲ቱ ሲሉ የውጣ ይላሉ አንዲት ጭራ ናት ዕዝል ቅጽል የላትም ። በኛም ፲ አንዲት ጭራ ናት ዕዝል ቅጥል የላትም ። አንድም ለኛ ፊደል ዐሥረኛው ተ ነው፤መስቀላዊት ሕገ ክርስቶስ ወንጌል ከኦሪት ከነቢያት ተለይታ ወደሰው ልቡና አትገባም ብየ እነግራችኋለሁ ። ወኀሰፈት ሰንበት እንዲል ፤ አብራ ትነገራለች እንጂ ማለት ነው ፤ ውኀጣ የሚል አብ ነት ይገኛል ። የውጣ ማለት ነው ። በዳር ሮ ሎ ብሎ ይገኛል ፡ ሮ ቢል ከመንግሥተ ሮም የምትበልጥ ሎ ቢል ልዕልት የምትሆን ወንጌል ከኦሪት ከነቢ ያት ተለይታ ወደሰው ልቡና አትገባም ብየ እን ዳትገባ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፲፱ ዘኪ ፈትሐ አሐተ እምእላ ትእዛዛት እንተ ተሐጽጽ ወይሜህር ከመዝ ለሰብእ ሕጹጸ ይከውን በመንግሥተ ሰማያት ። ያዕ፤ ፪ ፤ ፲ ።

፲፱ ካ፲ቱ ቃላት አንዲቱ ታናሽ ናት ብሎ ለራሱ የሚሠራ ለሌላው የሚያስተምር ውፁእ ሲል ነው ከመንግሥተ ሰማያት የወጣ ይሆናል ፡ መኑ አብኦ ለዝ እግዚአብሔር አሕጸጾ ወሐጽ መንፈቅ ወየሐጽጾሙ እመንግሥተ እቡሁ እንዲል ፤ ወዘሰ ይገብር ወይሜህር ከመዝ ለሰብእ ውእቱ ዐቢየ ይከ ውን በመንግሥተ ሰማያት፤ከዐሥርቱ ቃላት አንዲቱ ደግ ናት ብሎ ስራሱ የሚሠራ ለሌላው የሚያስተ ምር ግን ለመንግሥተ ሰማያት ባለቤት ይሆናል ። አንድም ይከውን ሕጹጸ ፤ እንደ ጨረቃ እንደ ንኡስ ኮከብ ይሆናል ፤ ይከውን ዐቢየ እንደ ፀሐይ እንደ ዐቢይ ኮከብ ይሆናል ።

፳ ናሁ እብለከሙ ከመ ለእመ ኢፈድፈደ ጽድ ቅክሙ እምጸሐፍት ወፈሪሳውያን ኢትበውኡ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ። ሉቃ ፤ ፲፩ ፤ ፴፱ ።

፳ በቁሙ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ናቸው ብሎ ፤ ሥራችሁ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ሥራ ካልበለጠ እያፈድፈድክሙ ጽዲቀ አብዝታችሁ ሥራ ካልሠ ራችሁ መንግሥተ ሰማያት አትገቡም ብየ እንዳት ገቡ በውነት እነግራችኋለሁ ። እኒያም አልገቡ እና ንተም አትገቡ ማለት ነው ። አንድም ደጋጎች እለ አብርሃም እለ ሙሴ እለ ዳዊት ናቸው ብሎ ሊቁ ወስዶታል ብሎ በሥራ መበላለጥ ከሌለ በክብርም መበላለጥ የለም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ። ሥራው ምንድ ነው ቢሉ እፍቅሮ ጸላዕት ተዐፍዖ መል ታሕት መንና ጥሪት ነው ። ይህንማ እነሱስ አድር ገውት የለም ለእመ ርኢከ እድግ ፀላዒከ ዘኃየሎ ጾሩ ኢትትዓደዎ አላ እስተልዕል ምስሌሁ እንዲል ዘፀ ፳፫፤፭ ፡ አድርገውት የለም ቢሉ መጥዎተ ርእስ ነው ይህንስ አድርገውት የለም ሙሴ እምትጥስዮሙ ለእሉ ሕዝብከ ጠስየኒ እመጽሐፈ ሕይወትከ ብሏል ዘፀ ፴፪፤፲፩ ፡ ዳዊትስ ምንተ ገብሩ እሉ አባግዕ እንዘ ኖላዊሆሙ አነ ዘአበስኩ ፤ ዳዕሙ ለትረድ እዴከ ላዕሌየ ወላዕለ ቤተ እቡየ ብሎ የለም ቢሉ ፤ እኒያ ለዘመዶቻቸው ነው ፤ እናንተ ግን ለሁሉ አድርጉት ሲል እኒያ አስበውት ቀርቷል እናንተ ግን አድርጉት ሲል ነው ፤ ዳግመኛ ሕግ ሁኖ ስላልተጻፈ ተጽፎ የለም ቢሉ ገብሩ ተብሎ ተጽፏል እንጂ ግበሩ ተብሎ ተጽፏልን ፤ በሥራም ካልተበላለጣችሁ ማለቱስ እንደ ምነው ቢሉ ለእኒያ አብነት አልነበራቸውም ለኒህ ግን አብነት ጌታ አላቸውና ፤ እኒያ በልጅነት አልታደሱም እኒህ ግን በልጅነት ታድሰዋልና ። ለኒያ አጋዥ አልነበራቸውም ለኒህ ግን አጋዥ ሥላሴ መላእከት መጻሕፍት መምራን አሏቸውና ።

፳፩ ሰማዕከሙ ዘተብህለ ለቀደምትከሙ ኢት ቅትል ነፍሰ ።

፳፩ ለቀደሙ ሰዎች ነፍስ አትግደል የተባ ለውን ዘጸ ፳፤፲፫ ዘከመ ተብህለ ሎሙ እንደተባለላቸው ዘይቤልዎሙ ያሏቸውን ዘከመ ይቤልዎሙ እንዳሏቸው ሰምታች ኋል ።
ወዘሰ ቀተለ ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ።
ነፍስ የገደለ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል
የተባለውን ሰምታችኋል ።

፳፪ ወአንሰ እብለከሙ ኵሉ ዘያምዕዕ እኅዋሁ በከንቱ ረስሐ ውእቱ ለኵነኔ ።

፳፪ እኔ ግን ወንድሙን በከንቱ ያሳዘነ ሁሉ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል ብየ እነግራ ችኋለሁ ፤ ሐተታ ኦሪትንስ ወንጌልንስ የሠራ እሱ አይደለም እኔ ግን

ማለቱ ስለምን ቢሉ ጌታ ሁን እንዳሻህ ሁን እንዲሉ ይህስ በጌታ የለበትም ብሎ ኦሪትን በሙሴ በኢያሱ አድሮ ሠርቷታል ወንጌልን ግን እሱ ሰው ሁኖ ሠርቷታልና ፤ እንድም ለቀደሙ ሰዎች እንዲህ ብየ ነበር ዛሬ ግን እንዲህ እልሁ ። እንድም እሚሄኒ ዮምኒ ያን ጊዜ እንዲህ ብየ ነበር ዛሬም እንዲህ እልኩ ። በከንቱ እለ ቦ መዓት ዘበርትዕ እንዲል ፤ የሚገባ ቁጣ አለና ሕፃናት ያል ተማሩትን እንዲማሩ የተማሩትን እንዳይገድፉ መናፍቃን እንዳይሠለጥኑ ሃይማኖት እንዳይጠፋ ክህደት እንዳይሰፋ ፥ እንድም በከንቱ ያለውን መፍ ቀርያን መዓት የጨመሩትን ነው በሐጌ መጽሐፍ ፪ ፰ ፥ ዝወርቅ ወዝ ብሩር ዘዚአየ ባለው መፍቀርያን ብሩር ወለዘፈቀድኩ እሁቦ ባለው እንደጨመሩበት ወዘሂ ይቤሎ ኅሥር ዘጸርቅ ረሰሐ ።

ወንድሙን ጨርቅ ለባሽ አባተ ታናሽ ብሎ የሰደበ በደለ ፤
ወይትኴነን በዐውድ
በዐደባባይ ይፈረድበታል ።
ወዘሂ ይቤሎ ለእኁሁ ዓብድ ረስሐ ውእቱ ።
ወንድሙን ዲዳ ደንቆሮ ያለው እሱ በደለ ።
ወይትኴነን በእሳተ ገሃነም ።

በእሳተ ገሃነም ይፈረድበታል ሐተታ ወንድሙን ጨርቅ ለባሽ አባተ ታናሽ ቢለው ባደባባይ ፤ ድዳ ደንቆሮ ቢለው በገሃነም ይፈረድበታል አለ ምነው ቢሉ ፥ ከተፈጥሮተ ሥጋ ተፈጥሮተ ነፍስ እንዲበልጥ ከስድቡም ስድቧ ይበልጣልና ፥ ከፍዳውም ፍዳውን አበለጠ ፤ እንድም በዓውድ ገሃነም በገሃነም ዓውድ ያሰነው።በአክብርዎ ፍርሀዎ በፍርሀዎ አክብርዎ እን ዳለ ። ይህንም ሊቁ ዘለ ፀረፈ ላዕለ ለብእ ጸረፈኬ ላዕለ እግዚአብሔር ብሎ ወስዶታል ። መጽሐፉን አይቶ መንቀፍ ጸሐፊውን ሕንጻውን አይቶ መንቀፍ ሐናጺውን መንቀፍ እንደሆነ ፍጥረቱንም አይቶ መንቀፍ እግዚእብሔርን መንቀፍ ነውና ።

፳፫ ወእምከመኬ ታብውእ መባዓከ ውስተ ምሥ ዋዕ ወበህየ ተዘከርከ ከመ ቦ እኁከ ዘተኃየሰከ ።

፳፫ መባህን ለቤተ እግዚአብሔር በምትሰጥ በት ጊዜ እንተ ወንድምህን የነቀፍህበት ፥ ዘተኃየ ሰከ እሱ እንተን የነቀፈበት ነገር እንዳለ ብታስብ ።

፳፬ ኅድግ ህየ መባዓከ ቅድመ ምሥዋዕ ።

፳፬ መባውን ከደጇ ስላም አኑረህ ወሑር ቅድመ ተኳነን ምስለ እኁከ ።

አስቀድመህ ከወንድምህ ተወቃቅሰህ ታረቅ ።
ወእምዝ ገቢአከ አብእ መባዓከ፥ ከዚህ በኋላ ተመል ስህ መባህን ስጥ ። ሰጥቶ ቢሄድ መባው እንኳን የገ ባልኝ እንጂ ብሎ ዕርቁ በቀረ ነበርና ፤ ይዞ ወደ ቤቱ ተመልሶ ቢሆን ዕርቁም መባውም በቀረ ነበርና ልብ እንዲቀረው ከእዳሪ እኑራለሁ ብሎ ፈጥኖ ታርቆ እንዲመለስ እንዲህ አለ እንድም ወእምከመኬ ብለህ መልስ ጸሎት በምትጸልይበት ጊዜ የነቀፈህ ወንድ ምህ የነቀፍከው ወንድምህ እንዳለ ብታስብ ጸሎቱን ትተህ ሂድ አስቀድመህ ከወንድምህ ተወቃቅሰህ ታረቅ ከዚህ በኋላ ተመልሰህ ጸሎትህን ጸልይ ። በቂም በበቀል ሁኖ የጸለዩት አይረባም አይጠቅም ምና እስመ ዘያነብር ቂመ ውስተ ልቡ ኢይውክፍት ጸሎቱ ቅድመ እግዚአብሔር ጸሎቱ ለመስተቀይም ከመ ዘርዕ ዘወድቀ ማእከለ አስዋክ እንዲል ።

፳፭ ኩን ጠቢበ ለዕድውከ ፍጡነ እንዘ ሀሎከ ምስሌሁ ውስተ ፍኖት ።

፳፭ በመንገድ ከሱ ጋራ ሳለህ በባላጋራህ ፊጥ ነህ ዕወቅበት ታረቅ በፍኖት ብሎ በሉቃስ ያቀና ዋል ።

ከመ ኢይመጡከ ዕድውከ ለመኰንን
ባላጋራህ ለዳኛ አሳልፎ እንዳይሰጥህ ።
ወመኰንን ይሜጥወከ ለወዓሊሁ ።
ዳኛውም አሳልፎ ለሎሌው ይሰጥሃል ።
ወወአሊሁ ይሞቅሐከ ።
ሎሌውም ያግዝሃል ።

፳፮ አማን እብለከ ከመ ኢትወፅእ እምህየ እስከ ሶበ ትሜልጥ ደኃሪተ ገመለ ዘሳዕሌከ ።

፳፮ ሌላው ገንዘብህስ ይቅርና ሰንኪቶ የምት ባል ቀለበትህን እስከምስጠት ደርሰህ ፤ እንድም ገመሰ ደኃሪት ይላል ፤ የታናሽ ጣትህን ቀለበት እስከ መስጠት ደርሰህ ከግዞት ቤት አትወጣም ብየ እንዳ ትወጣ በውነት እነግርሃለሁ ። እንድም ኩን ጠቢበ ብለህ መልስ በዚህ ዓለም ሳለህ በባለጋራህ በዲያብ ሎስ ዕወቅበት ። ይህን ዓለም ፍኖት አለው በመን ገድ እንዱ ሲያልፍ እንዱ ሲተርፍ እንደሆነ በዚህም ዓለም እንዱ ሲያልፍ እንዱ ሲተርፍ ነውና ። ባለ ጋራህ ዲያብሎስ ለጌታ አሳልፎ እንዳይሰጥህ ። ጌታም አሳልፎ ለዲያብሎስ ይሰጥሃል ። ዲያብሎስ ያግዝሃል ። ወዓሊሁ አለ የግድ ነው የፈቃድ አይደ ለም ። ሥራ ሠርተህ ያገኘኸው ጸጋ ክብር ይቅርና ባርባቀን ያገኘኸውን ልጅነት እስከ ማጣት ደርሰህ ከገሃነም አትወጣም ብየ እንዳትወጣ በውነት እነግ ርሃለሁ ። እንድም ፥ በዚህ ዓለም ሳለህ በባለጋ ራህ በፈቃደ ሥጋህ ፈጥነህ ዕወቅበት ። ባላጋራህ ፈቃደ ሥጋ አስፈርዶ ለጌታ እንዳይሰጥህ ። ጌታም አሳልፎ ለዲያብሎስ ይሰጥሃል ፤ ዲያብሎስ ያግዝሃል አማን እብለከ ። በነቢብ በገቢር በሠራኸው ኃጢ አት ቀርቶ በሐልዮ በሠራኸው ኃጢአት ተፈርዶብህ ከገሃነመ እሳት አትወጣም ብየ እንዳትወጣ በውነት እነግርሃለሁ ። ከሐልዮ ኃጢአት የሚነጻ አለን ቢሉ

የሚየሲዝ ሐልዮ የሚያሲዝ ሐልዮ አለ ። የሚያሲዝ ሐልዮ አስርቃለሁ አቀማለሁ ብሎ ሂዶ ሰው ነቅቶ በት ውሻ ጩሆበት እጥር ጠንቶበት ቢመለስ ያሲዛል ፤ የማያሲዝ ሐልዮ አስርቃለሁ አቀማለሁ ብሎ ይሄዳል ከመንገድ ሲደርስ ፈጣሪየ ቢፈርድብኝስ ብሎ የተመለሰ እንደሆነ ይህ አያሲዝም ። አንድም ሁሉም ያሲዛል ለዚህ ቅሉ ጥቂት ቀኖና ያሻዋል በሰይጣን ጸር ተወግቷልና ፤ ሁለት ሰዎች ከስልፍ ይገባሉ ሁለቱ ሁሉ ተወግተው ይመለሳሉ አንዱ ይሞታል አንዱ ይድናል ከዳነው ላይ እትራት ይጠፉልን ፤ ይህም በአቡነ እንጦንስ ታውቋል በማሞቱ በት ጊዜ መላእክተ ጽልመት ቀረቡ መላእክተ ብርሃን መጥተው ከዚህ ሰው ምን አላችሁ አሏቸው ፤ ምነው ያስ የሐልዮው አሏቸው ከቶብ በኋላ ነው ከቶብ በፊት አሏቸው ከቶብ በፊት ነው እንጂ ከቶብ በኋላማ በእንጦንስ ምን ተገኝቶበት አሉ ። ያማ በቶብ ታርቶበት የለም ወግዱ ብለዋቸዋል ።

፳፯ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኢትዘምው ። ዘፀ ፳ ፡ ፲፬ ።

፳፯ ለቀደሙት ሰዎች አትስስኑ የተባለውን ሰምታችኋል ።

፳፰ ወአንሰ እብለክሙ ኵሉ ዘርእያ ለብእሲት ወፈተዋ ወድአ ዘመወ ባቲ በልቡ ።

፳፰ እኔ ግን ቤትን ያየ ሁሉ ፈጽሞ በደለ ብየ እነግራችኋለሁ ርእይን መከልከሉ ነው ቢሉ አዎን እርቆ ማጠር ነው ፤ አንድም ፈተዋ ያለውን ይሻል አይቶ ባገኘኋት ቢል ።

፳፱ እመኒ ዓይንከ ዘየማን ታስሕተከ ምልሖ ወግድፍ እምላዕሌከ ማር ፱ ፡ ፵፯ ፤ ማቴ ፲፰ ፡ ፱ ።

፳፱ ቀኝ ዓይንህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆን ብህ ከንተ አውጥተህ ጣላት ።

እስመ ይኄይስከ ነቋሪከ ትባእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት እምትባእ ውስተ እሳተ ገሃነም ምስለ ክ፪ ሆን አዕይንቲከ ፡ ዛሬ ሁለት ዓይን ኑሮህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ በዚህ ዓለም ሳለህ ከሁለት ዓይንህ አንዱ ጠፍቶ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን ስምአን ስፉዬ አሣዕን ፤ አንዲት ሴት ወይዘሮ መጥታ ጫማ ስፋልኝ አለችው ሰፍቶ ሰጣት እየተመላለሰች አስችገረችው ጫማውን ነው ስፍቶ ስጥቸሻለሁ ምን ያመላልስሻል አላት ፤ ይህ ሁሉ ምክንያት ነው አንተን ብወድህ ነው አለችው በምን ነገር አላት ፤ መልክ መልካም ነህና አለችው ምኔ መልካም ነው ቢላት ሁለንተናህ መልካም ነው ይልቁንም በዓይንህ ይጸናብኛል አለችው ትወጅዋለሽ አላት አዎን አለችው ። ይህማ ምን ቁም ነገር አለው ውጋ አይደለም ብሎ በያዘው መንጉል አውጥቶ ሰጥቷታል።

፴ ወእመኒ እዴከ ዘየማን ታስሕተከ ምትሯ ወግድፋ እምላዕሌከ ።

፴ ቀኝ እጅህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆንብህ ቁርጠህ ጣላት ። እስመ ይኄይስከ ይታጐጐል አሐዱ እምአባልከ እምዘ ኵሉ ሥጋከ ይትወደይ ውስተ እሳተ ገሃነም ።

በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ሳይጐል ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ጎድሎ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ። ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ። ከዚያው ግን አባስ ካህነ ሮሜ አትናቴዎስ ሊቀ ጳጳሳት ዘሀገረ እንጾኪያ ፤ አባስ ካህነ ሮሜ በተአምረ ማርያም ታውቋል አትናቴዎስ ሊቀ ጳጳሳት ዘአንጾኪያ ቀድሞ አረማዊ ነበረ ኋላ አምኖ ተጠምቆ ተምሮ ተሾሟል በሀገራቸው የተሾመው ፯ ቀን ቀድሶ ያቈርባል በዚያ ልማድ በመስቀል እየባረከ ሲዞር ቀድሞ በአረማዊነት ሳለ በግብር የምታውቀው ቤት መስያ ይሁነኝ ብላ እጁን ነከሰችው ጦር ተነግባበት ከዚህ ሁሉ ያደረሰችኝ ይህች እጅ አይደለችም ብሎ ከዕቃ ቤት ገብቶ እጁን ቆርጦ ጣላት ፤ አባታችን ገብተህ ቀድስልን አሉት አይቻለኝም አላቸው ። ሁለተኛ ገብተህ ቀድስ አሉት አይቻለኝም አላቸው ፤ ይህ ሰው ወደ ቀደሞ ግብሩ ተመለሰን ብለዋል ወደ እመቤታችን አመለከተ እድ ብርህት ቀጠለችለት ገብቶ ሲቀድስ የእጁ ብርሃን እየበዘበዘ የማያሳያቸው ሆነ ወጥተው አባታችን ነገሩ ምንድነው ግለጥልን አሉት ምንጣፉን ግለጡት አላቸው ቢገልጡት ወድቃ አገኙዋት ይህች የኔ እጅ ናት ይህች እመቤታችን የሰጠችኝ ናት ብሏቸዋል ።

ወእመኒ እግርከ ዘየማን ታስሕተከ ምትራ ወግድፋ እምላዕሌከ ።

ቀኝ እግርህ ምክንያተ ስሕተት ብትሆንብህ ቆርጠህ ጣላት ፤ እስመ ይኄይስከ ይትጐጐል ፩ዱ እምአባልከ እምዘ ኵሉ ሥጋከ ይትወደይ ውስተ እሳተ ገሃነም በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ሳይጎድል ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ፤በዚህ ዓለም ከሕዋሳትህ አንዱ ጐድሎ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ። ይህን ያደረጉ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን አባ መርትያኖስ፡በዓቱ ከመንደር አጠገብ ነው ከበረሃ ውሎ ወደማታ ሲመለስ ዘማት ተሰብስበው አይተው ይህ መነኮስ ኃያል ጽኑዕ ነው የሚያስተው የለም አሉ ፤ አንዲቱ እኔ ባስተውስ ባታስችውስ ተባብለው ተወራርደዋል ፤ አሁን በጊዜ የሄድኩ እንደሆነ አይቀበለኝም ብላ ሲመሽ ሒዳ እጅ ጸፋች ፤ ወጥቶ ማነሽ አላት ከሩቅ አገር የመጣሁ የእግዚአብሔር እንግዳ ነኝ የምጠጋበት አጥቸ አውሬ ይጣላኛል ወምበዴ ይቀጠቅጠኛል ብየ ቈሚያለሁ አለችው አዕም ባስገባት ጸር ይነግብኛል አይሆንም ብላት

ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክሙኒ ያለው ይፈርስብኛል እያለ ያወጣ ያወርድ ጀመረ ። ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክሙኒ ያለውስ ቢፈርስብኝ ጦሩን አታግሠዋለሁ ብሎ እሳቱን እንድዶላት እሱ እልፍ ብሎ ጸሎቱን ያዘ እሷም የምትቀባውን ትቀባ የምታጤሰውን ታጤስ ጀመር ። መዓዛው ቢያስቸግረው እግሩን ከእሳቱ ማገዶው የእሷን መዓዛ እስኪያጠፋው እስኪለውጠው ፤ ምትራ ያለው ለዚህ ይመቻል ፤ እሷም አባቴ አላበጀሁም ብላ ንስሐ ገብታለች አንድም ገልጣ አንተኛ አለችው እንተኛማ ካልሽ ከእሳቱ ላይ እንተኛ እሳት ይህማ ይፈጅን የለም አለችው የዚህን ዓለም እሳት ያልቻልነው የወዲያኛውንማ ዓለም እሳት እንደምን እንችለዋለን አላት አባቴ አላበጀሁም ማረኝ ብላ ንስሐ ገብታለች እሱም አመንኵሷት በእቴን ለቀላትሂደል አንድም ዓይን የቲባለች ሚስት ናት። ከዓይን የሚሰወር እንደሌለ ከሚስትም የሚሰወር የለምና ፤ ሚስትህ ያልሆነ ሥራ ላሠራህ ብትል ፈቃዷን አፍርስባት ዛሬ በዚህ ዓለም የሚስትህን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ፡ በዚህ ዓለም የሚስትህን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ እጅ የተባሉ ልጆች ናቸው ወድቆ ይነሡ በእጅ ዘግቶ ይከብሩ በልጅ እንዲሉ ። ልጆችህ ያልሆነ ሥራ እና ሠራህ ቢሉ ፈቃዳቸውን አፍርስባቸው ፤ በዚህ ዓለም የልጆችህን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትወርድ፤ በዚህ ዓለም የልጆችህን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና እግር የተባሉ ቤተሰብእ ናቸው ቤተሰቦችህ ምክንያተ ስሕተት ሁነው ያልሆነ ሥራ እና ሠራህ ቢሉ ፈቃዳቸውን አፍርስባቸው ፤ በዚህ ዓለም የእሳቸውን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም እሳት ከምትገባ ፤ በዚህ ዓለም ፈቃዳቸውን አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ አንድም እንዳይንህ እንደ እጅህ እንደ እግርህ የምትወደው ወዳጅህ ያልሆነ ሥራ አሠራሃለሁ ቢልህ ፈቃዱን አፍርስበት በዚህ ዓለም የሱን ፈቃድ ፈጽመህ ኑረህ ኋላ ገሃነም ከምትገባ ። በዚህ ዓለም የሱን ፈቃድ አፍርሰህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፤ አንድም ምድራውያን ነገሥታት ዓይን በፍላት እጅ እግር በስለት ፤ እንዲቀጹ ሌዋውያን ካህናት ዓይንን በአንቃዕድዎ እጅን በሰፊህ ፤ እግርን በቀዊም ፡ ሠርተው ቀጽተው እንዲኖሩ ፤ አንተም ዓይንህን በአንቃዕድዎ እጅህን በሰፊህ እግርህን በቀዊም ሥራ ቅጻ ።

፴፩ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ይጽሐፍ ላቲ መጽሐፈ ሕዳጋታ ወየሀባ ። ዘዳ ፳፬፡ ፩ ማቴ ፲፱፡፯፡፱ ማር ፲፡፬፡፲፪ ሉቃ ፲፮ ፡ ፲፰ ፡ ፩ ቆሮ ፯ ፡ ፲ ።

፴፩ ከናንት አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች ሚስቱን የሚፈታ ሰው ሁሉ የምትፈታበትን ነውር የሚናገር ደብዳቤ ጽፎ ሰጥቶ ይፍታት የተባለላቸውን ሰምታችኋል ፤ እንዳለፈው በል ።

፴፪ አንሰ እብለክሙ ከመ ኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ በላዕሌሁ ለሊሁ ረሰያ ዘማ

፴፪ እኔ ግን ሳትሰስንበት ሰንፈች ደረቀች ብሎ ሚስቱን የፈታ ሰው ሁሉ ዘማ አሰኛት ብየ እነግራችኋለሁ ።

ወዘሂ አውሰበ ኅድግተ ዘመወ በነውር የተፈታችውን ያገባ በደለ ፤ በምን ያውቀዋል ቢሉ አቡን ፅጬኒ ይፍቱኝ ባለማለቷ ፤ ኋላ እንደምን ትሁን ቢሉ የፍርድ መጽሐፍ በጉቱዓ ብሎ ወስዶታል ። ንስሐ መግባቷን መምህረ ንስሐዋ ጉረቤቶቿ መስክረውላት ታግባ ብሏል ። አንድም ሰማዕክሙ ብለህ መልስ ። አሪትን የሚተው ሰው ሁሉ ወንጌልን ተከቶ ይተው የወንጌልን ሥራ ሳይሠራ ግን አሪትን የተወ ሰው ወንጌልን ኃላፊት ሕግ አደረጋት ። ከተዋትም በኋላ ወደ አሪት ቢመለስ በደለ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል አንድም መልስ ይህን ዓለም የሚተው ሰው ሁሉ መንግሥተ ሰማያትን ተከቶ ይተው ። የምናኔ ሥራ ይሥራ ። ወአንሰ እብለክሙ ፤ የምናኔ ሥራ ሳይሠራ ይህን ዓለም ተውሁ የሚል ሰው ግን መንግሥተ ሰማያትን ኃላፊት ርስት አደረጋት ። ከመነነም በኋላ ወደኋላም ቢመለስ በደለ ኃጥእ ተብሎ ይፈረድበታል።

፴፫ ወካዕበ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ለቀደምትክሙ ኢትምሐሉ በሐሰት ፤ ወባሕቱ አግብኡ መሐላክሙ ለእግዚአብሔር ። ዘሌዋ ፲፱፡፲፪ ዘፀ ፳፡፯ ዘዳ ፳፡፲፩ ያዕ ፭፡፲፪ ፤

፴፫ ለቀደሙ ሰዎች በእውነት እንጂ በሐሰት በስመ እግዚአብሔር እንጂ በስመ ጣዖት ዳኛ ፈርዶባችሁ ባለጋራ አውርዶላችሁ እንጂ ዳኛ ሳይፈርድባችሁ ባለጋራ ሳያወርድላችሁ አትማሉ ያሏቸውን ሰምታችኋል ።

፴፬ ወአንሰ እብለክሙ ኢትምሐሉ ግሙራ ።

፴፬ እኔ ግን ፈጽማችሁ አትማሉ እላችኋለሁ ኢበሰማይ ።
በሰማይም ሁኖ ከሰማይ የመጣ መቅሠፍት አይላተን ሰማይ ተንዶ ይጫነን እያሉ ይምላሉና ፤ እስመ መንበሩ ለእግዚአብሔር ውእቱ ።
የእግዚአብሔር ዙፋኑ ነውና ።
ወኢበምድር ።

በምድርም ሁኖ ምድር ይክዳን ምድር ተከፍቶ ይዋጠን እያሉ ይምላሉና ።
እስመ መከየደ እገሪሁ ይእቲ ፤
መመላለሻው ናትና ።

፴፭ ወኢበኢየሩሳሌም ፤

፴፭ በኢየሩሳሌምም ሁኖ ከበረከተ ርስት እያ ሳትሬን ከምድረ ርስት ያወጣን እያሉ ይምላሉና ።
እስመ ሀገሩ ይእቲ ለንጉሥ ዓቢይ ።
የደግ ንጉሥ የእግዚአብሔር የመመስከያው አገር ናትና ።

፴፮ ወኢበርእስከሙ ኢትምሐሉ ፤

፴፮ በራሳችሁም አትማሉ እንዲህ ያድርገን እያሉ ይምላሉና ።
ወኢበስእርተ ርእስከሙ ፤
በራሳችሁ ጸጉር አትማሉ ፤ እንደ ራሳችን ጸጉር ያጥቁረን የራሳችንን ጸጉር ያህል አምራ መጥቶ ይብላን እያሉ ይምላሉና ።
እስመ ኢትክሉ አሐተ እምስእርተ ርእስከሙ ኢአ ጸዐድዎ ወኢአጽልሞ ።
ከራሳችሁ ጸጉር አንዱን ነጩን ጥቁር ጥቁሩን ነጭ ማድረግ አይቻላችሁምና ።

፴፯ ወይኩን ባሕቱ ነገርክሙ እመሂ እወ እወ ወእመሂ አልቦ አልቦ ። ያዕ ፭ ፣ ፲፪

፴፯ ነገራችሁ እውነቱን እውነት ሐሰቱን ሐሰት ይሁን እንጂ ፣ ሐቲታ እወ ቢለው ያምንለታልን ቢሉ ይመንለት ወንጌል መሠረቷ ለሁሉ ነው እንጂ ላንድ ብቻ ነውን ይላሉ ባያምንለትስ ቢሉ መሐላውን በገንዘብ ያስቀረው ገንዘብ ባይኖረውሳ ቢሉ ይማል ዕዳው ባማይው ይሆናል እንጂ በማዩ አይሆንምና ወለእመ ኢተክህለ ይከውን ጌጋይ ላዕለ ዘአምሐሎ እንዲል ፣ ሐዋርያ ጳውሎስ ጠመዓው ለቅሥት የሐልቅ በመሐላ ጆላል ፤ ከዚህ ጌታ ኢትመሐሉ አለ እንደምነው አይማላም ቢሉ አይማላም ። ሐዋርያ የርትዑን ጌታ የትሩፋቱን ተናገረ እንድም ሁሉም ርትዕ ነው ። ሐዋርያ ዳኛ ፈርዶባችሁ ባላጋራ አውርዶላችሁ ማሉ ሲል ነው ። ጌታ ዳኛ ሳይፈርድባችሁ አትማሉ ሲል ነውና እንድም ኢበሰማይ ብለህ መልስ በመለኮት አትማሉ ባሕርዩ ነውና ፣ ወኢበምድር በትስብእት አትማሉ ባሕርዩ ነው ። ወኢበኢየሩሳሌም ፤ በሥጋው በደሙ አትማሉ ባሕርዩ ነውና ፤ ወኢበርእስከሙ በክርስቶስ አትማሉ ፤ ንሕነ አባል ወውእቱ ርእስ እንዲል ፣ ወኢበስእርተ ርእስከሙ ፤ በጻድቃን በሰማዕታት አትማሉ ፤ እስመ ኢትክሉ ከጻድቃን ከሰማዕታት አንዱን ኃጥእ ጻድቅ ጻድቁን ኃጥእ ማድረግ አይቻላችሁምና ፤ ወፈድፋደሰ እምእሉ እምእኩይ ውእቱ ፤
ከእወና ከአልቦ የወጣ ግን ከሰይጣን የተገኘ ነው

፴፰ ሰማዕክሙ ዘተብህለ ዓይን ቤዛ ዓይን ወሥን ቤዛ ሥን ። ዘፀ ፣ ፳፩ ፣ ፳፬ ። ዘሌ ፣ ፳፬ ፣ ፳ ፤ ዘዳ ፣ ፲፱ ፣ ፳፩ ።

፴፰ ዓይን ቢጠፋ ዓይን ይጥፋ ጥርስ ቢሰበር ጥርስ ይሰበር የተባለውን ሰምታችኋል ፤ ቢሣትቱ ለሚመጣው ለሌላው ነው ።

፴፱ ወአንሰ እብለክሙ ኢትትቃወምዎ ለእኩይ በእኩይ ። ሉቃ ፣ ፮ ፣ ፳፱ ። ፩ ቆሮ ፣ ፮ ፣ ፯ ።

፴፱ እኔ ግን ክፉውን ሰው በክፉ ነገር ድል አትንሱት ክፉን ግብር በክፉ ግብር አታጥፉት እላችኋለሁ ። ወኀበዚ ጸፍዓከ መልታሕቴከ እንተ የማን ሚጥ ሎቱ ካልዕታሂ ፤
ቀኝ ፊትህን ቢመታህ ግራ ፊትህን አዙረህ ስጠው ፊቃደ ሥጋህን ተው ቢልህ ፊቃደ ነፍስህን ተውለት

፵ ወለዘሂ ይፈቅድ ይትዓገልከ መልበስከ ኅድግ ሎቱ ክዳነከሂ

፵ መጐናጠፊያህን ሊቀማህ ቢወድ ቀሚስህን ጀርብለት ። ታሪክ እንዳንድ ባሕታዊ ወምበዶች እንግዶች መስለው መጡ እግራቸውን አጥቦ አብልቶ አጠጥቶ አሳደራቸው ሌት ተነሥተው እሉን አስረው መብራት አብርተው ያለ ገንዘቡን ይዘው ሄዱ ከሄዱ በኋላ መብራት አብርቶ ቢያይ ሁለት ድሪም የምታወጣ ጸምር አገኘ ይህችም ላንድ ጉዳይ ትሆናችኋለች ብሎ ተከትሎ ወስዶ ሰጣቸው ይህ ሰው እንዲህ ማድረጉ ከዚህ የበለጠ ዋጋ እንዳለ ቢያውቅ እንጂ ነው ብለው ተመልሰው ንስሐ ገብተው የሚኖሩ ሁነዋል ። እንድም አፍአዊ ግብርህን ሊያስተውህ ቢወድ ውሣጣዊ ግብርህን ተውለት

፵፩ ወለዘሂ አበጠከ አሐደ ምዕራፈ ሑር ምስሌሁ ፪ተ ።

፵፩ ትብትብ አሸክሞ አንድ ምዕራፍ ቢወስድህ ይህማ የግድ አይደለምን ብለህ የፈቃድ ሁለት ምዕራፍ ተሸክመህ ውሰድለት መምህረ ንስሐህ አንድ ሱባዔ ቀኖና ቢሰጥህ ይህስ ተስማምቶኛል ጨምርልኝ ። ብለህ ከሱ አስፈቅደህ ሁለት ሱባዔ ጹም ፤

፵፪ ወስቱ ዘሰአለከ ሀቦ ። ዘዳ ፲፭ ፣ ፯፣፰

፵፪ ለለመነህ ሁሉ ስጠው ፤
ወለዘይፈቅድ ይትለቃሕ እምኔከ ኢትክልዖ ።
ካንተ ሊበደር የሚወደውን አትከልክለው እንደ ዮሐንስ መሐሪ መፕተው አበድረን ሲሉት መክፈቻውን ሰጥቶ ወደ ዕቃ ቤቱ ይሰዳቸዋል የሚበቃቸውን ያህል ይዘው ይሔዳሉ አምጥተው የሰጡት እንደሆነ ይቀበላል ባይሰጡት ግድ የለውም ነበር ።

፵፫ ሰማዕክሙ ዘከመ ተብህለ ለቀደምትክሙ አፍቅር ቢጸከ ወጽላእ ጸላኢከ ። ዘሌ ፲፱ ፣ ፲፰ ።

፵፫ ከናንተ አስቀድሞ ለነበሩ ሰዎች ወዳጅህን ውደድ ጠላትህን ጥላ ያላቸውን ሰምታችኋል ።

አፍቅሮ ቢጸከ ይሁን ጽላእ ጸላኢከ የሚል በኦሪት ወዴት አለ ቢሉ ባጸፈው ተናገረ ወዳጅህን ውደድ ማለት ጠላትህን ጥላ ማለት ነውና ፤ አንድም ተጻ ረርዎሙ ለሚደናውያን ኢትርስዮ ለአማሌቅ ያለ ውን ለውጦ አነበበው ።

፴፱ ወአንስ እብለክሙ አፍቅሩ ጸላእተክሙ ሉቃ ፣ ፮ ፣ ፳፯ ሮሜ ፣ ፲፪ ፣ ፲ ግብ ሐዋ ፣ ፯ ፣ ፶፱ ሉቃ ፣ ፳፫ ፣ ፴፬ ።

፵፬ እኔ ግን ጸላታችሁን ውደዱ እላችኋለሁ ፤ ወባርክዎሙ ለእለ ይሰድዱክሙ ከሀገራችሁ አስወ ጥተው የሚሰዷችሁን መርቋቸው ከቦታችሁ ከሀ ገራችሁ አያናውጣችሁ ከመንግሥተ ሰማያት አያ ውጣችሁ እያላችሁ ። ሠናየ ግበሩ ለእለ ይጸረፉክሙ ለሚጠሏችሁ በጐ ሥራ ሥሩላቸው ።

ወጸልዩ በእንተ እለ ይትዔገሉክሙ ።

ሥቃይ ለሚያጸኑባችሁ ጸልዩላቸው አንዳንድ ምእ መን ዘመነ ዓላውያን ሁኖ አንድ ዓላዊ መከራ ያጸ ናበታል ጌታዬ ምረረ ገዛነምን ባዕመ መንግሥተ ሰማያትን ባያውቅ እንጂ ነው እንዲያውቅ አድርገው እያለ ይጸልይለታል ኋላ ዘመነ ዓላውያን አልፎ ዘመነ ክርስቲያን ሆነ ያ ክርስቲያን ዛሬ ቢያገኘኝ እንደ ምን ባደረገኝ ነበር አለ ። እሱስ ቀድሞም እንዲህ እያለ ይጸልይልህ ነበር አሉት እነሆ ክርስቲያን ምግባራቸው የቀና መሆኑ ሃይማኖታቸው እንጂ የቀና ቢሆን ነው ብሎ ተመልሶ አምኗል፣ ተጠምቋ ።

፵፭ ከመ ትኩኑ ውሉዶ ለአቡክሙ ዘበሰማያት

፵፭ የሰማያዊ አባታችሁ ልጆች ትሆኑ ዘንድ ዘንድ ማለት ሰማያዊ አባታችሁን ትመስሉ ዘንድ ። እስመ ውእቱ ያሠርቅ ፀሐየ ላዕለ ኄራን ወእኩያን ፀሐይን ለበጐዎችም ለክፉዎችም ያወጣልና ። ወያዘንም ዝናመ ላዕለ ጻድቃን ወኃጥአን ። ዝናምን ለጻድቃንም ለኃጥአንም ያዘንማልና ። ፀሐይ ሥጋው ደሙ ዝናም ወንጌል ነው በአንቢተኝነታ ቸው ይቅርባቸው እንጂ ሥጋው ደሙ ወንጌል የተሠራ ለሁሉ ነውና ።

፵፮ ወእመሰ ዘአፍቀረክሙ ታፈቅሩ ምንትኑ ዕሤትክሙ ።

፵፮ የወደዳችሁንማ ብቻ ብትወዱ ዋጋችሁ ምንድነው ።

አኮሁ መጸብሐንሂ ከማሁ ይገብሩ ።

የወደዳቸውንማ ብቻ መውደድ አጣሮችስ ያደርጉት የለምን ይህንስ አጣሮችም ያደርጉታል ባንዱ አገር ያሉ አጣሮች ባንዱ አገር ካሉ ጋራ ይጠቃቀ ማሉና ።

፵፯ ወእመሂ ተአማኅክሙ ቢጸክሙ ባሕቲቶ ምንት እንከ ፍድፉዴ ዝብርክሙ ።

፵፯ ወንድሞቻችሁን ብቻ የምታከብሩ ከሆነ አብ ልጣችሁ ምን ትሩፋት ሠራችሁ ፣ ምንት ፍድፉዴ ዘገበርክሙ ፤ የሠራችሁት ትሩፋት ምንድነው ፤ አኮኑ አሕዛብኒ ከማሁ ይገብሩ ወንድሞቻቸውንማ ብቻ መውደድ አሕዛብስ ያደርጉት የለም ይህንስ አሕዛብም ያደርጉታል ።

፵፰ አንትሙሰ ኩኑ ፍጹማነ ከመ አቡክሙ ሰማያዊ ፍጹም ውእቱ ።

፵፰ እናንተስ ሰማያዊ አባታችሁ ሁሉን አስ ተካክሎ በመውደድ ፍጹም እንደሆነ ሁሉን አስተ ካክላችሁ በመውደድ ፍጹማን ሁኑ ።

በእንተ ጾም ወጸሎት ወምጽዋት

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወባሕቱ ዑቁ ምጽዋተክሙ ኢትግበሩ ለዓ ይነ ሰብእ ከመ ያስተርእዩ ሎሙ ።

፩ ባሕቱን የሚጽፍም የማይጽፍም አለ ምጽዋታችሁን ሰው ይይልን ብላችሁ እንዳታደርጉ ዕወቁ ።

ወእመ አኮስ ዓስብ አልብክሙ በኀበ አቡክሙ ዘበ ሰማያት ያለዚያ ግን በሰማይ አባታችሁ ዘንድ ዋጋ የላችሁም ።

፪ ወሶበሂ ትገብሩ ምጽዋተክሙ ኢትንፍሑ ቀርነ በቅድሜክሙ በከመ ይገብሩ መደልዋን በመ ራኅብት ወበአስኳት ።

፪ በምትመጸውቱበትም ጊዜ ግብዞች ሰው ሰብስበው ቀን ቀጥረው በተመሳቀለ ጎዳና ባደባባይ እንዲያደርጉት ቀን ቀጥራችሁ ዐዋጅ ነግራችሁ አታድርጉት ። አንድም ውዳሴ ከንቱ ሽታችሁ አታ ድርጉት ። አንድ ባለጸጋ አፈ ወርቅን እንደጠየቀው ይህን ሲያስተምር አንድ ባለጸጋ መጥቶ ምጽዋት መመጽወት እወዳለሁ ውዳሴ ከንቱም እወዳለሁ አለው ውዳሴ ከንቱውን ትተህ መጽውት አለው አይሆንም ሁሉንም እወዳለሁ ይህ ከቀረ ምጽዋ ቱም ይቅር አለው እንኪያስ አትተው መጽውት ሰው ዘር ይዘራል ባይጠብቀው የእሸት ያህል ያጣ ለታልን አንተም የዚያን ያህል ጥቂት ዋጋ አታጣም ስጥ ብሎታል ።

ከመ ይትአኰቱ እምነበ ሰብእ ሰው ያይላቸው ይሰ ማላቸው ዘንድ ።

አማን እብለክሙ ኃጕሉ ዕሤቶሙ ።

ኃጕሉ ቢል የወዲያኛውን ዋጋቸውን አጡ ነሥኡ ይላል ውዳሴ ከንቱን አገኙ ብየ እንዳገኙ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፫ ወአንተሰ ሶበ ትገብር ምጽዋተከ ኢታእምር ፀጋምከ ዘትገብር የማንከ ።

፫ እንተ ግን በምትመጸውትበት ጊዜ ቀኝ እጅህ የምትሠራውን ግራ እጅህ አትወቀው ። ማለት በቀኝ እጅህ የያዝከውን በግራ እጅህ አትያዘው ግራ ደካማ ነው ጥቂቱን ብዙ ያስመስለዋል ልክፈልለት ያሰኛ ልና ቀኝ ኃያል ነው ብዙውን ጥቂት ያስመስላል ፤ ከዚህ ምን እከፍልለታለሁ ልስጠው ያሰኛልና ፣ አን ድም ሚስትህ አትወቅብህ ሲለው ነው ፀጋም እላት የባልና የሚስት ክብት ሎሚ ከሁለት እያለች ታዳከ ማለችና እንዳታዳክመው ከሚስት የሚሠወር ምን አለ ቢሉ ቅንንቱማ ካለ ገንዘቡ ሁሉ ያለ በአሱ እጅአይ ደለምን ከዚያው ይስጥ ይህማ ስርቆት አይሆንበትም ቢሉ ስጥቶ ይንገራት አይሆንም ብትለውላ ቢሉ ይለ ያዩ ጥንቱን መጋባታቸው ሰጥተው መጽውተው ሊጸድቁ ነውና ። አንድም ልጆችህ ዐይወቁብህ ሲል ነው ዐጋም አላቸው ያባታችን የቁም ወራሽ የሙት አልቃሽ እያሉ ያዳከማሉና እንዳያዳከሙት አንድም ቤተሰቦችህ ዐይወቁብህ ፀጋም አላቸው የጌታችን ወርቁ ለዝና ልብሉ ለእርዝና እህሉ ለቀ ጠና እያሉ ያዳከማሉና እንዳያዳከሙት ።

፬ ከመ በኅቡእ ይኩን ምጽዋትከ ፤

፬ ምጽዋትህ በስውር ይሆን ዘንድ ።
ወአቡከ ዘይሬእየከ በኅቡእ የአስየከ ክሡተ ። ስትመጸውት ተሰውሮ የሚያይህ አንድም ተሰው ረህ ስትመጸውት የሚያይህ ሰማያዊ አባትህ ጉባኤ ውንስ ከሻኸው በጻድቃን በሰማዕታት በመላእክት በኃጥአን በአጋንንት ፊት ገልጾ ዋጋህን ይሰጥሃል ።

፭ ወሶበሂ ትጼልዩ ኢትኩኑ ከመ አሕዛብ ።

፭ በምትጸልዩበትም ጊዜ እንደ ግብዞች አትሁኑ እስመ ያፈቅሩ በመኳርብት በውስተ መዓዝነ መራ ህብት ቀዊመ ወጸልዮ ከመ ያስተርእዩ ለዓይነ ሰብእ ሰው ይይልን ሰው ይስማልን ብለው በምኵራብ ባደ ባባይ ቁሞ መጸለይን ይወዳሉና ፣ በምኵራብማ መጸ ለይ እንዲገባ ለማጠየቅ ሙሴን ወንድምህ አሮን ድምጽ ያለው ልብስ ለብሶ ያን እያሰማ ገብቶ ይጸ ልይ ሕዝቡም እሱን አብነት አድርገው ገብተው ይጸልዩ ብሎት የለምን ቢሉ ከዚያው መካነ ጸሎት መካነ ትምህርት መካነ ተማኅጽ አለ ፣ እኒህ ግን መካነ ጸሎቱን ትተው በመካነ ተግሣጽ ቁመው ይታያሉና ። አማን እብለክሙ ኃጕሉ ዕሤቶሙ ።

፮ እንዳለፈው በል ፤
ወአንተሰ ሶበ ትጼሊ ባእ ቤተከ ወዕጹ ሆኅተከ ወጸሊ ለአቡከ ።

፮ አንተ ግን በምትጸልይበት ጊዜ ከቤትህ ገብ ተህ ደጅህን ዘግተህ ወደ ሰማያዊ አባትህ ጸልይ ። አን ድም በምትጸልይበት ጊዜ ሕዋሳትህን ሰብስበህ በስ ቂለ ሕሊና በነቂሐ ልቡና ሁነህ ወደ ሰማያዊ አባትህ ወደ እግዚአብሔር አመልክት ።

ወአቡከ ዘይሬእየከ በኅቡእ የዓሥየከ ክሡተ ። ተሰውረህ ስትጸልይ የሚያይህ ሰማያዊ አባትህ ዋጋ ህን ይሰጥሃል ወእንዘ ትጼልዩ ።

፯ ኢትዘንግዑ ከመ አሕዛብ ።

፯ ስትጸልዩ እንደ አሕዛብ አብዝታችሁ አት ጸልዩ ። ግብር ዘአልቦ ምግኔ ገዓር ውእቱ ወስገዓርኒ ይተልዎ ዝንጋኤ እንዲል አንድም ጮሃችሁ አት ጸልዩ ኢትከላህ በሕቁ አላ ዘምር በመጠን ከመ ኢይዘንግዑ አኃው እንዲል ።
እስመ ይመስሎሙ በአብዝኀ ንባቦሙ ዘይሰምዖሙ አብዝተው ጮኸው በመጸለያቸው የሚሰማቸው ይመስላቸዋልና ።

፰ ኢትትመሰልዎሙኬ ፣

፰ አብነት አታድርጓቸው ፣ እስመ የአምር አቡ ክሙ ሰማያዊ መፍቅደክሙ ዘእንበለ ትስአልዎ ፤ እናንተስ አብዝታችሁ ጮሃችሁ ሳትለምኑት ሰማ ያዊ አባታችሁ የምትሹትን ዐውቆ ያደርግላችኋል ።

፱ አንትሙሰ ሶበ ትጼልዩ ከመዝ በሉ ።

፱ ሉቃ ፡ ፲፩ ፣ ፪ እናንተስ በምትጸልዩበት ጊዜ እንዲህ በሉ ። ሐተታ አብዝታችሁ አትጸልዩ ብሎ ነበርና አጭር ጸሎት ጮኻችሁ አትጸልዩ ብሎ ነበርና የሕሊና ጸሎት ቋሚ ለንሚ ገረድ ደን ገጽር ሲቆሙ ሲቀመጡ ሲተኙ ሲነሡ የሚጸልዩት አጭር ጸሎት ሠራልን ።
አቡነ ዘበሰማያት ።
በሰማይ ያለህ አባታችን ፣ አቡነ በሉኝ አለ አምላክነ እግዚእነ መምህርነ በሉኝ አላለም ቀድሞ ነቢያት ከግብርናተ ዲያብሎስ እንዲልወጡ ሲያጠይቅ አምላክነ እያሉ ይጸልዩ ነበር እኛ ግን ከግብርናተ ዲያብሎስ እንዳወጣን ሲያጠይቅ አቡነ በሉኝ አለ እግዚእነ መምህርነ በሉኝ አላለም ። ጌታ ሎሌውን መምህር ደቀ መዝሙሩን ቢወደው ያበላዋል ያጠ ጣዋል የልቡናውንም ምሥጢር ያጫውተዋል እንጂ ርስቱን አያወርሰውም ርስቱን ግን የሚያወርስ ለልጁ ነው ። እሱ ግን የማታልፍ ርስቱን መንግሥተ ሰማያትን ያወርሰናልና ። አንድም ወበከመ ይም ህር አብ ውሉዶ ከማሁ ይምህሮሙ እግዚአብ ሔር ለኵሉ ይፈርህዎ እንዲል አባት ለልጁ እንዲራራ ይራራልናልና ፣ ዘበሰማያት አለ ከምድራዊ አባት ሲለይ ምድራዊ አባት ሲወልድ በግዘፍ ሲያሳድግ በግዘፍ ነው ኋላም ኃላፊ ርስቱን ያወርሰዋል ኋላ ሞትን ያስከትልበታል እሱ ግን ሲወልደን በረቂቅ ሲያሳድገንም በረቂቅ ነው ኋላም የማታልፍ ርስቱን መንግሥተ ሰማይን ያወርሰናል ኋላም ሐይው ከመ መላእክትን ያስከትልልናልና ፣ አንድም ጌታ በሁሉ ምሉእ ሲሆን ስለልዕልናው በሰማይ አለ ይባላልና ዘበእንተ ዕበይከ ትትሜሰል በደመናት እንዲል፡

እንድም ጸሎቱ በስቂለ ሕሊና ይሁን ሲል እንዲህ አለ ፤
ይትቀደስ ስምከ ፡
ስመ ወላዲ ስመ ተወላዲ ስመ ሠራጺ ይለይልን በሉኝ ። እንድም ስምየስ መሐሪ ወመስተሣህል ያልኸው ይጽናልን በሉኝ ። እንድም መላእክት ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ ብለው ስምህን አመስግነው ቅድስናህን ተሳትፈው እንዲኖሩ እኛም ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ ብለን አመስግነንህ ቅድስናህን ተሳትፈን እንድንኖር አድርገን በሉኝ አለ ።

፲ ትምጻእ መንግሥትከ ፤

፲ መንግሥተ ሰማይ ትምጣልን በሉኝ ትምጻእ ማለቱ ግን ከወዲያ ያለች ከወዲህ የሌለች ሁና ከወዲያ ወዲህ የምትመጣ ፥ ከወዲህ ያለች፥ ከወዲያ የሌለች ሁና ከወዲህ ወዲያ የምትሄድ ሁና አይደለም ትገልጽልን በሉኝ ሲል ነው እንጂ አኮ እምከልዕ መካን ዘይመጽእ ለአስተርእዮ ኀቤሆሙ አላ ሀሎ ኀቡአ ወምሉአ ማእከሌሆሙ ወውሣጤሆሙ እንዲል እንድም ልጅነት ትሰጠን በሉኝ ሲል ነው ። መተርጕምኒ ሰመያ ለትምጻእ መንግሥትከ ሱታፌ መንፈስ እንዲል ፥ ወይኩን ፈቃድከ በከመ በሰማይ ። መላእክት በሰማይ ሊያመሰግኑህ ፈቃድህ እንደሆነ እኛም እናመሰግንህ ዘንድ ፈቃድህ ይሁን በሉኝ እንድም ኋላ ሙተን ተነሥተን ልናመሰግንህ ፈቃድህ እንደሆነ ዛሬም በሕይወተ ሥጋ ሳለን እናመስግንህ ዘንድ ፈቃድህ ይሁን በሉኝ ከማሁ ማንሻ እንድም መላእክት በሰማይ አመስግነውህ ያውምስጋናው ምግብ ሆኑዋቸው እንዲኖር ።

፲፩ ከማሁ በምድር ሲሳየነ ዘለለዕለትነ ሀበነዮም

፲፩ ዘፍጥ ፳፰ ፥ ፳ ምሳ ፴፡፰፡፩፡ ጢሞ ፮ ፥ ፰ ማር ይስ ፲፪ ም ለኛም በዚህ ዓለም ሳለን የዕለት ምግባችንን ስጠን በሉኝ በዚህም መጻሕፍት ተባብረውብታል ያዕቆብ በአሪት እምከመ ረከብኩ እክለ ዘእበልዕ ወልብሰ ዘእትኤረዝ ይኩውንኒ እግዚአብሔር አምላኪየ ብሏል ጳውሎስም እምከመ ረከብነ ሲሳየነ ወአራዘነ የአክለነ ብሏል ። ፫ቱ ምእትም በሕንጸ ሥነኮላት ኢትኩን መፍቀሬ ወርቅ ወብሩር ዘእንበለ በአምጣነ ዘየአክል ለሕይወትከ ለሲሳይከ ወለአራዝከ በዐቅም ብለዋል ። ማር ይስሐቅም እመቦ ዘተርፈ እምፍቃደ ዕለትከ ሀቦ ለነዳይ ብሏል ፥ ለፍጹማን የሆነ እንደሆነ በቁሙ የዕለት ምግብ ነው ። ለሰብአ ዓለም ግን ያሙት ልብስ ያሙት ምግብ ዘር አስቀርቶ የቀረውን መስጠት ነው ። እንድም ሥጋህን ደምህን ንስሐን ትምህርትን ዓስበ ጸሎታችንን ስጠን በሉኝ ።

፲፪ ኅድግ ለነ አበሳነ ወጌጋየነ ከመ ንሕነኒ ንኅድግ ለዘአበሰ ለነ ።

፲፪ እኛም የበደለንን ይቅር እንል ዘንድ በደላችንን ይቅር በለን በሉኝ ፥ ይህማ ማስተባለፍ አይሆንም ቢሉ አይሆንም ሰው ይቅር ማለቱ እኔንም እግዚአብሔር ይቅር ይለኛል ብሎ ነውና ፥ እንድም ከእኃው እንዱ ተነሥቶ አብሑኒ ከመ እወስከ አሐደ ቃለ ላዕለ አቡነ ዘበሰማያት አላቸው ። አባሕናከ ንብብ አሉት ረስየነ ያለበት ነው ብሏል ። ይቅር ማለቱ ቅሉ ያማንተ ፈቃድ አይሆንም ሲል ፤

፲፫ ኢታብአነ እግዚአ ውስተ መንሱት ።

፲፫ አቤቱ ወደ ኃጢአት ወደ ክህደት ወደ መከራ ወደ ገሃነም አታግባን በሉኝ ።
አላ አድኅነነ ወባልሐነ እምኵሉ እኩይ ።
ከኃጢአት ከክህደት ከመከራ ከገሃነም አድነን እንጂ።
እስመ ዚአከ ይእቲ መንግሥት መንግሥተ ሰማይ ገንዘብህ ናትና ፤
ኃይል ወስብሐት ለዓለመ ዓለም ከሃሊነት ጌትነት ለዘላለሙ ገንዘብህ ናትና ፥ አሜን በውነት ።

፲፬ እስመ ለእመ ኃደግሙ ለሰብእ አበሳሆሙ የኃድግ ለከሙኒ አበሳክሙ አቡክሙ ሰማያዊ ፤
ሲራክ ፳፰ ፥ ፫፪ ፥ ፩ ማቴ ፥ ፲፰ ፥ ፴፩ ማር ፥ ፲፩ ፥ ፳፭

፲፬ እናንተ ይቅር ብትሉ ሰማያዊ አባታችሁ የናንተንም ኃጢአት ይቅር ይላችኋልና ይቅር ይላችሁ ዘንድ ይቅር በሉ ።

፲፭ ወእመሰ ኢኃደግሙ ለሰብእ አበሳሆሙ ለክሙኒ ኢየኃድግ አበሳክሙ አቡክሙ ሰማያዊ

፲፭ የሰውን ኃጢአት ይቅር ባትሉ ግን ሰማያዊ አባታችሁ ይቅር አይላችሁምና ይቅር ይላችሁ ዘንድ ይቅር በሉ እንድም ይቅር ብትሉ ይቅር ይላችኋል ይቅር ባትሉ ይቅር አይላችሁም አብዝታችሁ አትጸልዩ ብሎ ነበረና አጭር ጸሎት ጨምችሁ አትጸልዩ ብሎ ነበርና የሕሊና ጸሎት ቋሚ ለንሚ ገረድ ደንገጽር ሲቆሙ ሲቀመጡ ሲተኙ ሲነሡ በ፯ቱ ጊዜያት የሚጸልዩት አጭር ጸሎት ሠራልን ። እንዲህ ግን ስለሆነ ከ፹፩ መጻሕፍት ያለ ፳ ነገር አለበት ሃይማኖት ተስፋ ፍቅር ትሕትና ጸሎት ሃይማኖት ያላዩትን እግዚአብሔርን አቡነ ማለት ተስፋ ትምጻእ መንግሥትከ ማለት ፍቅር ለነ ብሎ አንዱ ላንዱ መጸለይ ትሕትና ቅዱሳን ከበቁ በኋላ ኅድግ ለነ አበሳነ ማለት ጸሎት መላው ጸሎት ነው ።

፲፮ ወሶበ ትጾውሙ ኢትኩኑ ከመ መደልዋን ።

፲፮ በምትጸልዩበት ጊዜ እንደ ግብዞች አትሁኑ እስመ እሙንቱ ይትሜጻለው ወይቴጽሩ ገጾሙ ፥ ወያማስኑ ። እነዚያ ፊታቸውን አጠውልገው ግንባራቸውን ጭምረው ሰውነታቸውን ለውጠው ይታያሉና ከመ ያእምር ሰብእ ከመ ጾሙ ።

እንደ ጾሙ ሰው ያውቅላቸው ዘንድ ።
እማን እብለክሙ ነሥኡ ዕሤቶሙ ነሥኡ ቢል የወ ዲህኛውን ውዳሴ ከንቱአገኙጋኑሉ ቢል የወዲያኛ ውን ዋጋቸውን አጡት ብየ በውነት እነግራችኋለሁ

፲፯ ወአንትሙሰ ሶበ ትጸውሙ ቅብዑ ርእ ሰክሙ ።

፲፯ እናንተስ በምትጾሙበት ጊዜ ራሳችሁን ተቀቡ ።
ወሕፅቡ ገጸክሙ ።
ፊታችሁን ታጠቡ የተቀባ የታጠበ እንዳይታወቅበት አይታወቅባችሁ ቢል ነው ። ይህስ በጌታ ጾም ነው በጾመ ፊታድ ቢሉ በጾመ ፊቃድ ነው እንጂ በጌታ ጾምማ ምን ውዳሴ ከንቱ አለበት ፣ ይኸውስ በከተማ ነው በገዳም ቢሉ በከተማ ነው እንጂ በገ ዳምማ ምን ውዳሴ ከንቱ አለ ይህም ሊታወቅ ዳን ኤል አምእመቦቦእኩ ገዳመ ሰሳ ኢ.ዓርገ ቅብዕ ዲበ ርእስየ ወኢቦእ ሥጋ ወወይን ውስተ አፉየ ብሏል ። አንድም ቅብዑ ፍቅርን ያዙ ቅብዕ ኢይርኅቀ ቅብ ዕሰ ፍቅረ ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው እንዲል ፣ ወሕ ፅቡ ንጽሕናን ገንዘብ አድርጉ እንድም ቅብዑ ትሕትናን ያዙ ፣ ወሕፅቡ ገጸክሙ ፣ በእንብዓ ንስሐ ታጠቡ ።

፲፰ ከመ ኢያእምር ሰብእ ከመ ጾምክሙ ።

፲፰ እንደ ጾማችሁ ሰው እንዳያውቅባችሁ ።
ዘእንበለ እቡክሙ ማእምረ ኅቡአት ።
ሁሉን መርምሮ ከሚያውቅ ከሰማያዊ አባታችሁ በቀር ሰማያዊ አባታችሁ ነው እንጂ ።
ወአቡክሙ ዘይሬእየክሙ በኅቡእ የዓስየክሙ ክሙተ ። ጉባኤውን ከሻችሁ ተሰውራችሁ ስትጾሙ ተሰውሮ የሚያያችሁ ሰማያዊ አባታችሁ በጻድቃን በመላእክት በኃጥአን በአጋንንት መካከል ዋጋችሁ ይሰጣችኋል ።

፲፱ ኢትዝግቡ ለክሙ መዝገበ ዘበምድር ኀበ ይበሊ ወይማስን ፣ እንቀጸ ምጽዋት ነው ። በመካ ከል ፣ እንቀጸ ጾምን አንቀጸ ጸሎትን አግብቶበት ነበረና አሁን አመጣው ስለ ሦስት ነገር ያመጣ ዋል ።

፲፱ እህሉን ነዳያን ሲበሉት ብለው እኑረውት ነቀዝ ቢበላው ፣ ልብሱን ነዳያን ቢለብሱት ብለው እኑረውት ነቀዝ ቢበላው ፣ ልብሱን ነዳያን ሲለ ብሱት ብለው እኑረውት ብል ቢበላው ምቀኝነት ነውና ፣ ዳግመኛ ለከፉ ጊዜ ይሆነኛል ብሎ ማኖር እግዚአብሔርን ከዳተኛ ማድረግ ነው ። በዝናብ አብቅሎ በፀሐይ አብስሎ አይመግበኝም ማለት ነውና ፣ አንድም ምንም እጅ እግር ባያወጡለት ገን ዘብ ማኖር ጣዖት ማኖር ነውና ፣ ኀልፈት ጥፋት ያለበትን ምድራዊ ድልብ አታድልቡ ።

ኀበ ጸጌ ወቁንቁኔ ያማስና ፣ ብል የሚበላውን ነቀዝ የሚያበላሸውን ።
ወኀበ ሰረቅት ይከርዩ ወይሰርቅዎ ።
ሌቦች ናሱን አፍርሰው ግድግዳውን ምሰው የሚወ ስዱትን ከሚወስዱት ቦታ አታድልቡ ።

፳ ዝግቡ ለክሙ መዝገበ ዘበሰማያት ኀበ ኢይበሊ ወኢይማስን ። ሉቃ ፣ ፲፪ ፡ ፴፫ ፡ ፩ ጢሞ ፮ ፡ ፲፱ ።

፳ እላ ያሰበት ነው ። ኀልፈት ጥፋት የሌለበ ትን ሰማያዊ ድልብን አድልቡ እንጂ ።
ወሀበ ኢያማስኖ ጸጌ ወቁንቁኔ ።
ብል የማይበላውን ነቀዝ የማያበላሸውን ።
ወኀበ ሰረቅት ኢይከርዩ ወኢይሰርቅዎ ።
ሌቦች ናሱን አፍርሰው ግድግዳውን ምሰው የማይ ወሰዱትን ከማይወስዱበት አድልቡ እንጂ ።

፳፩ እስመ ኀበ ሀሎ መዝገብክሙ ሀየ ይሄሉ ልብክሙኒ ።

፳፩ ገንዘባችሁ ካለበት ዘንድ ልቡናችሁ ከዚያ ይኖራልና ፣ አንድም ፣ ኢትዝግቡ ብሏህ መልስ ውዳሴ ከንቱ ያለበትን ምጽዋት አትመጽውቱ ዘይ በሊ ውዳሴ ከንቱ የሚያስቀርባችሁን ወኀበ ሰረቅት አጋንንት በውዳሴ ከንቱ የሚያስቀሩባችሁን እላ ያለበት ነው ። ውዳሴ ከንቱ የማያስቀርባችሁን ውዳሴ ከንቱ የሌሰበትን ምጽዋት መጽውቱ እንጂ አጋንንት በውዳሴ ከንቱ የማያስቀሩባችሁን ምጽዋ ታችሁ ካለበት ልቡናችሁ ከዚያ ይኖራልና ። እስመ ዘይገብሩ ለሠናይት ይሴፈዋ ለሠናይት እንዲል ።

፳፪ ማኅቶቱ ለሥጋከ ዓይንከ ውእቱ ። ሉቃ ፣ ፲፩ ፡ ፴፬ ።

፳፪ የሥጋህ ፋና ዓይንህ ነው ማለት የሥራ መከናወኛ ዓይንህ ነው ፣
ወእምከመ ዓይንከ ብሩህውእቱ ኵሉ ሥጋከ ብሩሃ ይከውን ፣ ዓይንህ ብሩህ የሆነ እንደሆነ አካልህ ሁሉ ብሩህ ይሆናል ዓይንህ የቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ የቀና ይሆናል ።

፳፫ ወእመሰ ዓይንከ ሐማሚ ውእቱ ኵለንታከ ጽልመተ ይከውን

፳፫ ዓይንህ የሚታመም የሆነ እንደሆነ እካ ልህ ሁሉ ጨለማ ይሆናል ማለት ዓይንህ ግን ያል ቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ ያልቀና ይሆናል ።
ወሶበ ብርሃን ዘላዕሌከ ጽልመተ ውእቱ ጽልመትከ እፎ ይከውነከ ።
ባንተ ያለ ብርሃን ጨለማ ከሆነ ጨለማህ እንደምን ይሆን ፣ በተፈጥሮ የተሰጠህ ዓይንህ የታመመ ከሆነ ጨለማ እንደምን ይጸናብህ ይሆን ፣ እንድም ጽል መትከ እፎ ብርሃነ ይከውነከ ፣ የታመመው ዓይንህ እንደምን ያይልሃል ፣ እንድም ማኅቶቱ ብለህ መልስ

የሥራህ መከናወኛ አእምሮ ጠባይህ ነው ወእም ከመ ዓይንከ ፡ አእምሮ ጠባይዕህ የቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ የቀና ይሆናል ወሶበ ብርሃን ፡ አእምሮ ጠባይዕህ ያልቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ ያልቀና ይሆናል በተፈጥሮ የተሰጠህ አእምሮ ጠባይዕህ ያልቀና ከሆነ ፍዳ እንደምን ይጸናብህ ይሆን አንድም ጽልመትከ ያልቀና አእምሮ ጠባይዕህ እፎ ብርሃነ ይከውንከ ። እንደምን መከበሪያ መጽደቂያ ይሆንሃል ። አንድም የሥራህ መከናወኛ ምጽዋትህ ነው ፡ ምጽዋትህ ውዳሴ ከንቱ የሌለበት እንደሆነ ሥራህ ሁሉ የቀና ይሆናል ። ምጽዋትህ ግን ውዳሴ ከንቱ ያለበት እንደሆነ ሥራህ ሁሉ ያልቀና ይሆናል ወሶበ ብርሃን ከንተ የሚሰጥ ምጽዋትህ ውዳሴ ከንቱ ያለበት ከሆነ ፍዳ እንደምን ይጸናብህ ይሆን ፤ አንድም ጽልመትከ ውዳሴ ከንቱ ያለበት ምጽዋትህ እፎ ብርሃነ ይከውንከ እንደምን መከበሪያ መጽደቂያ ይሆንሃል ፡ አንድም የሥራህ መከናወኛ ኤጲስ ቆጶስህ ነው ። ኤጲስ ቆጶስ የቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ የቀና ይሆናል ። ኤጲስ ቆጶስህ ግን ያልቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉያልቀና ይሆናል ፤ ኤጲስቆጶስህ ግን ያልቀና እንደሆነ ሥራህ ሁሉ ያልቀና ይሆናል ። ወሶበ ብርሃን ባንተ የተሾመ ኤጲስ ቆጶስህ ያልቀና ከሆነ ፍዳ እንደምን ይጸናብህ ይሆን አንድም ጽልመትከ ፤ ባንተ የተሾመ ኤጲስቆጶስህ እፎ ብርሃነ ይከውንከ እንደምን መከበሪያ መጽደቂያ ይሆንሃል ።

፳፬ ኢይከል ፩ዱ ገብር ተቀንዮ ለ፪ኤ አጋዕዝት ከፍለን መጽውተን ከፍለን ብንኖር ምንዋ ትሉኝ እንደሆነ ። ሉቃ ፡ ፲፮ ፡ ፲፫ ።

፳፬ አንድ ባሪያ ለሁለት ጌታ መገዛት አይቻለውም ።
ወእመአኮስ ፩ደ ይጸልእ ወካልአ ያፈቅር ፤
ይህም ባይሆን ማለት እገዛለሁም ቢል አንዱን ይጠላል አንዱን ይወዳል ፤ ወእመ አኮ ለአሐዱ ይትኤዘዝ ።

ያፈቅር ያለውን ይትኤዘዝ ይይጸልዕ ያለውን ኢይትኤዘዝ አለ ላንዱ ይታዘዛል ለአንዱ አይታዘዝም እንጂ ፡ ሐተታ ፤ አንዱ ቆላ ውረድ ሲለው አንዱ ደጋ ውጣ ቢለው ከሁለት ይሆናልን አይሆንም ሲል ። ኢትክሉኬ ተቀንዮ ለእግዚአብሔር ወለንዋይ ፡- እንደዚሁም ሁሉ እናንተም ለእግዚአብሔርና ለገንዘብ መገዛት አይቻላችሁም ። ወለንዋይ ባለው ወለማሞ ይላል ጥሬ ።

፳፭ ወበእንተዝ እብለከሙ ኢትተከዙ ለነፍስከሙ ዘትበልዑ ወዘትሰትዩ ወኢለሥጋከሙ ዘትለብሱ ። መዝ ፶፬ ፡ ፳፭ ሉቃ ፲፪ ፡ ፳፪ ፊልጵ ፬ ፡ ፮ ። ፩ ጢሞ ፮፡ ፯ ፩ ጴጥ፡ ፭፡ ፯ ።

፳፭ ስለዚህ ነገር ለነፍሳችን ምን እንበላለን ምን እንጠጣለን ለሥጋችን ምን እንለብሳለን ብላችሁ አታስቡ መብል መጠጥን ለነፍስ ሰጥቶ ተናገረ የበሉት የጠጡት ደም ይሆናል በዚህ ምክንያት ነፍስ ከሥጋ ጋራ ተዋሕዳ ትኖራለችና ፡ እስመ ነፍስ ተጋድር በደም እንዲል ልብስን ለሥጋ ሰጥቶ ተናገረ ምንም የምታፍር ነፍስ ብትሆን አጊጾ ከብሮ የሚታይ ሥጋ ነውና ።

አኮሁ ነፍስ ተዓፅብ እምሲሲት ምግብ ከመስጠትማ ነፍስን እምኃበ አልቦ አምጥቶ መፍጠር ጭንቅ አይሆንምን ።
ወሥጋ የዓፅብ እምልብስ ።

ልብስ ከመስጠትማ ሥጋን ካራቱ ባሕርያት አዋሕዶ መፍጢር ጭንቅ አይሆንምን ፡ ነፍስን እምኀበ አልቦ አምጥቼ ሥጋን ካራቱ ባሕርያት አዋሕጄ የፈጠርኋችሁ ለናንተ ምግብ ልብስ እንደምን እነሣችኋለሁ ለማለት እንዲህ አለ ። አንድም አኮሁ ብለህ መልስ ፡ ለናንተ ምግብ ከመስጠትማ ነፍስን ካለችበት ማምጣት ጭንቅ አይሆንምን ? ወሥጋ የዓፅብ ፡ ልብስ ከመስጠትማ ሥጋን ካለበት ማንሣት ጭንቅ አይሆንምን ? ነፍስን ካለችበት አምጥቼ ሥጋን ካለችበት ኋላ በመንግሥተ ሰማይ መንፈሳዊ ምግብ የምመግባችሁ ዛሬ ለናንተ ምግብ ልብስ እነሣችኋለሁን ለማለት ፡ አንድም ወበእንተዝ እብለከሙ ብለህ መልስ ሥጋውን ደሙን ወለሥጋከሙ ዘትለብሱ ። ልጅነትን ማን ይሰጠናል ብላችሁ አታስቡ ሥጋየን ደሜን ከመስጠትማ ነፍስ? ሥጋን መዋሐድ ጭንቅ አይሆንምን ነፍስን ሥጋን የተዋሐድሁላችሁ ፡ ሥጋየን ደሜን እነሣችኋለሁን ለማለት እንዲህ አለ ፡ ጭንቅነቱ በሌላ ነው እንጂ በሱ አይደለም

፳፮ ነጽሩ አዕዋፈ ሰማይ እለ ኢይዘርዑ ወእለ ኢየዓርሩ ወኢያስተጋብኡ ውስተ አብያት ወአቡከሙ ሰማያዊ ይሴስዮሙ ።

፳፮ ከፍለን መጽውተን ከፍለን ካላኖርን ምን እንመገባለን ትሉኝ እንደሆነ ዘር መከር የሌላቸውን በጎታ በጎተራ በረቅ የማይሰበስቡን ሰማያዊ አባታችሁ የሚመግባቸው አዕዋፍን እዩ ማለት አዕዋፍን አብነት አድርጉ ። ከመ ኢይዘርዑ ይላል ዘር መከር እንደሌላቸው በጎታ በጎተራ በረቅ እንዳይሰበስቡ ሰማያዊ አባታችሁ እንዲመግባቸው ዕወቁ ።
አኮኑ አንትሙ ፈድፋደ ትኄይስዎሙ ።

ለኒያማ እንዴታ ትሉኝ እንደሆነ ከተፈጥሮተ አዕዋፍማ ተፈጥሮተ ሰብእ አይበልጥምን ለኒያ ምግብ የሰጠ ለናንተ ይነሣችኋል ለማለት እንዲህ አለ ታሪክ እንደ ሁለት መነኰሳት ይኸን ይዘው በተባሕትዎ ሁነው በረኃብ በጽምዕ የሚያልቁ ሁነዋል ። ኋላ መልአክ እለኢይዘርዑ አለ እንጂ እለ ኢይሰርሩ አለ አላቸው ከዚህ በኋላ ተግባረ እድ ይዘው ራሳቸውን ረድተው የሚኖሩ ሁነዋል ። ከአባ ስልዋኖስ ገዳም እንደ ገባ መነኰሴ እንደምን ሁናችሁ ትኖራላችሁ

አላቸው ተግባረ እድ ይዘን እንኖራለን አሉት ።
እናንተስ ወንጌላውያንም አይደላችሁ ጌታ በወንጌል
ነጽሩ አዕዋፈ ሰማይ ቢል አላቸው ፣ ይህ ነገሩ ሲሳ
ሳብ ከእብ ምኔቱ ደረሰ እናንተ ሥራችሁን አትተው
ሰሱም የሚሻውን መጽሐፍ ባጡት ይመልከት አላ
ቸው ። ቦታ መጣፍ ሰዋተውት ሲመለከት ዋለ ፣
ምግብ የሚመገቡ በደወል ነውና ፤ ደወል አትምቱ
ጊዜያት አይታችሁ ተመገቡ አላቸው ። ጊዜያት
አይተው ተመገበው በየበዓታቸው ሔዱ ። ይጠሩ
ኛል ብሎ ቢያይ የማይጠሩት ሆነ ተደሩት እኃው
እያለ እሱ ካለበት ሄደ ፤ እወ ተደሩ ኢለው በሀገራ
ችሁ እንግዳ አኑሮ መብላት ሥራትን ነው አለው ፤
አንተማ መንፈሳዊ ነህ አትሻውም ብለን እኛ ሥጋ
ውያኑ ተመገብነው አለው ፤ አባቴ አላበጀሁም ብሎ
አነሱን መስሎ የሚኖር ሁነዋል ። አንድም ነጽሩ
ብለህ መልስ ዘር መከር የሌላቸውን ሰማያዊ አባታ
ችሁ የሚመግባቸው እሥራኤልን አብነት አድርጉ
እንዲመግባቸው ዕወቁ እሥራኤል ልብስ አላለቀ
በትርሀ አልወደቀ እንዲሉ ፤ ከውቂያኖስ በደመና
አይበት ተቋጥሮ በነፋስ ወደልጋዝ ተጭኖ መጣኑ
ድምብላል አህሎ መልኩ በረድ መስሎ ወእንዘ
የኃድግ ህቦ ይላል የውርጭ ገበታ ሲነጠፍ እየዘነ
መላቸው ፵ ዘመን መናውን ተመግበዋል ።
አኮኑ አንትሙ ትኄይስዎሙ ።
ለኢያማ እንዴታ ትሉኝ እንደሆነ በዘመነ ብሉይ
ከነበሩ ከኢያማ በዘመነ ሐዲስ ያላችሁ እናንተ ትበ
ልጡ የለምን ለኢያ የሰጠው ለናንተ እንማችኋለሁ
ለማለት እንዲህ አለ ። እንድም ነጽሩ ብለህ መልስ
ትንቢት ያልተነገረላቸውን ሱባዔ ያልተቈጠረላቸ
ውን ሰማያዊ አባታችሁ ሥጋውን ደሙን የሚመ
ግባቸው አሕዛብን አብነት አድርጉ እንዲመግባቸው
ዕወቁ ። ለኢያማ እንዴታ ትሉኝ እንደሆነ
ትንቢት ካልተነገረላቸው ሱባዔ ካልተቈጠረላቸው
ከአሕዛብማ ትንቢት የተነገረላችሁ ሱባዔ የተቈ
ጠረላችሁ እናንተ የምትበልጡ አይደለምን ።

፳፯ መኑ እምኔክሙ በተከዞ ዘይክል ወስኮ
በዲበ ቆሙ አሐደ እመተ ።

፳፯ በዚያውስ ላይ ራሳችሁንማ አስባችሁ ታሳ
ድሩ ዘንድ ከናንተ ወገን እጠርሁና ልርዘም
ብሎ በቁመቱ ላይ ከንድ ሙሉ ቁመት መጨመር
የሚቻለው ማነው እንደዚህም ሁሉ በቃሁ ነቃሁ
ብሎ ሥልጣነ ክህነትን ለራሱ ገንዘብ ማድረግ የሚ
ቻለው ማነው ።

፳፰ ወበእንተ ዓራዝኒ ምንተኑ ትሔልዩ ።

፳፰ የልብሳንስ ነገር ለምን ታስባላችሁ ።
ርእዩ ጽጌያተ ገዳም ዘከመ ይልሕቁ ኢይጻምዉ
ወኢይፈትሉ ።
ሳይደክሙ ሳይፈትሉ እንዲያድጉ ማለት ገዳማት
ዕፀዋትን ዕፀዋት ጽጌያትን ጽጌያት መወደድን አጊ
ጸው እንዲኖሩ ዕወቁ ።

፳፱ እብለክሙ ከመ ሰሎሞን ጥቀ ኢለብሰ
በኵሉ ክብሩ ከመ ፩ እምእሉ ።

፳፱ ሰሎሞንስ እንኳ በዚያ ሁሉ ባለጠግነቱ
ከጽጌያት አንዳንዱ አለበሰም ብየ እንዳለበሰ እነግ
ራችኋለሁ ። ሐተታ አበባ ያለበት ቀፈግ የተሳበበት
ወርቅ ዘቦ ግምጃ ይለብስ አልነበረም ቢሉ የሱ የባ
ሕርዩ አይደለም የእሳቸው ግን የባሕርያቸው ነውና
እሱ እነዚያን አብነት አድርጎ ነው ፤ እነዚያ ግን
እሱን አብነት አያደርጉምና በሁሉ ክብሩ ማለቱ
ብፅልን ካንተ ፀሬት እንዳልተነሣ ካንተም በኋላ
እንዳይነሣ አድርጌ ሰጥቸሃለሁ ብሎታልና ፤ አን
ድም ወበእንተ አራዝኒ ብለህ መልስ የልጅነትን
ነገር ለምን ታስባላችሁ ትንቢት ያልተነገረላቸው
ሱባዔ ያልተቈጠረላቸው ልጅነትን ያገኙ አሕዛብን
አብነት አድርጉ ። እብለክሙ ከመ ሰሎሞን እሥራ
ኤልን በመከበባቸው ሰሎሞን አላቸው እሥራኤልስ
እንኳ በዚያ ሁሉ ትንቢት በዚያ ሁሉ ሱባዔ ከአ
ሕዛብ እንዳንዱ ልጅነትን አላገኙም ብየ እንዳላ
ገኙ እነግራችኋለሁ ።

፴ ወናሁ ሣዕረ ገዳም ዘዮም ሀሎ ወጌሠመ
ውስተ ዕቶነ እሳት ይትወደይ ወእግዚእብሔር ዘከ
መዝ ያለብሶ ።

፴ የሚያስተምርበት ደጋ ነው ቢሉ ነገ በቆላ
መንደድ ጸዐተ ክረምት ነው ቢሉ ነገ በበጋ መንደድ
የሚነድ ሣዕረ ገዳምን ዛሬ በልምላሜ የሚያኖር እግ
ዚአብሔር ፤
እፎ እንከ ፈድፋደ ኪያክሙ እሕጹጻነ ሃይማኖት ፤
እናንት ሃይማኖት የሌላችሁ ለናንተማ እንደምን
ልብስ ምግብ ይነሣችኋል ፤ ወሊእመ ኮነ ሥርወ ጽጌ
ይላል ፣ በሉቃስ ሥርወ ጽጌ ዛሬ በልምላሜ የሚኖር
ከሆነ ኋላ በቆላ መንደድ የሚነድ ከሆነ እግዚአብ
ሔርም እንዲህ በልምላሜ የሚያኖረው ከሆነ ። እፎ
ኪያክሙ እንድም ወናሁ ሣዕረ ገዳም ብለህ መልስ
ዛሬ በተድላ የሚኖር ኋላ በገሃነም ፍዳ የሚቀበል
አይሁዳዊን በተድላ የሚያኖር እግዚአብሔር እፎ
ኪያክሙ ። እንድም አይሁዳዊ ዛሬ በተድላ የሚኖር
ከሆነ ኋላ በገሃነም ፍዳ የሚቀበል ከሆነ እግዚአብ
ሔር ይህነን በተድላ የሚኖር ከሆነ እፎ ኪያክሙ
እናንት ሃይማኖት የሌላችሁ እናንተንማ እንደምን
ቸል ይላችኋል ።

፴፩ ኢትተከዙኬ እንከ እንዘ ትብሉ ምንተ
ንበልዕ ወምንተ ንሰቲ ወምንተ ንትከደን ።

፴፩ ምን እንበላለን ምን እንጠጣለን ምን እን
ለብሳለን ብላችሁ አታስቡ ።

፴፪ እስመ ዘንተሰ ኵሎ አሕዛበ ዓለም ዘእፍአ የኀሥሥዎ ፤

፴፪ ይህንስ ሁሉ ከምግባር ከሃይማኖት በእፍአ ያሉ አሕዛብ ይሹታልና ፡፡
ወለክሙሰ የአምር አቡክሙ ሰማያዊ ከመ ትፈቅዱ ዘንተ ኵሎ ፡፡
ለናንተስ ሰማያዊ አባታችሁ ይህን ሁሉ እንድትሹት ያውቅባችኋል ማለት ፀውቆ ይሰጣችኋል ፡፡

፴፫ አ ንትሙሰ ኅሡ መቅድመ መንግሥቶ ወጽድቆ ፡፡

፴፫ እናንተስ አስቀድሞ ሃይማኖትን ምግባርን ሹ ፤ አንድም ፡ ልጅነትን መንግሥተ ሰማይን ሹ ፡፡
ወዝንቱ ኵሉ ይትዌሰከክሙ ፡፡
ይህሉ ሁሉ ማለት የዚህ ዓለምስ ነገር ሁሉ በእሩቅ ላይ ዳረጎት እንዲጨመር ይጨመርላችኋል ፡፡

፴፬ ኢትበሉኬ ለጌሠም ፡፡

፴፬ ለነገ አታስቡ ማለት ለነገ ይሆናል ብላችሁ አታሳድሩ ፡፡
እስመ ጌሠምሰ ትሔሊ ለርእሳ ነገ ለራሱ ያስባል ማለት የነገውን ነገ ታስቡታላችሁና ፡፡
የእክላ ለዕለት እኪያ ወሥራኃ የዕለት ጻሕ ጋሕ ይበቃታል ፤ የበጐ ጻር የበጐ ጋር ፡ አንድም ኢትበሉ እያልክ መልስ ፤ ለነገ ያጸናናል ብላችሁ አብዝታችሁ አትመገቡ ፡፡ የነገውን ነገ ትመገቡታላችሁና ፡ አንድም ነገ እንናዘዝዋለን ብላችሁ ኃጢአታችሁን አታሳድሩ የነገውን ነገ ትናገሩታላችሁና ፡፡ የነገውንስ ነገ ትናገሩታላችሁ ፡፡

በእንተ ትእዛዛት ፡፡

ምዕራፍ ፯ ፡፡

፩ ኢትኰንኑ ከመ ኢትትኰነኑ ሉቃ፡ ፮፡ ፴፯ ፡ ሮሜ ፪ ፡ ፩ ፡፡

፩ አንቀጸ መምህራን ነው ፤ እንዳይፈረድባችሁ አትፍረዱ ማለት ንጹሐን ሳትሆኑ አትፍረዱ

፪ እስመ በኵነኔ ዘኰነንክሙ ትትኰነኑ አንትሙ ፡፡ ማር ፬ ፡ ፳፬ ንጹሕ ሳትሆኑ ብትፈርዱ ይፈርድባችኋልና ፡፡ ይህስ አይደለም ሰማይኒ ኢኮነ ንጹሐ በቅድሜሁ ይላል ብሎ ሳትሾሙ አትፍረዱ ተሾሞ መፍረድ እንዲገባ ሙሴ በሰለጳድ ኢያሱ በአካን ፤ ቅዱስ ጴጥሮስ በሐናንያ ቅዱስ ጳውሎስ በበርያሱስ ፈርደዋል ፡፡ እስመ በኵነኔ ዘኰነንክሙ ትትኰነኑ አንትሙ ሳትሾሙ ብትፈርዱ ይፈረድባችኋልና ፡፡
ወበመሥፈርት ዘሰፈርክሙ ይሰፍሩ ለክሙ ፡፡

በሰፈራችሁበት ይሰፍሩላችኋልና ፤ በሰፈርህበት ላንን በመዘንህበት ሚዛን እንዲሉ ፡፡

፫ ለምንት ትሬኢ ኃሠረ ዘውስተ ዓይነ ቢጽከ ወሠርዌ ዘውስተ ዓይንከ ኢትኄጽር ፡፡

፫ ባንተ ዓይን ያለ ሠረገላ ቻልታየህ በወንድምህ ዓይን ያለ ጉድፍ ለምን ታያለህ ፡፡
ኢታቢይንኑ ፤
አታስተውልም ፤

፬ ወእፎ ትብሎ ለእኁከ ኅድገኒ አውፅእ ኃሠረ እምውስተ ዓይንከ ፡፡

፬ ወንድምህን ባንተ ዓይን ያለ ጉድፍ ተወኝ ላውጣልህ ለምን ትለዋለህ ፡፡
ወናሁ ኢትሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዓይንከ ፤
ባንተ ዓይን ያለውን ሠረገላ ሳታይ ፡፡

፭ አ መድልው ቅድመ አውፅእ ሠርዌ እምውስተ ዓይንከ ፡፡

፭ አንተ ግብዝ አስቀድመህ ባንተ ዓይን ያለ ሠረገላን አውጣ ወእምዝ ትሬኢ ከአውፅኦ ሐሠረ ዘውስተ ዓይነ እኁከ ፡፡
ከዚህ በኋላ በወንድምህ ዓይን ያለውን ጉድፍ ላውጣልህ ትለዋለህ እንድታወጣለት ትሆናለህ ፤ ምንቱ ትኄጽር ብለሁ መልስ በወንድምህ ልፍረድብህ እንደምን ትለዋለህ አንተ እንዲፈረድብህ ሁነህ ሳለህ አታስተውልም ፡ ወንድምህን ተወኝ ልፍረድብህ እንደምን ትለዋለህ ባንተ እንዲፈረድብህ ሁነህ ሳለህ ፤ አንተ ግብዝ አስቀድመህ አንተ እንዳይፈረድብህ ሁን ከዚህ በኋላ ወንድምህን ልፍረድብህ ትለዋለህ ፡ እንድትፈርድበት ትሆናለህ ሐተታ የወንድሙን ኃጢአት በጉድፍ የሱን በሠረገላ መስሎ ተናገረ የወንድሙን ኃጢአት የሚያውቀው በከፊል ነው የሱን ግን መላውን ነውና ዳግመኛ ልፍረድብህ በማለቱ ይፈረድበታልና ፡ አንድም ኢትኰንኑ ፡ ከጉባኤ ሳትውሉ ምሥጢር ሳታደላድሉ እናስተምራለን አትበሉ ፡፡ እናስተምራለን ብትሉ ይፈረድባችኋልና ፡፡ ወንድምህን ላስተምርህ እንደምን ትለዋለህ አንተ ሳትማር አታስተውልም ወንድምህን ተወኝ ላስተምርህ እንደምን ትለዋለህ ፡፡ አንት ሳትማር ፡ አንት ግብዝ አስቀድሞ አንተ ተማር ዕወቅ ፡፡ ከዚህ በኋላ ወንድምህን ላስተምርህ ትለዋለህ እንድታስተምረው ትሆናለህ ፡፡ አንድም ለራሳችሁ ጦር ሳይጠፋላችሁ ጾር የሚጠፋበትን ግብር ለሌላው እናስተምራለን አትበሉ ፡፡ ጾር ሳይጠፋላችሁ እናስተምራለን ብትሉ ይፈረድባችኋልና ፡፡ ወንድምህን ጾር የሚጠፋበትን ግብር ላስተምርህ ለምን ትለዋለህ ላንተ ጾር ሳይጠፋልህ አታስተውልም ፡፡ አንተ ግብዝ አስቀድመህ አንተ ጾር እንዲጠፋልህ ሁን ከዚህ በኋላ ወንድምህን ጾር የሚጠፋበትን ግብር ላስተ

ምርህ ትለዋለህ እንድታስተምረው ትሆናለህ ።

፮ ኢተሀቡ ቅድሳተ ለከለባት ። ማቴ ፳፩ ፳፪ ማር ፲፩ ፥ ፳ ፥ ፱ ፥ ሉቃ ፲፩ ፥ ፱ ፥ ዮሐ ፲፬ ፥ ፲፫ ፥ ያዕቆብ ፩ ፥ ፮ ።

፮ የተቀደሰውን ለውሾች አትስጡ ማለት ሊት ኩንን ካለንስ ብላችሁ ሥጋዬን ደሜን በአይሁዳዊ ነት ግብር ላለ ሰው አትስጡ ።
ወኢትደዩ ባሕርየክሙ ቅድመ አኅርው ፤
ዕንቋችሁንም በእሪያ ፊት አታኑሩ ።
ከመ ኢይኪድዎ በእገሪሆሙ ፤
በእግራቸው እንዳይረግጡት ።
ወተመይጦሙ ይሥጥጡክሙ
ተመልሰው ይጸዷችኋል ። ሐተታ በእግራቸው ተን ጥዕየ ፀሐይ ይጸናል ። ሌሊት ፅንቍ ከተራራ ላይ አኑረው የሚጸፍ ሲጸፍ የሚያድን ሲያድን ያድራል። እሪያ መልክ ጥሩ ነው ባጠገቡ ፤ ሲሄድ የገዛ መልኩን አይቶ ደንግጦ ሲሔድ ሰብሮት ይሄዳል ዕንቍ የጌታ እሪያ የአይሁድ ምሳሌ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እያለ በገዛ ኃጢአታቸው ቢዘልፋቸው ጠልተው ተመቅኝተው ሰቅለው ገድለውታልና ፤ ከመ ኢይኪድዎ እንዳይነቅፉት ወተመይጦሙ አማርኛችን ካማርኛችሁ ኃይለ ቃላችን ከኃይለ ቃላችሁ እያሉ ተመልሰው ፍትሐ ርትዑ ሥላሴን ያስፈርዱባችኋልና አንድም ኢተሀቡ እያልሀ መልስ ሃይማኖታችሁን ለመናፍቅ አትንገሩ ከመ ኢይኪድዎ እንዳይነቅፉት ወተመይጦሙ ፤ አማርኛን ካማርኛችሁ ኃይለ ቃላችን ከኃይለ ቃላችሁ አንድ ነው እያሉ ይከራከሯችኋልና አንድም መልስ በተዓቅቦ ያገኛችሁትን ምሥጢር ላልበቃ ሰው አትንገሩ ሰው ሲሆኑ ስዚህን ይበቃሉ እንዳይሏችሁ ፤ ወተመይጦሙ ተመልሰው ፍትሐ ርትዑ ሥላሴን ያስፈርዱባችኋል ።

፯ ሰአሉ ወይትወሀበክሙ ፤
የበቃውን ያልበቃውን በምን እናውቀዋለን ትሉኝ እንደ ሆነ ፥
፯ ለምኑ ይሰጣችኋል ሐተታ እንደ ዮሐንስ ዘደማስቆ ፥ እንደ ድሜጥሮስ የበቃና ያልበቃ ለይተው ይሰጡ ነበር ።
ኅሡ ወትረክቡ ።
ሹ ታገኛላችሁ ።
ጐድጕዱ ወይትረኃወክሙ ፤
አጅ ጽኑ ይከፈትላችኋል ።

፰ እስመ ኵሉ ዘሰአለ ይነሥእ ።
፰ የለመነ ሁሉ ያገኛልና ፥ በእሉ ለምነው ያገኙ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን አዳም ፤
ወዘኂሠ ይረክብ ፤
የሻም ያገኛልና ኅሡ ፤ ሽተው ያገኙ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን ከቀደሙ ሰዎች አብርሃም ከኋላ ሰዎች ሙሴ ጸሊም በዐሐይ ብሥነ ጉጥረት ተመራምረው አምነዋል ።
ወለዘኂ ጐድጐደ ይትረኃዎ ።
እጁን ለጸፋም ይከፈትለታልና ጐድጕዱ ሳለው እንደ ፊያታይ ዘየማን ።

፱ መኑ ውእቱ እምኔክሙ ዘይሰእሎ ወልዱ ወእብነ ይሁቦ ፤

፱ እኛ ለሌላው በጐ ነገር ስንለምን በኛ ክፉ ነገር ቢደረግብንሳ ትሉኝ እንደሆነ ከናንተ ወገን ልጁ ዳቦ የሚለምነው አባቱ ደንጊያ የሚሰጠው ማን አለ ፤ አንድም እብነኑ ይሁብ ልጁ ዳቦ ቢሏም ነው ቀርሱን ይስበረው ብሎ ደንጊያ ይሰጠዋልን ከዚያው ቅሉ ሳይላዩን ትቶ ልብ ልቡን ይሰጠው የለምን ።

፲ ወእመኂ ዓሣ ሰአሎ ወአርዌ ምድር ይሁቦ ።

፲ ከናንተ ወገን ልጁ ዓሣ የሚለምነው አባቱ እባብ የሚሰጠው ማን አለ አርዌ ምድርኑ ይሁብ መርዙ ይገድለው ብሎ እባብ ይሰጠዋልን ፤ ከዚያው ቅሉ አጥንት አጥንቱን ትቶ ሥጋ ሥጋውን ይሰጠው የለም ቢሉቃስ ወእመኒ አንቆቅሆ ሰአሎ አቅረበኑ ይሁቦ ይላል ። ልጁ ዕንቁላል የሚለምነው አባቱ እምቧይ የሚሰጠው ማን አለ ፥ አንድም ልጁ ዕንቁላል ቢለምነው አባቱ እንቧይ ይሰጠዋልን ከዚያም ቅሉ ቅርፍት ቅርፍትን ትቶ አስኳል አስኳሉን ይሰጠው የለምን ።

፲፩ ወሶበ አንትሙ እኩያን አንትሙ ተአምሩ ሠናየ ሀብተ ወሂበ ለውሉድክሙ እፎ እንከ ፈድፋደ አቡክሙ ዘበሰማያት ይሁቦሙ ሠናይተ ለእለ ይሰእልዎ ።

፲፩ ክፉ ወገን እንዲህ የሚያደርግ ስ የሰም ትሉኝ እንደሆነ ዘአንትሙ እንዘ አንትሙ ይላል ሰባሕርያችሁ ክፋት ጥመት የሚስማማችሁ ስትሆኑ እናንተ ለልጆቻችሁ በጐ ነገርን የምታደርጉላቸው ከሆነ ቸርነት የባሕርዩ የሚሆን ሰማያዊ አባታችሁማ በጐ ነገርን ለሚለምኑት እንደምን በጐ ነገርን ያደርግላቸው ይሆን ።

፲፪ ኵሎ ዘትፈቅዱ ይግበሩ ለክሙ ሰብእ ከማሁ አንትሙኒ ግበሩ ሎሙ ።

፲፪ ሰዎች ሊያደርጉባችሁ የምትወዱትን ሁሉ እናንተም አድርጉላቸው እስመ ከማሁ ኦሪትኒ ወነቢያትኒ ኦሪት ነቢያት እንዲህ ብለዋልና ባኡ ማንሻ ፤

፲፫ ባኡ እንተ ጸባብ አንቀጽ ።

፲፫ ኦሪትም ነቢያትም ባኡ እንተ ጸባብ አንቀጽ ብለዋልና ወደ ጸባብ በር ግቡ በጸባብ መንገድ ሂዱ ።

እስመ ርሒብ አንቀጽ ወሰፊሕት ፍኖት እንተ ትወስድ ውስተ ኃጉል ።

ወደ ጥፋት የምታደርስ ሰፊ በር ሰፊ መንገድ አለችና፤ ወብዙኃን እሙንቱ እለ ይበውኡ ውስቴታ ፤ ወደርሷ የሚገቡ ብዙ ናቸው ።

፲፬ ጥቀ ጸባብ አንቀጽ ወጽዕቅት ፍኖት እንተ ትወስድ ውስተ ሕይወት ።

፲፬ ወደ ሕይወት የምታደርስ እጅግ ጭንቅ በር እጅግ ጭንቅ መንገድ አለችና ።
ወውኁዳን እሙንቱ እለ ይበውእዋ ፤

ወደሷ የሚገቡ ጥቂት ናቸውና ሰፊውን በር ሰፊውን መንገድ ተታችሁ በጸባብ በር በጸባብ መንገድ ሂዱ ። ሐተታ ሰፊ በር ሰፊ መንገድ የተባለች አሪተ ናት ለእመ ዓቀብከ አሪተከ ትበልዕ ከራሚከ ወይሰፍሕ ማኅበብተ ወያንከ ወትሬኢ ውሉደ ውሉድከ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትውልድ ትላለችና ጠባብ በር ጭንቀ መንገድ የተባለች ወንጌል ናት ለዘሂ ጸፍዓከ መልታሕቴከ እንተ የማን ሚጥ ሎቱ ካልዕታሂ ወለዘሂ አበጠከ አሐደ ምዕራፈ ሑር ምስሌሁ ወአብጽሖ ሎቱ ፪ተ ምዕራፈ ወለዘሂ ይፈቅድ ይትዓገልከ መልበስከ ኅድግ ሎቱ ከዳንከሂ ትላለችና ። አንድም ሰፊ በር ሰፊ መንገድ የተባለ ፈቃደ ሥጋ ነው ጠባብ በር ጠባብ መንገድ የተባለች ፈቃደ ነፍስ ናት።አንድም ሰፊ በር ሰፊ መንገድ የተባለ ባለጸጋን መጽውት ድኃን ጹም ማለት ነው፤ ጠባብ በር ጠባብ መንገድ ባለጸጋን ጹም ድኃን መጽውት ማለት ነው ። አንድም ቆዝራ ደየት መንገድ ናት ። የማና እሳት ወፀጋማ ቀላይ ወኢታገምር ዘእንበለ ቢደተ ፩ዱ እግረ ብእሲ እንዲል ያሳንድ ጫማ የማታበቆም መንገድ አይ ቷል ፤ እሷ ቅሉ በሕገ ነፍስ ካልሆኑ አትገባም ሲል ነው እንጂ በቁሙ አይደለም ከዚህም ጌታን የጸድቃን ማኀበ የኃጥአን መብዛት እያሳዝነውም ጥቂት ፅንቍ ያለው ብዙ ወርቅ ባለው ጥቂት ወርቅ ያለው ብዙ ብር ባለው ጥቂት ብር ያለው ብዙ ብረት ባለው ጥቂት ብረት ያለው ብዙ ሸክላ ባለው ጥቂት ሸክላ ያለው ብዙ ደንጊያ ባለው እንዲይቀጭ ።

፲፭ ተዓቀቡኬ እምሐሳውያን ነቢያት እለ ይመጽኡ ኀቤክሙ በአልባሰ አባግዕ ።

፲፭ የበግ ለምድ ለብሰው ማለት እውነተኞች መስለው ከሚመጡ ከሐሰተኞች ሃይማኖታውያን መስለው ከሚመጡ ከመናፍቃን መንፈሳውያን መስለው ከሚመጡ ከሥጋውያን መምህራን ተጠበቁ ። ወእንተ ውስጠሙሰ ተኩላት መሰጥ እሙንቱ ። በውስጥ ግን ነጣቂ ተኩላ ናቸው ማለት ቢመረምሯቸው ግን ሰውን እየነጠቁ ወደ ገሃነም የሚያወርዱ ናቸው ። በከመ ይቤ ኢዮብ የሚል አብነት ይገኛል ተናግሮ ሳይጻፍ የቀረ ነው ።

፲፮ ወእምፍሬሆሙ ተአምርዎሙ ፤ እውነተኛ መስለው የሚመጡ ሐሰተኞችን ሃይማኖታውያን መስለው የሚመጡ መናፍቃንን መንፈሳውያን መሰለው የሚመጡ ሥጋውያኑን መምህራን በምን እናውቃቸዋለን ትሉኝ እንደሆነ በሥራቸው ታውቁአላችሁ ።

፲፮ ይቀስሙሁ እምአሰዋክ አሰካለ ወእምአሜከላ በለሰ ።
በዚያውስ ላይ ሥራቸውን አንሠራም እንጂ ትምርታቸውንማ ብንማርም ምን ዕዳ ይሆናል ትሉኝ እንደ ሆነ ከሾህ ፍሬን ከደንደር በለስን ይለቅማሉ ከመናፍቅ መምህር ሃይማኖትን ከሥጋዊ መምህር መንፈሳዊ ትምህርትን ከሐሰተኛ መምህር እውነተኛ ትምህርትን ይማራሉን ፡ ከማሁኬ ፤

፲፯ መርዝ መርዝን ኮሶ ኮሶን እንዲያፈራ ፤ መናፍቅ መምህር ክህደትን ኑፋቄን ሥጋዊ መምህር ሥጋዊ ትምርትን ሐሰተኛ መምህር ሐሰትን እንዲያስተምር ።

፲፯ ኵሉ ዕፅ ሠናይ ፍሬ ሠናየ ይፈሪ ። ወይን ወይንን በለስ በለስን ያፈራል ፤ ሃይማኖታዊ መምህር ሃይማኖትን መንፈሳዊ መምህር መንፈሳዊ ትምህርትን እውነተኛ መምህር እውነተኛ ትምህርትን ያስተምራል ።
ወእኩይሰ ዕፅ ፍሬ እኩየ ይፈሪ ።
መርዝ መርዝን ኮሶ ኮሶን ያፈራል ፥ መናፍቅ መምህር ክህደትን ሥጋዊ መምህር ሥጋዊ ትምህርትን ሐሰተኛ መምህር ሐሰትን ያስተምራል ።

፲፰ ኢይክል ዕፅ ሠናይ ፍሬ እኩየ ፈርየ ፤
፲፰ ወይን ኮሶን በለስ መርዝን እያፈራም ። ሃይማኖታዊ መምር ክህደትን መንፈሳዊ መምር ሥጋዊ ትምርትን አያስተምርም ፥ ወኢዕፅ እኩይ ፍሬ ሠናየ ፈርየ ኮሶ ወይንን መርዝ በለስን አያፈራም መናፍቅ መምህር ሃይማኖትን ሥጋዊ መምህር መንፈሳዊ ትምህርትን አያስተምርም ።

፲፱ ኵሉ ዕፅ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይገዘምዎ ። ማቴ ፲፫ ።

፲፱ በጐ ፍሬ የማያፈራውን ዕንጨት ሁሉ ይቆርጡታል ።
ወውስተ እሳት ይወድይዎ ።
ከእሳትም ይጨምሩታል ። አንድም በጎ እምነት በጐ ሥራ የማይሠራውን ሁሉ ሥጋዊ ነፍሱን ከሥጋው ይለዩታል በገሃነም ፍዳ ያጸኑበታል ።
፳ ወእምፍሬሆሙሰ ተአምርዎሙ ።
፳ ቢርቀው ቢያምረው ደገሙው እኮ ዙሉ ዘይብለኒ እግዚአ ።
፳፩ እግዚአ ዘይበውእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ። ማቴ ፳፭ ፡ ፲፩ ፡ ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፵፮ ።

፳፩ ሁሉ አቤቱ አቤቱ ይልሃል የሚገባውንስ የማይገባውንስ በምን እናውቀዋለን ትሉኝ እንደሆነ አቤቱ አቤቱ የሚለኝ ሁሉ መንግሥተ ሰማያት አይ ገባም ። እኮ ዘይበውእ ። የሚገባ አይደለም ። ዘእንበለ ዘይገብር ፈቃዶ ለአቡየ ዘበሰማያት ፤ የሰማያዊ አባቴን ፈቃድ የሠራ ይገባል እንጂ ።

፳፪ ወብዙኃን ይብሉኒ በይእቲ ዕለት እግዚኦ እግዚኦ ።

፳፪ በዕለተ ምጽአት ብዙ ሰዎች አቤቱ አቤቱ ይሉኛል ።

አኮኑ በስምከ ተነበይነ ። ዘኍ ፳፬ ፤ ፩ ፤ ፲፯ ። በስምህ መጻእያትን ተናግረን የለም ይሉኛል እለ ። በስዓም ኮከብ ይሠርቅ እምያዕቆብ ብሎ ተናግሯልና ። ወበስ ምከ አጋንንተ አውፃእነ ። ግብ. ፲፱ ፤ ፲፪ ። በስምህ አጋንንትን ስናወጣ አልነበርንም ይሉኛል ደቂቀ አስቂዋ ጋኔን ያወጡ ነበር ። ወበስምከ ኃይ ላተ ብዙኃ ገበርነ በስምህ ፍጹም ታምራት ስናደርግ አልነበርንም ይሉኛል ። ይሁዳ ሙት እስከ ማንሣት ደርሶ ነበርና ።

፳፫ ወይእተ ጊዜ እብሎሙ ግሙራ ኢየአምረ ክሙ ረኃቁ እምኔየ ኵልክሙ እለ ትገብሩ ዓመፃ ። መዝ. ፮ ፤ ፱ ፤ ማቴ. ፳፭ ፤ ፵፩ ፤ ሉቃ. ፲፫ ፤ ፳፯ ።

፳፫ ያን ጊዜ ከቶ አላውቃችሁም ዓመፅን የም ትሠሩ ሁላችሁም ከኔ ራቁ እላቸዋለሁ ። ሐተታ ፤ ፈጥርስ አላውቃችሁም አይልም ። ወስድ ኋችሁ ካድኋችሁ እላቸዋለሁ ።

፳፬ ኵሉ ኬ ዘይሰምዖ ዘንተ ቃልየ ወይገብር ይመስል ብእሴ ጠቢበ ዘሐነጸ ቤቶ ዲበ ኰኵሕ ሉቃ. ፮ ፤ ፵፰ ፤ ሮሜ ፪ ፤ ፲፫ ፤ ያዕ. ፩ ፤ ፳፪ ።

፳፬ ይኸን የኔን ነገር ሰምቶ የሚሠራው ሰው ሁሉ ቤቱን በጭንጫ ላይ የሠራ ብልህ ሰውን ይመ ስላል ።

፳፭ ዘነመ ዝናማት ።

፳፭ ዝናም ዘነመ ።

ወውኅዙ ወሐይዝት ።

ጎርፍ ጎረፈ ።

ወነፍሑ ነፋሳት ።

ነፋስ ነፈሰ ።

ወገፍዕዎ ለውእቱ ቤት ።

ያን ቤት እናናውጽሕ አሉት ፣ ወኢወድቀ ፣ አልተና ወጸም እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ከጭንጫ ላይ ተሠርቷልና ሐተታ ፣ እንደምን አድርገው ይሠሩታል ቢሉ ዘይት ያፈሱበታል ይላሳል ያን እየቆፈሩ ይመ ሠርቱበታል ይጸናል ። እንድም ኵሉ ዘይሰምዕ ብስሀ መልስ ። ይህን የኔን ቃል ሰምቶ የሚሠራው ሁሉ ሃይማኖቱን በበጐ ልቡና የያዘ ብልህ ሰውን ይመስላል ዘነመ ዝናማት ከዓላውያን ነገሥታት ከዓላውያን መኳንንት የሚመጣ መከራ ነው ። ውኅዙ ወኃይ ዝት መከራ እቀበላለሁ ባለ ጊዜ ሕዋሳቱ ይፈሩበታል ነፍሑ ነፋሳት ። ቤተሰቦቹ ንጉሥ የወደደውን ዘመን የወሰደውን ይዘህ አትኖርም ይሉታል ። ያን ሰው ሃይማኖትህን እናስለቅቅህ ይሉታል ። ወኢወድቀ አለቀቀም ። እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ፣ ሃይማኖ ቱን በበጐ ልቡና ይዟልና ፣ እንድም የኔን ቃል ሰምቶ የሚሠራ ሰው ሁሉ ሃይማኖቱን ምግባሩን እንደ ኢዮ ብባለ ሰውነት የያዘ ብልህ ሰውን ይመስላል ። ዘነሙ ሞተ ውሉድ ጥፍዓተ ንዋይ ነው ። ወውኅዙ ። በራሱ የሚመጣ ደዌ ነፍሑ አጋንንት በሚሰቱ አድረው እስከ ማእዜኑ ትብል ኢዮብ እትዔገሥ ለእግዚአብ ሔር በየውሃት እምእይዜሰ ባርኮሁ ወሙት ብለው ታል ። ወገፍዕዎ ይህን ሰው ሃይማኖቱን ምግባሩን እናስለቅቅህ አሉት አለቀቀም ። እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ሃይማኖቱን ምግባሩን እንደ ኢዮብ ባለ ሰውነት ይዟልና ። እንድም የኔን ቃል ሰምቶ የሚ ሠራው ሰው ሁሉ በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን የሚ ኖር ብልህ ሰውን ይመስላል ነፍሑ ባሰው ይነሷል ነፍሑ ። አጋንንት በሕሊና ያወጡታል ያወርፉታል እንደ እንጦስ እንደመቃርስ ንጽሕ ጠብቄ ከቤት ርቄ እኖራለሁ ያሰኙታል ሂዶ ስመምሀረ ንስሐው ይነግረዋል ቆይ ይለዋል ። ዘነሙ ዝናማት ፣ እንደ እንጦስ እንደ መቃርስ ንጽሕ ጠብቄ ከቤት ርቄ መኖር አይቻለኝም እንደ ኢዮብ እንደ አብርሃም በሕግ ጸንቼ እኖራለሁ ያሰኙታል ይህን ሂዶ ስመምሀረ ንስሐው ይነግረዋል ። እሉም የሰይጣን ጾር እንደሆነ በሙቶ ቆይ ይለዋል ፤ ወውኅዙ ፤ ሁሉም አይሆ ንልኝም ያሰኙታል ፤ ወገፍዕዎ እናስለቅቅሃለን ይሉ ታል አለቀቀም ። እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ። በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን ይኖራልና ። ይህ ሰው ወድቆ ተነሥቶ በሕሊናው ድል ነሥቷቸዋል ፣ ወመ ዊቶ ተንሢኦ ስፈኖሙ ስሕያዋን ወስሙታን እን ዳስው ጌታን ።

፳፮ ወኵሉ ዘይሰምዕ ዘንተ ቃልየ ወኢይገብር ይመስል ብእሴ ዓብደ ዘሐነጸ ቤቶ ዲበ ኆፃ ።

፳፮ ይህን የኔን ቃል ሰምቶ የማይሠራው ሰው ሁሉ ቤቱን በድብሽት ላይ የሠራ ሰነፍ ሰውን ይመ ስላል ።

፳፯ ዘነሙ ዝናማት ፤

፳፯ ዝናም ዘነመ ፤

ወውኅዙ ወኃይዝት ፤

ጐርፍ ጐረፈ ፤

ወነፋሑ ነፋሳት ፤

ነፋስ ነፈሰ ፤

ወገፍዕዎ ለውእቱ ቤት ፤

ያን ቤት እናናዋውጽሕ አሉት ወወድቀ ፤

ወደቀ ፤

ወኮነ ድቀቱ ዓቢየ ፤
የንፍስ ነውና ዓቢየ አለ ፤

፳፰ ወሶበ ፈጸመ እግዚእ ኢየሱስ ዘንተ ነገረ ተደሙ አሕዛብ ወአንከሩ ምሕረቶ ፤

፳፰ ጌታ ይህን አስተምሮ ከፈጸመ በኋላ ሕዝቡ ትምህርቱን አደነቁ ፤

፳፱ እስመ ከመ መኰንን ይሜህሮሙ ፤ ማር ፩ ፡ ፳፪ ፡ ሉቃ ፬፡፴፪ ።

፳፱ እንደ ንጉሥ አንስ እብለክሙ እያለ ያስተምራቸዋልና ፤ ወአኮ ከመ ጸሐፍቶሙ ከመዝ ይብሉክሙ ንጉሥ እንደሚሉ እንደ ሹማምንቱ ያይደለ እንድም እንደ አብ አንስ እብለክሙ እያለ ያስተምራቸዋልና ፤ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር እንደ ሚሉ እንደ ዓበይተ ነቢያት ያይደለ ፤ እንድም ሠራዒ ሕግ እንደመሆኑ ያስተምራቸዋልና ፤ ከመዝ ይቤ ሙሴ ከመዝ ይቤ ሳሙኤል እንደሚሉ እንደ ደቂቀ ነቢያት ያይደለ ፤ እንድም ፈጻሚ ሕግ እን ደመሆኑ ያስተምራቸዋልና ፤ ወለሊሆሙስ በአጽባዕ ቶሙ ጥቀ ኢይለክፍዎ ለውእቱ ጾር እንዳላቸው እንደ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ያይደለ ። እንድም ከመ ሥል ጣን ቦ ይላል አብነት ላንደ ጌትነቱ በርኅራኄ ያስ ተምራቸዋልና ፤ እስመ ቅንየትከ ወምልክናከ ይሬ ስየከ ትሠሃል ላዕለ ኵሉ እንዲል ።
ወአኮ ከመ ጸሕፍቶሙ ።
ከወርቁ የጸራውን ከግምጃው ያማረውን ከላሙ የለባውን እንደሚሉ እንደ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ያይደለ ።

በእንተ አድኅኖተ ለምጽ ።

ምዕራፍ ፰

፩ ወእንዘ ይወርድ እምደብር ተለውዎ ሰብእ ብዙኃን ።
በጌታ ከብፁዓን ጀምሮ እስከዚህ ያንድ ቀን ነው

፩ ጉባኤው ሲፈታ ብዙ ሰዎች ተከተሉት የቀሩትን አይከተሏቸውም እሱን ተከተሉት አስ ቢራቡ ይመግባቸዋል ቢታመሙ ይፈውሳቸዋል ቢሞቱ ያነሣቸዋልና ።

፪ ወናሁ መጽአ ፩ ብእሲ ዘለምጽ ቀርበ ወሰ ገደ ሎቱ ። ማር ፩ ፡ ፵ ሉቃ ፡ ፭ ፡ ፲፪ ።

፪ ብዙኃን ካላቸው ለምጽ የያዘው አንድ ሰው ቀርቦ ሰገደለት ።

እንዘ ይብል እግዚኦ እመሰ ፈቀድከ ትክል አንጽሖትየ አቤቱ ከወደድክስ እኔን ከለምጽ ማዳን ይቻልሃል ሐተታ ለምጻምን የምታስተራኩስ አሪትን እሱ እንደሠራት ለማጠየቅ እንዳሳለፋትም ለማጠየቅ ለልማዱ ለምጻም አይቀርብም ነበር ።

፫ ወሰፍሐ እዴሁ ወገሠሦ ።

፫ እጁን ዘርግቶ ዳሠሠው በሁለንቱናው ሕይ ወት እንደሆነ ለማጠየቅ ምትሐት እንዳይደለ ለማ ጠየቅ አሪትን እንዳሳለፋት ለማጠየቅ ለልማዱ ለም ጻም አይዳሰስም ነበርና ።
ወይቤሎ እፈቅድ ንጻሕ ፤
መዳንህን እወዳለሁ ዳን አለው ወነጽሐ እምልምጹ በጊዜሃ ፤ ያን ጊዜ ከለምጹ ዳነ በሐልዮ ፈውሶ በነ ቢብ አዳነው ። እስመ ህብተ ፈውስ ዘይከውን እምኔሁ ይቀድሞ ለንባቡ እንዲል ።

፬ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዑቅ ኢትንግር ወኢለመኑሂ ዘሌዋ ፡ ፲፬ ፡ ፪ ።

፬ ለማንም ለማን እንዳትነግር ዕወቅ አለው ። ውዳሴ ከንቱ አይሻምና የሚያምኑበት ጊዜ አልደ ረሰምና እስከ ትንሣኤ ድረስ ወባሕቱ ሑር አፍትን ርእሰከ ለካህን ፤
ሂደህ ራስህን ለካህን አስመርምር እንጂ ፤
ወአብእ መባዓከ በእንተ ዘንጻሕከ ፤
ከለምጽሕ ስለ ዳንህ መባሕን ስጥ እንጂ ።
በከመ አዘዘ ሙሴ ።
ሙሴ እንዳዘዘ ።
ከመ ይኩን ስምዓ ላዕሌሆሙ በለመኑ መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ምነው ያላመናችሁ ይሏቸዋል ምን አይተን እንመን ይላሉ ያውሳ ለምጻሙን እያ ዳነ መባው እየመጣላችሁ ትበሉ የነበረ ተብሎ አፍትን ርእሰከ ለካህን ማለቱ የሆነውንም ያልሆነ ውንም ለምጻም አዳንኩ እያለ ምኩራባችንን ቢያ ሳድፍብን ከሞቱ ገባንበት ባሉ ነበርና እንዳይሉ የለምጽን ነገር ከዚህ ይናገሩታል ለምጽ በብዙ ነገር ይመጣባቸዋል ባልና ሚስት የታመሙ እንደ ሆነ ካሊጋው ከምንጣፉ የሜኝ ዋጋ ቢያስቀሩ በመ ሜኛው ባይበቱ የጸሐፊ ዋጋ ቢያስቀሩ በመጽሐፉ የሐናጺ ዋጋ ቢያስቀሩ በሕንፃው ተወግቶ ኑሮ እሳትም ፈጅቶት ኑሮ ሲሽር ከትራቱ ይወጣል ። ፍጹም ለምፃም አለ ፤ ህንብርብር አለ ፍጹም ለም ጻሙን አይለዩትም ከቀቢጸ ተስፋ ደርሱዋልና ወደ አሕዛብ ይሄዳል ፤ ብለው ህንብርብሩን ይለዩታል ከቀቢጸ ተስፋ አልደረሰምና ወደ አሕዛብ አይሄ ድም ብለው ፍጹም ለምጻሙን ሥራት ይሠሩብታል አትከናነብ እፍህን ሽፍን ወገብህን አትታጠቅ ጫማ አታድርግ ይሉታል ፤ ይህ የከሃዲ ምሳሌ ነው ። አትከናነብ ማለታቸው ለጊዜው ደዌው ተገልጦ እንዲታይ ነው ። ፍጻሜው ግን ልዕልና ሃይማኖት የለህም ሲሉት ነው ። እፍህን ሽፍን ማለታቸው ለጊዜው ደዌው በእስትንፋሱ ወደ ሕያዋን እንዳ ይናኝ ነው ፍጻሜው ግን ማስተማር አይገባህም

ሲሉት ነው ። ወንብህን አትታጠቅ ማለታቸው ለጊዜው ሰውነቱ ልህሉህ ነውና እንዳይሰማው ነው ፍጻሜው ግን ንጽሕና የለህም ሲሉት ነው ። ጫማ አታድርግ ማለታቸው ምግባረ ወንጌል የለህም ሲሉት ነው ፤ አይለዩትም አለ ከሃዲ የታወቀ ነው፡አይስ ብምና፡ ህንብርብር የመናፍቅ ምሳሌ ይለዩታል አለ ነኝ እያለ ይሰባልና ፡ አንድም ወእንዘ ይወርድ ብሉሀ መልስ ከልዕልና ወደ ትሕትና በመጣ ጊዜ ነቢያት በግብር መሰሉት ። ወናሁ መጽአ ፤ በፍዳ የተያዘ አዳም መጥቶ ሰገደለት ። እግዚእ እመሰ ፈቀድከ እቤቱ ከወደድህስ እኔን ከፍዳ ማዳን ይቻልሃል ። ወሰፍሐ እዴሁ ፤ እጁን ዘርግቶ ተሰቀለለት ። የማነ እዴየ መጠውክምሙ ወትነትሙ ቀምቀተ እንዲል ፡ እፈቅድ ንጻሕ መድኃኒነ እወዳለሁ ዳን አለው ። ወነጽሐ እምለምጹ በጊዜሃ ያን ጊዜ ፈጥኖ ከፍዳው ዳነውቅ ኢትንግር ፤ ኃጢአትህን ለማንም ለማን አትናገር አለው ፡ በአዳም መላውን መናገር ነው ። ሑር ወአፍትን ለመምህረ ንስሐህ ንገር እንጂ ፤ ወአብእ መባኣከ ፤ ከፍዳህ ስለ ዳንከ ቀኖናህን ፈጽም እንጂ ፤ በከመ አዘዘ ሙሴ ፡ ቄሱ እንዳዘዘ ፡ ከመ ይኩን ስምዓ ፤ በኢተነሳሕያን መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ።

፭ ወበዊአ ቅፍርናሆም መጽአ ኀቤሁ መስፍን ምእት ፤ ሉቃ ፡ ፯ ፡ ፩ ።

፭ ቅፍርናሆም ብገባ ጊዜ የመቶ አዝማች መጣ

፮ ወይቤሎ ብቁዓኒ እግዚእ ቍልዔየ ድውይ ወሕሙም ጥቀ ።

፮ ልጄ ታሟል ፡ ደዌ ጸንቶበታል ወይሰክብ ውስተ ቤተ መዋርዕ ፤ ከሕሙማን ቤት ተኝቷል አለው ፤ በሀገራቸው የድውያን ቤት አንድ ነው ለባለጸጋው የመጣው ምግብ ለድሃው እንዲተርፈው ደዌ ከሕሙማን ወደ ሕያዋን እንዳይተላለፍ ፤ ያል ጸናበት የጸናበትን አይቶ እግዚአብሔርን እንዲያ መሰግን ። አንድም ወይሰክብ ውስተ ቤት ብሎ ወመፃጕዕ ጥቀ ይላል ፈጽሞ ጸንቶበታል ።

፯ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ነየ እነ እመጽእ ወእፌውሶ ።

፯ እኔ መጥቼ እድነዋለሁ አለው ።

፰ ወአውሥአ ውእቱ ህቤ ምእት ሉቃ ፡ ፯ ፡ ፯

፰ የመቶ አዝማች መለሰ ።

ወይቤ እግዚእ ኢይደልወኒ ከመ እንተ ትባእ ታሕተ ጠፈረ ቤትየ ።

ጥፋር ቤትየ ሲል ነው ፤ ስጠተ ልብሰ ንፍቀ ታቦት እንዲል ፡ ስጡጠ ልብሰ ንፉቀ ታቦተ ሲል ፡ ከኔ ቤትልትገባአይገባኝም አንተን ልቀበል አልበቃሁም አለው ። ወባሕቱ እዝዝ በቃልከ ይሕየው ቍልዔየ ልጄ ይድን ዘንድ በቃልህ እዘዝ እንጂ ነገር ግን በቃልህ እዘዝ ።

ወየሐዩ ቍልዔየ ፤
ልጄም ይድናል ።

፱ እስመ አነኒ ብእሲ መኰንን እነ ፤

፱ እኔም እንጂ እኔም አኮን እንዳቅሜ ገዥ ነኝ ። ወብየ ሐራ ዘእኬንን ።
የምገዛቸው ጭፍሮች አሉኝ ፤ ወእብሎ ለዝ ሑር ወየሐውር ፡ ደጅ ሲጠና የሰነበተውን ሂደህ ዕረፍ እለዋለሁ ይሄዳል ።
ወለካልኡኒ ነዓ ወይመጽእ ፤
ዐርፎ የሰነበተውን መጥተህ ደጅ ጥናኝ እለዋለሁ ይመጣል ።
ወለገብርየኒ ግበር ከመዝ ወይገብር ።
ባርያየንም የቆመውን ቁረጥ የተኛውን ፍለጥ ብለው ያዘዝሁትን ሁሉ ያደርጋል ። ደዌያትስ ባንተ ዘንድ ምን ቁም ነገር ናቸው ግቡ ብትላቸው የሚገቡ ውጡ ብትላቸው የሚወጡ አይደሉምን ።

፲ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ አንከረ ፤

፲ ጌታ ይህን ሰምቶ አደነቀ ። ሦስት ነገር አግኝቶ ያደንቅለታል ሃይማኖት ፡ ጥበብ ፡ ትሕትና ፤ ሃይማኖት ያድነልኛል ብሎ መምጣት ፤ ጥበብ ምሳሌ መስሎ መናገር ፤ ትሕትና ኢይደልወኒ አይገባኝም ማለት ነው ።
ወይቤሎሙ ለእለ ይተልውዎ አማን እብለክሙ ፤ ኢረከብኩ ከመዝ ዘይትአመን በውስተ ኵሉ እስራኤል ።
ለተከተሉት በእስራኤል ዘንድ እንዲህ ያለ እማኒ አላገኘሁም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ። አንድም ወበዊአ ብሏህ መልስ ። ከልዕልና ወደ ትሕትና በመጣ ጊዜ የሁሉ መገናኛ አዳም መጣ ። ቍልዔየ ድውይ፡ አቤቱ ነፍሴ በፍዳ ተይዛለች አለው ። ወሕሙም ጥቀ ፍዳ ጸንቶባታል ፡ ወይሰክብ ውስተ ቤተ መፃጕዕ ፡ በኃጥአን ቤት በሲኦል በፍዳ ተይዛለች ። ነየ እነ እመጽእ ወእፌውሶ ። በሐሙስ ዕለት ወበመንፈቃ ለዕለት እትወለድ እምወለተ ወለትከ ያለውን መናገር ነው ። ኢይደልወኒ አዳም አድነኝ አለ እንጂ ሰው ሁንልኝ አለማለቱን መናገር ነው ። እስመ እነሂ ፡ እኔም እንጂ እኔም እኮን እንዳ ቅሜ ገዥ ነኝ። ወብየ ሐራ የማወጣቸው የማገባቸው ሕሊናት አሉኝ ። ወእብሎ ለዝ ሑር ከፉውን ሕሊና ውጣ ብለው ይወጣል ወለካልኡኒ ነዓ ወይመጽእ ። በጐውን ሕሊና ግባ ብለው ይገባል ። ወለገብርየኒ ሥጋዬን ለነፍሴ ተገዛ ብለው ይገዛል ። አጋንንትስ ባንተ ዘንድ ምን ቁም ነገር ናቸው ። ግቡ ብትላቸው የሚገቡ ውጡ ብትላቸው የሚወጡ አይደሉምን አለው ። ወሰሚዖ አይለወጥም ።

፲፩ ወባሕቱ እብለክሙ ብዙኃን ይመጽኡ እም ሥራቅ ወእምዕራብ ወይረፍቁ ውስተ ሕፅነ አብርሃም ይስሐቅ ወያዕቆብ በመንግሥተ ሰማያት ።

ይህ ሰው ትውልዱ ከእስራኤል ነው ያሉ እንደሆነ ፤ ይህስ የተገኘ ከኛ አይደለም እንዳይሉት ።

፲፩ ነገር ግን ካራቱ ማዕዘን የሚያምኑብኝ ብዙ አሉ ። ይህ ሰው ትውልዱ ከአሕዛብ ነው ያሉ እንደሆነ አንድ ሰው ቢያምንበት እንዲህ ያደንቃል እንዳይሉት ሌሎችም ካራቱ ማዕዘን መጥተው የሚያምኑብኝ አሉ ፤ ወይረፍቁ ፣ በምስቱ ሕፅን ይቀመጣሉ ማለት በአብርሃም በይስሐቅ ፣ በያዕቆብ ፣ ቃል ኪዳን በምትወረስ በመንግሥተ ሰማይ ይኖራሉ ።

፲፪ ወለውሉደ መንግሥትሰ ያወፅእዎሙ ውስተ ጸናፌ ጽልመት ሚልክ ፩፥፲፩ ።

፲፪ ይገባናል የሚሉ እስራኤልን ግን ከመንግሥተ ሰማይ አፍአ ወደ ገሃነም ያወጣቸዋል ።
ኀበ ሀሎ ብካይ ወሐቀየ ስነን ፣
ልቅሶ ጥርስ ቁርጥማት ወዳለበት

፲፫ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለውእቱ ኅቤ ምእት ሑርኬ ይኩንከ በከመ ተአመንከ ።
፲፫ ጌታም የመቶውን አዝማች ሂድ እንዳመንህ ይደረግልህ አለው ።
ወሐደወ ወልዱ በይእቲ ሰዓት ልጁም ያንጊዜ ፈጥኖ ዳነ ። የአዳም ነፍሱ ከፍዳ ዳነች ።
ወገቢእ መስፍን ውስተ ቤቱ ረከቦ ለወልዱ ሕያዎ ። ወደቤቱ በተመለሰ ጊዜ ሐደዎድኖ ሕያወ የዳነ ሁኖ በዘሐይወ በዳነ ገንዘብ አገኘው ።
በእንተ ሐማተ ጴጥሮስ ።
፲፬ ወበዊአ ቤቶ ለጴጥሮስ ረከባ ለሐማተ ጴጥሮስ እንዘ ትሰከብ ወትፈጽን ።
፲፬ ከጴጥሮስ ቤት በገባ ጊዜ ሐማተ ጴጥሮስን ሆድ ዝማ ታማ ተኝታ አገኛት ።
፲፭ ወአኃዛ እዴሃ ወገሠሣ ።
፲፭ እጇዋን ይዞ ዳሰሳት ፣ ወኃደጋ ፈጸንታ ። ሆድ ዝማዋ ተዋት ። ወተንሥአት ወተልእከቶሙ ። ተነሥታ አገለገለቻቸው ። መፈትፈት ማሳለፍ አይደለም ለጊዜው የሚበሉትን እያዘጋጀች አቀረበችላቸው ፍጻሜው ግን ከ፴፮ቱ ቅዱሳት አንስት ገብታ ተቈጠረች ፤ አንድም ወበዊአ ብሰሀ መልሰ እሥራኤልን በመከበባቸው ጴጥሮስ አባቸው ጌታ ወደ እሥራኤል በመምርነት በገባ ጊዜ ረከባ ለሐማተ ጴጥሮስ ፤ ኦሪትን ሰብ ሰታጤስ ደም ስታፈስ አገኛት ወአኃዛ እዴሃ ፲ቱ ቃላትን ባሉት አጽንቶ አሳሰፋት ። ወኃደጋ በኦሪት ሥራት ደም ማፍሰስ ሰብ ማጤስ ቀረ ። ወምሴተ ከዊኖ አምጽኡ ኅቤሁ

፲፮ ብዙኃን እለ አጋንንት ማር ፣ ፩ ፣ ፴፪ ።

፲፮ ወምሴተ ከዊኖ ወሰብ መስየ ይላል ። ሲመሽ በመሽ ጊዜ ብዙ አጋንንት ያደሩባቸው ሰዎች ይዘው መጡ ። ፈውሱ ከዓቀብተ ሥራይ ልዩ ነውና እነ ዚያ በዚህ ዕለት እንጂ በዚህ ዕለት በዚህ ሰዓት እንጂ በዚህ ሰዓት አይቻለንም ይላሉ ፣ እሱ ግን በመጡበት ሰዓት ሁሉ ያድናቸዋልና ።
ወአውጽኦሙ በቃሉ ።
ዓኡ መናፍስት ርኩሳን ብሎ አወጣቸው ።
ወፈወሰ ዙሎ ሕውያነ ።
ሕሙማኑን አዳነ ። ከመ ይትፈጸም ቃል

፲፯ ኢሳይያስ ነቢይ ዘይቤ ውእቱ ነሥአ ደዌነ ወጾረ ሕማመነ ኢሳ ፣ ፶፫ ፣ ፬፥፩፥ጴጥ ፣ ፪ ፣ ፳፬ ።

፲፯ ደዌያችንን ተሸከመ ማለት ኢሳይያስ ደዌ ሥጋችንን በታምራት ደዌ ነፍሳችንን በትምህርት አራቀልን ብሎ የተናገረው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ድውያነ ሥጋን በተአምራት ድውያነ ነፍስን በትምህርት አዳነ፤ አንድም ድውያነ ነፍስን በትምህርት አዳነ ብሎ ኢሳይያስ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ድውያነ ሥጋን በታምራት አዳነ ሞተ ሥጋው ለሞተ ነፍስ ምልክት እንደሆነ ድኅነተ ሥጋው ስድኅነተ ነፍስ ምልክት ነውና አንድም እስከ አፅርዓ ወአሰሰለ ይላል አብነት ደዌ ነፍሳችንን በመስቀል ተሰቅሎ እስኪያርቅልን ድረስ ደዌ ሥጋችንን በታምራት አራቀልን ብሎ ኢሳይያስ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ፈወሰ ድውያንን አዳነ ። አንድም ነቢይ ነሥአ ደዌነ ወጾረ ሕማመነ እንዳለ ፣ ወንጌላዊ ነሥአ ደዌነ ወጾረ ሕማመነ ፤ ደዌያችንን ነሣ አለ ታሪክ ከራድዮን የሚባል ጸዓዳ ዖፍ አለ ይዘው ከቤተ መንግሥት ወስደው ያኖሩታል ሰው ሲታመም ወስደው ያቀርቡታል የሚሞት የሆነ እንደሆነ አያየውም ፊቱን ይመልስበታል የሚድን የሆነ እንደሆነ ያየዋል ቀርቦ አፉን ከፉ አድርጎ እስትንፋሱን ይቀበለዋል በእስትንፋስ ምክንያት ደዌ ወደሱ ይመለሳል ነጭ የነበረ ይጠቁራል ብርድ ብርድ ይለዋል ዋዕይ ሲሻ ወደ አየር ይወጣል ዋፅይ ሲሰማው ከባሕር ይገባል ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት በባሕር ኑሮ የቀደመ ጠጕሩን መልጦ ታድሶ ይወጣል ፤ ከራድዮን የጌታ ምሳሌ ጸዓዳ እንደሆነ ጸዓዳ በመለኮቱ ይለዋልና ድውይ የአዳም ምሳሌ እንደ ማየት በዓይን ምሕረት አይቶታልና ቀርቦ እስትንፋሱን እንደመቀበል ባሕርዩንባሕርይ አድርጎለታል በእስትንፋስ ምክንያት ደዌ ወደሱ እንደ ተመለሰ ፤ በአዳም የተፈረደውን መከራ ጌታ ለመቀበሉ ምሳሌ ። ወቦአ እግዚእነውስተ ኵሉጸዋተወመከራ እንተ ባቲ አመከረነ ጸላዒ እንዲል ፣ ወደዓየር ወደ አየር እንደመውጣት በመስቀል ተሰቅሏልከባሕርእንደመግባትወደመቃብር ወርዷል ፫ ሌሊት ፫ መዓልት በከርሠ ባሕር ኑሮ የቀደመ ጠጕሩን ትቶ እንደመነሣት ፫ መዓልት ፫ ሌሊት በከርሠ መቃብር ኑሮ ሙስና መቃብርን አጥፍቶ አንድ ወገን ሁኖ ለመነሣቱ ምሳሌ ፣ ኅደገ ንዴተ ሀላዌ ተመይጠ ወገብአ ኀበ ስብሐቲሁ ወክብሩ እንዲል

በእንተ ዘከመ ይደሉ
ተሊዎተ እግዚእ ኢየሱስ ።
ወሶበ ርእየ ብዙኃን ሰብአ ዘተለውዎ አዘዘ ይሑሩ
ማዕዶተባሕር የተከተሉትን ብዙ ሰዎች ባየ ጊዜ
ባሕሩን ተሻግራችሁ ቆዩኝ አላቸው ። አሁን ብሔረ
ጌርጌሴኖን ገባ ብሎ እንዲያመጣው ፤ ሐተታ ፤
እስራኤል አሕዛብን ይጸየፏቸዋልና እንዳይጸየፉ ጌታ
ኢያሱን አሕዛብን ፈጽመህ አታጥፏቸው ብሎ
ታል ። ከመ ኢትኩን ምድር አጸ ። ምድረ በዳ እንዳ
ትሆን እስራኤል እየቀደሙ እየበዙ ሊወርሷት ቢታ
በዩ ሊቀጣቸው ጾር ሊያስተምሯቸው እንደዚህም
ሁሉ ጌታ ኢጋንንትን ፈጽሞ አላጠፋቸውም የምእ
መናን ልቡና ከትሩፋት ባዶ እንዳይሆን ቢታበዩ
ሊያዋርዷቸው ጾር ሊያስተምሯቸው ።

፲፱ ወመጽአ ኀቤሁ አሐዱ ጸሐፊ

፲፱ ጸሐፊ ማለት ዐዋቂ ነኝ የሚል ሰው ወደሱ
መጣ ።
ወይቤሎ ሊቅ እትሉከ ኀበ ሖርከ ።
መምህር ልደርልህ አለው ።

፳ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለቈናጽልኒ ግበብ
ቦሙ ።

፳ ለቀበሮች ፍርክታ አላቸው ።
ወለአዕዋፈ ሰማይኒ ምጽላል ቦሙ
ለአዕዋፍም ማረፊያ መኖሪያ ዛፍ አላቸው ።

፳ ወለወልደ ዕጓለ እመሕያውሰ ወአልቦቱ
ኀበ ያሰምክ ርእሶ ። ሉቃ ፱ ፶፰ ።

፳ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ለኔ ግን ራሴን
የማስጠጋበት ቦታ የለኝም ፤ ለመኳንንቱ ለካህናቱ
አደርሳቸው እንጂ ለኔ ለምን ታደርልኛለህ አለው ።
ቈናጽል አላቸው መኳንንትን ቈንጽልን ተመያኒ
ይለዋል ቴንኮለኛ ነው ወያወዕኢ ፊሳዮ እንዲል ፤
ከፉ መዓዛ አለው ያን አውጥቶ የሞተ መስሎ
ከጉድጓዱ አፍ ወጥቶ ይተኛል ። ተሐዋስያን
ሲሸቱት የሞተ መስሏቸው ሊበሉ ይቀርባሉ እያ
ነቀ ከጉድጓድ ይዞ ገብቶ ይመገባል ። መኳንንትም
በተሾሙበት አገር በኛ ጊዜ ርስትህን ጉልትህን
ከላስመለስህ በማን ጊዜ ልታስመልስ ነው ብለው
ይገጥሙታል ቢረታ ዳኝነት ቢረታ መማለጃ ይበ
ሉታልና ። ካህናትን አዕዋፍ አላቸው ለአ
ዕዋፍ ዘር መከር እንደሌላቸው ለካህናትም ዘር
መከር የላቸውምና ፤ አንድም በቈንጽል በዖፍ
ለተመሰለ ለገንዘብ አንተ ማደሪያ አለኸው ። ቈን
ጽል አለው ይተነኩሉበታልና ። ዖፍ አለው ፈጥኖ
ይጠፋልና ። ወልደ ዕጓለ እመሕያውስ ፤ ልደርልህ
ማለት እንጂ አደርብኝ ማለት ነው የገንዘብ ማደ
ሪያ ሁነህ በየት ልደርብህ አለው ። አንድም ቈን
ጽል ዖፍ ለተባለ ለዲያብሎስ ማደሪያ አንተ አለ
ኸው የተመቸ ተንኮለኛ ነውና ። ዖፍ ፈጥኖ ያስታ
ልና በውሳጤ ቤትከ ኢትርግም ብዑላነ እስመ ያፈ
ሰማይ ያወፅኦ ለነገርከ እንዲል ። ወልደ ዕጓለ እመ
ሕያውስ የዲያብሎስ ማደሪያ ሁነህ ሳለህ በየት
ልደርብህ አላድርብህም አለው ። አንድም ለቈ
ንጽል ለዖፍ ላንተ ማደሪያ ገሃነም አለህ ፤ እኔ ግን አላ
ድርብህም ። ቈንጽል አለው ጥንቆላ መስሎት ተምሬ
በታምራቱ እበላበታለሁ ብሎ በተንኮል መጥቷ
ልና ፤ ዖፍ አለው በጥቂት ቀን ነጥቄ እሄዳለሁ ብሎ
መጥቷልና ፤ አንድም ለቆናጽል ለአይሁድ ማደ
ሪያ ገሃነም አላቸው ። በአዕዋፍ በሐዋርያት እኔ
አድርባቸዋለሁ በአይሁድ ግን አላድርባቸውም ።
ምጽላል ባለው አበኳር የሚል አብነት ይገኛል
የጭቃ ቤት የምትሠራ ዖፍ አለችና ።

፳፩ ወይቤሎ ካልእ እምአርዳኢሁ እግዚእ አብ
ሐኒ እቅድም ወእሑር ወእቅብር ለአቡየ ።

፳፩ ከሕዝቡ አንዱ አሰናብተኝ አስቀድሜ ሂጄ
አባቴን ልቅበር አለው ። ከጉባኤው ከዋለ ሁሉንም
ደቀ መዝሙር ማለት ልማድ ነውና እንዲህ አለ
እንጂ ከሕዝቡ አንዱ ነው ። ሙቷል ቢሉ ልቅበ
ረው አልሞተም ቢሉ ልርዳው አለው ፤

፳፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንተሰ ትልወኒ

፳፪ አንተስ ተከተለኝ አለው ። ለጊዜው በእ
ግር ተከተለኝ ፍጻሜው በግብር ምሰለኝ አለው ።
ወኅድጎሙ ለምውታን ይቅብሩ ምውታኒሆሙ ።
ሙተዋል ቢሉ ሙታን እናት አባትህን ሙታን ሕሊና
ዘመዶቻቸው ይቅበሯቸው አንድም አልሞቱም ቢሉ
ሙታን ሕሊና እናት አባትህን ሙታን ሕሊና ዘመ
ዶቻቸው ይርዷቸው ያጥቧቸው ፤ አንድም ሙታን
ሕሊና እናት አባትህን ምውት ገንዘባቸው ይርዳቸው
ያጥባቸው ።
በከመ አኀደኖ ለባሕር
፳፫ ወዓሪጎ ውስተ ሐመር ተለውዎ አርዳ
ኢሁ ። ማር ፬ ፴፮ ።
፳፫ ከመርከብ በወጣ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ
ተከተሉት ።
፳፬ ወናሁ ዓቢይ ድልቅልቅ ኮነ በውስተ
ባሕር ።
፳፬ ባሕሩ ተናወጸ ።
እስከ ሶበ ይደፍኖ ለሐመር ማዕበለ ባሕር ።
ማዕበሉ መርከቡን እስጥመዋለሁ እስኪል ድረስ
ወወእቱሰ ይነውም ።
እሱ ግን ተኝቶ ነበር ኖመ ከመ ውሉደ ሥጋ እን
ዲል ።
፳፭ ወቀርቡ አርዳኢሁ ወአንቅሕዎ ፤
፳፭ ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው ቀሰቀሱት ፤
ወይቤልዎ እግዚእ አድኅነነ ከመ ኢንሙት ።
አቤቱ ከሰጥመት አድነን አሉት ።

፳፮ ወይቤሎሙ ምንት ያፈርሃክሙ አሕጹጻነ ሃይማኖት ።

፳፮ እናንት ሃይማኖት የሌላችሁ ምን ያስፈራችኋል ከሱ ጋራ ሳለን ጥፋት አያገኘንም በሱ ስም አምነን እንድናለን እትሉም አላቸው ።
ወተንሢኦ ገሠጾሙ ለነፋሳትኒ ወለማዕበለ ባሕርኒ።
ተነሥቶ ነፋሳትን ማዕበለ ባሕርን ገሠጻቸው ።
ወኮነ ዓቢይ ዛኅን ።
ታላቅ ጸጥታ ተደረገ ማለት ጸጥ አለ ።

፳፯ ወአንከሩ ሰብእ ።
፳፯ ሕዝቡ አደነቁ ።

ወይቤሉ መኑ እንጋ ውእቱ ዝንቱ ዘይትኤዘዙ ሎቱ ባሕርኒ ወነፋሳትኒ ።
ባሕር ነፋሳት የሚታዘዙለት ይህ ማነው አሉ ። እንድም ወዓሬነ ብለህ መልስ አሪትን በሠራ ጊዜ ነቢያት ፣ ወንጌልን በሠራ ጊዜ ሐዋርያት በግብር መሰሉት ።
ወናሁ ዓቢይ ድልቅልቅ ኮነ በውስተ ባሕር ።
በሰውነታቸው መከራ ጸናባቸው ። እስከ ሶበ ይደፍና ለሐመር ። ሕጋቸው አሪትን ሕጋቸው ወንጌልን አስተዋቸዋለሁ እስኪል ድረስ ፣ ወእቱሰ ይነውም ትዕግሥቱን መናገር ነው ። ቀርቡ ወአንቅሕዎ ፣ አቤቱ ከመከራ አድነን ብለው ለመኑት ፣ ምንት ያፈርሃክሙ አኅጹጻነ ሃይማኖት፣መከራ ብትቀበሉ ክብር ይበዛላችኋል እንጂ ምን ያደርጋችኋል ምን ያስፈራችኋል አላቸው ። ወተንሢኦ ገሠጾሙ ፣ ከትዕግሥቱ ወጥቶ መከራውን አራቀላቸው ወኮነ ዓቢይ ዛኅን ። መከራው ራቀላቸው እንድም ወዓሬነ ፣ ታባሕትዎ በያዘ ጊዜ ባሕታውያን ፣ ወደ መስቀል በወጣ ጊዜ ሰማዕታት በግብር መሰሉት በሰውነታቸው መከራ ጸናባቸው ፣ ገድላቸውን እስኪያስተዋቸው ድረስ ፣ ትዕግሥቱን መናገር ነው ። ለመኑት እናንት ሃይማኖት የሌላችሁ ምን ያስፈልራችኋል ፣ መከራ ክብር ያበዛላችኋል እንጅ ምን ያደርጋችኋል አላቸው ከትዕግሥቱ ወጥቶ ለሰማዕታት ነበልባል እብርዶ እንበሳ አስግዶ ለባሕታውያን ቆራ እንዲታለብላቸው ዛፍ እንዲያፈራላቸው አንድርጎ ረዳቸው ፤ መከራው ቀረ ።

በእንተ አጋንንት
ዘብሔረ ጌርጌኖን ።

፳፰ ወበጺሖ ማዕዶተ ጌርጌሴኖን ተቀበልዎ ፪ቱ እለ አጋንንት ወፂአሙ እመቃብራት ። ማር ፭ ፣ ፩፡ ሉቃ ፰ ፣ ፳፮ ፣

፳፰ ጌርጌሴኖን በደረሰ ጊዜ አጋንንት ያደሩባቸው ሁለት ሰዎች ከመቃብር ወጥተው ተቀበሉት ። ባንዱ ሽህ ባንዱ ሽህ አድረውባቸዋል ሰው ከሚቀበርበት ላም ከሚታረድበት ጸጅ ከሚጣልበት መኖር ለጋኔን ልማዱ ነውና ፣ እንድም ነፍስ በሕያው አድራ መቃብሯን ትጠብቃለች የሚሉ አሉና ለማስመሰል ፣ እንድም የምውት ነፍስ በሕያው አድራ የዘመዶችዋን ጠላት ታጠፋለች የሚሉ አሉና ያን ለማስመሰል ይህን ይዘው የዘመዶቻችን ነፍስማ ጠላቶቻችንን የምታጠፋልን ከሆነ የልጆቻችን ነፍስማ እንደምን ታጠፋልን ብለው ልጆቻቸውን አርደው የፈጁ ብዙ ናቸው ። እንድም በሕያዋኑ አድረውባቸዋል በምውታኑ አድረን እንኖራለን ፣ ዲያብሎስ እግዚእ ሕያዋን ወሙታን ነኝ ሲል ፣ ወወፂአሙ እመቃብራት አለ ።
መእኩያን ጥቀ ወኢያበውሐ መኑሂ ይኅልፍ እንተ ይእቲ ፍኖት ።
እጅግ ክፉ ናቸው ማንንም ማን በዚያች መንገድ ሊሄድ አያስናብቱትም ነበር ፣ እንድም ኢያበውሖ መነሂ ይላል በዚያች መንገድ ይሄድ ዘንድ ማንንም አያስናብቱም ነበር ።

፳፱ ወናሁ ጸርሑ እንዘ ይብሉ ምንት ብነ ምስሌከ ኢየሱስ ወልደ እግዚአብሔር ሕያው

፳፱ የሕያው የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጁ ኢየሱስ ክርስቶስ ሆይ ካንተ ጋራ ምን ጸብ አለን ፣ እንድም ካንተ ጋራ የምንቃወምበት ምን ኃይል ምን ሥልጣን አለን ብለው አሰምተው ተናገሩ ።
መጻእከኑ ዝየኒ ትስድደነ ፣
ከዚህም አስወጥተህ ልትሰደን መጣህን ሐተታ ዝየኒ ማለታቸው ቀድሞ ከኢየሩሳሌም ኋላ ከሄሮድስ ከተማ አስወጥቶ ሰዷቸው ነበርና ፣ ወዘእንበለ ይብጻሕ ጊዜሁ ትሣቅየነ ፣ ፍዳ የምንቀበልበት ጊዜ ሳይደርስ ሥቃይ ልታጸናብን መጣህን አሉት ፣ ጊዜው ዕለተ ዓርብ ዕለተ ምጽአት ነው ፣

፴ ወቦ ህየ መራዕየ አሕርው ይትረአዩ ርሑቀ እምኔሆሙ ማር ፭ ፣ ፲፩ ፣ ሉቃ ፣ ፰ ፣ ፴፪

፴ የእሪያ መንጋ ከዓቸው ርቀው ተሰማርተው ነበር ።

፴፩ ወአስተብቍዕዎ እሙንቱ አጋንንት ፤
፴፩ አጋንንት ማለዱት ።
ወይቤልዎ እመሰ ታወፅአነ ፈንወነ ኀበ መራዕየ አሕርው ፤ ከሰዎቹስ ካወጣኸን በአሕርው እናድርባቸው ዘንድ እዘዘን አሰናብተን አሉት ፤ ሐተታ ፣ ስንኳን አእምሮ ንባብ ባለው ሰው አእምሮ ንባብ በሌላቸው በአሕርው ያለሱ ፈቃድ ማደር እንዳይቻላቸው ለማጠየቅ ።
፴፪ ወይቤሎሙ ሑሩ ።

፴፪ ሂዱቹሁ እደሩባቸው አላቸው እኮ ከመዶግበር ሰእለቶሙ ብሎታል ሊቁ ፣ አሁን ጌታን ስለእለተ አጋንንት ደስ አሰኝቶት አይደለም በተንኮል መጥተዋል እሕዛብ እሪያውን እንደ ከብት እያረቡ ሥጋውን ይበሉታል ፣ ወተቱን ይጠጡታልና

እኒህን ያጠፋንባቸው ጌዮደሆን እሱን ይጣሉልናል ብለው መጥተዋል ። ጌታም ሑሩ እደሩባቸው አላቸው እኒህ ገደል ወድቀው ባሕር ጠልቀው ሲያልቁ ምድር ተከፍቶ የሚያስጥማቸው ነውና ፣ በዚያው ሥራውን ለመሥራት ሂዱ እደሩባቸው አለ ።

ወወፂአሙ ሖሩ ወቦኡ ውስተ አሕርው ከሰዎች ወጥተው በእሕርው አደሩ ። ወሮጹ ኵሉ መራዕየ አኅርው ወጸድፉ ውስተ ባሕር ወሞቱ ውስተ ማይ ጥቂት የደመ ነፍስ አእምሮ ነበራቸው ያችኑ አጥተ ዋት ገደል ወድቀው ከባሕር ጠልቀው አልቀ ዋል ። አሕርው የአይሁድ አጋንንት በአይሁድ ያደሩ የአጋንንት ምሳሌ ሠረውንም እውረውንም አንድ አድ ርጎ ገሃነም እንዲያወርድ ለማጠየቅ ፣ አንተ ወጣያ ታቲከ ኀቡረ ትወርዱ ውስተ ገሃነም እንዲል ።

፴፫ ወጐዩ ኖሎት ወአተው ሀገረ ወዜነው ኵሎ ዘኮነ ።

፴፫ ጠባቆች ሸሽተው አገር ገብተው የአ ሕርውን ስጥመት ተናገሩ ወዘእለ አጋንንትኒ ፣ የአጋንንትንም ጥፋት የሰዎችንም ድኅነት ተናገሩ ።

፴፬ ወናሁ ወፅአ ኵሉ አሐ ውስተ ሀገር ይት ቀበልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፴፬ በሀገር ያሉ ሰዎች ሁሉ ሊቀበሉት ወጡ ወሰበ ርእዮ አስተብቍዕዎ ይኅልፍ እምደወሎሙ ባዩት ጊዜ ካገራችን አለፍልን ብለው ለመኑት ። ንባብ አእምሮ በሌላቸው በአሕርው እንዲህ አድ ርጎ የፈረደ ንባብ አእምሮ ያለን የኛን ኃጢአትማ መርምሮ ዐውቆ እንደምን ይፈርድብን ብለው ።

በእንተ መጻጕዕ ።

ምዕራፍ ፱ ።

፩ ወዓረገ ውስተ ሐመር ዓደወ ወበጽሐ ሀገሮ፣ በመርከብ ተጭኖ ባሕሩን ተሻግሮ ወደ አገሩ ወደ ኢየሩሳሌም ገባ ።

፪ ወአምጽኡ ኀቤሁ ድውየ መፃጕዓ እንዘ ይጸውርዎ በዓራት ማር ፪ ፣ ፫ ፣ ሉቃ ፣ ፭ ፣ ፲፰ ።

፪ ደዌ የጸናበት አንድ ሰው ባልጋ ተሸክመው ወደሱ መጡ ። ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ሃይማ ኖቶሙ ይቤሎ ለውእቱ መፃጕዕ ተአመን ወልድየ ያድንልናል ብለው መምጣታቸውን ፣ አንድም ሃይ ማኖቶ ይላል ያድነኛል ብሎ መምጣቱን አይቶ ልጄ ሃይማኖትህ አድኖሃልና በሃይማኖትህ ጽና ወተኀደገ ለከ ኃጢአትከ ። ኃጢአትህም ተሰርዮ ልሃል አለው ።

፫ ወናሁ እለ እምውስተ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ይቤሉ ዝሰ ይፀርፍ ።

፫ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ወገን የሚሆኑ ይህስ ይሳደባል አሉ ፤

፬ ወአእሚሮ እግዚእ ኢየሱስ ሕሊናሆሙ ወይ ቤሎሙ ለምንት ትሔልዩ እኩየ በአልባቢክሙ ።

፬ ጌታ እንዲህ ማለታቸውን ዐውቆ በልቡ ናችሁ ክፉ ነገርን ለምን ታስባላችሁ አላቸው ።

፭ ምንት ይቀልል እምብሂለ ተኃደገ ለከ ወእ ምብሂለ ተንሥእ ወንሣእ ዓራተከ ወሑር ፤

፭ ተነሥተህ አልጋህን ተሸክመህ ሂድ ከማ ለትና ኃጢአትህ ተሰርዮልሃል ከማለት ማናቸው ይቀላል አላቸው ።

፮ ከመ ታእምሩ ከመ ብውሕ ሎቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ይኅድግ ኃጢአተ በዲበ ምድር ።

፮ ለሰው ልጅ ለክርስቶስ በዚህ ዓለም ኃጢ አት ማስተስረይ እንዲቻለው ታውቁ ዘንድ ፣ ሐተታ ፣ ኃጢአት ከማስተስረይ ድውይ መፈወ ሱን ማብለጡ ነው ፤ ሁሉስ የጌትነት ሥራ አይደ ለም ቢሉ ኃጢአት ሲሰረይ አይታይም ድውይ ሲፈ ውስ ይታያልና ፣ ሰውም ካላየው ያየውን ማድነቅ ልማድ ነውና ፣ ሰው በሚያደንቀው ተናገረ ። አን ድም ኃጢአት ተሰረየልህ ከማለትና ተነሥተህ አል ጋህን ተሸክመህ ሂድ ከማለት ማን ይቀላል ፣ ድውይ ሲፈውስ አይታችሁ ኃጢአት ያስተሰርያል አት ሉም አላቸው ሞተ ሥጋ ለሞተ ነፍስ ምልክት እንደሆነ ድኅነተ ሥጋው ለድኅነተ ነፍስ ምልክት ነውና ።

ወእምዝ ይቤሎ ለውእቱ መፃጕዕ ተንሥእ ወንሣእ ዓራተከ ወሑር ቤተከ ።

ተነሥተህ አልጋህን ተሸክመህ ወደ ቤትህ ሂድ አለው ፣ ሐተታ ፣ ተረፈ ደዌ የለበትምና ፈውሱ ከዓቀብተ ሥራይ ልዩ ነውና እነዚያ እዳንን ካሉ በኋላ እህል ይቅመስ ይዋል ይደር ይጽናና ይላሉ ፤ እሱ ግን ተረፈ ደዌ የለበትምና ። አንድም እነዚያ እዳን ብለው የሚጠጣበት ጽዋው የሚተኛበት አል ጋው ምንጣፉ ይገባልና ይላሉ እሱ ግን ይህ ሁሉ የለበትምና ተነሥተህ አልጋህን ተሸክመህ ሂድ

፯ አለው ። ወተንሢኦ ነሥአ ዓራቶ ወሖረ ቤቶ ፤

፯ ተነሥቶ አልጋውን ተሸክሞ ወደ ቤቱ ሄደ።

፰ ወርእዮሙ ሕዝብ አንከሩ

፰ ሕዝቡም አይተው አደነቁ ፤ ወአእኰትዎ ለእግዚአብሔር ዘወሀበ ዘከመዝ ሥልጣነ ለሰብእ ለሰው እንዲህ ያለ ሥልጣን የሰጠው ማለት አላመ ኑም ቢሉ እንዲህ ያለ ነቢይ ያሥነሣልን ብለው፣ አም ነዋል ቢሉ ለራሱ ድኅነት ይኛ የነበረ ሥጋን ከባ

ሕርይ ልጅህ ጋራ አዋሕደህ ለሌላው ድኅነትን እንዲያድል ያደረግኸው ብለው እግዚአሐርን አመሰገኑት ።
ዘከመ ተጸውዓ ማቴዎስ ።

፱ ወኃሊፎ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ ረከበ ብእሴ እንዘ ይነብር ውስተ ምጽባሕ ዘስሙ ማቴዎስ ፤ ማር ፪ ፡ ፲፬ ፡ ሉቃ ፡ ፭ ፡ ፳፯

፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚያ አልፎ ሲሄድ ማቴዎስ የሚባል ሰው ከሚያስገብርበት ቦታ ተቀምጦ አገኘ ፤ ሐተታ ፡ ሲያስገብር አላለም የሰው ገንዘብ ይዞ ሄደ ብለው ምክንያት እንዳያደርጉበት ።
ወይቤሎ ትልወኒ ።
ተከተለኝ ማለት ስጊዜው በእግር ፍጻሚው ግን በግብር ምሰለኝ አለው እንዲሻው ከፍጹምነት እንዲደርስ ዐውቆ ።
ወተንሥአ ተለዎ ።
ተነሥቶ ተከተለው ማለት ስጊዜው በእግር ፍጻሚው በግብር መሰለው ።

በእንተ ዘከመ ይደልዎሙ

ለክርስቲያን ጸዊመ ፤

፲ ወእንዘ ይረፍቅ ውስተ ቤት ናሁ መጽኡ ብዙኃን ኃጥአን መጸብሓን ።

፲ ከቤት ገብቶ ሲበላ ብዙ ኃጥአን መጸብሓን መጡ ።
ወረፈቁ ምስለ እግዚእ ኢየሱስ ወአርዳኢሁ ።
ከደቀ መዛሙርቱም ከሱም ጋራ ተቀምጠው በሉ ። እንዲያው አይደለም ተከተለኝ ካልኸኝስ ከቤት ገብተህ ምሳ ብላልኝ ብሎታል ፤ የቤቱን ትዳር ያየእንደሆነ አከብሮ ያኖረኛል ብሎ አሁን ዛሬ ለጌታ የሚያድር ሰው ፈረሱን በቅሎውን ሎሌውን ገረዱን አብዝቶ እንዲታይ ። አንድም ፡ ትእምርተ ምናኔ ነው ፩ ፡ ነገ ፡ ፱ ፡ ፱ ። ኤልሳዕ ፲ ፡ ሁለት ጥንድ በሬ አስጠምዶ ሲያሳርስ ኤልያስ ሐሚለቱን ከራሱ ላይ ጥሎ ተከተለኝ አለው ። አባቴ ተከተለኝ ካልኸኝስ ቆየኝ አንድ ጊዜ ብሎ ፲፪ቱን ጥንድ በሬ አርዶ ለነዳያን አብልቶ ተከትሎታልና በዚያ ልማድ ።

፲፩ ወርእዮሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ይቤልዎሙ ለአርዳኢሁ ለምንት ይበልዕ ሊቅክሙ ምስለ ኃጥአን ወመጸብሓን ።

፲፩ ጸሐፍት ፈሪሳውያን አይተው መምህራችሁ ከኃጥአን ከመጸብሓን ጋራ ለምን ይባላል አሏቸው

፲፪ ወሰሚዖ እግዚእ ይቤሎሙ ሕሙማን ይፈቅድዎ ለዓቃቤ ሥራይ ።

፲፪ ጌታም በሰማ ጊዜ ባለመድኃኒትን የታመሙ ሰዎች ይሹታል ። ሐተታ ያበጠውን ሊፈርጥላቸው የጎረበጠውን ሊልጥላቸው ፤
ወአኮ ጥዑያን ።
ጤነኞች ግን አይሹትም ። አንድም ዓቃቤ ሥራይ ዘነፍስ እኔን ሕሙማን ነን የሚሉ ኃጥአን መጸብሓን ይሹኛል ደኅነኞች ነን የምትሉ እናንተ ግን አትሹኝም ።

፲፫ ሑሩ ወአእምሩ ምንት ውእቱ ዘይቤ ምጽዋተ እበድር እመሥዋዕት ። ሆሴ ፡ ፯ ፡ ፮ ። ማቴ ፡ ፲፪ ፯ ። ፩ ፡ ጢሞ ፡ ፩ ፡ ፲፫ ።

፲፫ ሑሩ በእግረ ሕሊና ነው ምጽዋተ እበድር እመሥዋዕት ያለው ምንም እንደሆነ መርምራችሁ ዕወቁ ማለት እኒህን መጸየፍ መሥዋዕት እኒህን አለመጸየፍ ምጽዋት እንደሆነ ዕወቁ ። እስመ ኢመጻእኩ እጸውዕ ጻድቃነ ።
ጻድቃን ነን የምትሉ እናንተን ልጠራ አልመጣሁምና ።
አላ ኃጥአን ለንስሐ ።
ኃጥአን ነን የሚሉ እኒህን ወደ ንስሐ ልጠራ መጥቻለሁ እንጂ ፡ በዓለሙ አንድ ጻድቅ ኑሮ ያን ልጠራ አልመጣሁምና ሁሉ ኃጥእ ሁነዋልና ያን ልጠራ መጥቻለሁ እንጂ ።

፲፬ ወእምዝ መጽኡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ለዮሐንስ ወይቤልዎ በእፎ ኢይጸውሙ አርዳኢከ ። ማር ፪ ፡ ፲፰ ። ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፴፫ ።

፲፬ ለምንት ሲል ነው በእፎ ትጼዕል ሊቀ ካህናቲሁ ለእግዚአብሔር እንዲል ፤ ከዚህ በኋላ የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት መጥተው ደቀ መዛሙርትህ ለምን አይጾሙም አሉት ።
ንሕነሰ ወፈሪሳውያን ንጸውምብዙኃ ።
እኛ ፈሪሳውያን ግን ብዙ እንጾማለን ። ሐተታ ፡ ምን ጾም አላቸው ቢሉ እሑድና ማክሰኞ ሐሙስ ይጾማሉና ፤ አንድም ጾመ ረቡዕ ጾመ ሐሙስ ጾመ ሰቡዕ ጾመ እሱር የሚባል ጾም አለና ።

፲፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢይክሉ ደቂቀ ለመርዓዊ ጸዊመ ወላህዎ እምጣነ ሀሎ መርዓዊ ምስሌሆሙ ።

፲፭ የመርዓዊ ሚዜዝት መርዓዊ ከሳቸው ጋራ ሳለ መጾም ማልቀስ አይቻላቸውም ።
ወባሕቱ ይመጽእ መዋዕል አመ ይነሥእዎ ለመርዓዊ እምኔሆሙ ውእተ አሚረ ይጸውሙ ነገር ግን መርዓዊ ከሳቸው የሚለይበት ጊዜ ይደርሳል ያን ጊዜ ይጾማሉ አለ ፤ ዐሥርቱ ቢወጣ ፡ አንድም የኔ ደቀ መዛሙርት ከኔ ጋራ ሳሉ መጾም ማልቀስ አይቻላቸውም እኔ ከሳቸው የምለይበት ጊዜ ይደርሳል ያንጊዜ ይጾማሉ ፡ ይነሥእዎ ፀሞት ቢሉ

ሁለት ቀን ያከፍላሉና በዕርገት ቢሉ ፯ ቀን መን ፈስ ቅዱስን ተቀብለው ይጾማሉና ።

፲፮ ወአልቦ ዘይጠቅብ ግምደ ደርግህ ውስተ ሰጠተ ልብስ ብሉይ ።

፲፮ አዲስ ቁራጭ ባረጀ ልብስ ላይ የሚጥፍ የለም ።
እስመ ይትመላዕ ሕያዎ ለልብስ ።
ደጎነኛውን ተሚልቶት ይሄዳልና ።
ወያዓብዮ ለስጠቱ ።
ቀዳዳውንም ያሰፋዋልና ፤ እንድም ሐዋርያትን በመንፈስ ቅዱስ ባልታደሰ ሰውነታቸው ጾምን ጹሙ የሚላቸው የለም ጾሙም ይቀራል ሰውነታ ቸውም ይጎዳልና ።

፲፯ ወአልቦ ዘይወዲ ወይነ ሐዲሰ ውስተ ዝቅ ብሉይ ።

፲፯ ባረጀ ራዋት ጉሽ ጠጅ የሚሾም የለም፤
ወእመ አኮስ ዝቁኒ ይነቅዕ ወወይኑኒ ይትከዓው ።
ቢሾሙ ግን ራዋቱም ይቀደዳል ወይኑም ይፈሳል።
ወባሕቱ ለወይንስ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ሐዲስ ይወ ድይዎ ፤
ጉሹን ጠጅ ግን ባዲስ ራዋት ይሾሙታል ፡ ወይ ትዓቀቡ ፪ሆሙ በበይናቲሆሙ ።
እርስ በርሳቸው ባንድነት ይጠባበቃሉ ፡ አዲሱ ራዋት የጠጁን ፍላሎት ይችለዋል የጠጁም ፍላሎት አዲ ሱን ራዋት ያለፋዋልና ፡ አንድም ሐዋርያትን በል ጅነት ባልታደሰ ሰውነታቸው ሕግ ጠብቁ የሚላ ቸው የለም ፤ ወእመ አኮስ ፤ ጠብቁ ቢሏቸውም ሕጉም ይፈርሳል ሰውነታቸውም ይጎዳልና ፡ ወባሕ ቱ ፡ በልጅነት በታደሰ ሰውነታቸው ግን ወንጌልን ጠብቁ ይሏቸዋል ፡ ወይትዓቀቡ ፡ እርስበርሳቸው ይጠ ባበቃሉ እሳቸውም ሕጉን ይጠብቁታል ሕጉም እሳቸውን ይጠብቃቸዋል ። እኮ ንሕነ ዘነዓቅቦሙ ለሕገጋት አላ እሙንቱ ሕገጋት የዓቅቡነ ለዓቂብ ወለተጸውኖ እንዲል ።

በእንተ ወለተ ኢያኢሮስ ፡

ወበእንተ ደም ዘይውኅዛ ።

፲፰ ወእንዘ ዘንተ ይነግሮሙ ናሁ መጽአ አሐዱ መኰንን ወሰገደ ሎቱ ። ማር ፭፡፳፪፡ሉቃ፡ ፰፡ ፵፩።

፲፰ ይህን ሲነግራቸው ኢያኢሮስ መጥቶ ሰገደለት ። እንዘ ይብል ወለትየ ይእዜ ሞተት ። ልጄ ዛሬ ሞተች አለው ።
ወባሕቱ አንብር እዴከ ላዕሌሃ ወተሐዩ ።
ነገር ግን መጥተህ እጅህን ጫንባት ትነሳለች አለው።

፲፱ ወተንሢኦ ሖረ ።

፲፱ ተነሥቶ ሄደ ።
ወተለውዎ ብዙኃን ሰብእ ።
ብዙ ሰዎች ተከተሉት ።
ወአርዳኢሁኒ ምስሌሁ ፤
ደቀ መዛሙርቱን አስከትሎ ሄደ ፡

፳ ወናሁ መጽአት ብእሲት እንተ ደም ይውኅዛ እም፲ወ፪ቱ ክረምት ወቀርበት እንተ ድኅሬሁ ። ማር ፭፡ ፳፭ ። ሉቃ ፰ ፡ ፵፫ ።

፳ ካሥራሁለት ዓመት ጀምሮ ደም የሚፈሳት ሴት መጣች ። ዘ፲ቱ ወ፪ቱ ዓመት ይላል ደም መፍ ሰስ ከጀመራት ፲፪ ዓመት የሆናት ሴት ከወደኋላው መጣች ።

፳፩ ወገሠሠት ጽንፈ ልብሱ እንዘ ትብል በልባ እምከመ ገሠሥኩ ጽንፈ ልብሱ እሐዩ ።

፳፩ የልብሱን ዘርፍ የዳሰስሁ እንደሆነ እድ ናለሁ ብላ የልብሱን ዘርፍ ዳሰሰች ።

፳፪ ወተመይጠ እግዚእ ኢየሱስ ርእያ ።

፳፪ ጌታም ተመልሶ አያት ።
ወይቤላ ተአመኒ ወለትየ ሃይማኖትኪ አሕየወተኪ ልጄ ሃይማኖትሽ አዳነችሽ በሃይማኖትሽ ጽኚ አላት እንዲያው አይደለም ወደ ኋላ ተመልሶ ደቀ መዛ ሙርቱን መኑ ገሠሠኒ ጽንፈ ልብስየ አላቸው ከዚህ በኋላ ናሁ ብዙኅ ሰብእ ይጸዓቅ ወይጣወቅ አንተስ ትብል መኑ ገሠሠኒ ጽንፈ ልብስየ አሉት ፤ ታም ራት ያደርጋል ነገር ግን ይሰረቀዋል እንጅ እንዳ ይሉ አአምር ከመ ወፅአ ኃይል እምኔየ ብሏቸዋል ነገሩ ካልቀረስ ብላ ወደፊቱ አልፋ ሰገደችለት ። ከዚህ በኋላ ተእመኒ ወለትየ ብሏታል እንተ ደም ይውኅዛ የቤተ አይሁድ ልብስ የሐዋርያት አልባሲ ሁስ ለክርስቶስ መሃይምናን እሙንቱ እንዲል ፤ ጽንፈ ልብስ ከሐዋርያት ቀጥለው የተነሡ መም ህራን ፡ እንተ ደም ይውኅዛ የልብሱን ዘርፍ ይዛ እንደተፈወሰች ቤተ አይሁድም ከሐዋርያት ቀጥ ለው ከተነሡ መምህራን ተምረው ስብ ማጤሳቸውን ደም ማፍሰሳቸውን መተዋቸውን መናገር ነው ወሐ ይወት ሶቤሃ ይእቲ ብእሲት ።
ፈጥና ያን ጊዜ ዳነች ።

፳፫ ወመጺኦ እግዚእ ኢየሱስ ቤቶ ለውእቱ መኰንን ረከበ ሰብአ ብዙኃነ መብክያነ እንዘ ይትሀወኩ ።

፳፫ ጌታችን ከኢያኢሮስ ቤት በደረሰ ጊዜ ብዙ ሰዎች ሲያለቅሱ ሲወጡ ሲገቡ አገኘ ፤ ሹም ቢሞት ፺ የሹም ልጅ ቢሞት መቶ ታምሳ እንዲሉ ።
፳፬ ወይቤሎሙ ተገኃሡ ።
፳፬ ተመለሱ አላቸው ።
እስመ ኢሞተት ሕፃን ።
ብላቴናይቱ አልሞተችምና ።
አላ ትነውም ።

ተኝታለች እንጂ ፣ እንዲያሥነሣት ዮውቃልና በነ
ፍስ ሕያዊት ናትና ትቀድሰዋለችና ።
ወሰሐቅዎ ፤
በኢያኢሮስ ሳቁበት የሞተና ፤ ያልሞተ የማያውቅ
ያሥነሣልኛል ብሎ ይዞ መጣ ብለው ፣ አንድም የጌ
ታን ነገሩን እንደ ዋዛ አዩበት ያጠብን የገነዝን ።
እኛ እያለን አልሞተችም ይለናል ፣ ብለው ።

፳፭ ወእምዝ ወፅአ ሰብእ ቦአ ወአኃዛ እደ.ሃ፤
፳፭ ሰዎቹ ከወጡ በኋላ ገብቶ እጇዋን ይዞ
አሥነሣት ።
ወተንሥአት ሕፃን ።
ብላቴናይቱ ተነሣች ። ሐተታ እንተ ደም ይው
ኅዛ የታመመችበት ይሆች ብላቴና የተወለደች
በት እንተ ደም ይውኅዛ የተፈወሰችበት ይሆች
ብላቴና የተነሣችበት ቀኑ አንድ ነው ።

፳፮ ወወፅአ ስሙዓተ ነገሩ ውስተ ኵሉ በሐ
ውርት ።

፳፮ የተአምራቱ ዜና ስሙዓተ ነገራ
ይላል ቀድሞ መሞቷ ኋላ መነሣቷ በራቱ
ማዕዘን ተነገረ ፤

በእንተ ፪ቱ ዕውራን

፳፯ ወኃሊፎ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ ተለ
ውዎ ፪ቱ ዕውራን
፳፯ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚያ አልፎ
ሲሄድ ሁለት ዕውራን ተከተሉት ።
እንዘ ይጸርሑ ወይብሉ ተሣሃለነ ወልደ ዳዊት ።
ወልደ ዳዊት እዘንልን ይቅር በለን እያሉ ።
፳፰ ወበዊአ ቤተ መጽኡ ኀቤሁ እሙንቱ
ዕውራን ።
፳፰ ለዕውራን ርቆ መሄድ አይሆንላቸውምና
ከቤት ገብቶ ቆይቷቸዋል ከቤት በገባ ጊዜ ዕውራን
ወደሱ መጡ ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ተአምኑሁ ከመ እክል
ዘንተ ገቢረ ።
ጌታም ዕውር ማዳን እንዲቻለኝ ታምናላችሁን አላ
ቸው ።
ወይቤልዎ እወ እግዚኦ ።
አቤቱ አዎን እናምናለን አሉት ፣ ሐተታ እወ እን
ዲሉት ያውቅ የለም ቢሉ ዐላዋቂ ሥጋን እንደተ
ዋሐደ ለማጠየቅ ፣ አኮ ኢያእምሮ ኅቡአተ ፣ አላ
ከመ የሀብ መካነ ሰጥንተ ትሰብእቱ ዘኢየአምር
ኅቡአተ ፣ እንዲል ፣ አንድም ፣ ዐወቅሁት ብሎ ሥራ
ውን አይተውምና ፤ በዚያው ሥራውን ለመሥራት
አንድም ፣ ሃይማኖታቸውን ለማስገለጽ ።
፳፱ ወገሠሦሙ አዕይንቲሆሙ ።
፳፱ ዓይናቸውን ዳሠሣቸው ።
ወይቤሎሙ በከመ ሃይማኖትክሙ ይኩንክሙ ።
እንደ ሃይማኖታችሁ ይደረግላችሁ አላቸው ።

፴ ወሶቤሃ ተከሥተ አዕይንቲሆሙ
፴ ያን ጊዜ ዓይናቸው ዳነ ።
ወገሠጾሙ እንዘ ይብል ዑቁ ኢትንግሩ ለመኑሂ ።
ለማንም ለማን እንዳትነግሩ ዕወቁ ብሎ አስተማ
ራቸው ውዳሴ ከንቱ አይሻምና የሚያምኑበት ጊዜ
አልደረሰምና ፣ አንድም እስከ ትንሣኤ ፣

፴፩ ወወፂኦሙ ነገሩ ለኵሉ ብሔር

፴፩ ወጥተው ለሰው ሁሉ ተናገሩ አትንገር
ያሉት ሰው መንገር ልማድ ነውና ፣ አንድም ጊዜው
ቢደርስ ።
በእንተ ጽሙም ዘቦቱ ጋኔን ፤

፴፪ ወእምዝ አምጽኡ ኀቤሁ ዘጋኔን ጽሙመ
ወበሀመ ፣ ማቴዎስ ፲፪ ፣ ፳፪ ፣ ሉቃ ፣ ፲፩ ፣ ፲፬ ።

፴፪ ከዚህ በኋላ ጋኔን ድዳ ደንቆሮ ያደረገውን
ሰው ይዘው መጡ ። ድዳ ደንቆሮ ጋኔን ሲያድርበት
ሰውም ድዳ ደንቆሮ ይሆናልና ፣ አንድም ጽሙም
ወበሐም ይላል ድዳ ደንቆሮ ጋኔን ያደረበትን
ሰው ይዘው መጡ ፣ ቀድስ ቢሉት አልቀድስም
ብሏልና ፣ ድዳ አለው ። ትእዛዘ እግዚአብሔርን
ስማ ቢሉት አልሰማም ብሏልና ደንቆሮ አለው ።
፴፫ ወወፂኦ ጋኔኑ ነበበ ውእቱ በሐም ወሰምዓ
ውእቱ ጽሙም

፴፫ ጋኔኑ በተለየው ጊዜ ድዳ የነበረው ተና
ገረ ደንቆሮ የነበረው ሰማ ።

፴፬ ወፈሪሳውያንሰ ይቤሉ በመልአኮሙ ለአ
ጋንንት ያወፅኦሙ ለአጋንንት ።

፴፬ ፈሪሳውያን ግን ታምራት ያደርጋል ሰው
ይሳባል አሪት ትጠፋለች ወንጌል ትሰፋለች ብለው
የንጉሥን ጭፍራ በንጉሥ ቀላጤ እንዲያስወጡት
ካለቃቸው ከብዔል ዜቡል ተጨዋውቶ ያስወጣቸ
ዋል እንጂ እሰዚያ ግን አያስወጣቸውም አሉ ። አሁን
ለነዚህ ዛሬ አይመስላቸውም በሚመጣው ጉባኤ
ይመልስላቸዋል ።

በኪመ አንሶሰወ ኢየሱስ ውስተ ገሊላ

፴፭ ወአንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ኵሉ
አህጉር ወበሐውርት እንዘ ይሜህር በምኵራባቲ
ሆሙ ። ማር ፮ ፣ ፮ ።

፴፭ ጌታ በምኵራባቸው እየገባ ሲያስተምር ኖረ
ወይሰብክ ወንጌለ መንግሥት ጌትነቱን የምትናገር
ወንጌልን ሲያስተምር ኖረ ። ሐተታ እንዳለፈው
ምዕ ፣ ፬ ፣ ፳፫ ።

ወይፈውስ ኵሎ ድውያነ ወኵሎ ሕማመ ዘውስተ
ሕዝብ ለዚያው ምልክት በሕዝቡ ዘንድ ያሉ ድው
ያንን ሁሉ ይፈውስ ነበረ ።

፴፮ ወርእዮ ብዙኃነ ሰብአ አምሀርዎ ፡ ወተ ማሃሎሙ ።

፴፮ ብዙ ሰዎችን ባየ ጊዜ አሳዘኑት ፤ አዘነላቸው አስመ ስሩሃን አሙንቱ ።
በጾማ አሪት በጾማ ኃጢአት ደክመዋልና ።
ወግዱፋን ከመ አባግዕ ዘአልቦ ኖላዊ ።
ጠባቂ እንደሌላቸው አባግዕ ሁነዋልና ።

፴፯ ወእምዝ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ፡ ሉቃስ ፲ ፡ ፪ ።

፴፯ ከዚህ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው ።
ማዕረሩስ ብዙኅ
መከሩ ብዙ ነው
ወገባሩ ኅዳጥ ።
ሠራተኛው ግን ጥቂት ነው ።

፴፰ ሰአልዎ ለበዓለ ማዕረር ።
፴፰ የመከሩን ባለቤት ለምኑት ።
ከመ ይፈንዉ ገባሬ ለማዕረሩ ።

ለመከሩ አጫጅ ሠራተኛ ይጨምር ዘንድ ፤ አንድም ማዕረሩስ ብዙኅ ሰማዕያኑ ብዙ ናቸው ። ወገባሩ ኅዳጥ መምሩ አንድ የሐንስ ነው ወኅዳጥ ቅዋእንዲል ሰአልዎ የመምርነት ባለቤት እኔን ለምኑኝ ፡ ከመ ይፈንዉ እናንተን መምሁራን አድርጌ እልካችሁ ዘንድ ወይፈሩ በሚያመጣው ፈተና አትለምኑ ይል የለም ከዚህ ምነው እንዲህ አለ ቢሉ ፤ ያ ሥጋዊ ነው ይህ ግን መንፈሳዊ ነውና የሚጠቀሙበትም ነውና ፤ አንድም እስፈቅዶ ለመሾም መከራ በመጣባቸው ጊዜ ተሾሙ ተሾሙ ያለን ለዚህ ነው እን ዳይሉ ፤ ምነዋ መከራ ብንቀበል ወደን እንጂ ተሹ መነዋል እንዲሉ ፤ አንድም ማዕረሩ ብዙኅ ፤ መጻሕ ፍተ ነቢያት ንባባቸው ብዙ ነው ወገባሩ ሕዳጥ ፤ ትርጓሚያቸው ጥቂት ነው ። ድኅነት አያሰጡም ። ሰአልዎ ፤ የብሉይ የሐዲስ ባለቤት እኔን ለምኑኝ ከመ ይወስክ ገባሬ ፤ መተርጕማን አድርጌ እሥነ ማችሁ ዘንድ ድኅነት እንድታሰጡ አደርጋችሁ ዘንድ

በከመ ተፈነወ ሐዋርያት ።

ምዕራፍ ፲ ።

፩ ወጸውዖሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ። ማር ፫ ፡ ፲፫ ። ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፲፫ ፡ ፱ ፡ ፩ ።

፩ ዐሥራ ሁለቱን ደቀ መዛሙርቱን ጠራቸው ማለት ሾማቸው ወወሀቦሙ ሥልጣነ ዲበ መናፍ ስት ርኩሳን ከመ ያውፅእዎሙ ወይፈውሱ ኵሎ ድውያነ ወሕሙማነ ።

አጋንንት ያወጡ ድውያን ይፈውሱ ዘንድ ሥልጣን ሰጣቸው ማለትለሹመታቸውምልክትዱውያንፈውሱ ሙታን እንሥኡ አለ ለምጽ አንጽሑ ብሎ ገቢረ ታም ራትን ሰጣቸው ፤ ንጉሥ ደጃዝማች በሾመ ጊዜ ለሹ መቱ ምልክት ለንደቅ አላማ ማሠሪያ ነጋሪት ሰጥቶ እንዲሰደው ዐሥራ ሁለት መሆናቸው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፡ ትንቢት ፤ ኤርምያስ ለሊሁ ኢየሱስ አምላክ ወልደ አምላክ ይመጽእ ውስተ ዓለም ወየኀሪ ፲ተ ወ፪ተ ሐዋርያተ ወይከይድ ውስተ ደብረ ዘይት ዘእነ ርኢኩ ሥግወ ብሂል ፤ ኤልሳዕም በራእዩ ወናሁ ይወርድ እግዚእነ እምሰ ማይ ዲበ ምድር ወየኃሪ ፲ተ ወ፪ተ ዕፀወ ባሉጥ ብሂል ፤ ምሳሌም ያዕቆብ ከአዋልደ ከነዓን አልተጋባም ሶርያ ወርዶ ፲፪ ሕፃናት ወልዷል ጌታም ባሕርየ መላእክትን ባሕርይ አላደረገም የአዳምን ባሕርይ ባሕርይ አድርጎ ፀሥራሁለቱን ሐዋርያት ሹሞ መስ ደዱን መናገር ነው ። ኢንሥኦ ለዘንሥእ እመላእክት ዘእንበለ ዳዕሙ እምዘርዓ አብርሃም እንዲል ፤ ለኑ ዚያ ሦስቱም ምውታን ዐሥራው አብርሃም ይስ ሐቅ ያዕቆብ አኗቸው ለነሀም ፫ ሕያዋን ዐሥራው ሥላሴ አኗቸውና በዐሥራሁለቱ ምዕዛረ ፀሐይ በእ ሥራሁለቱ አልህምተ ብርት በዐሥራሁለቱ መን ብተ ሰሎሞን በዐሥራ ሁለቱ የቤት አለቆች በፀሥራ ሁለቱ ጉበኞች ምሳሌ ፤ ወማእዘ እሥራኤል ወበጽ ጽሑ ኀበ ዐ ፲ቱ ወ፪ቱ አንቅዕት ወ፸ ተመርት ይላል ዐሥራ ሁለቱ አንቅዕት ያሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ፸ ተመርት የ፸ አርድእት ምሳሌ ። አንድም በልብሰ እሮን ባሉ በዐሥራ ሁለት አይናቍ ምሳሌ ። በደ ብረ ሲና ከዙፋኑ እግር በተገኙ በ፲፪ቱ አዕናቍ ፤ ኤልያስም ፬ ቻል ውኃ አምጡ ብሎ ደግሙ ሠልሱ ብሏቸዋል በዚያ ምሳሌ ኢያሱ ዮርዳኖስን ሲሻገር ዐሥራሁለት ድንጊያ ከአፍአ አግብቶ ዐውስጥ ተክ ሏል ዐሥራ ሁለት ድንጊያ ከባሕሩ አውጥቶ አሽ ክሞ ወስዶ፲፪ቱንበጌባል፲፪ቱን በገሪዛን አስተክሏቸዋል ሰዎቹ የሐዋርያት ድንጊያው የመከራቸው ምሳሌ ትንቢቱን ዐውቆ አናግሯል ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ አስመስሏል ምሥጢሩ እንደምን ነው ቢሉ ለአራት ባሕርያት ሦስት ሦስት ግብር አላቸው ። ዐሥራ ሁለት ይሆናል ካራቱ ባሕርያት የተፈጠረ ሰውን እጠብቅባቸዋለሁ ሲል ።

፪ ወዝውእቱ አስማቲሆሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሐዋ ርያት ።

፪ ያሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ስማቸው ይህ ነው። ሐዋርያት ማለት ደጃዝማች ቀላጤ ምጥው ፍንው ሃያጅ ማለት ነው ። ደጃዝማች በተሾመበት አገር ገብቶ የተቀበለውን ሹመት ሽልማት ሰጥቶ ያከብ ረዋል ። ካህን ቢሆን ዐሥራቱን በኩራቱን ሰጥቶ ያከብረዋል ። ይህን የማይሻ መነኰሴ ቢሆን ከእ

ግሩ ቆድቆ እቡነ ዘበሰማያት ይቀበላል ለመንሶቤው ክብሩ ነው ያልተቀበለውን ዓይን በፍላት እጅ እግር በበሉት ይቀጣል ። ሐዋርያት ትምህርታቸውን የተቀበሏቸውን በልጅነት ያከብራሉ ሀብት ሥርየት ይሰጣሉ ያልተቀበሏቸውን በሌጊዎን ይነጹሉ በኑፋቄ ይበቅላሉና ፣ ቀላጤም በደለኛ ወታደር ካልገዛው አገር ገብቶ ያልፈላ ያስጠምቃል ያልቦካ ያስጋግራል ። የተበደለ ድኃ ከንጉሥ ሄዶ ይጮሃል ባዳራሽ ተገኝቶ ቀላጤ ሰጥቶ ይሰደዋል ፤ ያ ቀላጤ በብርሃን የገባውን በጨለማ በፀሐይ የገባውን በዝናም አስወጥቶ የተሰበረ ዕንጨቱን የተቀዳ ውኃውን ያስመልስለታል ። በደለኛ ወታደር ካልገዛው አገር ገብቶ ያልፈላ እንዲያስጠምቅ ያልቦካ እንዲያስጋግር ፤ ዲያብሎስ ያልፈጠረውን ፍጥረት ያልገዛውን ሰውነት ፭ ሽህ ካ፭፻ ዘመን ኃጢአት ሲያሰራ ጣዖት ሲያስልክ መኖሩን መናገር ነው የተበደለ ድኃ ከንጉሥ ሄዶ እንደመጮህ ነቢያት አንሥእ ኃይለከ ፈኑ እዴከ ማለታቸውን መናገር ነው ንጉሥ ባዳራሽ ተገኝቶ ቀላጤ ሰጥቶ እንደ መስደድ ቃለ እግዚአብሔር ሰው ሁኖ በሥራ ሁሉቱን ሐዋርያት ሹሞ መስደዱን መናገር ነው ። ቀላጤ በብርሃን የገባውን በጨለማ በፀሐይ የገባውን በዝናም እንዲያስወጣ ሐዋርያትም በደዌ የገባውን በታምራት በክህደት የገባውን በትምህርት ማስወጣታቸውን መናገር ነው። የተሰበረ ዕንጨቱን እንዲያስመልስለት በአዳም የሄደውን ልጅነት አስመልሰዋልና ፤ ፍንው ፤ ወናሁ አነ እፌንወከሙ ከመ አባግዕ ማእከለ ተኩላት ብሎ እንዲያመጣው ምጥው ። ከፍንው ይገባል ፤ ሃያጅም እለ ይህ ሁሉ ካልሄዱ አይገኝምና ።

ቀዳሚ ስምዖን ዘተሰምየ ጴጥሮስ ።

አንዱ መጀመሪያው ጴጥሮስ የተባለ ስምዖን ነው ። ሐተታ ፤ ጴጥሮስ ማለት መርግ ማለት ነው መርግ ከወደላይ ቢመጣ ያስፈራል ። እሱም ሞተ በሥጋ ወሐይወ በመንፈስ እያለ ሲያስተምር ያስፈራልና አንድም ሻፎ ደንጊያ ማለት ነው ይህ ሥጋን ካጥንት ይሰያል ። እሱም ምእመናንን ከመናፍቃን ይለያልና ፤ አንድም ደንጊያ ማለት ነው ይህን የቀን ሐሩር የሌሊት ቁር አይሰውጠውም ። እሱም በመከራ አይለወጥምና ፤ አንድም ከዋው ደንጊያ ማለት ነው ያ እየፈጋ ይሄዳል ። እሱም ካ፲፩ዱ ስብከት ሁሉ እየገባ ያስተምራልና ፤ ወእንድርያስ እኁሁ ። ወንድሙ እንድርያስ ነው ። ሐተታ ፤ እንድርያስ ማለት ተባእ ለመስቀል በሦረ ሐዋርያት ማለት ነው ።

፫ ወያዕቆብ ወልደ ዘብዴዎስ

፫ የዘብዴዎስ ልጅ ያዕቆብ ነው ሐተታ ፤ ያዕቆብ ማለት እዕቃጺ እኃዚ ማለት ነው ። የቀደመው ያዕቆብ ሰኰና ኤሳውን ይዞ እንደተወለደ ፤ እሱም ሰኰና ወንጌልን ይዞ ሲያስተምር ይሞታልና ሰኰና ኤሳውን እንዳሰናከለ እሱም የመናፍቃንን ትምህርት ያሰናክላልና ።

ወዮሐንስ እኁሁ ።

ወንድሙ ዮሐንስ ነው ። ዮሐንስ ማለት ፍሥሐ ወኀሤት ማለት ነው ። ወብዙኃን ይትፌሥሑ በልደቱ እንዲል ፤ ፊልጶስ ።

ፊልጶስ ነው ፤ ፊልጶስ ማለት ረያጼ አፍራስ ማለት ነው እኃዜ ኩናትም ማለት ነው መፍቀሬ አኃው ማለት ነው ፊልሳዳፎስ እንዲል ።

ወበርተሎሜዎስ

በርተሎሜዎስ ነው በአብራይስጥ በር ልጅ ማለት ነው ። ተክል የማጠጣት ግብር ያለው ልጅ ማለት ነው ወልደ ኃይል ወልደ የማን እንዲል ፤ አንድም ወይን ተክሎ ዕለቱን አድርሷልና ፤

ቶማስ ።

ቶማስ ነው፤ቶማስ ማለት ፀሐይ ማለት ነው ። ፪ቱ አስማቲሁ ለፀሐይ አሐዱ ቶማስስ ወ፩ዱ አርያሬስ እንዲል ።

ወማቴዎስ መጸብሐዊ ።

አንዱ ማቴዎስ ነው ። ማቴዎስ ማለት ኅሩይ ማለት ነው ከዚህ አውጥቶ ለዚህ ማዕርግ አበቃው ሰማለት ስሙን ከነግብሩ ጠራው ።

ወያዕቆብ ወልደ እልፍዮስ ።

የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ ነው ሐተታ ፤ እንዳሰፈው ወልብድዮስ ዘተሰምየ ታዴዎስ፤ታዴዎስ የተባለ ልብድዮስ ነው ልብድዮስ ማለት ልብደ ሠሪ ዓሣ ወጋሪ ማለት ነው ። ልበ ድዮስ ይላል ካህነ አምላክ ማለት ነው ። ወእምጽአ‧ማሬ ዘድዮስ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሕዝበ ድዮስጳራ እንዲል ፤ አንድም ዘርዕ ወማዕረር ማለት ነው አሪትን እንደ ዘር ወንጌልን እንደ መከር አድርጎ አስተምሯልና አንድም ሥንዴ ዘርቶ ዕለቱን ለመሥዋዕት አድርሷልና

፬ ወስምዖን ቀነናዊ ።

፬ ባልተነበበ ስሙ ይተረጐማሉ ስምዖን ያለው ናትናኤል ነው ናትናኤል ማለት ውሁብ ሀብተ እግዚአብሔር ማለት ነው ቀነናዊ የቃና ሰው ቀሬናዊ የቀራንዮ ሰው ቀናዒ ለሕገ እምላኩ ።

ወይሁዳ እስቆሮታዊ ዘውእቱ እግብኦ ።

የአስቆሮት ሰው የሚሆን ያስያዘው ይሁዳ ነው ። ይህ ሰው ስሙ ከግብሩ ያልተባበረ ነው ይሁዳ ማለት ተአማኒ በእግዚአብሔር ማለት ነበር እሱ ግን እላ ደረገውም ለዚህ ማዕርግ ቢያበቃው ከሞቱ ገባበት ለማለት ጸፈው እንዳወጣው ለማጠየቅ በመጨረሻ አመጣው ።

፭ እሉንተ ዐሠርተ ወ፪ቱ ሐዋርያተ ፈነዎሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

[illegible] እውነተ ካለ ፈንወ ፈነዎሙ ካለ ለእውነቱ [illegible] ነበር ፤ ጌታ እኒህን ፲፪ቱን ሐዋርያት ላከ [illegible] ሐተታ ካ፩ ወገን መርጧቸዋል፤ [illegible] ከፈናጽያን ከመጸብሐን ከመሠግራን [illegible] ፡ ቤትን ባምስት ወገን ያጸኑታል [illegible] በገለባ በግር በደንጊያ በእንጨት ካራት [illegible] ካ፩ኛ ባሕርየ ነፍስ የተፈጠረ ስውን [illegible] እጠብቅባችኋለሁ ሲል ፤ ከነዚህም [illegible] ያስወጠውም አለ ። በእ [illegible] ያላባለፈውም ግብር እንዳለ ለማ [illegible] ፤ [illegible] ግመዓትም የገዢና የተገዢ ምልክት [illegible] ቤተ ሰው ስሙን ለውጦ እንዲያወጣ [illegible] እንዘ ይብል ፍኖተ አሕዛብ ኢትሑሩ ፤ [illegible] መንገድ አትሂዱ ማለት የአሕዛብን ሥራ [illegible] ። ወውስተ ሀገረ ሳምር ኢትባኡ ፤ [illegible] አገር አትግቡ ብሎ አዘዛቸው ።

፮ [illegible] ኀበ አባግዕ ዘተኀጕላ እምቤተ [illegible] ።

፮ [illegible] ወደጠፉ በጎች ሂዱ ማለት መምህር [illegible] ወደ ተጎዱ ወደ እሥራኤል ሂዳችሁ አስተምሩ እንጂ ትንቢት የተነገረ ሱባዔ የተቆጠረ ለነዚህ ነውና አንድም ። ትንቢት የተነ ገረልን ሱባዔ የተቈጠረልን እኛ ባለን ትምህርቱን [illegible] ነበርና ፤ [illegible] ፡ አንድም [illegible] [illegible] ነበርና እንዳይሉ ፤

፯ ወሐዊረክሙ ስብኩ እንዘ ትብሉ ቀርበት መንግሥተ ሰማያት ፤

፯ ሂዳችሁ ጽጌቱ በልጅነት ልጅነት በሃይማ ኖት የምትሰጥበት ጊዜ ደርሷል እያላችሁ አስተምሩ

፰ ድውያነ ፈውሱ ።

፰ ድውያንን ፈውሱ ።       ሙታነ አንሥኡ ፤
ሙት አንሡ ።
እለ ለምጽ አንጽሑ ፤
ለምጽ አድኑ ።
አጋንንተ አውጽኡ ፤
አጋንንትን አውጡ ።
በጸጋ ዘነሣእክሙ በጸጋ ሀቡ
በለጋስነት የተማራችሁትን በለጋስነት አስተምሩ
በከንቱ ዘነሣዕክሙ በከንቱ ሀቡ
ዋጋ ሳትሰጡ የተማራችሁትን ዋጋ ሳትቀበሉ አስ ተምሩ አንድም በጸጋ ዘነሣእክሙ ፥ በታምራት የተ ማራችሁትን በታምራት አስተምሩ ፡ በከንቱ ዘነሣ እክሙ ፥ ሳትጽና የተማራችሁትን ሳይጽና አስተምሩ

፱ ኢታጥርዩ ለክሙ ወርቀ ወኢብሩረ ፡ ማር
፮ ፡ ፰ ፡ ሉቃ ፡ ፱ ፡ ፫ ፡ ፲ ፡ ፬

፱ ወርቅ ብር አትያዙ ።
ወኢጸሪተ ውስተ ቅናውቲ ክሙ ።
በዝናራችሁ ቍናማቺክሙ ይላል ፡ በተረንተራ ችሁ ሻሚ መሐልቅ አትያዙ ።

፲ ወኢጽፍነተ ለፍኖት ።

፲ የስንቅ አቅማዳም አትያዙ ።
ወኢ፪ኤ ክዳናተ ።
ሁለት ልብስም አትያዙ ፡ ይህን የሚሹ ሥጋውያን ናቸው እሳቸው ግን መንፈሳውያን ናቸውና ይህን አይሹም ፤   አንድም ሁለትም ልብስ ባይኖረን አንዱን ለብሰን አንዱን ሸጠን ባንመገብ እንደምን በሆን ነበር ብሎ ያዳክማልና እንዳያዳክማቸው ነው
ወኢጫማ ።
ጫማ አታድርጉ ይህ ለሥጋውያን ነው ፤ እሳቸው ግን መንፈሳውያን ናቸውና ይህን አይሹትም ፤ አንድም ጫማ ባይኖረን እሾሁን ዕንቅፋቱን ዋዕዩን እንደምን ባለፍነው ነበር ብሎ ያዳክማልና እንዳያ ዳክማቸው ነው ። አንድም ጌጸኛውን ሲል ነው።
ወኢበትረ ።
በትርም አትያዙ ። ይህ ለሥጋውያን ነው ፤ እሳቸው ግን መንፈሳውያን ናቸውና ይህን አይሹትም ፡ አን ድም በትር ባንይዝ ውሻው ጸባቡ እንደምን ባደረ ግን ነበር ብሎ ሃይማኖት ያዳክማልና እንዳያዳክም ነው አንድም ጌጸኛውን ሲል ነው እስመ ይደልዎ አስቡ ለዘይትቀነይ ።
ለሚሠራ ዋጋ ይገባዋልና ለሚያስተምር መምህር የዕለት ራት አንድ እንጀራ ጽዋ ውኃ ይገባዋልና ። ኢታጥርዩ ። አንድም በናስተምር ውለን ምን እን መገባለን ትሉኝ እንደሆነ ለሚያስተምር ለመምህር እንጂ የለት ራት አንድ እንጀራ ጽዋ ውኃ ይገባዋል እነዚያው ይመግቧችሁ ።

፲፩ ወውስተ ሀገር እንተ ቦእክሙ ወኀመኒ አብያት ተስአሉ ወበሉ ለመኑ ይደልዎ ሰላም በው ስቴታ ።

፲፩ ከገባችሁበት አገር ከገባችሁበት ቤት ደግ ሰው የበቃ ማን አለ ብላችሁ ጠይቁ ።
ወሀየ ኀድሩ እስከ አመ ትወጽኡ ፤
ለማስተማር ወጥታችሁ እስክትሄዱ ድረስ ከዚያ ኑሩ ። ሐተታ፡ምእመናን ለመማር በመጡ ጊዜ እንዳ ያጧቸው ነው ። አንድም ካንዱ ወዳንዱ ሲሉ ያይ ዋቸው እንደሆነ እኒህማ ምግብ ለማሻሻል መጥተ ዋል እንጂ መቼ ለማስተማር መጥተዋል እንዳይሏ ቸው ።

፲፪ ወበዊአክሙ ውስተ ቤት ተአምኅዎሙ ።

፲፪ ከቤት በገባችሁም ጊዜ እጅ ንሷቸው ማለት አክብሯቸው እንጂ አክብሩን አትበሉ ።
ወለእመ ይደልዎ ለውእቱ ቤት ይኅድር ሰላምክሙ

ላዕሌሁ የበቃ ደግ ሰው የተገኘ እንደሆነ ሰላማችሁ እኔ አደርበታለሁ ።

፲፫ ወእመሰ ኢይደልዎ ይግባእ ሰላምክሙ ላዕሌክሙ ።

፲፫ የበቃ ደግ ሰው ያልተገኘ እንደሆነ ግን ሰላማችሁ በናንተ ይደር ማለት ሰላማችሁ እኔ በናንተ እንዳደርኩ እቀራለሁ ።

፲፬ ወለዘሰ ኢተወክፈክሙ ወኢሰምዓ ነገረክሙ ወጺአክሙ እፍአ እምውእቱ ቤት ወእም ውእቱ ሀገር ንግፉ ጸበለ እገሪክሙ ።

፲፬ እናንተን እልቀበልም ትምህርታችሁንም አል ሰማም ያለ ሰው ካለበት ቤት ካለበት አገር ወጥታችሁ የግራችሁን ትቢያ አራግፉ ። ሐተታ ፡ ስንኳን ገንዘባችሁ ትቢያችሁ አልተከተለንም ለማለት ። እኛ ያክመንላችሁ በእምቢታችሁ ቢቀርባችሁ ፍዳችሁ በራሳችሁ ነው ለማለት ፡ አንድም ይህ ትቢያ ከኛ እንደተለየ እናንተም ከኛ ልዩ ናችሁ ለማለት ፡ አንድም ትቢያ እንደ ረገፈ እናንተም በሥጋችሁ በመቅሠፍት በነፍሳችሁ በገሃነም ትጠፋላችሁ ለማለት ፡ አንድም በቁማር ልማድ ፡ የተበደለ ሰው ቢኖር ስንጨት ተክሎ ማር ጽጥሮ መጥቶ ይንገረኝ ብሎ ነበርና ።

፲፭ አማን እብለክሙ ከመ ይረክባ ሳሕለ ምድረ ሰዶም ወገሞራ አመ ዕለተ ደይን ፈድፋደ እምይእቲ ሀገር ።

፲፭ እናንተን አልቀበልም ትምርታችሁን አል ሰማም ያለ ሰው ሁሉ ካለበት አገር ይልቅ ሰዶም ገሞራ በፍርድ ቀን ዕረፍትን ያገኛሉ ብዬ እንዲያገኙ በእውነት እነግራችኋለሁ ። በሀገሩ ሰዎቹን መናገር ነው ፍዳ ይቀልላቸዋል ማለት ነው ።

፲፮ ወናሁ አነ እፌንወክሙ ከመ አባግዕ ማእከለ ተኩላት ። ሉቃ ፲፥ ፫

፲፮ ተኩላ አለና ብለው አባግዕን ከቤት እንዳያ ውሏቸው ተኩላ ወዳለበት እንዲያስማሯቸው ፡ ወደ ነገሥተ አሕዛብ ወደ መኳንንት አሕዛብ እሰዳ ችኋለሁና ። ኩኑ እንከ ጠቢባነ ከመ አርዌ ምድር ወየዋሃነ ከመ ርግብ እንደ እባብ ብልህ ሁኑ እንደ ርግብም የዋህ ሁኑ ። አንድም በሉቃስ እፌንወክሙ ማእከለ ተኵላት ይላል ። ወደ ነገሥተ አሕዛብ ወደ መኳንንተ አሕዛብ እሰዳችኋለሁና ኩኑ ጠቢባነ ። ሐተታ የእባብ ብልሐቱ ምንድነው ቢሉ ከመንገድ ዳር ሲተኛ ራሱን ቀብሮ ይተኛል እናንተም ራሳችሁን እኔን አትካዱኝ ሲል አንድም ውኃ ሲጠጣ መርዙን ከየብስ አኑሮ ነው ፡ ከውኃው የገባ እንደ ሆነ ተሰራጭቶ ያጠፋኛል ብሎ እናንተም ቂም በቀል ይዛችሁ አትጸልዩ ሲል ቂም በቀል ይዞ የጸለዩት ጸሎት አይረባም አይጠቅምምና ። እስመ ዘያነብር ቂመ ውስተ ልቡ ኢይሰጠፍት ጸሎቱ ቅድመ እግዚአብሔር እንዲል አንድም በኖኅ ጊዜ አፉን ከፍቶ ሳለ ርግብ ዋሻ መስሏቸ ገብታ እንቁላሏን ጣለች እሷን የበላኋት እንደሆነ ኖኅ አስወጥቶ ይጥለኛል ብሎ እስክትወጣ አፉን እንደከፈተ ቆይቷል ምክንያት አድርጎ እናንተን የሚያጠፋብትን ሥራ አትሥሩ ሲል ነው ። አንድም ዕፀ ዘዌ የሚባል አለ ፍሬውንይወደዋልጥላውሲያርፍብትያደክመዋልብልህ ነውና ቢት በምሥራቅ ማታ በምዕራብ ሁኖ ይመገበዋል ምክንያት አድርጎ እናንተን የሚያደክምበትን ሥራ አትሥሩ ሲል ፡ አንድም ጥግ ሳይዝ አይጣላም ምክንያት አድርጎ እናንተን የሚጣላበትን ሥራ አትሥሩ ሲል ራቁቱን የሆነ አይነድፍም ምክንያት አድርጎ እናንተን የሚጥልበትን ሥራ አትሥሩ ሲል ፡ ርግብ የዋህ ናት በቀል ጥላትም እናንተም ኃዳግያነ በቀል ሁኑ ሲል በኖኅ ጊዜ ዋሻ መስ ሏት ከዘንዶ አፍ ገብታ በየውሃት ተጠብቃለች እናንተም በየውሃት ሆናችሁ ተጠብቃችሁ ኑሩ ሲል አንድም ከዕፀ ዘዌ ሥር ዐርፋ በየውሃት ትጠበቃለች እናንተም በየውሃት ተጠብቃችሁ ኑሩ ሲል ፡ ዑሐይ ልትሞቅ ስትወጣ በምዕራብ ሽምቆ ቆይቶ እያናቀ ይፈጇታል ። እናንተም በየውሃት ሁናችሁ መከራውን ተቀበሉ ሲል ።

፲፯ ወተዓቀቡ እምሰብእ እኩያን

፲፯ ከክፉ ሰዎች ተጠበቁ ።
እስመ ያገብኡክሙ ውስተ ሕፅዋዳት ።
አደርቡን ብለው ወደ ዐደባባይ ይወስዳችኋልና ፡
ወይቀሥፉክሙ በምኵራባቲሆሙ ።
በምኵራባቸው አግብተው ይገርፏችኋልና ፡

፲፰ ወይወስዱክሙ ኀበ መሳፍንት ወነገሥት በእንቲአየ ፡

፲፰ በሰሜ ስለ አመናችሁ በስሜ ስለ ተጠራችሁ በስሜ ስለ አስተማራችሁ ወደ መኳንንተ አሕዛብ ወደ ነገሥተ አሕዛብ ይወስዷችኋልና ፡ ከመ ይኩን ስምዓ ላእሌሆሙ ዘእብራኤል መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ፡ ምነው ያላመናችሁበት ይሏቸዋል ምን አይተን እንመን ይላሉ ያውሳ በጸዓብ ደረት ባጭር ቁመት ተወስኖ ቢያስተምራችሁ ጡልታችሁ ተመቅኝታችሁ ሰቅላችሁ የገደላችሁት ተብሎ ፡ አንድም ምነው ያላመናችሁበት ይሏቸዋል ምን አይተን እንመን ይላሉ ያውሳ ሐዋርያት የሱን ነገር ቢያስተምሯችሁ እንቀበላችሁ ብላችሁ ለአሕዛብ ኤያሳለፋችሁ ትሰጧቸው የነበረ ተብሎ ፡ ወላዕለ አሕዛብ ።
በአሕዛብም መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ፡ ምነው ያላመናችሁበት ይሏቸዋል ምን አይተን እንመን ይላሉ ፡ ያውሳ ሐዋርያት የሱን ነገር ወረደ ተወለደ

፳፱ አኮኑ ፪ቱ አዕዋፍ ይሰየጣ ለ፩ኤ ጸሪቀ አሰርዮን ።
እንዲህማ ከሆነ ወድቀን ወድቀን መቅረታችን አይ ደለም ተሉን እንደሆነ ። ፪ ፡ ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፲፩ ።

፳፱ ግዕ ፡ ፳፮ ፡ ፴፬ ። ሁለት አዕዋፍ በሁለት ሻሚ መሐለቅ ይሸጡ የለምን አሰርዮን የገበያ የሚዛን ስም ወአሐቲ እምኔሆን ኢትወድቅ ውስተ ምድር ዘእ ንበለ ያእምር አቡክሙ ሰማያዊ ።
ሰማያዊ አባታችሁ ሳያውቅ ከሁለቱ አንዲቱ አት ወፋም በወጥመድ አትያዝም ።

፴ ወለክሙሰ ሰእርተ ርእስክሙኒ ሆሉ ጉሉቀ ውእቱ ።

፴ እናንተስ የራሳችሁ ጸጉር ሳይቀር የተቈ ጠረ ነው የተቈጠረ እንዳይጠፋ አትጠፉም ።

፴፩ ኢትፍርሁኬ እስመ እምብዙኃን አዕዋፍ ትኄይሱ አንትሙ

፴፩ ከተፈጥሮተ አዕዋፍ ተፈጥሮተ ሰብእ ይበ ልጣልና አይዟችሁ ። አንድም አኮኑ ብለህ መልስ በአሪት በነቢያት ያሉ ሰዎች በሃይማኖት በጥምቀት ይኖሩ የለምን ወአሐቲ እምኔሆን ፤ በአሪት በነቢ ያት ካሉ ሰዎች ሰማያዊ አባታችሁ ሳያውቅ አንዱ አይጠፋም ፤ ወለክሙሰ የናንተስ ደቀመዛሙርቶ ቻችሁ ሳይቀሩ የተቈጠሩ ናቸው ሥእርት አላቸው አርድእትን ጸጉር የራስ ጌጽ እንደሆነ ደቀ መዝሙር ለመምህሩ ጌጽ ነውና ጸጉር ያደገው ሲወድቅ ያላ ደገው ሲወጣ ደስ እንዲያሰኝ ደቀ መዝሙር ያጠ ናው ሲወጣ ያላጠናው ሲገባ ደስ ያሰኛልና ኢት ፍርሁኬ በአሪት በነቢያት ካሉ በሃይማኖት በጥ ምቀት ያላችሁ እናንት ትበልጣላችሁና አይዟችሁ አንድም አኮኑ ብለህ መልስ በሃይማኖት በጥምቀት ያሉ ሰዎች በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን ይኖሩ የለምን ወአሐቲ እምኔሆን በሃይማኖት በጥምቀት ካሉ ሰማያዊ አባታችሁ ሳያውቅ አንዱ አይጠፋም ወለክሙሰ እንዳለፈው ኢትፍርሁ በሃይማኖት በጥም ቀት ካሉ በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን ያላችሁ እናንተ ትበልጣላችሁና አትፍሩ ።

፴፪ ኵሉ ዘየአምን ብየ በቅድመ ሰብእ እነኒ እአምኖ በቅድመ አቡየ ዘበሰማያት ፤ ማር፡፰ ፡ ፴፰ ። ሉቃ ፡ ፱ ፡ ፴፮ ፡ ፲፪ ፡ ፰ ። ፪ ፡ ጢሞ ፡ ፪፡፲፪ ።

፴፪ በሰው ፊት ያመነብኝ ማለት ዘመን የወለደውን ንጉሥ የወደደውን ሳይል በሰው ፊት ያመነብኝን በሰማያዊ አባቴ ፊት ልጅ ወዳጅ እለዋለሁ

፴፫ ወለዘሰ ክህደኒ በገጸ ሰብእ እነኒ እክህዶ በገጸ አቡየ ዘበሰማያት ።

፴፫ ዘመን የወለደውን ንጉሥ የወደደውን ብሎ በሰው ፊት ያላመነብኝን ግን እኔም በሰማያዊ አባቴ ፊት ወለድኩህ ካድኩህ እለዋለሁ አንድም በቤተ ክርስቲያን በሰው ፊት ያመነብኝን ልጅ ወዳጅ እለዋለሁ ። ከቤተ ክርስቲያን በሰው ፊት ያላመነብኝን ግን በሰማያዊ አባቴ ፊት ወለድኩህ ካድኩህ እለዋለሁ

፴፬ ኢይምሰልክሙ ዘአምጻእኩ ሰላመ ለምድር

፴፬ ለሰው ፍቅርን አንድነትን ያመጣሁ አይ ምሰላችሁ ኢያምጻእኩ ይላል አላመጣሁም ።
አላ መጥባሕተ ።
ሰይፍን ነው እንጅ ማለት ጾብን ክርክርን መለያየትን ነው እንጂ ።

፴፭ ወመጻእኩሰ እፍልጥ ብእሴ እምአቡሁ

፴፭ ወንድ ልጅን ከአባቱ ።
ወወለተኒ እምእማ ።
ሴት ልጅን ከናቷ ።
ወመርዓተኒ እምሐማታ ።
መርዓትን ካማቷ ልለይ መጥቻለሁ እንጅ ፤ ሐተታ ፤ አማትና ምራት ሳይስማሙ ከመሬት እንዲሉ የማ ይስማሙ ያሉ እይደለምን ቢሉ በሚስማሙት መና ገር ነው ። አንድም ወመጻእኩ እፍልጥ ብእሴ እም አቡሁ ብለህ መልስ ወንጌልን ከአሪት ወወለተኒ ዐሠርቱ ቃላትን ከሥርዓተ ሪበናት ወመርዓትኒ ነቢያት ካህናትን ከምኵራብ ልለይ መጥቻለሁ እንጅ አንድም ብእሴ እምአቡሁ ሰውን ከግብር አባቱ ከሰይጣን ፤ ወወለተኒ ፈቃደ ነፍስን ከፈቃደ ሥጋ ፤ ወመርዓተኒ ውሣጣዊት ግብርን ከአፍአዊት ግብር ልለይ መጥቻለሁ እንጅ ።

፴፮ ወሰብእ ቤቱ ይፃረር ለዐብእ
፴፮ ግር ፡ ፯ ፡ ፮ ። ሰውን ቤተሰቦቹ ይጣሉ ታል ዘመን የወለደውን ንጉሥ የወደደውን ይዘህ መሰለህ አትኖርም ይሉታል አንድም መከራ እቀ በላለሁ ባለ ጊዜ ሕዋሳቱ ይፈሩበታል አንድም ሰብእ ቤቱ ይሁዳ ክርስቶስን ያፀቅለዋል ።

፴፯ ዘያፈቅር አባሁ ወእሞ እምኔየ ኢይደሉ ሊተ ወኢይክል ይፀመደኒ ። ሉቃ ፲፬ ፡ ፳፮ ።
፴፯ አባት እናት ከደዋል ልጆች እልካዱም ፤ በሃይማኖት እናት አባቴን ካልመሰልኩ ርስቱን ጉል ቱን ለሌላ ያወርሱብኝ የለም ብሎ በሃይማኖት ጊዜ ከኔ ይልቅ አባት እናቱን የወደደ ሰው የኔ ደቀ መዝሙር ሊባል አይገባውም እኔን ሊያገለግለኝ አይቻለውም ።
ወዘያፈቅር ወልዶ ወወለቶ እምኔየ ኢይደሉ ሊተ ፤ አሁን ልጆች ከደዋል አባት እናት አልካዱም በሃይ ማኖት ልጆቼን ካልመሰልኳቸው ኋላ ማን ይረዳኛል ማን ያጠባኛል ብሎ በሃይማኖት ጊዜ ከኔ ይልቅ ልጆቹን የወደደ የኔ ደቀ መዝሙር ሊባል አይገባውም ወኢይክል ይፀመደኒ ።
ሊያገለግለኝ አይችልም

የቀንቀኑ አርድእተ ዮሐንስ ፣ እንድም ምስቁ ሃታ ናቸው አንዱ ሃታ የዘፈን ዜማ ቀንቀኑ አንዱ ሃታ ተቀበሉ አንዱ ሃታ ዝም አሉ እነሆ ሲቀበሉ እኒያ ዝም ማለታቸው ደስ ባይላቸው እንጅ ነው ብለው የዘፈን ዜማ የተነቀነት መልሰው የልቅሶ ዜማ ቀንቅ ነዋል የተቀበሉ ተቀበሉ አንቀበልም ያሉ ዝም አሉ የተቀበሉ ጋዋእን መጽብሐን አንቀበልም ያሉ ጸሐፍት ፈሪሳውያን የጌታን ትምህርት በዘፈን ዮሐንስን በልቅሶ መስሉ ተናገረ በለምን ቢሉ በጌታ ትምህርት ታምራት ተደርጓበታል ልጅነት ተገኝቶ በታል ። በዮሐንስ ትምህርት ግን ልጅነት አልተገኘበትም ታምራት አልተደረገበትምና ምነው ያውስ ቢሆን የዮሐንስ ቀድሞ የጌታ አይከተልም ነበር ቢሉ የጌታ ቃል ሳለ የባሪያ ቃል እናስቀድምም ብለው በብያኔ አስተድመውታል ነገር ግን ሁሉም አንድ ነው ። ዮሐንስ ሳይበላ ሳይጠጣ ማስተማሩ ታምራት መስሏቸው ይሳቡ እንደ ሆነ ብሎ ፣ ጌታ እየበላ እየጠጣ ማስተማሩ በፍቅር ለመሳብ ነው ። ከዚያም ቢያጣምሙ ከዚያም ቢያጠምሙ ለመያዝ እንደሆነ ።

ወጸደቀት ጥበብ እምደቂቃ ወእምግባራ ።

ጥበብ ወልድ ከሥራዋ ከልጆቹዋ የተነሣ ከበረች ጸድቀት እምኔየ ትዕግር እንዲል አንድም ደቂቃ በምግባራ በሥራዋ ልጆቹዋን ረታች ጸድቀተኒ ትዕግር እንዲል አንድም ጥበብ ወልድ ከልጆቹዋ ይልቅ በሥራዋ ከበረች ።

ዘከመ ጌሰን ፤

ለእሁጉር ኢንሳሕያት ።

፳ ወእምዝ አኀዘ እግዚእ ኢየሱስ ይጌሥን ለእሁጉር እለ በውስቴቶን ገብረ ኃይለ ብዙኃ ።

፳ ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ክርስቶስ ደጋግ ታምራት ያደረገባቸውን ምኵራባት ይነቅፋቸው ጀመር። እስመ ኢነስሐ ።

አላመኑምና ።

፳፩ ወይቤሎን አሌ ለኪ ኮራዚ

፳፩ ስመ ምኩራብ ነው ኮራዚ ወዮልሽ እያለ ሉቃ ፣ ፲ ፣ ፲፫ ። አሌ ለኪ ቤተ ሳይዳ ።

ቤተ ሳይዳ ወዮልሽ ።

እስመ ሶበ በጢሮስ ወበሲዶና ተገብረ ኃይል ዘተገብረ በውስቴትክን ።

በናንተ የተደረገው ታምራት በጢሮስ በሲዶና ተደርጎ ቢሆን ።

እምነስሑ በሐመድ ።

ማቅ ለብሰው አመድ ነስንሰው ንስሐ በገቡ ነበር ። ሐተታ፣ በጢሮስ ኪራም ፳፪ ዘመን ኑሮ የለምን በሲዶናስ ኤልያስ አንድ ምውት ኤልሳዕ ሁለት ምውት አስነሥቶ የለም ቢሉ በኒያ ሕጸጽ አለበት በጌታ ግን ሕጸጽ የለበትምና የኒያ የጸጋ ነው የጌታ ግን የባሕርይ ነውና ።

፳፪ ወባሕቱ እብለክሙ ጢሮስ ወሲዶና ይረክባ ሳሕተ ፈድፋደ እምኔክን አመ ዕለተ ደይን ።

፳፪ ነገር ግን ጢሮስ ሲዶና በፍርድ ቀን ከናንተ ይልቅ ዕረፍትን ያገኛሉ ፣ ብየ እነግራችኋለሁ ።

፳፫ ወአንቲኒ ቅፍርናሆም ለእመ እስከ ሰማይ ትትሌዓሊ እስከ ሲኦል ትወርዲ ።

፳፫ አንቺም ቅፍርናሆም እስከ ሰማይ ብትደርሺ እስከ ሲኦል ትወርጃ ዘንድ አለሽ ። አንቺም ቤተ አይሁድ ክርስቶስን ዕሩቅ ብእሲ እስከ ማለት ብትደርሺ ገሃነም ትወርጂ ዘንድ አለሽ ።

እስመ ሶበሁ ተገብረ ኃይል ዘተገብረ በውስቴትኪ እምሀለወት እስከ ዮም ።

ባንቺ የተደረገ ታምራት በሰዶም ተደርጎ ቢሆን ንስሐ ገብታ ከተፈረደበት ፍርድ ድና እስከሁን ፀሕይወት በኖረች ነበር ። ሐተታ ፣ በሰዶም ሎጥ በእንግዉ ደረቅ ዕንጨት አለምልሟል መላእክትንስ ዕንግድነት ተቀብሉ የለም ቢሉ የሱ የጸጋ ነው የጌታ ግን የባሕርይ ነውና ፣ በሱ ሕጸጽ አለበት በጌታ ግን ሕጸጽ የለበትምና ።

፳፬ ወባሕቱ እብለክሙ ከመ ምድረ ሰዶም ሳሕተ ትረክብ ፈድፋደ እምኔኪ አመ ዕለተ ደይን ።

፳፬ ነገር ግን በፍርድ ቀን ካንቺ ይልቅ ሰዶም ዕረፍትን ታገኛለች ብየ እነግራችኋለሁ ።

፳፭ ወይእተ ጊዜ አውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤ እእምነከ አባ እግዚእ ሰማያት ወምድር ። ሉቃ ፣ ፲፩ ፣ ፩ ።

በዚህ ያልተያዘ በሉቃስ የተያዘ ነው ። ሰብዓ አርድእት መጥተው አጋንንት ገረሩ ለነ በስምከ ብለውታል እነሱ ማመለገን ባይቻላቸው በዓቸው ተገብቶ ያመሰግንላቸዋል ።

፳፭ ያን ጊዜ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዩን ምድሩን የፈጠርህ አባቴ አመሰግንሃለሁ አለ ወልድየ እመና እንዲል አእኰቶ ሲል ።

ዘኀባእኮ ለዝንቱ እምጠቢባን ወማእምራን ወከሠትኮ ለሕፃናት ።

የኔን እምላክነት ዐዋቆች ነን ከሚሉ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ሰውረህ ለሕፃናት እአምሮ ለሐዋርያት የገለጥኸው ።

፳፮ እወ አባ እስመ ከመዝ ኮነ ሥምረትከ በቅድሜከ ።

፳፯ እዎን አባቴ አዋቂ ነን ከሚሉ መሰወር አላዋቂ ነን ለሚሉ መግለጥ ቀድሞም ልማድህ ነው፤ ምሥጢረ ድኅነትን ከሰብእ ትካት ሰውረህ ለኖኅ ከሰብእ ሰዶም ሰውረህ ለሎጥ እንደገለጥህ ።

፳፯ ኵሉ ተውህበኒ እምኀበ አቡየ ።

ዮሐንስ ፺፬፪ ። ፺ ፣ ፳፰ ፣ ፳፬ ። ፹ ፣ ፲፬ ። ፲ ፣ ፲፰ ።

፳፮ ሁሉ ከባቴ ዘንድ ተሰጠኝ ። የተሰጠውስ በማኀፀን ሲዋሐድ ነው ፣ ወለዘፈቀደ ወልድ ይከሥት ሎቱ ለማለት ነው እንጂ

ወአልቦ ዘየአምሮ ለወልድ ዘእንበለ አብ

አብን ወላዲ ካላለ ወልድን ተወላዲ ብሎ የሚያ ምን የለም ።

ወአልቦ ዘየአምሮ ለአብ ዘእንበለ ወልድ ።

ወልድን ተወላዲ ካላለ አብን ወላዲ ብሎ የሚያምን የለም አንድም አብ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ባይ መሰከርለት ወልድን የሚያውቀው አልነበረም ።

ወአልቦ ፣ ወጸአኩ እምኀበ አብ ወመጻእኩ አቡየ ፈነወኒ ዘርእየ ኪያየ ርእዮ ለአቡየ አነ ወአብ አሐዱ ንሕነ ብሎ ሳይመሰክር አብን የሚያውቀው አል ነበረም ፣ አንድም ፣ ከአብ በቀር አብ ያውቀዋል እንጂ ያለ አብ ወልድን በባሕርዩ የሚያውቀው የለም ፣ ወአልቦ ፣ ከወልድ በቀር ወልድ ያውቀዋል እንጂ ያለ ወልድ አብን በባሕርዩ የሚያውቀው የለም ።

ወለዘፈቀደ ወልድ ይከሥት ሎቱ ።

ወልድ ሊገልጽለት ለወደደው ይገልጽለታል ፈቀደ ለሁለቱም ።

፳፰ ንዑ ኀቤየ ኵልክሙ ስሩሃን ወክቡዳን ጾር

፳፰ ሸክም የከበዳችሁና የደከማችሁ ሁሉ ወደኔ ኑ ማለት በጸማ ኦሪት በጸማ ኃጢአት የደከማችሁ ጾረ ኀጢአት የረበናች ትብትብ ያልፈታችሁ ወደ እኔ ኑ ።

፳፱ ወአነ አዐርፈክሙ ። ኢሳ ፣ ፲ ፣ ፲፱ ፣ ዮሐንስ ፣ ፳ ፣ ፫ ።

ዕረፍተ ነፍስ ሰጥቼ አሳርፋችኋለሁ ።

፳፱ አብነት ንሥኡ ጾሩ ይላል ። ቀንበሬን ተሸከሙ ማለት ሕጌን ያዙ ። ሐተታ ቀንበር አላት ወንጌልን ቀንበር ሁለቱን በሮች አንድ አንድታ ደርግ ወንጌልም ሕዝብና አሕዛብን አንድ ታደርጋ ለችና ።

ተመሀሩ ወአእምሩ እምኔየ ከመ የዋህ አነ ወትሑት ልብየ የዋህ ትሑት እንደሆንኩ መጠን ከኔ ተም ራችሁ ዕወቁ ። ወትረክቡ ዕረፍተ ለነፍስክሙ ዕረፍተ ነፍስ ታገኛላችሁ ።

፴ እስመ አርዑትየኒ ሠናይ ።

፴ ቀንበሬ ልዝብ ነውና ።

ወጾርየኒ ቀሊል ።

ሸክሜ ቀሊል ነውና ።

ሕጌ ወንጌል ደግ ሕግ ናትና ፣ ትእዛዜም ቀሊል ነውና ከዚህ የከበደን አለ ለዚህ ጸፍአከ መልታሕቲከ ዘየማን ሚጥ ሎቱ ካልዕታሂ ወለዘሂ አበጠከ አሐደ ምዕራፈ ሑር ምስሌሁ ፪ተ ወለዘሂ ይፈቅድ ይት ዓገልከ መልበስከ ኅድግ ሎቱ ክዳንከሂ ትላለች ከዚህ የከበደ ምን አለና እንዲህ አለ ቢሉ አደርጋ ዋለሁ በሚል ዘንድ ቀሊል ነውና ፣ አንድም ለወጣ

ኒያን ክቡድ ቢሆን ለፍጹማን ቀሊል ነውና ፤ አንድም ፣ ከሕገ ኦሪት ሲለይ ነው ፤ ኦሪት ወገሩ ስቀሉ ብላ ካሰናበተች በኋላ ምኅትናለትም ወንጌል ግን በንስሐ ትላለችና ፤

ንስሐውን ቅሉ ሰበዓ በበስብዕ ትላለችና ፤ ሕግሰ መሲሐዊት ተራኀርኃት እንዲል ፣ አንድም ኦሪት ፈጽማችሁ ጽደቁ ትላለች ፣ ወንጌል ግን በክ ርስቶስ ፈጻሚነት ትላለችና ፣ አንድም ከሕገ አረ ሚ ሲለይ ። ሕገ አረሚ ላህምን ቁልቋ ሙዕ ሰብእ ትላለች በወንጌል ግን ይህ ሁሉ የለምና ፤ ከሕገ አሕዛብ ሲለይ አሕዛብ ከዱር ገብተው ባሩን ቆር ጠው እጅ እግር ሲያወጡ ቀለሙን ግድፉን ሲያከ ናውኑ ይኖሩ ነበርና

ምዕራፍ ፲፪ ።

በእንተ ሰንበት ።

፩ ወበውእቱ መዋዕል ወፈረ እግዚእ ኢየሱስ በሰንበት እንተ ማዕከለ ገራውህ ። ማር ፪ ፣ ፳፫ ፣ ሉቃ ፣ ፮ ፣ ፩ ።

፩ በዚያ ወራት ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቅዳሜ በእሻ መካከል ሄደ ።

አርዳኢሁስ ርኅቡ ወአኀዙ ይምሀዉ ሰዊተ ወይ ብልዑ ፤ ደቀ መዛሙርቱ ግን ተርበው እሸርና እሸት እያሹ ይበሉ ጀመር ።

፪ ወርእዮሙ ፈሪሳውያን ይቤልዎ ርኢ ዘይገብሩ አርዳኢከ ዘኢይከውን ገቢረ በሰንበት ።

፪ ፈሪሳውያን ሰምተው ደቀ መዛሙርትህ በሰ ንበት ሊሠሩት የማይገባ ሥራ ሲሠሩ አስተውል አሉት ።

፫ ወይቤሎሙ ኢያንበብክሙኑ ዘገብረ ዳዊት አመ ርኅበ ።

፫ ዳዊት በተራበ ጊዜ ያደረገውን አልተመለ ከታችሁም አላቸው ።

ውእቱኒ ወእለ ምስሌሁ ።

እሱም ከሱ ጋራ ያሉ ብላቴኖቹ ያደረጉትን ።

፬ ዘከመ ቦአ ቤቶ ለእግዚአብሔር ወበልዓ ሐባውዘ ቍርባን ዘኢይከውኖ ለበሊዕ ።

፬ ከቤተ እግዚአብሔር ገብቶ ሊበላው የማ ይገባውን መሥዋቱን እንደበላ ።

ወኢ ለእለ ምስሌሁ ።

ከሱም ጋራ ያሉ ሊበሉት የማይገባውን ።

ዘእንበለ ለካህናት ለባሕቲቶሙ

ለካህናት ብቻ ይገባቸዋል እንጂ ።

፭ ወካዕበ ኢያንበብክሙኑ ዘሀሎ ውስተ ኦሪት ከመ ካህናት እለ ውስተ ቤተ መቅደስ ያረኵስዋ ለሰንበት ። ዘሌ ፳፬፣፰ ፣ ዘኍ ፳፰ ፣ ፱ ።

፭ ይስዕርዋ ሲል ነው ። በቤተ መቅደስ ያሉ ካህናት ቅዳሜን እንዲሽሯት በኦሪት የተጻፈውን አል

ሕይወቱ መንፈስ ቅዱስ ለህልውና የመረጠችው ወዳጄ ።
ወእነግር መንፈስየ ላዕሌሁ ።
ሕይወቴ መንፈስ ቅዱስን ሕይወት የማደርግለት።

፲፱ ውእቱ ይሜህር ፍትሕየ ለአሕዛብ ወኩነኔየ ለሕዝብ ።

፲፱ እሱ ሃይማኖተ ወንጌልን ለአሕዛብ ሃይማኖተ አሪትን ለእሥራኤል ሲያስተምር ።
ኢይደምፅ ወኢይጸርኅ ።
አይሰማም ፤ ወአልቦ ዘይሰምዕ ቃሎ በምኵራባት ።በምኵራባት ሲያስተምር የሚሰማው የለም ተብሎ በኢሳይያስ የተነገረው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ። ሐተታ በዮሐንስ ወዓልዓለ ቃሉ በምኵራብ ይሳል በዚህ እንዲህ አለ አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር አንዱ ዮሐንስ ነው አለሞቶ ነው የሚያስተምር ፤ ከዚህ እንዲህ ማለቱ ውዳሴ ከንቱ አይሰማበትም ቢል ነው ።

፳ ብርዕ ቅጥቁጥ ኢይሰብር ፤
፳ ከእግሩ ጭምትነት የተነሣ እስኪሉ የወጣለት የፀንቀላል ቅርፍት አይደቅበትም ።
ወሡዕነ ዘይጠይስ ኢይጠፍዕ ከቃሉ ልዝብነት የተነሣ የሚጤያጤያስ የጧፍ ኩስታሪ አይጠፋበትም እስከ ያገብእ ፍትሐ መዊኦቱ
አሸናፊ ፍርዱ በአይሁድ በአጋንንት እስኪመለስ ድረስ ።

፳፩ ወበስሙ ዚአሁ ይትአመኑ አሕዛብ ።
፳፩ አሕዛብም በስሙ እስኪያምኑ ድረስ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ተግኀሠ እምሀየ ። አንድም በንስሐ በኀዘን የሚቀጠቀጥ በተስፋ የሚጤያጤያስ አዳም አይጠፋም በዕለተ ዓርብ አሸናፊ ፍርዱ በአጋንንት እስኪ መለስ ድረስ አሕዛብ በስሙ እስኪያምኑ ድረስ ብሎ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ። አሕየዎሙ ። ሞተ ሥጋው ለሞተ ነፍሱ ምልክት እንደሆነ ድኅነተ ሥጋውም ለድኅነተ ነፍሱ ምልክት ነውና ። አንድም በቅንዓት የሚቀጠቀጥ በቅንዓት የሚጤያጤያስ አይሁዳዊ አይጠፋም ። አሸናፊ ፍርዱ በአይሁድ በ፵ ዘመን እስኪ መለስ ድረስ ። አሕዛብም በስሙ እስኪያምኑ ድረስ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ፤ ተማከሩ ይቅትልዎ ፣ አንድም መቃ መስየ የፍግ እሳት ወንጌል አትጠፋበትም አሸናፊ ፍርዱ በአይሁድ በአጋንንት እስኪመልስ ድረስ ፣ አሕዛብም በስሙ እስኪያምኑ ድረስ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።
ገሠፆሙ ሐተታ ፣ መቃ መስየ እሳት ወንጌልን ፣ መቃ መሰየ በጋውን ማንም ሲጠቀጥቀው ይባጃል ። ክረምት በሆነ ጊዜ በያለበት ያፈላል ወንጌልም ስትነገር አንድ ሰው በሰማዕትነት ይሞታል ታምራት ይደረጋል ብዙ ሰው ያምናል ። የፍግ እሳት ካንድ ላይ ያቃጠሉት እንደሆነ ሁለተኛ ሦስተኛ እቃጥሉት አይልም ተያይዞ ይነዳል ወንጌልም በመቶ ሐያ ቤተሰብ ተጀምራ እስከ ምጽአት ድረስ ስትነገር ትኖራለችና ።
እንደገና ብርዕ ቅጥቁጠ ኢይሰብር ወሡዕነ ዘይጠይስ ኢይጠፍዕ ይላል እብነት በቀር ያጠፉ ችኋል ቢሏቸው ስንኳን እኛን ሊያጠፉ እስኪሉ የወጣለት የፀንቀላል ቅርፍትስ እንኳ አያደቅም ። የሚጤያጤስ የጧፍ ኩስታሪስ እንኳ አያጠፋም ይሉታል ብሎ ኢሳይያስ የተናገረው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ፈለሰ እምሀየ ።

በእንተ ዕውር ወጽሙም

ዘቦቱ ጋኔን ።

፳፪ ወአምጽኡ ኀቤሁ ዘጋኔን ዕውረ ወጽሙመ ወበሐመ ፤

፳፪ ከዚህ በኋላ ጋኔን ዕውር ደንቆሮ ድዳ ያደረገውን ሰው ወደሱ አመጡ ።
ወፈወሶ እስከ ውእቱ ዕውር ወጽሙም ነበበ ወር እየ ወሰምዐ ።
ዕውረ ሥጋው በታምራት ዕውረ ነፍሱ በትምህርት እስኪያይ በሐመ ሥጋው በታምራት በሐመ ነፍሱ በትምህርት እስኪናገር ፤ ጽሙመ ሥጋ በታምራት እስኪሰማ ድረስ አዳነው
፳፫ ወተደሙ ኵሎሙ አሕዛብ ፤
፳፫ አሕዛብ ሁሉ አደነቁ ።
ወይቤሉ አኮኑ ዝንቱ ወልደ ዳዊት ።
ያላመኑት ። የቀቡዕ የዳዊት ልጅ አይደለምን ይህን ይህል ርኅራኄ ከማን አገኘው ብለው ። ያመኑት ግን የርኅሩኅ የዳዊት ልጅ አይደለምን ምነዋ ቢያደርግ አሉ ።
፳፬ ወፈሪሳውያንሰ ሰሚዖሙ ይቤሉ ዝንቱሰ ኢያወፅእ አጋንንተ ዘእንበለ በብዔል ዜቡል መልአ ከሙ ለአጋንንት ። ማቴ ፱ ፣ ፴፬ ማር ፡ ፫ ፣ ፳፪ ፡ ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፲፭ ።
፳፬ ፈሪሳውያን ግን ሰምተው ታምራት ይደረጋል ሰው ይሰበሰባል ወንጌል ትሰፋለች ኦሪት ትጠፋለች ብለው የንጉሥን ጭፍራ በንጉሥ ቀላጤ እንዲያስወጡት ካለቃቸው ከብዔል ዜቡል ተጨዋውቶ ያወጣቸዋል እንጂ ያለዚያ አያወጣቸውም አሉ ።
፳፭ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ሕሊናሆሙ ይቤሎሙ ኩላ መንግሥት እንተ ትትናፈቅ በበይናቲሃ ትማስን ። ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፲፯ ።
፳፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነገራቸውን ዐውቆባቸው እርስ በርሷ የምትለያይ መንግሥት ሁሉ ትጠፋለች አላቸው ንጉሡ እንዝመት ሲል ሠራዊቱ አንዘምትም ቢሉ ።

ወዙላ ሀገር ።
እርስ በርሷም የምትለያይ ሀገር አትጸናም ፤ ትፈ ታለች ኹሙ አንገብር ሲል ሕዝቡ አንገብርም ቢሉ ። ወእመኒ ቤት እንተ ትትናፈቅ በበይናቲሃ ኢትቀውም እርስ በርሷም የምትለያይ ቤትም አትጸናም ትፈ ርሳለች ። ባለቤቱ ደጋ እንሁን ሲል ቤተሰቡ ቆላ እንሁን ቢሉ ።

፳፮ ወእመሰ ሰይጣን ያወፅእ ሰይጣነ ተናፈቀኬ በበናይቲሁ ፤ ሰይጣንም ሰይጣንን የሚያወጣው ከሆነ እርስ በርሱ ተለያየ ።

፳፮ እፎ እንከ ትቀውም መንግሥቱ ።
መንግሥቱስ እንደምን ትጸናለች ፤ ሐተታ ምን መንግሥት አለው ቢሉ ዮሐንስ ወልደ ማሪት እን ዳየው ፤ አባቱ መምለኬ ጣዖት ነበረ ለጣዖት ሊሰዋ ሲሄድ አስከትሎት ሄደ ሠውቶ እስኪወጣ ዕንቅ ልፍ መጣበት ተኛ በሕልሙ ዲያብሎስ በአምሳለ ንጉሥ ዘውዱን ደፍቶ ከዙፋኑ ሁኖ ኃያላኑን በቀኝ በግራ በፊት በኋላ አቁሞ ያየዋል ከዳሪ መጥቶ ንገ ሩልኝ ይላል ይነግሩለታል ይገባል ወዴት ነበርህ ይለዋል ከሀገር ፤ ምን አድርገህ መጣህ ይለዋል ባልና ሚስቱን ነገር ካለቶ በኋላ አጣልቼ አለያይቼ መጣሁ ይለዋል በስንት ቀንህ ነው አለው ባ ፲፭ ቀኔ ነው አለው ። አስወጣው አለው ። ሌላው መጥቶ ንገሩልኝ አለ ይነግሩለታል ገባ በሉት ይላል ይገባል ወዴት ነበርህ አለው ከምድር ድምበር ፤ ምን አድርገህ መጣህ ይለዋል ወንድማማች አጣ ልቼ አጋድዬ መጣሁ ይለዋል በስንት ቀንህነው ፰ ቀኔ ነው አለው ይለዋል አስወጣው ይላል ይወጣል

ደግሞ መጥቶ ንገሩልኝ ይላል ይነግሩለታል ይገባል ወዴት ነበርህ ይለዋል ከባሕር ፤ ምን አድ ርገህ መጣህ ይለዋል ነፋስ አምጽቼ ማዕበል ሞገድ አስነሥቼ መርከቡን ገልብጬ ሰውን አስጥሜ መጣሁ ይለዋል ስንት ቀንህ ነው ፴ ቀኔ ነው አለ አስወጣው አለ ። ደግሞ ሌላው መጥቶ ንገሩልኝ ይላል ይነግሩለታል ገባ በሉት ይላል ይገባል ወዴት ነበርህ ይለዋል ከገዳም ምን አድርገህ መጣህ ይለ ዋል ፵ ዘመን የዘጋውን መነኮሴ እስቼ ዓለማዊ ሥራ አሠርቼው መጣሁ አለው በስንት ቀንህ አለው በዘመኑ ልክ ተዋግቼ አለው አንተንስ ሊያነግሡህ ይገባል ብሎ ከዙፋኑ ወርዶ ዘውዱን ደፍቶ ሲያነ ግሠው አየ ። ሲነቃ የመነኮሳት መከራቸው የጸና ክብራቸው እንጂ ቢበዛ ነው ብሎ አምኑዋል ተጠ ምቋል መንኩሷል ።

፳፯ ወእመሰ አነ በብዔል ዜቡል አወፅእሙ ለአጋንንት ውሉድክሙ በምንት ያወፅእዎሙ ፤

፳፯ እኔ አጋንንትን በብዔል ዜቡል የማወጣ ቸው ከሆነ ልጆቻችሁ ሐዋርያት በማን ስም ያወጧ ቸዋል በኔ ስም አይደለምን ወበእንተዝ እሙንቱ ፈታሕተ ይከውኑክሙ ።
ስለዚህ ነገር ማለት እናንተ በብዔል ዜቡል ያወ ጻል ስላላችሁኝ ሐዋርያት በኔ ስም የሚያወጣቸው ስለሆነ እነሱ መፈራረጃ ይሆኑባችኋል ።

፳፰ ወእመሰ አነ በመንፈሰ እግዚአብሔር አወ ፅእሙ ለአጋንንት የጊኬ በጽሐት ላዕሌክሙ መን ግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፰ እናንተ አጋንንትን በብዔል ዜቡል ያወ ጣቸዋል የምትሉኝ ከሆነ እኔ ግን አጋንንትን በመ ንፈሰ እግዚአብሔር የማወጣቸው ከሆነ ሥልጣነ እግዚአብሔር ልታጠፋችሁ ተቃጥታባችኋለች አን ድም እናንተ በመንፈሰ እግዚአብሔር ያወጣቸዋል ካላችሁኝ እኔም በመንፈሰ እግዚአብሔር የማወጣ ቸው ከሆነ መንግሥተ እግዚአብሔር ልጅነት ልት ሰጣችሁ ቀርባለች ።

፳፱ ወአልቦ ዘይክል መኑሂ በዊአ ቤተ ኃያል ወበርብሮ ንዋዮ ፤

፳፱ ካርበኛ ቤት ገብቶ ገንዘቡን መዝረፍ የሚ ቻለው የለም ።
እመ ኢተደመ ዓሚሮቶ ለኃያል
አስቀድሞ እጁን ካልያዘው ወእምዝ ይበረብር ቤቶ እጁን ከያዘ በኋላ ገንዘቡን ይወስዳል እንደዚህም ሁሉ ሰይጣንን በሮቱ አርእስተ ኃጣውእ ድል ነሥቼ ዋለሁና አወጣዋለሁ እንጂ ያለዚያ አላወጣውም።

፴ ዘኢኮነ ምስሌየ ፅድውየ ውእቱ
፴ በቦታ በቅዳሴ ከኔ ጋራ አንድ ያይደለ ዲያ ብሎስ ባለጋራዬ ነው ፤
ወዘኢይትጋባእ ምስሌየ ይዘርወኒ ።
በቦታ በቅዳሴ ከኔ ጋራ አንድ ያይደለ ዲያብሎስ በምእመናን እንዳላድርባቸው ያደርገኛል ።
የምእመናንን ዝርወት አንድ አድርጎ ይዘርወኒ አለ። አንድም ዘኢኮነ ምስሌየ ፤ በሃይማኖት በጉባኤ ከኔ ጋራ አንድ ያይደለ ይሁዳ ባለጋራዬ ነው ። ወዘ ኢይትጋባእ ፤ በሃይማኖት በጉባኤ ከኔ ጋራ አንድ ያይደለ ይሁዳ ፤ በመእመናን ፤ አንድም በሱ እንዳ ላድርበት ያደርገኛል ።

፴፩ ወበእንተዝ እብለክሙ ኵሉ ኃጢአት ወጽ ርፈት ይትኃደግ ለሰብእ ። ማር ፫ ፡ ፳፰ ፡ ሉቃ ፡ ፲፪፡፲
፴፩ ስለዚህ ሰውን የሰደበ ሁሉ ኃጢአቱ ይሰ ረይለታል ብዬ እነግራችኋለሁ ።
ወዘሰ ጸረፈ ላዕለ መንፈስ ቅዱስ ኢይትኃደግ ሎቱ መንፈስ ቅዱስን የሰደበ ግን ማለት ሕጹጽ ያለ ኃጢ አቱ አይሰረይለትም ።

፴፪ ወዘሰ ነበበ ቃለ ላዕለ ወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ይትኃደግ ሎቱ ።

፴፪ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስን ግን ዕሩቅ ብእሲ ያለ ይሰረይለታል ።

ወዘሰ ነበበ ላዕለ መንፈስ ቅዱስ ኢይትኀደግ ሎቱ መንፈስ ቅዱስን ሕጹጽ ያለ ግን ኃጢአቱ አይሰረ ይለትም ፣ ይህን ማለቱ ይገባዋል ብሎ አይደለም ለወልድ ምክንያት አለው ሥጋ ለብሷል ። ለመንፈስ ቅዱስ ግን ምክንያት የለውምና፡ከቲዘጋ ቤቱ ከተ ዳፈነ እሳቱ እንዲሉ እንድም አብ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ካመሰከረለት ዕሩቅ ብእሲ ያለ ኃጢአቱ ይሰረይ ለታል ።

አብ ዝንቱ ውእቱ ብሎ ከመሰከረ በኋላ መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ከመሰከረለት በኋላ ግን ዕሩቅ ብእሲ ያለ አይሰረይለትም ። እንድም ሕዝባዊን የሰደበ ኃጢአቱ ይሰረይለታል ። ኤጲስ ቆጶሱን የሰደበ ግን ኃጢአቱ አይሰረይለትም ።

እንድም ሥጋዊ ተዘምዶን ያፈረሰ ኃጢአቱ ይሰረይለታል መንፈሳዊ ተዘምዶን ያፈረሰ ግን ኃጢአቱ አይሰረይለትም ኃጢአት ሥጋውያት ይሰ ረያ በጾም ወበጸሎት ፣ ኃጢአትሰ መንፈሳውያት ኢይሰረያ በጾም ወበጸሎት ዘእንበለ ዳዕሙ በምን ዙስና እንዲል ፤ እንዲህ ማለት ንስሐ ከገባ አይሰ ረይለትም ማለት አይደለም ከቀኖና ቀኖናውን ከፍዳ ፍዳውን ማብለጥ ነው ።

ኢበዝ ዓለም ።
በዚህም ዓለም ሁኖ ።
ወኢበዘይመጽእ ዓለም ።
በሚመጣውም ዓለም ሁኖ አይሰረይለትም ። በወ ዲህስ ይሁን በወዲያማ ምን ንስሐ አለ አልቦቱ ለሰብእ ንስሐ እምድኅረ ሞት ይል የለም ቢሉ ፣ ኃጢአቱን ሰቂሉ ነግሮት ቀኖና ተቀብሎ ጀምሮት ቢሞት ሳይጀምረውም ቢሞት መካነ ንስሐ አለ ከዚያ አድርሶ ይወጣልና እንዲህ አለ ። እንድም ወትጼሎ አበሳነ ምስለ ኵሉ ዘገበርነ እንዲል ያለ ማነውም ያጠፋነውም በፍትሐ እግዚአብሔር ይመ ረመራል ያለማነው በዝቶ ያጠፋነው ያነሰ እንደሆነ እንገባለን ያለማ ነው አንሶ ያጠፋነው የበዛ እንደ ሆነ ግን አንገባምና ።

፴፫ እመ አኮ ግበሩ ዕፀ ሠናየ ወፍሬሁኒ ሠናይ

፴፫ እመ አኮ ዋዌ ነው መልካም ዛፍ አድርጉ ፍሬውም መልካም ማለት የአብርሃም ልጆች ነን በሉ የአብርሃምን ሥራ ሥሩ ። እንድም ተነሣሒያን ነን በሉ እኔም ተራድቼ የተነሳ ሕያንን ሥራ ሳሠ ራችሁ ።

ወእመ አኮ ግበሩ ዕፀ እኩየ ወፍሬሁኒ እኩይ ።

ወይም ከፉ ዛፍ አድርጉ ፍሬውም ክፉ ማለት የሰይጣን ልጆች ነን በሉ የሰይጣንን ሥራ ሥሩ እሱስ አያዛቸውም እንዳይተውት ያውቃልና ፤ እን ድም ፣ በአፋቸው እንወድሃለን ይሉታል በልቡ ናቸው ይጸሉታል በአፋችሁም በልቡናችሁም ውደ ዱኝ ፤ ያለዚያ ግን በአፋችሁም በልቡናችሁም ጥሉኝ ፣ እንድም ሥራውን የአምላክ ሥራ ነው ይላሉ እሱን ዕሩቅ ብእሲ ይሉታል ሥራየን የአ ምላክ ሥራ ነው በሉ እኔንም አምላክ ነው በሉ ያለ ዚያ ግን እኔንም ዕሩቅ ብእሲ በሉ ሥራዬንም የዕ ሩቅ ብእሲ ሥራ ነው በሉ ። እንድም ታምራቱን ይወዳሉ ትምርቱን ይጸላሉ በእንተ ሠናይሰ ግብ ርከ ኢንዌግረከ አላ በበይነ ፅርፈትከ እንዲል ታም ራቱንም ትምርቱንም ውደዱ ያለዚያ ግን ትምር ቱንም ታምራቱንም ጽሉ ። እስመ እምፍሬሁ ይት ዓወቅ ዕፅ ።

ዛፍ በፍሬው ይታወቃልና ።

በእንተ ጽልሁት ዘፈረሳውያን

፴፬ ኦ ትውልደ ዓራዊት ምድር በአይቴ ትክሉ ሠናየ ተናግሮ እንዘ እኩያን አንትሙ ።

፴፬ እናንተ የእባብ ልጆች ክፉዎች ስትሆኑ መልካም መናገር እንደምን ይቻላችኋል በልቡናችሁ ዕሩቅ ብእሲ የምትሉ ስትሆኑ እኔን የባሕርይ አም ላክ ማለት እንደምን ይቻላችኋል ።

እስመ እምተረፈ ልብ ይነብብ አፍ ፤
ልብ ያሰበውን አፍ ይናገራልና ።

፴፭ ኄር ብእሲ እምሠናይ መዝገበ ልቡ ያወ ፅእ ሰሠናይት ሉቃ ፣ ፮ ፣ ፵፭ ።

፴፭ በጐ ሰው በጐ ነገር ከሚያስብበት ልቡ ናው በጐ ነገርን አውጥቶ ይናገራል ።

ወእኩይሰ ብእሲ እምእኩይ መዝገበ ዓመጻሁ ያወ ፅእ ለእኪት ክፉ ሰው ግን ክፉ ነገር ከሚያስብበት ልቡናው ክፉ ነገርን አውጥቶ ይናገራል ።

፴፮ እንሰ እብለክሙ ኵሉ ሰብእ ዘይነብብ ንባበ ጽሩዓ ያገብኡ ሎቱ በእንቲአሁ ቃለ በዕለተ ደይን ።

፴፮ እኔ ግን ተርታ ነገርን በሚናገር ሰው ሁሉ በፍርድ ቀን ፍዳውን ያመጡበታል ብየ እነ ግራችኋለሁ ። ታሪክ እንዳንድ ባሕታዊ ከሚረዳ በት ገዳም ወጥቶ በተባሕትዎ ይኖራል ከማኅበሩ አንዱ ሊጠይቀው ሄደ እነ እገሌ እንደምን ሁነዋል ብሎ ጠየቀው የበቁ ሁነዋል አለው ። እንድ ሕ ሙየ ግብር ነበር እገሌስ አለው እሱስ ከሁሉ በልጧል አለው አፍ ፣ እስካሁን የነገርኸኝ ሁሉ ሐሰት ነው ለልማዱ ጌታ በአምሳለ ንጉሥ ሲገኝለት እሱም የብ ርሃን ካባ ለብሶ በቀኝ ሲቆም የሚያየው ነው ። እን ደወትሮ የብርሃን ካባ ለብሶ በቀኝ እቆማለሁ ብሎ ሲሄድ ምስለኔየ ወሬኛየ መንግሥት ተበሳልጬ መጣሀ ንሳ ያዘው ሲል እሻላሁ ብሎ ሲሄድ ካባው ተገፎ ሲቀር አየ እንዲህ ብየ በተናገርሁት ፈጣሪየ ፈርዶብኝ ነውን ብሎ ንስሐ ቢገባ በሰባት ዓመቱ ጌታ እንደ ጥንቱ በአምሳለ ንጉሥ ሲገኝ እሱም የብር ሃን ካባ ለብሶ በቀኝ ሲቆም አይቷል ።

፴፮ እስመ እምቃልከ ትጸድቅ

፴፯ ከነጋገርህ የተነሣ ትከብራለህና ወእምቃልከ ትትኴነን

ከነጋገርህ የተነሣ ይፈረድብሃልና ፡ ኢዮብ ፦ ጠንከ እምቃለ አፉከ ፤ ሰሎሞን ሕይወት ወሞት ውስተ እደ ልሳን ፡ ሲራክ ኃሳርከሂ ወክብርከ እምቃለ አፉከ ያሉትን ቃል ሰውጦ አነበበው

በእንተ ትእምርተ ዮናስ ።

፴፰ ወአሜሃ መጽኡ ሰብአ እምጸሐፍት ወእምፈሪሳውያን ወይቤልዎ ሊቅ ንፈቅድ እምኔከ ትእምርተ ንርአይ ።

፴፰ ያን ጊዜ ከጸሐፍት ከፈሪሳውያን ወገን የሚሆኑ ሰዎች መጥተው መምር ምልክት ልታሳየን እንወዳለን አሉት ። ሐተታ ፡ እሉ ሰው ሆኖ በቋንቋቸው በዕብራይስጥ ቢያስተምራቸው እንደ ሙሴ ባሕር ከፍለህ ጠላት ገድለህ ደመና ጋርደህ መና አውርደህ እንደ ኢያሱ በረድ አዝንመህ ፀሐይ አቁመህ እንደጌዴዎን ፀምር ዘርግተህ ጠል አውርደህ እንደ ኤልያስ ሰማይ ለጉመህ እሳት አዝንመህ ልታሳየን እንወዳለን አሉት ።

፴፱ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ትውልድ ዕሉት ወዓማፂት ወዘማዊት ትእምርተ ተኃሥሥ ፡ ማቴ ፲፮ ፡ ፬ ። ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፳፱ ፡ ፩ ፡ ቆሮ ፩ ፡ ፳፪ ፡

፴፱ ሴሰኛ አሉተኛ ትውልድ ቤተ አይሁድ ምልክትን ትሻለች ። ቤተ አይሁድን ዘማ አላቸው ዘማ ነገሩ አንድ ሲሆን ዕስት ዕለት ወንድ ሊለወጥላት እንድትወድ ቤተ አይሁድም ዕለት ዕለት ትምህርት ቢለወጥላቸው ይወዳሉና ። ወትእምርትሰ ኢተውህባ ዘእንበለ ትእምርተ ዮናስ ነቢይ ፡ ምልክት ግን ዮናስ ካደረገው ምልክት በቀር ያልተደረገላት የቀረበት የማይደረግላት የማይቀር ላት የለም ። ሁሉን ስትዘነጋው ይህን አትዘነጋው ምና ኋላ በመጨረሻ ተዘከርነ ዘይቤ ቅንቱ መስሐቲ እመ ሕያው ውእቱ እመ ግልስት ዕለት እትነሣእ አዝዝ እንከ ይዕቀቡ መቃብሮ ይላሉና ።

፵ እስመ በከመ ነበረ ዮናስ ውስተ እንበሪ ሠሉስ መዋዕለ ወሠሉሰ ለያልየ ከማሁ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ይንበር ውስተ ልበ ምድር ሠሉሰ መዋዕለ ወሠሉሰ ለያልየ ። ዮሐ ፡ ፪ ፡ ፩ ።

፵ ዮናስ በከርሠ አንበሪ ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት እንደ ኖረ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶ ስም ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት በከርሠ መቃብር ይኖር ዘንድ አለውና ።

፵፩ ሰብአ ነነዌ ይትነሥኡ እመ ዕለተ ደይን ምስለ ዛ ትውልድ ። ዮሐ ፡ ፫ ፡ ፭ ።

፵፩ የነነዌ ሰዎች በፍርድ ቀን በቤተ አይሁድ በጸላትነት ይነሡባታል ።

ወይትፋትሕዋ ።

ይከራከሯታል ።

ወያስተሐፍርዋ ።

ምላሽ ያሳጧታል ።

እስመ ነስሑ በስብከተ ዮናስ ፤

ዮናስ ቢያስተምር አምነዋልና ።

ወናሁ ዘየዓቢ እምዮናስ ሀሎ ዝየ ።

ከዮናስ የሚበልጥ እነሆ ከዚህ አለ ማለት ቤተ አይሁድ ግን እግዚእ የናስ ክርስቶስ ቢያስተምራቸው አናምንም ብለዋልና ።

ጌታ ዮናስን እሱስኑ ሠሉሰ ዕለት ትትገ ፈታዕ ነነዌ ሀገር ሀባይ እያልህ አስተምር አለው ኢይሆንም አንተ መሐሪ ነህ እኔ እንዲህ ብየ አስተምሬ ብትምራቸው ነቢየ ሐሰት እባል የለም አለው ሁለተኛ ሂድ አላልሁምን አለው ዮናሰ ማለት ርግብ የዋህ ማለት ነውና ይህ ሁሉ የሚዘበዝበኝ ከፊቱ ቢያገኘኝ አይደለም ብሎ ውቱንቱአ እምገጸ እግዚአብሔር ወሖረ ተርሴስ ይላል ተርሴስ ወደሚባል ሀገር ሲሄድ ኢዮጴ ከሚ ባል ባሕር ደረሰ ወረከበ ሐመረ ዘይነግድ ብሔረ ተር ሴስ ይላል ፤ በሀገራቸው ከየብሱ ባሕሩ ይበዛልና ነጋድያን በመርከብ ተጭነው ወደ ተርሴስ ሲሄዱ አገኘ ወተአሰበ ሐመረ በንዋይ ይላል ገዘቶ ባን ድነት ተጭኖ ሂደ ምንት ተግባርከ ወአይ ብሔርከ ወአይ ሕዝብከ አሉት አይ ብሔርከ ላሉት እይመ ልበላቸውም አይ ሕዝብከ ላሉት ዕብራዊ ነኝ ። ወም ንት ተግባርከ ላሉት የማመልከው ሰማይን ምድርን የብስን ባሕርን የፈጠረ እግዚአብሔር ነው አላቸው ከጥልቅ ባሕር ሲደርሱ ነፋስ መጣ ማዕበል ሞገድ ቀነሣ መርከባቸው ሊሰጥም ሆነ ወገደፉ ማህሎሙ ይላል ፡ ገንዘባቸውን እያወጡ ይጥሉ ጀመር እንደ ማሚረት ፤ ወንሕረ ዮናስ ውስተ ከርሠ ሐመር ይላል ሊቀ ሐመር ከሚተኛበት ገብቶ ተኝቷል እንዲ ሄዶ ተንሥኡ ወጸውእ ስመ አምላክከ አለው እግዚአ ብሔርን አመልክተሁ ብሏቸው ነበርና ነገሩን አይቶ ይህ የመጣ በኔ ምክንያት ነው እኔን ካልጣላችሁኝ ጸጥ አይልላችሁም አላቸው እባቸውም ሰውስ ብን ጥል እዳ ይሆንብናል ዕጣ እንጣጣል ብለው ዕጣ ቢያወጡ ወወረደ ዕፃ ላእለ ዮናስ እንዲል በዮናስ ዕጣ ወጣበት ወረደ ማለቱ ግን ከራሳቸው አድርገው ያወጡታልና ፈቃድህስ ከሆነ ዕዳ አይሆንብንም ብለው አውጥተው ጣሉት የታዘዘ አንበሪ ተቀብሎ ዋጠው ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት አሳድሮ በአ ንጻረ ነነዌ አውጥቶ ጣለው ከዚህ በኋላ ወሰበከ ምህዋረ አሐቲ ዕለት ይላል ያንድ ቀን መንገድ ሲቀር ያኑ አስተማረ ።

ያገሩ ንጉሥም ይኸን ነገር በሰማ ጊዜ ከዙ ፋኑ ወርዶ ማቅ ለብሶ አመድ ነስንሶ ንስሐ ገባ የወንድ ሙሽራ ከጫጉላው የሴት ሙሽራ ከመጋረ

ሉውንም እንጂ ባወቀ አስመስሏል ምሥጢሩ እንደ ምን ነው ቢሉ ለአዳም ለሔዋን ለሕፃናቱ ለሥጋ ለነፍሲ ለደመ ነፍስ እንደ ካሠለማጠየቅ ፤ አንድም ፫ቱ እድዋኒሁ ለሰብእ እንዲል ኃጢአትን ምክን ፍዳን እንዳጠፋ ለማጠየቅ ። አንድም በዕውነትም እንደሞተ ለማጠየቅ ፈላስፎች ነፍሉ ከሥጋው ከይለይ ደም ከልቡ ወድቆ እስትንፋሱን ይከለክ ለዋል ብለው ከሞተበት ሰዓት ጀምረው እስከ ቀተ ዘት ሰዓት ድረስ አቆይተው ነው ቀሚቀብሩ የሚ ድንም አለ የሚሞትም አለ ረዋና ተነሥቶ ቢሆን አልሞተም ባሉ ነበርና በውቅት እንደሞተ ለማጠ የቅ ያውስ ቢሆን ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት ወዴት ይገኛል ቢሉ መዓልተ ዓርብ ሌሊት ዓርብን ሰቦ ሌሊተ እሑድ መዓልተ እሑድን ሰቦ አንድም ከርሠ ሐዋርያቶን መቃብር ብሎ አንድም ዓርብ ከነግህ እስከ ቀትር ብርሃን ከቀትር እስከ ሰዓት ጨለማ ሁኑዋል ፤ በሠርክ ብርሃን ሁኑዋል ።

ወፍና ሠርክ ይበርህ ብርሃን እንዲል ይህ ሁለት መዓልት አንድ ሌሊት የቅዳሚ ሌሊትና መዓልቱ የእሑድ ሌሊት ይህ ነው ።

፵፪ ንግሥተ ዓዜብ ትትነሣእ ሎሙ ዕለተ ደይን ምስለ ዛ ትውልድ ። ፩ ፡ ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፪ ፡ ሕጹ ፡ ፱ ፡ ፩።

፵፪ ንግሥተ ዓዜብ በፍርድ ቀን በቤተ አይሁድ ትነሣባታለች ወትትፋታሕ ።
ትከራከራታለች ።
ወታስተሐፍራ ፤
ምላሽ ታሳጣታለች ።

እስመ መጽአት እምአጽናፈ ምድር ትስማዕ ጥበቢሁ ለሰሎሞን ።

የሰሎሞንን ጥበብ ልትሰማ ከጽንፈ ምድር መጥታለችና ወንጌላዊ በወዲያ ሁና ይጽፋልና የኛን አገር ጽንፈ ምድር አለው ።
ወናሁ ዘየዓቢ እምሰሎሞን ሀሎ ዝየ ።
ከሰሎሞን የሚበልጥ ከዚህ አለ ማለት ቤተ አይሁድ ግን እግዚአ ሰሎሞን ክርስቶስ ቢያስተምራቸው አናምንም ብለዋልና ።

ታሪክ የሰሎሞንን ጥበብ እያመጣ የሚነግራት ታምሪን የሚባል ነጋዴ ወዳጅ ነበራት ሂጂ ልረዳው ብላ መቶ ሃያ መክሊት ወርቅ ተንከራ በኢትዮጵያ ይለዋል ሉል በወዲያ የማይገኝ በኛ አገር የሚገኝ ዝባድ ገጸ በረከት ይዛ ሄደች ስትሄ ድም እያዘራች ሄዳለች ስትመለስ ስንቅ ሊሆናት አገር እንዳትዘርፍ ከእግሯ እንደ ምዳቋ ቀንድም እንደ አህያ ሰኰናም ቢሉ ነበረበት ከደባባይ ስት ደርስ ብላቴና አይቶ ገብቶ ንጉሥ በዘመንህ የማ ይመጣ የለም እንዲህ ያለች ሴት መጥታለች አለው ግቢ በላት አለው ስትገባ ከደጁ ወድቆ የሚኖር

ግንድ ነበር ብትራመደው ወልቆ ወደቀላት እሱዋን አይቶ በዓይን መዓት አየው ።

ንጉሥም ባላይ አልነገርሁህም ጠይቀህ ቅጣኝ አለው ፤ ቢጠይቃት እውነቱ ነው ነበረብኝ ነገር ግን ከደጅህ የወደቀ ገበሬ ታምራት ዕፀ አለ እሱ ፈወሰኝ እንጂ አለችው እሱ እንደ ብር እሱ አንድ ብር ሽበውበታል ከሱ በኋላ ሃያ ስምንት ነገሥታት ነግሠዋል ሃያ ስምንት ብር ይሸቡበታል ፤ ወርቁን ለይሁዳ ሰጥተው በዕንጨቱ ጌታን ሰቅለውታል።

ሐፍኖ ወይን ዘእምንጉሥያን ይትዓዘዝ ወበኀልኅኦ ይተክል ከኔ መድኃኒተየ እንዲል ። ብዙ አን ቀትልሽ ጠይቀዋለች ፤ ወአልቦ ዘኢፈከረ ላቲ ወዘ ተሰወረ እምኔሁ ፤ ተሰውሮት የቀረ ያልተረጐመላት የለም ።

እሱም ከዚያ ድረስ መጥታ ሥርዓተ መንግሥት እናሳያት እንጂ ብሎ እሱዋ ሁሉን ከምታይ በት እሷ ከማትታይበት ቦታ አኑሮ ሥርዓተ መንግሥት አሳያት ። ከዚህ በኋላ በ፯ ቦይኝ አላት የሀገራችን መንግሥት በድንግልና ነው አይሆንም አለችው እንኪያስ አንችም የኔን ገንዘብ አልነካም ብለሽ ማይ አላት ማለች ።

የሚያጸግ ምግብ ሰጥቶ የምትጠጣውን ነጣት ሰሎሞን ቢተኛ እንደ አንበሳ ዓይኑን ያፈጣል ሲነቃ ይጨፍናል ተኝቶ ሳለ ያየኛል ብላ ዝም ብላለች ነቅቶ ሳለ አሁንስ አያየኝም ተኝቷል ብላ በጥበብ ያገባው ውኃ አለ ቀድታ ልትጠጣ መንቀል ይዛ ቀረበች እጅዋን ያዛት አንች ከኔ ገንዘብ ላትነኪ አኔም ያንቺን ገንዘብ ላልነካ መሐላ አልነበረንም አላት ይህማ ውኃ አይደለም አለችው ከውኃ የበለጠ አለ አላት ያሁኑን ተወኝ ፈቃድህን ትፈጽማለህ አለችው ተገናኙ ምኒልክ ተፀነሰ ወጥታ ስትሄድ ዓምደ ብርሃን ተከትሏት ቢሄድ አይቶ መንግሥት ወደ ኢትዮጵያ ሄደች ብሎ ትንቢት ተናግሯል ።

ይህ ሁሉ ምሳሌ ነው ፤ ንግሥተ ዓዜብ የዚህ ዓለም ሰሎሞን የጌታ ፻፳ መክሊተ ወርቅ የመቶ ሃያ ቤተሰብ መቶ ሃያ መክሊተ ወርቅ የተገኘ ከሱዋ ነው መቶ ሃያ ቤተሰብ የተገኙ ከዚህ ዓለም ነውና ፤ ዕንቍ የሃይማኖት ዝባድ የተዋልጦተ ገድል ምሳሌ ፤

በእንተ መናፍስት ርኩሳን ።

፵፫ ወእምከመ ወፅአ መንፈስ ርኩስ እምሰብእ የዓውድ በድወ ኀበ አልቦ ማይ ፤ ሉቃ ፡ ፲፩፥፳፬።

፵፫ መንፈስ ርኩስ ሰይጣን በጾበል በጸሎት ከሰው ከተለየ በኋላ ወደሌለበት ወደ የብስ ይሄዳል ፤ እሱስ ወኃ ወዳለበት ይሄዳል ገላቸውን ሲታጠቡ ልብሳቸውን ሲያጥቡ አድርባቸዋለሁ ብሎ መንፈስ ቅዱስ ወደ የብስ የሚወስደው ስለሆነ እንዲህ አለ እንጂ አንድም ወደ ኢጥሙቃን ይሄዳል እሱስ የሚሄድ ወደ ጥሙቃን ነው መንፈስ ቅዱስ ግን

እሱዋንስ አይደለቅፋትም ይህም ሊታወቅ ይእቲ ተግቢ እምሁራፊል በንጽሕ ይላቃል ብሎ ከአክብሮተ አብ ወእምአክብሮተ እግዚአብሔር እንዲበልጥ ለማጠየቅ ፡ እንደም ከጉባኤ መካከል መነሣት ይገባል ብለው አብነት እንዳያደርጉበት ።

፵፱ ወአመረ እደሁ ኀበ አርዳኢሁ ።

፵፱ እጁን ወደ ደቀ መዛሙርቱ አመለከተ እጅ ሲነገር ያግዛልና ።
ወይቤሎሙ ናሁ እምየ ወአኀውየ ።
እናቴም ወንድሞቼም እነሆ በጉባዔ ያሉ ሕዝብ ናቸው አላቸው ፤

፶ እስመ ዙሉ ዘይገብር ፈቃዶ ለአቡየ ዘበሰማያት ውእቱ እኁየ ወእኅትየ ወእምየኒ ውእቱ ።

፶ የሰማይ አባቴን ፈቃድ የሚፈጽም ሁሉ ወንድሜም እኅቴም እናቴም እሱ ነውና ።

ምዕራፍ ፲፫ ።

፩ ወበይእቲ ዕለት ወፂኦ እግዚእ ኢየሱስ እምቤት ነበረ መንገለ ሐይቀ ባሕር ።

፩ በዚያች ቀን ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ከቤት ወጥቶ ከወደቡ ተቀመጠ ።

፪ ወተጋብኡ ኀቤሁ ሰብእ ብዙኃን እስከ ሶበ የዓርግ ውስተ ሐመር ወይነብር ማር ፡ ፪ ፡ ፩ ።

፪ ከመርከብ ወጥቶ እስኪቀመጥ ድረስ ብዙ ሰዎች ወደሱ ተሰበሰቡ ። ሐተታ ሰው ሲሰፋ ከመርከብ ከተራራ ሆኖ ማስተማር ልማድ ነው ። መምህር ከፍ ካለ ቦታ ሰማዕያን ዝቅ ካለ ቦታ ሲሆኑ ትምህርት ለሰማዕያን ይረዳልና ። ወይረድ ከመ ጠል ነቢብየ እንዲል ።
ወዙሉ ሰብእ ውስተ ሐይቅ ይቀውሙ ።
ሕዝቡ ሁሉ ከወደቡ ተቀምጠው ነበር ወትቀውም ንግሥት በየማንከ እንዲል ፤ ባሕር የመለኮት ፥ ሐመር የትስብእት ምሳሌ ፤ መለኮቱን ትስብእቱን ከማመን በአፍአ እንደ ነበሩ ለማጠየቅ ውስተ ሐይቅ ይቀውሙ አለ ። እንደም ባሕር የትስብእት ሐመር የመለኮት ፤ መለኮቱን ትስብእቱን ከማመን በአፍአ እንደነበሩ ለማጠየቅ ውስተ ሐይቅ ይቀውሙ አለ እንደም ባሕር የጥምቀት ሐመር የቤተ ክርስቲያን ምሳሌ ከጥምቀት ከቤተ ክርስቲያን አፍአ እንደ ነበሩ ለማጠየቅ ውስተ ሐይቅ ይቀውሙ አለ ።

፫ ወነገሮሙ ብዙኃ በምሳሌ እንዘ ይብል ።

፫ ሉቃ ፫፥ ፰ እንዲህ ብሎ በምሳሌ ብዙ ነገራቸው ። እንደም ብዙኃ ምሳሌ ብዙ ምሳሌ ነገራቸው እንደም ወመሰለ ሎሙ ብዙኃ ምሳሌ ብዙ ምሳሌ መሰለላቸው ሐተታ ምሳሌውም በሆነ ነው እንጂ ባልሆነ ምሳሌ አይደለም ለገበሬ በዘር ለሴት በርሾ ለነጋዴ በዕንቍ ለዓሣ ወጋሪ በዘረ መትራን መስሎ አስተምሯል ። በምሳሌ ማስተማሩ ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ትንቢት አከሥት በምሳሌ አፉየ ወእነግር እምሳለ ዘእምትካት ተብሎ ተነግሯል ፤ ምሳሌም ቀድሞ አባቶቹ ነቢያት በምሳሌ እንበለ ምሳሌ አስተምረዋል እሱም በምሳሌ ይኸን እንበለ ምሳሌ ብዙዓንን አስተምሯልና ትንቢቱን ዐውቆ አናግሯል ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ አይሰወርሏል ምሥጢሩ እንደ ምንው ቢሉ ላዋቂ ለመግለጽ ካላዋቂ ለመሠወር ። እንደም ደቀ መዝሙር ሁል ጊዜ ተርታ ነገር ቢነግሩት አይነቃምና ለማንቃት ።
ናሁ ወፅአ ዘራኢ ከመ ይዝራዕ ።
ገበሬ ሊዘራ መጣ ዘሩም የተበጠረ የተንጠረጠረ ነው

፬ ወእንዘ ይዘርዕ ቦ ዘወድቀ ውስተ ፍኖት ።

፬ ጫብጦ ሲዘራ ከመንገድ የወደቀ ዘር አለ ።
ወመጽኡ አዕዋፈ ሰማይ ወበልዕዎ ።
አዕዋፍ መጥተው የለቀሙት ።

፭ ወቦ ዘወድቀ ዲበ ኰኲሕ ኀበ አልቦ መሬት ብዙኀ ወወእቱ ጊዜ ሠረጸ ።

፭ ብዙ መሬት ከሌለው ከጭንጫ ላይ የወደቀ ፈጥኖ የበቀለ አለ ።
እስመ አልቦ ዕመቅ ለመሬቱ ።
ለመሬቱ ጥልቅነት የለውምና ፤

፮ ወሶበ ሰረቀ ፀሐይ መጽለወ ወየብሰ ፤

፮ ፀሐይ በወጣ ጊዜ ጠውልጎ ደረቀ ።
እስመ አልቦ ዕመቅ ለመሬቱ
ለመሬቱ ጥልቅነት የለውምና ፤

፯ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ።

፯ ከሾህ መካከል የወደቀ ዘር አለ ።
ወበቈሉ ሦክ ጠበቆ ወሐነቆ ።
በበቀለ ጊዜ እንዳያድግ እሾህ አንቆ አስቀረው ።

፰ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይ ።

፰ ከበጐ ምድር የወደቀ ዘር አለ ።
ወወፅአ ፍሬ ።
ፍሬ ያቀረጸ
ቦ ዘ፻ ።
መቶ ቅንጣት ።
ወቦ ዘ፷ ።
ስሳ ቅንጣት ።
ወቦ ዘ፴ ።
፴ ቅንጣት ያቀረጸ አለ ። እንደም ናሁ ወፅአ ብለህ መልበ ጌታ ቢያስተምር በው ሆነ ፀአተ ይሰሚ ሥጋዌሁ እንዲል ከዚህ ፀአተ አለ ሐዋርያው በኢተ ይለዋል ፤ ወእንዘ ይዘርዕ ፤ ሰው ሁኖ ሲያስተምር በልበ ዝንጉዓን ቋደረ ትምህርት አለ ። ወመጽኡ አዕዋፍ አጋንንት ያሳቱት አዕዋፍ አላቸው ለማሳት ይፈጥናሉና ። ኢትሕሚ ሰብአ ውስተ ቤትከ እስመ ዖፈ ሰማይ ያወፅአ ለነገርከ እንዲል

ሰሕቶም ማለቱ የበሉት ደስ እንዲያሰኝ ሲያስቱ ደስ ይላቸዋልና ወቦ ዘወድቀ ዲበ ኰኩሕ ፈጥና ፀመቶ ተረዳሁ ከሚል ስፍሐ አእምሮ ከሌለው ልቡና ያደረ ትምህርት አለ እስመ አልቦ ስፍሐ አእምሮ ማለት ጥልቅ ዕውቀት የለውምና ። ወሶበ ሠረቀ ፀሐይ መከራ በመጣበት ጊዜ ፈጥኖ የከዳ እሙ ጸሐዩ ። ስፍሐ አእምሮ የለውምና ። ወቦ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ከሐሳቦች ልቡና ያደረ ትም ትምህርት አለ ። ወዐርገ ተምር ዐውቶ ሥራ እሙ ሐሳብ ጊዜ እምነት ግብረት ያስቀሩበት ፤ ብዕል ሰፋጢት ማለት እንዳይ ብዕል ሐልዮ መንበርት ማለት ዐታ ማለት ትካዘ ዓለም ፍትወ ብእሲት ፍትወ ውሉድ ናቸው ፤ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይት በበጐ ልቡና ያደረ ትምህርት አለ ፴ ዘምአት ወቦ ፷ ወቦ ፻ ሥራውን በምስት ወገን ይመስላል በመሐይምናት በማእከላዊነት በፍጹምነት ከመሩጌው በዚያው ይመርሱታልና ፤ ባለ መቶ ባለ ስሳ ባለ ሠላሳ አለ ። እንድም ባለ መቶ ሰማዕታት ባለ ስሳ መነኰሳት ባለ ፴ በሕግ የጸኑ ሰብአ ዓለም ናቸው እንድም ሁሉም በሁሉ አሉ ብሎ ከሰማዕታት እንደ ቅዱስ ጊዮርጊስ እንደ ቂርቆስ እንደ ፋሲለደስ ያሉት ባለ መቶ ፤ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ስሳ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ሠላሳ ናቸው ። ከመነኰሳትም አቡነ ዕንጦንስ እንደ መቃርስ እንደ አቡነ ተክለ ሃይማኖት እንደ አቡነ ገብረ መንፈስ ቅዱስ ያሉት ባለ መቶ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ስሳ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ሠላሳ ናቸው ከሰብአ ዓለምም እንደ ኢዮብ እንደ አብርሃም ያሉት ባለ መቶ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ፷ ከነዚያ ዝቅ ያሉት ባለ ፴ ናቸው ። አንድም ቦ ዘወድቀ ውስተ ፍኖት ፤ ፍኖት የተባለ መንግሥተ ሰማያት ድሉት ለጻድቃን ገሃነመ እሳት ድሉት በኃጥአን እንደሆነች ተምሮ ዐውቆ ሥራ እሰራለሁ ሲል ኢጋንንት ያስቀሩበት ነው ። ወቦ ዘወድቀ ዲበ ኰኩሕ ፤ ኰኩሕ የተባለ ካልተማሩ አያውቁ ካላወቁ አይጸድቁ እን ዲሉ እማራለሁ አውቃለሁ ሲል ሳይማር ሳያውቅ የቀረ ነው ፤ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ።
ሦክ የተባለ ትሩፋት እፍአዊን ሠርቶ ትሩፋት ስው ርት የቀረችበት ነው ፤ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይት ምድር ሠናይት ያለው ሁሉንም የሠራ ነው ቦ ዘምእት ወቦ ዘስሳ ወቦ ዘሠላሳ ፤ ይህም ወሥርዓተ ፍድፋዴ ዓለማውያን እስተጋብአ ሰጉበ ሠለስቱ ክፍል እንዲል ሰማዕታትን በበጐ ልጅ መነኰሳትን በበጐ ሎሌ ሕጋውያንን በበ ጐ ባሕሪ መስሎ ይናገራል ፡፡ በጐ ልጅ አባቱ ሳለ ካባቱ ጋራ ይወጣል ይወርዳል አባቱ ከሞተ በኋላ ባባቱ ርስት ዘምቶ ይሞታል ፤ የሰማዕታት ሙደበኞች ሐዋርያት ናቸው በጐ ልጅ ካባቱ ጋራ እንዲወጣ እንዲወርድ ሐዋር ያትም ጌታ ሳለ ከጌታ ጋራ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር ሲወጡ ሲወርዱ ኑረዋል ። አባቱ ከሞተ በኋላ ባባቱ ርስት ዘምቶ እንዲሞት ጌታ ከሞተ በኋላ ወንጌልን ሲያስተምሩ በሰማዕትነት ሙተዋልና ፤ በጐ ሎሌም ጌታው ሸማ አጥበህ ማገር ቆርጠህ ና ያለው እንደሆነ ጌታዬ አይችልም ብሎ ነው እንጂ ልመጥ የሚሆን ዓሣ የሚማገርበት ልጥ ይገድ ብሄድ ይከፋልን ብሎ ልብሱን አጥቦ ዓሣውን ይዞ ማገሩን ቆርጦ ልጡን ጨምሮ ይዞ ይሄዳል ። መነኰሳትም ሚስት አግቡ ታችሁ ዐሥራት በኩራት ቀዳምያት አውጥታችሁ እንግዳ ተቀብላችሁ ሥጋውን ደሙን በሚገባ ተቀብላችሁ ኑሩ ቢላቸው ባሕርያቸው ደካማ ነው አይቻላቸውም ብሎ ነው እንጂ ከሕገ ሥጋ ሕገ ነፍስ ከሕገ እንስሳ ሕገ መላእከት እንዲበልጥ ታውቆ የለም ብለው ከቤት ርቀው ንጽሕ ጠብቀው ይኖራሉና በጐ ባሪያ የቆመውን ቁረጥ የተኛውን ፍለጥ ቢሉት ያዘዙትን ሁሉ ያደርጋል ። ሕጋውያንም ባዘዛቸው ትእዛዝ በሰራላ ቸው ሥራት ጸንተው ይኖራሉና ። ወእንዘ ዝሩት ይእቲ ማእከለ አድባር ወአውግር ወቆሳተ ገዳም ተጋ ቢአ ትከውን እሐተ ጽርስፎራ እንዲል መቶው ፤ ስሳው ፤ ሠላሳው ቅንጣት ተሰብስቦ አንድ ኅብስት እንዲሆን ሰማዕታትም መነኰሳትም ሕጋውያንም በግዕዝ ርትዕት አንድ ናቸው ።

፱ ዘቦ እዝን ሰሚዓ ለይስማዕ

፱ ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ ማለት ፍኖት የተ ባለ በቁሙ ፍኖት እንዳይደለ ልበ ዝንጉዓን እንደሆነ ኰኩሕ የተባለ በቁሙ ኰኩሕ እንዳይደለ ስፍ ሐ አእምሮ የሌለው ልቡና እንደሆነ ሦክ የተባለ በቁሙ ሦክ እንዳይደለ ብዕል ሰፋጢት ሐልዮ መንበርት ያስቀሩበት እንደሆነ እዝነ ልቡና ያለው ያስተውል ።

፲ ወቀረቡሙ አርዳኢሁ ይቤልዎ በእንተ ምንት በምሳሌ ትትናገሮሙ ለሕዝብ ፤

፲ ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው ለሕዝቡ በምሳሌ ስለምን ታስተምራቸዋለህ አሉት ።

፲፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እስመ ለክሙ ተውህበ አእምሮ ምሥጢራቲሃ ለመንግሥተ ሰማይ፤

፲፩ የመንግሥተ ሰማይን ምሥጢር ማወቅ ለናንተ ተሰጥቷልና ማለት የወንጌልን ምሥጢር ማወቅ ለናንተ ተገልጧልና ። ወሎሙሰ ኢተውህበሙ ፤ ለሳቸው ግን አልተገለጸላቸውም ።

፲፪ እስመ ለዘቦ ይሁብዎ ። ማቴ ፳፭ ፡ ፳፱ ።

፲፪ ላለው ይሰጡታልና ማለት አእምሮ ላለው ይሁብዎ ምሳሌውን ይነግሩታልና ፤ ወይዌስከዎ ። ምሥጢሩን ይጨምሩለታልና ለከሙ ተውህበ ላለው ወለዘሰ አልቦ እለሂ ቦ የኃይድዎ ። አእምሮ የሌለውን ግን ያለውን ይቀሙታልና ማለት እንዳያውቀው

አድርገው ይመስሉበታልና ለሙሰ ኢተውህበ ላለው አንድም ምሳሌውን ለያዘ ይሁብዎ ወይዌስክዎ እንድ ወገን ምሥጢሩን ትርጓሜውን ይነግሩታልና ስክሙ ተውህበ ላለው ወለዘሰ አልቦ ምሳሌውን ላልያዘ ግን ያለውን አእምሮውን ነሥተው በግእዙ እንስሳ ያቆሙታልና ወለሙሰ ኢተውህበ ላለው ።

፲፫ ወበእንተ ዝንቱ በአምሳል እትናገሮሙ ።

፲፫ ስለዚህ በምሳሌ እነግራቸዋለሁ እስመ እንዘ ይሬእዩ ኢይሬእዩ ።
እናያለን ሲሉ አያዩምና ።
ወእንዘ ይሰምዑ ኢይሰምዑ ፤ እንሰማለን ሲሉ አይሰሙምና ወኢያሉብው እናውቃለን ሲሉ አያውቁምና

፲፬ ከመ ይትፈጸም ላዕሌሆሙ ትንቢተ ኢሳይያስ ነቢይ ዘይቤ ፡ ኢሳ ፮፡፱ ። ማር ፬፡፲፪ ፡ ሉቃስ ፰፡፲ ፡ ዮሐ ፲፪፡፵ ። ግብ ፳፰፡፳፮ ፡ ፭ ፡ ሮሜ ፲፩ ፡ ፰ ። ሉቃ ፡ ፲ ፡ ፲፬ ።

፲፬ ነቢዩ ኢሳይያስ የተናገረው ትንቢት በላቸው ይፈጸም ዘንድ ።
ሰሚዐ ትሰምዑ ወኢትሌብዉ መስማቱን ትሰማላችሁ አታስተውሉም ኢይሰምዑ ላለው ነጸሮተ ትኔጽሩ ወኢትሬእዩ ፤ ማየትን ታያላችሁ ማለት እናያለን ትላላችሁ አታስተውሉም ኢይሬእዩ ላለው ።

፲፭ እስመ ገዝፈ ልቡ ለዝ ሕዝብ

፲፭ አለዋቆች ሁነዋልና ።
ወእዘኒሆሙ ደንቀወ እምሰሚዐ የኢሳይያስ ቃል መፍቻ ፤ ጆሮቸው ከመስማት ደንቁሯልና ኢይሰምዑ ላለው ።
ወክደኑ አዕይንቲሆሙ ከመ ኢይርአዩ በአዕይንቲሆሙ እንዳያዩ ዓይናቸውን ጨፍነዋልና ማለት ምሥጢር ከማየት ተከልክለዋልና ኢትሬእዩ ላለው ወበእዘኒሆሙ ኢይሰምዑ ። በጆሮቸው እንዳይሰሙ ወበልቦሙ ኢይሌብው ። በልባቸው እንዳያስተውሉ ከመ ኢይትመየጡ ኀቤየ ፤ ወደኔ እንዳይመለሱ ። ወኢይሰሃሎሙ ይቅር እንዳልላቸው ።

፲፮ ወለክሙሰ ብፁዓት አዕይንቲክሙ ።

፲፮ ለናንተ ግን ሳይናችሁ ምስጋና ማለት እናንተ ግን ንዑዳን ክቡራን ናችሁ ።
እስመ ይሬእያ ። ያያሉና ማለት አይታችሁኛልና ። ወእዕዛኒክሙ እስመ ይሰምዓ ። ጆሮቻችሁ ይሰማልና ማለት ሰምታችሁኛልና ንዑዳን ክቡራን ናችሁ ።

፲፯ አማን እብለክሙ ከመ ብዙኃን ነቢያት ወጻድቃን ፈተው ይርአዩ እንትሙ ዘትሬእዩ ወኢርአዩ ፡ ወፈተው ይሰምዑ እንትሙ ዘትሰምዑ ወኢሰምዑ ሉቃ ፲ ፡ ፳፬ ።

፲፯ ብዙ ነቢያት ጻድቃን እናንተ የምታዩትን የምትሰሙትን ማለት ዛሬ የምትሰሙኝ የምታዩኝ እኔን ሊያዩኝ ሊሰሙኝ እንደ ወደዱ እንዳላዩኝ እዳንልሰሙኝ በእውነት እነግራችኋለሁ ። ሐተታ ነቢያት አላቸው፣ ያበር የቸነፈር የጼዋዌን ነገር ተናግረዋልና ጻድቃን አላቸው እንደመጠናቸው ዋቂት ትሩፋት ሠርተዋልና ፤ ኢርእዩ ወኢሰምዑ አለ የሥጋዌ ነገር አልተገለጸላቸውምና ፤ አንድም ዶጋት አለ ኢሳይያስ እነ ኤርምያስ ናቸው ብሎ ወስዷቸዋል ብዙ ነቢያት አላቸው ፤ የሥጋዌ ነገር ተገልጾላቸው ቀና ግረዋልና ጻድቃን አላቸው ብዙ ትሩፋት ሠርተዋልና እንዳላዩኝ እንዳልሰሙኝ አለ ገልጾላቸው ተናግረውት ዐረፍተ ዘመን ስገቷቸው ሳያዩት ቀርተዋልና ።

፲፰ ወአንትሙሰ ስምዑ ምሳሌሁ ለዘይዘርዕ

፲፰ እናንተስ የሚዘራውን ምሳሌ ስሙ ።

፲፱ ኵሉ ዘይሰምዕ ነገረ መንግሥተ ሰማያት ወኢይሌቡ ይመጽእ እኩይ መይመሥጥ ቃለ ዘተዘርዐ ውስተ ልቡ ውእቱኬ ዘተዘርዐ ውስተ ፍኖት

፲፱ በመንገድ የወደቀው ዘር የመንግሥተ ሰማያትን ነገር ሰምቶ የማያስተውለው እኩይ ዲያብሎስ መጥቶ በልቡናው የተዘራውን የሚያጠፋበት ነው ።

፳ ወዘሰ ውስተ ኰኵሕ ተዘርዐ ውእቱ ዘነገረ ይሰምዕ ወሶቤሃ በፍሥሓ ይትዌከፎ ።

፳ ከቋንጣ ላይ የወደቀው ዘር ነገሩን ሰምቶ ለጊዜው ደስ ብሎት የሚቀበለው ነው ።

፳፩ ወባሕቱ አልቦቱ ሥርው ላዕሌሁ ለጊዜሁ ዳዕሙ ውእቱ ወከዊኖሰ ምንዳቤ ወስደት በእንተዝ ነገር በጊዜሃ የዓሉ ።

፳፩ ነገር ግን ለጊዜው ነው እንጂ ሥር የለውምና ስለዚህ ነገር መከራና ስደት በደረሰ ጊዜ ፈጥኖ ይክዳል ።

፳፪ ወዘሰ ውስተ ሦክ ተዘርዐ ዝውእቱ ዘነገረ ይሰምዕ ወትካዘ ዓለም ወስፍጠተ ብዕል ተሐንቆ ለነገር ወዘእንበለ ፍሬ ይከውን ።

፳፪ በሾህ የተዘራው ዘር ነገሩን ሰምቶ የብልጽግና ማታለልና ይህን ዓለም ማሰብ ሐንቆት ያለ ፍሬ የሚሆን እሱ ነው ።

፳፫ ወዘሰ ውስተ ምድር ሠናይት ተዘርዐ ዝውእቱ ዘነገረ ይሰምዕ ወይሌቡ ወይፈሪ ወይገብር ።

፳፫ በበጎ ምድር የተዘራው ዘር ግን ነገርን ሰምቶ የሚያስተውለው የሚሠራው ነው ።
ቦ ዘምእት ወቦ ዘ፷ ወቦ ዘ፴ ። መቶ ስሳ ሠላሳ የሚያፈራ አለ ።

በእንተ ምሳሌ ዘሥርናይ ሠናይ ወዘክርዳድ ።

፳፬ ካልዕተ ምሳሌ አምጽአ ሎሙ ። ማር ፬፡፳፮
፳፬ ሁለተኛ ምሳሌ ሌላ ምሳሌ መስሎ ነገራቸው እንዘ ይብል ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብእሴ ዘዘርዐ ሠናየ ዘርዐ ውስተ ገራኅቱ ።
መንግሥተ ሰማያት ሕገ ወንጌል ፡ ሕገ ወንጌል ተሰፋ ተሰፋ ኢየሱስ ክርስቶስ የተበጠረ የተንጠረጠረ

ዘርን የሚዘራ ገበሬን ትመስላለች ። ገራኅት ፡ ይህ ዓለም ፤ አንድም መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ትመ ስል ዘርዓ በአ ፤ ገበሬ በርሻው የሚዘራት የተበጠረ የተንጠረጠረ ዘርን ትመስላለች ገራኅት ልቡና ።

፳፭ ወእንዘ ይነውሙ ሰብእ መጽአ ጸላኢሁ ወዘርዐ ክርዳደ ማእከለ ሥርናይ ወኃለፈ ።
ተኝተው ፡ ሰዎች ...

፳፮ ወሶበ ተንሥአ ሣዕር ጠሊት መጥቶ በስንዴው መካከል ክርዳድ ዘርቶ ሄደ ።

፳፮ ወሶበ በቈለ ሥርናይ ወፈረየ አሜሃ አስተርአየ ክርዳድኒ ።

፳፮ ሥንዴው በበቀለና ባፈራ ጊዜ ያን ጊዜ ክርዳዱም ታየ ማለት ተለይቶ ታወቀ ።

፳፯ ወመጺኦሙ አግብርቲሁ ለበዓለ ገራኅት ይቤልዎ እኮሁ ሠናየ ዘርዐ ዘራዕከ ውስተ ገራኅትከ

፳፯ ባሪያዎቹ መጥተው ባለቤቱን አቤቱ በር ሻህ በጐ ዘር ዘርተህ አልነበረምን ።
እምአይቴ እንከ ሎቱ ክርዳድ ክርዳድ ከወዴት ተገኘ አሉት ።

፳፰ ወይቤሎሙ ብእሲ ፀራዊ ገብረ ዘንተ ።

፳፰ ጠላት ሰው ይህን አደረገ ። አንድም ዕንለ ፀራዊ ዲያብሎስ የጠላት ልጅ እንዲህ አደረገ ወአግብርቲሁ ይቤልዎ ትፈቅድኑ እንከ ንሑር ወንጸሕይዮ ባሪያዎቹም እንግዲህ ክርዳዱን ትቀልመን ልንሄድና እንድንጠፍለው ትወዳለህን አሉት ።

፳፱ ወይቤሎሙ አልቦ ።
አይሆንም አላቸው ።

፳፱ ከመ እንዘ ተዓርዩ ክርዳደ ኢትምሀውዎ ምስሌሁ ሥርናየኒ ።
ክርዳዱን እንነቅላለን ስትሉ ሥንዴውን እንዳትነቅሉ

፴ ኅድግዎ ይልሐቁ ኅቡረ እስከ ጊዜ ማዕረር

፴ ተዋቸው እስከ መከር ድረስ ባንድነት ይኑሩ ወበጊዜ ማዕረር እብሎሙ ለእለ የዓጽዱ ርእዩ ቅድመ ክርዳደ ወእሰርዎ በበከላስስቲሁ ወአውዕይዎ በእሳት መከር በደረሰ ጊዜ የሚያጭዱትን አስቀድማችሁ ክርዳዱን ከሥንዴው አይታችሁ በየነዶው እስራችሁ በእሳት አቃጥሉት ።
ወሥርናየሰ አስተጋብኡ ውስተ መዛግብትየ ።
ሥንዴውን ግን በጎታ በጎተራ በረቅ ሰብስቡት አላ ቸዋለሁ ። አንድም ወእንዘ ይነውሙ ሰብእ ብለህ መልስ ። ሐዋርያት ካለፉ በኋላ ዲያብሎስ አርዮስን ሠለስቱ ምእት ካለፉ በኋላ መቅዶንዮስን መቶ አም ሳው ካለፉ በኋላ ንስጥሮስን ማሥነሣቱ መናገር ነው ወሶበ በቈለ በተሾመ ባስተማረ ጊዜ ክህደቱ ኑፋ ቄው ተገልጾ ታወቀ ። ደቀ መዝሙር ከመምሩ ቤት ሳለ ክህደቱን ኑፋቄውን አይገልጸውምና ፤ ወመጺ ኦሙ አግብርቲሁ መላእክት ቀርበው እምጸሐፌ ዓለማት ፈጣሬ ዓለማት ጌታችን አቤቱ በዚህ ዓለም በጐ ትምርት አስተምረህ አልነበረምን ፤ እምአይቴ እንከ ሎቱ ክርዳድ ፤ ይህ ክህደት ኑፋቄ ከወዴት መጣ አሉት ። ወይቤሎሙ ፀራዊ ገብረ ዘንተ ፤ እኩይ ዲያ ብሎስ እንዲህ አደረገ አንድም የጠላቱ የዲያብሎስ የግብር ልጁ መናፍቅ እንዲህ አደረገ ። ሰው በባሕ ርይ እንዲራባ እሱም በግብር ይራባልና ፤ ሐተታ፡ መላእክት የሚጠይቁት ጌታ የሚመልሳቸው ሁኖ አይደለም ። በዚህ ዓለም በጐ ትምርት አስተምሮ አልነበረም ይህ ክህደት ኑፋቄ ከወዴት ተገኘ ብለው በመረመሩ ጊዜ ክህደት ኑፋቄ የተገኘ ከዲያብሎስ እንደሆነ የሚያውቁበትን ዕውቀት ከሱ ማግኘታቸ ውን መናገር ነው ። ወአግብርቲሁሰ ይቤልዎ ትፈቅ ድኑ ንሑር ንጸሕይዮ ። ኃጥኡን ከጻድቅ ለይተን ልናጠፋው ትወዳለህ አሉት ፤ ወይቤሎሙ አልቦ አይሆንም ከመ እንዘ ትጸሐይዩ ኃጥኡን እናጠፋለን ስትሉ ጻድቁን እንዳታጠፉ የኅጥእ ዳፋ ጻድቁን ይዳፋ እንዲሉ ፤ ለይቶ ማጥፋት ይቻላቸው የለም ፤ ይህም በኖኅ በሎጥ ታውቋል ብሎ ከነዚህ የሚወለዱ በንስሐ የሚመለሱ ብዙ አሉና ፤ ኅድግዎሙ ተዋ ቸው እስከ ዕለተ ምጽአት ባንድነት ይኑሩ ። ወበጊዜ ማዕረር ፤ ምጽአት በደረሰ ጊዜ መላእክትን አዛቸዋ ለሁ ። ርእዩ ቅድመ ፤ አስቀድማችሁ ኃጥአንን ከጻ ድቃን ለይዋቸው ፤ ወእሰርዎ በበከላስስቲሁ ፤ በየ ወገናቸው በገሃነም ሥቃይ እምጡባቸው ወሥርናየሰ ጻድቃንን ግን በመንግሥተ ሰማይ አኑሯቸው አላቸ ዋለሁ ። ሐተታ መዛግብት አላት በብዙ ወገን ትወ ረሳለችና ፤ እስመ ውስተ ቤተ አቡየ ብዙኅ ማኅደር ወምዕራፍ ቦቱ እንዲል ፤ አንድም ትመስል ብለህ መልስ ። መንግሥተ ሰማይ ሊቀ ማኅበር በርሻው የተበጠረች የተንጠረጠረች ዘርን የሚዘራ ገባሬን ትመስላለች ገራኅት ንዳም ፤ አንድም መንግሥተ ሰማይ ሥርዓተ ማኅበር ፤ ገበሬ በርሻው የዘራት የተበጠረች የተንጠረጠረች ዘርን ትመስላለች ። ገራ ኅት ልቡና ፤ ወእንዘ ይነውሙ አበው ሥርዓት ሠር ተው ካለፉ በኋላ ዲያብሎስ ክፉ ሕሊና ማምጣቱን መናገር ነው ። ወሶበ በቈለ ፤ ሥራ እሠራለሁ ባለ ጊዜ ክፉ ሕሊና ተለይቶ ታወቀ ወመጺኦሙ መላ እክት ቀርበው ጌታን ለሰው በጐ ሕሊናን ፈጥረህለት አልነበረምን ይህ ክፉ ሕሊና ከወዴት ተገኘ አሉት ብእሲ ፀራዊ ጠላቱ ዲያብሎስ እንዲህ አደረገ አላ ቸው ። ሐተታ መላእክት የሚጠይቁት እሱም የሚ መልስላቸው ሁኖ አይደለም ። ለሰው በጐ ሕሊና ፈጥሮለት አልነበረም ይህ ክፉ ሕሊና ከወዴት ተገኘ ብለው በመረመሩ ጊዜ ክፉ ሕሊና የሚገኝ ከዲያብ ሎስ እንደ ሆነ የሚያውቁትን ዕውቀት ከጌታ ማግኘ ታቸውን መናገር ነው ። ወአግብርቲሁሰ መላእክት ክፉውን ሕሊና ልናጠፋው ትወዳለህን አሉት ፤ ወይቤሎሙ አልቦ ፤ አይሆንም እስመ እንዘ ተአርዩ ክፉውን ሕሊና እናጠፋለን ስትሉ በጐውን ሕሊና

እንዲታጨፉ ፡ ጎድግዎሙ ቲዋቸው እስከ ተባሕቅዎ ድረስ ጥንድነት ይኑሩ ። ወበጊዜ ማዕረር ። በተባሕትዎ ጊዜ ሥርዓት የሚሠሩ አበውን አዛቸዋለሁ ፤ አስቀድማችሁ ክፉውን ሕሊና ከበጐው ሕሊና ለይታችሁ በየአገባቡ በቀኖና አርቁት ። ወሥርናዩስ በጐውን ሕሊና ግን በመንፈስ ቅዱስ አስጠብቁት አላቸዋለሁ ። መዛግብት አለው መንፈስ ቅዱስን ስለ ሀብቱ ብዛት ።

በእንተ ምሳሌ ዘሕጠተ ሰናፔ ።

፴፩ ካልዕተ ምሳሌ አምጽአ ሎሙ ሁለተኛ ምሳሌ ፡ ሌላ ምሳሌ መሰለላቸው ። ማር ፬ ፴፩ ሉቃ ፡ ፲፫ ፡ ፲፱

፴፪እንዘ ይብል ትመስል መንግሥተ ሰማያት ኅጠተ ሰናፔ እንተ ተነሥአ ብእሲ ወዘርዓ ውስተ ገራኅቱ ። መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ፤ ሕገ ወንጌል ተስፋ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስ በርሻው የሰናፍጭ ቅንጣት የሚዘራ ገበሬን ትመስላለች ። ገራኅት ይህ ዓለም ። አንድም መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ገበሬ በእርሻው የዘራት ሰናፍጭን ትመስላለች ገራኅት ልቡና ። ሐተታ ሰናፍጭ ፍጽምት ናት ነቅ የለባትም ወንጌልም ነቅዕ ኑፋቄ የለባትምና ። ሰናፍጭ ላይዋ ቀይ ውስጧ ነጭ ነው ። ወንጌልም በላይ ደማችሁን አፍሱ ትላለች በውስጥ ግን ሕገ ተስፋ ናትና ፡ አንድም ሰናፍጭ ጣዕሟ ምረሯን ያዘነጋዋል ፤ ወንጌልም ተስፋዋ መከራዋን ያዘነጋዋልና ። አንድም ሰናፍጭ ቁስለ ሥጋን ታደርቃለች ። ወንጌልም ቁስለ ነፍስን ታደርቃለችና ። አንድም ሰናፍጭ ደም ትበትናለች ወንጌልም አጋንንትን መናፍቃንን ትበትናለችና ። አንድም ከምትደቁስበት ተሐዋስያን አይቀርቡም ። ወንጌልም ከምትነገርበት አጋንንት መናፍቃን አይቀርቡምና ። ሰናፍጭ ስትደቁስም ስትበላም ታስለቅሳለች ። ወንጌልም ሲማሯትም ሲያስተምሯትም ታሳዝናለችና ። ሰናፍጭ ከበታችዋ ያሉትንም እታክልት ታመነምናለች ፡ ወንጌልም የመናፍቃንን ጉባኤ ታጠፋለችና ። ሰናፍጭ አንድ ጊዜ የዘሯት እንደሆነ ባመት ባመት ዝሩኝ አትልም ተያይዛ ስትበቅል ትኖራለች ። ወንጌልም በመቶ ሃያ ቤተሰብ ተጀምራ እስከ ምጽአት ድረስ ስትነገር ትኖራለችና ።

፴፪ ወይእቲ ትንእስ እምኵሉ አዝርዕት ። ፴፪ ስትዘራ ከአዝርዕት ሁሉ ታንሳለች ። ወሶበ ልህቀት ተዓቢ እምኵሉ አሕማላት ። ባደገች ጊዜ ግን ከአዝርዕት ሁሉ ትበልጣለች ፡ እንደ ሺ ካሉ ከዖፍ ዘር ከኅመን ዘር ። ወትከውን ዕፀ ዐቢየ ። ደግ ዕፅ ትባላለች ።
እስከ ይመጽኡ አዕዋፈ ሰማይ ወያጸልሉ ታኅተ አዕጹቂሃ ። አዕዋፍ መጥተው ማረፊያ መሰፈሪያ ዛፍ እስኪያደርጓት ድረስ ። አንድም ወይእቲ ትንእስ ብለህ መልስ ። ወንጌል ስትነገር ከሁሉ ታንሳለች

በመቶ ሐያ ቤተ ሰቡ መጀመሯን ትንእስ አለ ፤ በጉባኤ በተነገረች ጊዜ ግን ከሕገጋት ሁሉ ትበልጣለች ። ወትከውን ፡ ደግ ሕግ ትሆናለች ፤ ወይመጽኡ ሕዝብ አሕዛብ እስኪያምኑባት ድረስ ። አንድም ትመስል ብለህ መልስ ። በጥምቀት በተአምኖ ኃጣውእ ያሉ ሰዎች በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን ያሉ ሰዎችን ይመስላሉ ። ወይእቲ ትንእስ ፡ በጥምቀት የሚሰጠው ጸጋ በመጠኑ ነውና ፡ ትንእስ አለ ያም ኃጢአቱን ሲናገር ተዋርዶ ነውና ። ወሶበ ልህቀት ፤ በጥምቀት ያገኘውን ጸጋውን በሥራ ባስፋው ጊዜ ያም ቀኖናውን በፈጸመ ጊዜ ከሰው ሁሉ ይበልጣል ። ወትከውን ። ደግ ሰው ይባላል ፤ ወይመጽኡ ሰው ሁሉ መጥቶ ከእግሩ ወድቆ አትርሳኝ እስኪለው ድረስ ።

በእንተ ምሳሌ ዘብሑእ ።

፴፫ ካልዕተ ምሳሌ ነገሮሙ ። ሉቃ ፲፫ ፳፩ ።

፴፫ ሰቀረበው ካልዕት ይላል ሁለተኛ ምሳሌ ሌላ ምሳሌ ነገራቸው ።

ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብሑአ ዘነሥአት ብእሲት ወአብኅአቶ ውስተ ሠለስቱ መሥፈርተ ሐሪጽ መንግሥተ ሰማያት እንዳለፈው ፤ በሦስት መሥፈሪያ ዱቄት የሸሸገችው ማለት ሦስት መስፈሪያ ዱቄት የለወሰችበትን ሴት የያዘችውን ።
ወአብኅአ ኵሎ ።

ሁሉን ወደ ምጸት የሳበ እርሾን ትመስላለች ። ብኑእ ጌታ ብእሲት ጥበቡ ውስተ ሠለስቱ መሥፈርተ ሐሪፅ ፤ ሥጋን ነፍስን ደመ ነፍስን ያዋሐደችው ። ወአብኅአ ኵሎ በተዋሕዶ ሥጋን የባሕርይ አምላክ ማድረጉን መናገር ነው ። አንድም ብእሲት መምህራን ብኑእ ወንጌል ፡ ውስተ ሠለስቱ ወንጌል መሠራቷ ለሦስቱ ነገድ ነውና ለነገደ ሴም ለነገደ ያፌት ለነገደ ካም ፡ ወአብኅአ ኵሎ በወንጌል ሁሉ መክበሩን መናገር ነው ። አንድም ብእሲት መምህራን ብሑእ ጥምቀት ፤ ውስተ ፫ቱ ፤ ጥምቀት በሦስቱ ስም ነውና ወአብኅአ ኵሎ በጥምቀት ሁሉ መክበሩን መናገር ነው ። አንድም ብእሲት ቀሳውስት ብኁእ ፤ ሥጋው ደሙ ፤ ውስተ ሠለስቱ ። ለቀድሶተ ሥጋ ወነፍስ ወመንፈስ ብሰው ይሰጣሉና ወአብኅአ ኵሎ ፤ በሥጋው በደሙ ሁሉ መክበሩን መናገር ነው ። አንድም ብእሲት ቡርክት ነፍስ ፤ ብኁእ ጸጋ ጥምቀት ውስተ ፫ቱ መሥፈርተ ሐሪፅ ውስተ ፫ቱ መክፈልተ ሕሊናሃ እንዲል ፡ ሥራውን በሦስት ወገን ትሠራዋለች በወጣኒነት በማእከላዊነት በፍጹምነት ክብሩንም በዚያው ልክ ትወርሰዋለችና ፤ ወአብኅአ ኵሎ ። በሥራው ሁሉ መክበሩን መናገር ነው ፤ አንድም ብኁእ ጌታ ብእሲት ዮሴፍ ኒቆዲሞስ ። ውስተ ሠለስቱ ፡ ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት በከርሠ መቃብር መኖሩን

መናገር ነው ። ወአብነት ሁሉ ሙሴና መቃብርን አጥፍቶ አንድ ወገን ሁኖ መንግሥትን መናገር ነው ።

፴፬ ወዝንተ ኵሎ ተናገረ እግዚእ ኢየሱስ በምሳሌ ለአሕዛብ ። ማር ፬፥ ፴፫ ።

፴፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለአሕዛብ ይህን [illegible] በምሳሌ አስተማራቸው ።
[illegible] በምሳሌ ኢተናገሮሙ ።
ያለ ምሳሌ ግን አላስተማራቸውም አለ በዚህ ቀን አንድም በሆን ምሳሌ እንጂ ባልሆን ምሳሌ አላስተምራቸውም ።

፴፭ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ በነቢይ እንዘ ይብል እከሥት በምሳሌ አፉየ ወእነግር እምሳለ ዘእምትካት ።

፴፭ መዝ ፸፯፥፪ አፌን ምሳሌ አገልጣለሁ የተሰወረውንም ምሳሌ አስተምራለሁ ተብሎ በነቢይ የተነገረው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ። በከመ ይብ አሳፍ የሚል አብነት ይገኛል ሰዳዊት ሁለት ሙቶ ሰማንያ ስምንት መዘምራን ነበሩት አለቆቻቸው አሳፍ ቆሬኤማን ኤዶትም ይባላሉ በየአለቆቻቸው ኳሬት ተከፍለው ዐሥራ ሁለት ዐሥራ ሁለት እየ ሆኑ ወገን እራቱ ጊዜ ይጸልያሉ ።
ልክ የቸው እሱም ከዳባባይ በማይወጣበት ነገር በማ ይወጣበት ጊዜ እየገባ ይጸልያል ሥራ መፍቻት የሰም ዐዚህ ጊዜ እስታው ለአሳፍ ደርሶት ነበርና ስለዚህ በከመ ይብ አሳፍ የሚል አብነት ይገኛል ።

በእንተ ፍካሬ ዘምሳሌ ክርዳድ ።

፴፮ ወእምዝ ኀደጎሙ ለአሕዛብ ወቦአ ውስተ ቤት ።

፴፮ ከዚህ በኋላ ሕዝቡን በአፍአ ትቶ ከቤት ገባ ወቀርቡ ኀቤሁ እርዳኢሁ ። ደቀ መዛሙርቱም ወደሱ ቀረቡ ወይቤልዎ ፈክር ለነ ምሳሌ ዘክርዳድ ወዘገራህት ።
በክርዳድ በገራህት የመሰልከውን ተርጉመህ ንገረን አሉት እንደ ከተማ ደቀ መዝሙር አይደሉምና የከተማ ደቀ መዝሙር ቢያየውም ባያየውም ዝም ብሎ ይሄዳል ።

፴፯ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ዘይዘርዕስ ሠናየ ዘርዓ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ውእቱ ።
፴፯ ያ መልካም ዘር የዘራው የሰው ልጅ ነው ብሎ መለሰላቸው ።
፴፰ ወገራህትኒ ዓለም ውእቱ ፤
፴፰ እርሻውም ዓለም ነው ።
ወሰናይኒ ዘርዕ ውሉደ መንግሥት እሙንቱ ።
መልካም ዘር የመንግሥት ልጆች ናቸው ።
ወክርዳድኒ ውሉዱ ለእኩይ ።
ክርዳዱም የክፉ ልጆች ናቸው ።

፴፱ ወፀራዊኒ ዘዘርዖ ዲያብሎስ ውእቱ ።
፴፱ ራዕ ፲፬፡፲፭ ። የዘራውም ጠላት ዲያብሎስ ነው ።
ወማዕረርኒ ኀልቀተ ዓለም ውእቱ ።
መከሩም የዓለም ፍጻሜ ነው ወዓጸድኒ መላእክት እሙንቱ አጫጆችም መላእክት ናቸው ።

፵ ከመ ኬ የዓርይዎ ለክርዳድ ቅድመ ወያውዕይዎ በእሳት ።

፵ ክርዳዱን አስቀድመው መርጠው በእሳት እንዲያቃጥሉት ፤ ከማሁ ይከውን በኅልቀተ ዝንቱ ዓለም ።

በዚህ ዓለም ፍጻሜ እንዲህ ይሆናል ።

፵፩ ይፌንዎሙ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ለመላእክቲሁ ።
፵፩ የሰው ልጅ መላእክትን ያዛቸዋል ።
ወየዓርዩ እመንግሥቱ ኵሎ ዓላውያን ወእለ ይገብሩ አበሳ በደል የሚያደርጉትንና ወንጀለኞችን ከመንግሥቱ ላይ ለይተው ።
፵፪ ወይወድይዎሙ ውስተ እቶነ እሳት ኀበ ሀሎ ብካይ ወሐቅየ ሥነን ።
፵፪ ልቅሶ ጥርስ ቁርጥማት ወዳለበት እቶን እሳት ይጨምሯቸዋል ።
፵፫ አሜሃ ይበርሁ ጻድቃን ምስብዒተ እደ እምብርሃነ ፀሐይ በመንግሥተ አቡሆሙ ።
፵፫ ጥበ ፫፡፫ ። ዳን ፲፪፡፫ ። ያን ጊዜ ጻድቃን ሰማያዊ አባታቸው በሚያወርሳቸው በመንግሥተ ሰማይ ከፀሐይ ሰባት እጅ ያበራሉ ።
ዘቦ እዝነ ሰሚዓ ለይስማዕ ። ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ ማለት እዝነ ልቡና ያለው ያስተውል ።

በእንተ መድፍን ወባሕርይ ወገፋፍ ።

፵፬ ወካዕበ ትመስል መንግሥተ ሰማያት መድፍነ ዘኀቡዕ ውስተ ገራህት ።
፵፬ ለቀረበው ካዕበ ይላል ሁለተኛ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ሕገ ወንጌል ተስፋ ፣ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ዘኅቡእ ዝጉብ ይላል በእርሻ ውስጥ የተቀበረች ወርቅን ትመስላለች ። ወረኪቦ ብእሲ ኅብአ ሰው አግኝቶ የሰወራትን ፤ ወእምፍሥሐሁ ሖረ ወሤጠ ኵሎ ዘቦ ወተሣየጣ ለይእቲ ገራኅት ፤ ከደስታው የተነሣ ሂዶ ያለ ገንዘቡን ሽጦ ያቺን እርሻ የገዛላትን ። ሐተታ ምድሩን ካልገዛሁ ወርቁን አላገኝም ብሎ ባልሆን ምሳሌ አያስተምርምና የኢዶምያስ ሰዎች የቀበሩት ወርቅ ነው ። አንድም ካዕበ ትመስል መድፍነ ብለህ መልስ ብእሲ ጌታ መድፍን አዳም ገራኅት ይህ ዓለም ነው ፤ ወረኪቦ ጌታ አዳምን በዚህ ዓለም ንስሐ ገብቶ ባገኘው ጊዜ ባሕርየ አዳምን ባሕርየ አድርጎ አዳምን ማዳኑን መናገር ነው ። ኢ.ነዓሥእ ለዘነሥእ እመላእክት ዘእ

ንበለ ዳዕሙ እምዘርአ አብርሃም እንዲል ። አንድም ብእሲ ዮሴፍ ሐድፉን ጌታ ገራኅት አመቤታችን ፤ ዮሴፍ ጌታን እመቤታችንን ባገኛቸው ጊዜ ቤቱን ንብረቱን ትቶ ተከትሎ ግብጽ መውረዱን መናገር ነው አንድም ብእሲ ሐዋርያት መድፉን ጌታ ገራኅት ይህ ዓለም ወረኪቦ ሐዋርያት ጌታን በዚህ ዓለም ባገኙት ጊዜ መረባቸውን መርከባቸውን ትተው ጌታን መከተላቸውን መናገር ነው። አንድም አምስቱን ግብራት ባም ስቱ ግብራት ተሰውረው ባገኛቸው ጊዜ ትፍሥሕትን በኃዘን ኃይልን በድካም ብዕልን በንዴት ልዕልናን በትሕትና ግዕዛንን በግብርናት ተሰውረው ባገኛቸው ጊዜ ትፍሥሕቱን ለኃዘን ኃይሉን ለድካም ብዕሉን ለንዴት ልዕልናውን ለትሕትና ግዕዛኑን ለግብር ናት ሰጥቶ አዳምን ማዳኑን መናገር ነው ። አንድም ምእመናን አምስቱን ግብራት ገንዘብ ማድረጋ ቸውን መናገር ነው ። አምስቱ ግብራት የተባሉ ፤ ዓለም ተውላጠ ዓለም ምግባር መንፈሳዊ ቃለ መጻ ሕፍት ቃለ መምህራን ናቸው ። ዓለም ይህ ዓለም ነው ሁሉ የሚገኝ ከዓለም ነውና ፤ ተውላጠ ዓለም እንደ የዋህ ጳውሊ ባለጸጋ አባት ነበረው አባቱ ሙቶ በገንዘብ ከወንድሙ ጋራ ተጣልቶ ወደ ዳኛ ሲሄድ እንዳባቱ ያለ ባለጸጋ ሙቶ ወደ መቃብር ሲወስዱት አገኘ ይህ ምንድነው ብሎ ጠየቀ ባለጸጋ ነበር ሙቶ ሊቀብሩ ይወስዱታል አሉት ። ለዚህ ብየ ከወንድሜ ተጣላሁን አንተን ይምሰል ብሎ ጥሎስት ሄዷል ። ምግባር መንፈሳዊ እንደ አብ ርሃም መርዓዊ ነው እድ ብርሀት ከጫጉላው አው ጥታ እየመራች ገዳም ወስዳዋለች ቃለ መጻሕፍት እንደ አባ ዕንጦንስ ምንተ ይበቁዖ ለሰብእ ለእመ ዙሉ ዓለመ ረብሐ ወኅጕለ ኃጕለ የለውን ይዞ መንኖ ሄዷል።ቃለ መምህራን እንደ አትናስዮ፤ምእ መናንን የምትረዳ ዶግ ሴት ነበረች ሰይጣን በዝሙት ድል ነሣት ምእመናንን የማትጠይቃቸው ሆነ ሰይ ጣን ልጃችንን ቀማን በተቻለህ ርዳን ብለው ከዮ ሐንስ ሐጺር ላኩ ሂዶ ንገሩልኝ አለ ነገሩለት ግባ በሉት አለች ገባ አስነጥፋ ና ከጠገቤ ተቀመጥ አለ ችው በወንበር ከፊቷ ተቀምጦ እያያት ያለቅስ ጀመር ምነው ታለቅሳለህ አለችው መልከ መልካም ነሽና ብታሳዝኚኝ ነው አላት ይህማ ደስ ያሰኛል እንጂ ያሳዝናል አለችው መፍረስ መበስበስ አለና ምን ይሆናል አላት ለዚህ ምን ይበጃል አለችው ብትተ ይው አላት ብተወው ጌታዬ ይምረኛል አለችው ይምርሻል አላት አንድም እሱ በገባ ጊዜ ሲያስስ ንዋት የነበሩ አጋንንት መብራት እንደ አበሩባቸው አርጋብ ሲወድቁባት ሲነሱባት አየ እንዲህ ሲሆኑ ብሽ አየሁ አላት ለዚህም ይበጃኛል አለችው ብትተይው ብተወው ጌታዬ ይምረኛልን አለችው አዎን ይምርሻል ተከተይኝ ብሏት ወጣ አብራው ወጣች አባቱ ቆየኝ ትለዋለች ድረሽብኝ ይላታል አግሬ አልችል ቢል ከልብሷ እየቀደደች አጉደ ጫማ እያደረገች ትከተለዋለች ። አባቴ ቆየኝ ትለዋለች ድረሽ ይላታል ከጥታው ደረሱ አሳቱን እንድዶላት ተቀመጠች እሱ አልፍ ብሎ ጸሎቱን ያዘ በዚያ ሌሊት ዐረፈች ሰዋስወ ብርሃን ተተክሎ መላእክት ሲወጡ ሲወርዱ ያያል ማዕርጉ ጽማዌ ነውና የተላኩበትን ግን አያውቅም ሲነጋ መልአክ መጥቶ ያች ያመጣሃት ሴት ዐርፋለች መቃብሯን አንበሳ ይቆፍርልሃልና ቅበራት አለው ይህስ ይሁን ዛሬ ሌሊት ስትወጡ ስትወርዱ ያየኋችሁ ምንድን ነው አለው ነፍሷን በፍሳርግ ነው አለው ተቀበላትን አለው እዎን ተከተይኝ ብለሃት ተከትላህ በወ ጣች ጊዜ ተጋድሎ ለኪ ብሏታል ብሎ ነግሮታል ።

፵፭ ካዕበ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብእሴ ሠያጤ ዘየኃሥሥ ባሕርየ ሠናየ ።

፵፮ መንግሥተ ሰማያት ሕገ ወንጌል ሕገ ወንጌል ተሰፋ ፤ ተሰፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ብሩሃ ሲል ነው ዕንቍን የሚሻ ነጋዴን ትመስላለች ። ወረኪቦ አሐተ ባሕርየ እንተ ብዙኅ ሤጣ ሖረ ወሤጠ ኵሎ ዘቦ ወተሣየጣ ።

ዋጋዋ ብዙ የሆነ ዕንቍን ባገኘ ጊዜ ያለ ገንዘቡን ሽጦ የገዛትን ብእሲ ጌታ ዕንቍ አዳም ፤ አዳምን ንስሐ ገብቶ ባገኘው ጊዜ ባሕርዩን ባሕርይ አድ ርጎ አዳምን ማዳኑን መናገር ነው ። አንድም ብእሲ ጌታ ዕንቍ አዳም መንግሥተ ሰማይ ሐዋርያት አዳምን የሚሹ ጌታን ይመስላል ።

አንድም መንግሥተ ሰማይ ምእመናን ጌታን የሚሹ ሐዋርያትን ይመስላሉ ፤

ሐዋርያት የሚሹት ጌታን ይመስላሉ ።

፵፯ ካዕበ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ገሪፈ እንተ ተወድየት ።

፵፯ ውስተ ባሕር ወአስተጋብአት እምኵሉ ዘመደ ዓሣት ።

፵፯ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ሕገ ወን ጌል ተሰፋ፤ ተሰፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ከባሕር ላይ

፵፯ የጣሏትን ዓሣን ሁሉ ሰብስባ የያዘች ዘረ መትራንን ትመስላለች ።

፵፰ ወሶበ መልአት አዕርግዋ ውስተ ሐይቅ

፵፰ በመላች ጊዜ ከወደቡ ያወጧትን

ወነቢሮሙ ኅረዩ ሠናዮ ወወደዩ ውስተ ሙዳዮሙ ። ከወደቡ ተቀምጠው ደጋጉን እየመረጡ ከማጥና ቻው አኖሩ ። አረዩ ኃረዩ በየኑ ቤጹ ይላል ወእኩዮሰ ገደፍዎ አፍአ ፤

ክፉውን ግን መልሰው ከባሕር ጣሉት አጴራግዛ ራስ ከብዶ ይባላል ።

፵፱ ከማሁ ይከውን በኅልቀተ ዓለም

፵፱ በዕለተ ምጽአት እንዲህ ይደረጋል ።

፵፱ ወይመጽኡ መላእክት ወይፈልጡ ኃጥአነ እማእከሎሙ ለጻድቃን ወይወድይዎሙ ውስተ እቶነ እሳት ኀበ ሀሎ ብካይ ወሐቅየ ስነን።

፵፱ መላእክት መጥተው ጻድቃንን ለይተው በመንግሥተ ሰማይ ያኖሯቸዋል ፥ ኃጥአንን ከጻድቃን ለይተው ልቅሶ ጥርስ ቍርጥማት ባለበት በገሃነም ያኖሯቸዋል ። አንድም ትመስል ገሪፈ ብለህ መልስ ገሪፍ መንጌል በሕር ዘሀሎ ዓለም ። ወእስተጋብአቱ ሕዝቡን አሕዛቡን አንድ ያደረገች።ወዖበ መልአት ይህ ዓለም የሚያልፍ ጻድቃን በነገደ ዲያብሎስ ልክ ሲሞሉ ነውና ። አንድም ገሪፍ ሥርዓተ ማኅበር ባሕር ገዳም ። ወእስተጋብአት ሰውን ሁሉ የሰበሰበች ወዖበ መልአት ብዙ ዘመን ከረዳ በኋላ ትባሕትዎ ያዝ ይሉታል ። በ፫ በ፯ ፱ በ፲ ምልክት ይታ ይለታል ፤ በ፩ኛው በ፳ኛው በ፲ኛው ተባሕትዎ ይይዛል ምልክት ባይታይለት የረዳበት ዘመን ተቈ ጥሮ ይይዛል ምልክት ለሁሉ አይታይምና ወእኩየሰ ሳይረዳ ተባሕትዎ እይዛለሁ ያለውን ግን ገና ነህ ርዳ ይሉታል ወያወፅእዎ ዘበአኀሥሮት እንዲል ። ከማሁ ይከውን በህልቀተ ዝንቱ ዓለም።በዕለተ ምጽ አት እንዲህ ይደረጋል ።

፶፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለበውክሙኑ እንከ ዘንተ ኵሎ ።

፶፩ ጌታ ይህን ሁሉ ዐወቃችሁት አላቸው ። ሐተታ እንደ ከተማ መምህር አይደለምና የከተማ መምህር ቢያቀለትም ባያቀለትም ዝም ብሎ ይሄዳል ።
ወይቤልዎ እወ ፤
አዎን አሉት ፤ እላቸውም እንደ ከተማ ደቀ መዝሙር አይደሉምና ያወቁትን አዎን ያላወቁትን ፈክር ለን ይሉታልና ።

፶፪ ወይቤሎሙ በእንተ ዝንቱ ኵሉ ጸሐፊ ዘይፀመድ ለመንግሥተ ሰማይ ይመስል ብእሴ በዓለ ቤት ዘያወፅእ እመዝገቡ ሐዲሰ ወብሉየ ።

፶፪ ስለዚህ ነገር ወንጌልን የሚያስተምር ሁሉ አሮጌና አዲስ ከሣጥኑ የሚያወጣ ማለት ልልበስ ያለውን የማያጣ ባለጸጋን ይመስላል ። ልጥቀስ ቢል አያጣም ። አንድም አዲሱን ለመልበስ ብሉዩን ለማናፈስ ከሣጥኑ የሚያወጣ ባለጸጋን ይመስላል ። ሐዲሱን እያስተማረ ብሉዩን የሚማር ይሆናል ። አንድም ዘያወፅእ እመዝገቡ ብሉየ ። ወዘይወዲ ውስቴቱ ሐዲስ ብሉዩን ከሣጥኑ የሚያወጣ በሣጥኑ ሐዲሱን የሚያኖር ባለጸጋን ይመስላል አእምሮን ገንዘብ የሚያደርግ ውኀደተ አእምሮን የሚያርቅ ይሆናል ።

ዘከመ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ናዝሬት።

፶፫ ወሶበ ፈጸመ እግዚእ ኢየሱስ እሎንተ ምሳሌያተ ተንሥአ እምህየ ወሖረ ሀገሮ ፤

፶፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ይህን ሁሉ በምሳሌ አስተምሮ ከፈጸመ በኋላ ከዚያ ተነ ሥቶ ወደ ሀገሩ ወደ ናዝሬት ሄደ ።

፶፬ ወመሀሮሙ በምኵራቦሙ

፶፬ ማር ፤ ፮ ፤ ፩ ሉቃ ፤ ፬ ፤ ፲፮ ከምኵራብ ገብቶ አስተማራቸው ።
እስከ ሶበ ይደመሙ ወይብሉ እምአይቴ እንከ ሎቱ ዝንቱ ኵሉ ጥበብ ወኃይል ፤
ይህ ሁሉ ጥበብ ኃይል ከወዴት ተገኘለት ብለው እስኪያደንቁ ድረስ ጥበብ ምሳሌ መስሎ ወኃይል ትርጓሜ ተርጕሞ ማስተማር ። አንድም ጥበብ ምሳሌ መስሎ ተርጓሜ ተርጕሞ ማስተማር ወኃይል ታምራት ማድረግ ከማን አገኘው ።

፶፭ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልዱ ለፀራቢ ። ዮሐ ፮ ፥ ፵፪ ።

፶፭ የፀራቢ የዮሴፍ ልጅ አይደለምን አሉ ። በሀገራቸው ልጅ ያባቱን ሥራ ይማራል እንጅ ሌላ አይሠራምና ።
ወስማ ለእሙ ማርያም ።
እናቱስ ማርያም አይደለችምን ድኃ ማለት ነው ።
ወአኃዊሁኒ ያዕቆብ ወዮሳ ስምዖን ወይሁዳ ።
ወንድሞቹስ እነዚህ እነዚህ አይደሉምን ።

፶፮ ወአኃቲሁኒ ኵሎን ሀለዋ ኀቤነ

፶፮ እኅቶቹስ ቁኛ ዘንድ ያሉ አይደሉምን ። አንድም መንፈስ ቅዱስ ፊታቸውን ጸፍቶ አፋቸውን ከፍቶ ምንም ቢያደርግ የፀራቢ ሰማያት ወምድር የእብ ልጅ አይደለም እናቱስ እግዝእተ ብዙኃን ማርያም አይደለችም ሲያሰኛቸው ነው ።
እምአይቴ እንከ ሎቱ ዝንቱ ኵሉ ጥበብ ወኃይል።
ይህን ሁሉ ጥበብና ኃይል ከወዴት አገኘው እንዳሉ ።

፶፯ ወአኃዙ ያንጐረጕሩ በእንቲአሁ ።

፶፯ በሱ ነገር ይታወኩ ጀመር ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አይትሜነን ነቢይ ዘእንበለ በሀገሩ ወበቤቱ ።
ነቢይ ከቤቱና ከሀገሩ በቀር አይነቀፍም ማለት በሀገሩ አይከበርም አላቸው ።

፶፰ ወኢገብረ በህየ ኃይለ ብዙኃ በእንተ ሕጸተ አሚኖቶሙ ።

፶፰ ስለ አለማመናቸው ብዙ ታምራት አላ ደረገም ።

በእንተ ሀለየ ሄሮድስ ላዕለ ኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፲ወ፬ ።

፩ ወበውእቱ መዋዕል ሰምዓ ሄሮድስ ንጉሥ ነገሮ ለእግዚእ ኢየሱስ ። ማር ፮ ፤ ፲፬ ሉቃ ፱ ፤ ፯

፩ በዚያ ወራት ሄሮድስ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስን ነገር ሰምቶ ማለት ያደረጋውን ታምራት

የሠራውን ትሩፋት ሰምቶ ድምፀ ነገሩ ይላል አብ ነት የቃምራቱን ዜና ሰምቶ ።

፪ ወይቤ ዝውእቱ ዮሐንስ መጥምቅ ውእቱ ተንሥአ እምውታን ።

፪ ለብላቴኖቹ ይህ ዮሐንስ መጥምቅ ነው እሱ ከሙታን ተነሥቶ ይሆናል ።
ወበእንተዝ ይትገበራ ሎቱ ኃይላት ።
በግፍ አስገድየው ነበርና ስለዚህ ታምራት ይደረ ግለታል አላቸው ።

፫ እስመ ውእቱ ሄሮድስ አኃዞ ለዮሐንስ ወሞ ቅሖ በቤተ ሞቅሕ ማር ፯ ፡ ፲፯ ሉቃ ፫ ፡ ፲፱ ።

፫ ሄሮድስ ዮሐንስን ይዞ አስሮ አግዞት ነበርና በእንተ ሄሮድያዳ ብእሲተ እኁኁ ፊልጶስ ።
በወንድሙ በፊልጶስ ሚስት በሄሮድያዳ ምክንያት ።
እስመ ኪያሃ አውሰበ ።
እሷን ስለአገባ ።
፬ እስመ ይቤሎ ዮሐንስ ሎቱ ኢይከውንከ ታውስብ ብእሲተ እኁከ ፊልጶስ ።
፬ የወንድምህን የፊልጶስን ሚስት ማግባት አይገባህም ቢለው ።
፭ወእንዘ ይፈቅድ ይቅትሎ ይፈርሆሙ ለሕዝብ
፭ ሊገድለው ወዶ ሳለ ሕዝቡን ይፈራቸው ነበረ ።
እስመ ከመ ነቢይ ይሬእይዎ ለዮሐንስ ።
ዮሐንስን እንደ አባት ያፍሩታል እንደ መምህር ያከ ብሩታልና ።
፮ ወከዊኖ ዕለተ ልደቱ ለሄሮድስ ዘፈነት ሎቱ ወለተ ሄሮድያዳ በማእከሎሙ ።
፮ ሄሮድስ የተወለደበትን ቀን በዓል አድርጎ ሳለ ወለተ ሄሮድያዳ መጥታ በመኳንንቱ ፊት ዘፈ ነችለት፣ ሐተታ አሕዛብ የተወለዱበትኝ ቀን ያከብራ ሉና በዚህ ቀን ተወልደን ከዚህ ማዕርግ ደረስን ሲሉ ፤ አንድም ከጨለማ ወደ ብርሃን ከጾባብ ወደ ስፊ የወጣንበት ሲሉ ።
ወአደመቶ ለሄሮድስ ።
ሄሮድስን ደስ አሰኘችው ።
፯ ወበእንተዝ መሐለ ላቲ ከመ የሀባ ዘሰአለቶ ።
፯ ስለዚህ የለመነችውን እንዲሰጣት ማለላት።
፰ ወይእቲሰ አቅደሙት እእምሮ በኀበ እማ ።
፰ እሷ አስቀድማ ከናቷ ዘንድ ነገሩን ዐውቃው መጥታ ነበርና ታሪክ ከዕለታት ባንድ ቀን ካንች በቀር ሌላ የምወደው እንደሌለ አምላክ እስራኤል ያውቀዋል ። ነገር ግን ይኽ ነቢይ ይዘልፈናል አላት ለዚህማ ምን ቸገረህ በዓል የምታደርግበት ቀን ደር ቧል ልጇ መጥታ ትዘፍንልሃለች ቸብቸቦውን አስቆ ርጠህ ስጣት ከዚህ በኋላ የወደድነውን እናደርጋለን አለችው ከዚህ በኋላ ስትሄድ ምን ላድርግልሽ ያለሽ እንደ ሆን ሌላ ነገር አትለምኚ ቸብቸቦውን ቈርጠህ ስጠኝ በይው ብላ መከራ ሰዷታለች ። ሂዳ ዘፈነች ለት በማርቆስ እስከ መንፈቀ መንግሥቱ ይላል ፤ የመንግሥቱንም እኩሌታ ቢሆን እሰጥሻለሁ አላት ሂዳ ነገረቻት ይልቅስ የነገርሁሽን አድርጊ መንግ ሥቱንማ መላውን ማኝ ነሥቶናል አለቻት ሂዳ ፤
ወትቤሎ ሀበኒ ይእዜ ርእሶ ለዮሐንስ መጥምቅ በየ ሕል ።
የዮሐንስን ራሱን አስቆርጠህ በየሕል ስጠኝ አለችው

፱ ወተከዘ ንጉሥ በእንተ መሐላሁ ።
ስለመሐላው ማለት ከድታ አማለችኝ ብሎ አዘነ ።
ወበእንተ እለ ይረፍቁ ምስሌሁ ከሱም ጋር ሰለተቀ መጡት መሐላ አፍራሽ ይሉኛል ብሎ ፤ አንድም ወበእንተ እለ ይረፍቁ ነቢየ እግዚአብሔር አስገደለ ይሉኛል ብሎ ።
ወአዘዘ የሀብዋ ።
ቆርጣችሁ ስጧት ብሎ አዘዘ ።

፲ ወፈነዎ መስተራትዓተ ሐራ ።

፲ ጭፍራውን የሚሠሩ የሚቀጡ ባለወነችን ላከ ቤተ አንግሣ ቤተ እይጽ ሰቃይ ቀራጭ እንዳለ ።
ወመተሩ ርእሶ ለዮሐንስ በቤተ ሞቅሕ ።
በግዞት ቤት ሳለ የዮሐንስን ራስ ቀረጡ ።

፲፩ ወአምጽኡ ርእሶ በየሕል ወወሀብዋ ለይእቲ ወለት ።

፲፩ በየሕል አምጥተው ለብላቴናዪቱ ሰጧት ።
ሐተታለጊዜው እስራኤል ደም ይጸየፋሉ ፍጻሜው ግን የከበረ የዮሐንስ ራስ በዚች በርኩሰት እጅ እንዳት ያዝ ነው ።

ወይእቲ ወሀበት ለእማ ፤ እሷም ወስዳ ለናቷ ሰጠች ግዳይ ጣለች ። ሐተታ ትስፋም ትፈትልም ነበር ቢሉ ንጉሥ ንግሥት ስትዘልፍ አታፍር የነበረች እንደበት ታተመች ብላ በያዘችው ግልጽልጽ እደ ረገችው ወተሰፍሐት ይእቲ ርእሰ ወሠጠቀት ዓረፍተ ቤት እንዲል ፤ ሁለት ከንፍ አውጥታ ግንቡን ሠጥቃ ወጥታ ጌታ በደብረ ዘይት ሲያስተምር ሂዳ ሰገደች ለት ። ባለሽበት ተወሰነሽ አስተምሪ አላት ። ዐሥራ አምስት ዓመት አስተምራ በብሔረ ዓረቢያ ዐርፋለች ነጋድያን ሲያልፉ እንደ ዕንቍ ስታበራ አይተው የመምራችሁ ራስ ከዚያ ወድቃለች ብለው ለደቀ መዛሙርቱ ነገሯቸው ወስደው ቀብረዋታል ።
እሷስ እንደምን ሁናለች ቢሉ እናትና ልጁ ዘፈን እና ደርሳለን ብለው ሲሄዱ እናቲቱን ምድር ተከፍቶ ዋጣት ልጂቱ እናቴን ብላ እጅዋን ይዛ ቀርታለች ። ከዚህ በኋላ ሄሮድስን ኢይደልወከ ታውስብ ብእሲተ እኁከ ፊልጶስ አለችው ቀድሞ ያልሆነ ሥራ ታሠራ በኋላ ምሥጢር ታወጣንሳ በሰይፍ በላት ብሎ በሰ ይፍ አስመትቷታል ። ገድሉ እንበረ ዋጣት ይላልሳ ቢሉ ሁሉም ተደርጎባታል የሚሰይፍበት ቦታ ከባ

ሕር ፣ አጠገብ ነው በሰይፍ መታት ደም ተከሉዋት ወርዳ ከባሕር ወደቀች እንበሪ ተቀብሉ ዋጣት ። እንድም ገና ሳይቀጣት ፤ የታዘዘ እንበሪ ያዛት የንጉሥ ትእዛዝ አይቀርምና በሰይፍ መትቷት ሩጧል ተቀብሉ ውጧታል ። እንድም እናትና ልጁ ሂደው ሄሮድስን ኢይደልወከ ታውስብ ብእሲተ እኁከ ፊልጶስ እለት ቀድሞ ያልሆነ ሥራ ያሠራ ኋላ ምሥጢር ሆኖም ብሎ እስከንገለቸው አልቀበር ወገን አልንድቃባቸዋል ። እንድም እናትና ልጁ ዘፈን እና ድባለን ብለው ሲሄዱ እናቲቱን ምድር ተከፍቶ ዋጣት አንድ ሰው እጅዋን ይዞ ቀረ ልጂቱ ሂዳ ሄሮድስን ኢይደልወከ ታውስብ ብእሲተ እኁከ ፊልጶስ አለችው ቀድሞ ያልሆነ ሥራ ታሠራ ኋላ ምሥጢር ታወጣ ንሳ በሰይፍ በላት ብሎ በሰይፍ አስመትቷታል ። ያ ሰው እናቷም እንጂ እንዲህ ሁና ሞተች አሰ በምን ዐውቀህ አሉት እጅዋን አሳይቷል ። እሱስ እንደምን ሁነዋል ቢሉ አወጣ የሚባል አግች አሰው ዘማትን እየሰበሰበ ልጂን ያስቀናታል ሆነ ብሎ አገር መታ ቁማር ይህን ሰምቶ ያስደፈረኝ እሱ እኝጂ ነው ብሎ አስጠርቶ ወስዶ አጋዘው ከዚያ እእምሮውን አጥቶ የገዛ አካሉን እየነጨ እየበላ ሽቶ ተልቶ እብሉ ፈንድቶሙ ብሎ ደርቆ ተበላሽቶ ሙቷል ። ወመዊቶ ጻድቅ ይኩንን ረሚዓን ያለው ሊደርስ ሊፈጸም ።

፲፪ ወመጽኡ አርዳኢሁ ወነሥኡ በድኖ ወቀበርዎ ።

፲፪ ደቀ መዛሙርቱ በድኑን ወሰደው ቀበሩት ልቡ ለጻድቅ ውኩል ኪመ አንበሳ እንዲል ርሱን ያገኘ ያገኘናል ሳይሉ ወመጽኡ ዜነውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

መጥተው የዮሐንስን ሞት ለጌታ ነገሩት ።

በእንተ ቀዳሚት አብዝኆተ ኅብስት ።

፲፫ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ተግኅሠ እምህየ በሐመር ውስተ ገዳም እንተ ባሕቲቱ ።
ማር ፯ ፥ ፴፩ ። ሉቃ ፱ ፥ ፲ ፥ ዮሐ ፮ ፥ ፩ ።

፲፫ ጌታም የዮሐንስን ሞት ሰምቶ ከባሕር በመርከብ ተጭኖ ወደ ገዳም ሄደ ። ሐቂታ አርድእተ ዮሐንስ ኀዘንተኞች ናቸውና ለማሳረፍ ፤ አንድም ሰብአ ሁለቱ አርድዕት መጥተው እጋዓንቅ ገረሩ ሉነ ብለውታል ነገሩ እንደምን ነው ስማለት ።
ወሰሚዖሙ ሕዝብ ተለውዎ በእግር እምበሐውርት ሕዝቡ መሄዱን ሰምተው ከሀገሩ ተወጣጥተው የብሱን በእግር ተከተሉት ።

፲፬ ወወፂኦ ርእየ ብዙኃነ እሕዛብ ፤

፲፬ በወጣም ጊዜ ብዙ ሰው አየ ወምህሮሙ ። አዘነላቸው ወአሕየወ ድውያኒሆሙ ፤ ድውያኑን አዳነ ።

፲፭ ወምሴተ ኮነ ቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ወይቤልዎ ገዳም ውእቱ ብሔር ።

፲፭ ሲመሽ በመሸ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው እየሱ ምድረ በዳ ነው ።
ወሰዓትኒ ኃለፈ ፍትሖሙ ለሕዝብ ።
ጊዜውም መሽቷል ሕዝቡን አሰናብታቸው አሉት ከመ ይሑሩ ውስተ አህጉር ወይሳየጡ ለርእሶሙ መብልዓ ወደ ሀገር ገብተው ምግባቸውን ይገዙ ዘንድ ፣ ሐተታ በቤተሰብ ልማድ እሰን እሰን ባዮች ናቸውና እሁን ዝም ብለን ኋላ ለዚህ ሁሉ ሰው ምግብ አቅርቡ ቢለን ከወዴት እናመጣለን ብለው

፲፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አኮ መፍትው ይሑሩ ሩኀቀ ሆሙ ።

፲፮ እንደ ተራቡ ሲሄዱ አይገባም አላቸው እላ አንትሙ ሀብዎሙ ዘይበልዑ ።
የሚበሉትን እናንተ ስጧቸው እንጂ ።

፲፯ ወይቤልዎ አልብነ ዝየ ዘእንበለ ኃምስ ኅብስት ወ፪ቱ ዓሣ

፲፯ ከዚህ ከሁለት ዓሣና ካምስት እንጀራ በቀር ሌላ የለንም አሉት ።

፲፰ ወይቤሎሙ አምጽእዎን ሊተ ዝየ ።

፲፰ ይህስ ካለ ወዲህ አምጡልኝ አላቸው ።

፲፱ ወአዘዞሙ ለሰብእ ይርፍቁ ዲበ ሣዕር ።

፲፱ ከመስኩ ተቀመጡ አላቸው ። ወነሥአ ውእተ ኃምሰ ኅብስተ ወ፪ሆ ዓሣ ወነጸረ ሰማየ ። ሁለቱን ዓሣ አምስቱን እንጀራ ይዞ ወደ ሰማይ አየ ። ሐቲታ ይህን ኅብስት የማበረክትበት ሥልጣን ካንተ ጋራ አንድ ነው ሲል አንድም ታምራት ይደረግልን ባላችሁ ጊዜ ወደ እግዚአብሔር አመልክቱ ለማለት አብነት ለመሆን ። ባረከ ንመበ ቀረሰ ፣ ወፈተተ ፤ አጣቃቀን ። ወወሀቦሙ ለአርዳኢሁ ። ለደቀ መዛሙርቱ ሰጡ ብሎ ሰጣቸው ።
ወአርዳኢሁኒ አቅረቡ ለሕዝብ ደቀ መዛሙርቱም ለሕዝቡ አቀረቡ በሱም እጅ በሐዋርያትም እጅ ሳለ ይበረከት ነበር በረከት መንፈሳዊ እስከ ምጽአት እንዳያቋርጥ ያጠይቃል ።

፳ ወበልዑ ኵሎሙ ወጸግቡ ።

፳ ሁሉም በልተው ጸገቡ ።
ወአግኀዙ ዘተርፈ ፍተታተ ። የተረፈውን አነሡ ወመልዓ ዐሠርተ ወ፪ተ መዛርዓ ምሉእ ።
መሳይምት እክፋረ እስፈሬዳተ ይላል ጋዘና መሶብ ቅርጫት ማለት ነው ።

፳፩ ወእለሰ በልዕዎ የእከሉ ፶፻ ዕደው ዘእንበለ አንስት ወደቅ ።

፳፩ የበሉት ሰዎች ከሴቶችና ከሕፃናት በቀር ፭ሺህ ያህል ይሆናሉ በሀገራቸው ሴትና ወንድ አቀላቅሎ መቍጠር የለምና ዘእንበለ አንስት አለ ፤ ልጆችም አይበሉምና ፤ አንድም ሴቶች ወንድ ሲያያቸው

ያፍራሉና ሕፃናትም ከሚበሉት የሚያበሳሹት ይበዛልና ፲፪ ማንግታቸው ባሥራ ሁለቱ ሥዋማን ባሥራ ሁለቱ ከዋክብት ምሳሌ ፤ በልተውሎት የተረፈው በዘመነ ሐዲስ የተገለጸ ምሥጢር ነው ካራቱ ባሕርያት ካምስተኛ ባሕርየ ነፍስ የተፈጠረ ሰው የሚቻለውን ያህል ነሥቶለት የቀረው በልበ ሐዋርያት እንደ ቀረ ያጠይቃል ። አምስቱ ያምስቱ አዕማደ ምሥጢር ሁለቱ ዓሣ የፍቅረ ቢጽና የፍቅረ እግዚአብሔር አንድም የሥጋው የደሙ ምሳሌ ፤ የተረፈውንም ከማርያም መግደላዊት ቤት አትረውት በዘመነ ደዌ ለፈውስ በዘመነ ቀጠና ለበረከት ይወስዱት ነበር ሲመሽ ያደረገው ጧት ያላደረገው ስለምን ቢሉ ጧት አድርጎት ቢሆን ምሳቸውን የበሉ ምሳትንን በልተን ያልበሉ የበላነው ሳይሰማማን ብንበላው በረከተ እንጂ እንዳይሉ ሁሉም በሚሹበት ጊዜ አደረገው ምሥጢሩ ግን በፍጻሜ ዘመን መንፈሳዊ ምግብ እመግባችኋለሁ ሲል ነው በገዳም ያደረገው ስለምን ቢሉ ለጊዜው ከመንደር አጠገብ አድርጎት ቢሆን ፈጣን ፈጣን ደቀ መዛሙርት አሉትና ከዚያም ከዚያም እያመጡ በላይ በላዩ እየጨመሩበት በረከተ እንዳይሉ ፤ ፍጻሜው ግን እሥራኤል በገዳም ፵ ዘመን መና የመገብሁ እኔ ነኝ ሲል አንድም ከዚህ ዓለም አፍአ በምትሆን በመንግሥተ ሰማያት መንፈሳዊ ምግብ እመግባችኋለሁ ሲል ፤ በመስክ ያደረገው ስለምን ቢሉ ለጊዜው ለልብሳችን በንጠነቀቅ ባንበላው በረከተ እንጂ እንዳይሉ ፤ ምሥጢሩ ግን በምቹ ቦታ በመንግሥተ ሰማይ እኖራችኋለሁ ሲል ፤ በወኃ አጠገብ ያደረገው ስለምን ቢሉ ለጊዜው እጃችንን ባንታጠብ ተጸይፈን ባንበላው በረከተ እንዳይሉ ፤ ምሥጢሩ ግን በጥምቀት በሚገኝ ክብር አከብራችኋለሁ ሲል ።

ዘከመ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ መልዕልተ ማይ ።

፳፪ ወአገበሮሙ ሶቤሃ ለአርዳኢሁ ከመ ይእርጉ ውስተ ሐመር ወይቅድምዎ ኀበ ማዕዶተ ባሕር እስከ ሶበ ይፌንዎሙ ለአሕዛብ ። ማር ፮ ፣ ፵፭ ።

፳፪ ከዚህ በኋላ ሕዝቡ ቢራቡ ያመሳል ቢታመሙ ይፈውሳል ቢሞቱ ያሥነሣል እንዲህ ያለውን ቢያነግሡት ምን ይብላል ነገር ግን ግን ይይዝልናል ብለዋል ሐዋርያት እለን እለን ባዮች ናቸውና እኛ እያለን እኛ እንይዝላችኋለን ብለዋቸዋል፤ ሕዝቡን እስኪያሰናብት ድረስ በመርከብ ተጭነው ባሕሩን ተሻግረው ይቆዩት ዘንድ ተሻግራችሁ ቆዩኝ አላቸው ። አንድም ሲይዙት ወደው ፈርተው ቆመዋል ዐውቆባቸው ሒዱ ብላችሁ አላቸው ።

፳፫ ወእምዝ ፈቲሖ እሕዛበ ዓርገ ውስተ ደብር እንተ ባሕቲቱ ይጸሊ ። ዮሐ ፮ ፣ ፲፭ ።

፳፫ ከዚህ በኋላ ሕዝቡን አሰናብቶ ለብቻው ሊጸልይ ወደ ተራራ ወጣ ። ሐተታ ሰውም አያን ግሥኝ ልዑለ ባሕርይ ነኝ ሲል ይፀሊ ግለቱ ታምራት ተደረገልን ብላችሁ ጸሎታችሁን አትተው ልማ ለት አብነት ለመሆን ።

ወምሴተ ከዊኖ ባሕቲቱ ሀሎ ሀየ ሲመሽ ብቻውን ከዚያ ነበር ።

፳፬ ወሐመርሰ ናሁ ማእከለ ባሕር ሀሎ ።

፳፬ መርከቡ ግን እነሆ ከባሕር መካከል ነበር። ወርኁቅ እምሐይቅ መጠነ እሥራ ወኆቱ ምዕራፍ ከወደቡ ሃያ አምስት ምዕራፍ ያህል ርቆ ነበር ። ወይትሀወክ እሞገድ ።

ከማዕበሉ የተነሣ ይናወጽ ነበር እስመ እምቅድሜሁ ውእቱ ነፋስ ።

ነፋስ ከወደፊቱ ተነሥቶ ነበርና ።

፳፭ ወበራብዕት ሰዓተ ሌሊት መጽአ ኀቤሆሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ የሐውር ዲበ ባሕር ።

፳፭ ባራተኛው ሰዓተ ሌሊት ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በባሕር ላይ እየሄደ መጣ ። ሐተታ፥ ቀዳማይ እካች ካልዓይ እካች ሣልሳይ እካች ራብዓይ እካች አለና ፤ ምሥጢሩ ግን በአራተኛው ክፍለ ዘመን ጌታ ሰው መሆኑን ያጠይቃል ።

፳፮ ወሶበ ርእይዎ አርዳኢሁ እንዘ የሐውር ዲበ ባሕር ደንገጹ ወተሐውኩ እንዘ ይብሉ ምትሐት ውእቱ ።

፳፮ ደቀ መዛሙርቱ በባሕር ሲሄድ ባዩት ጊዜ ምትሐት መስሏቸው ፈሩ ደነገጡ ። ሐተታ ፤ ከሄሮድስ ከተማ ያስወጣነው ሰይጣን በየብስ መጣላት ባይሆንለት ነፋስ አምጥቶ ማዕበል ሞገድ አስነሥቶ ሊያስጥመን መጣ ብለው ። ወእምግርማሁ እውየው እሉን ከመፍራታቸው የተነሣ አሰምተው ተናገሩ ።

፳፯ ወበጊዜሃ ተናገሮሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይብል እነ ውእቱ ወኢትፍርሁ ።

፳፯ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፈጥኖ እኔ ነኝ አትፍሩ አላቸው ።

፳፰ ወአውሥአ ጴጥሮስ ወይቤሎ እመሰ አንተሁ እግዚኦ አዝዘኒ እምጻእ ኀቤከ እንተ ዲበ ማይ

፳፰ ጴጥሮስ መሰስ አቤቱ አንተስ ከሆንህ በውኃው ላይ ወዳንተ እመጣ ዘንድ እዘዘኝ አለው ።

፳፱ ወይቤሎ ነዓ ።

፳፱ ና አለው ።

ወወሪዶ ጴጥሮስ እምዲበ ሐመር ሖረ ዲበ ማይ ይብጻሕ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።

ጴጥሮስ ወደ ጌታ ሊደርስ ከመርከብ ወርዶ በወኃው ላይ ሄደ ሃይማኖቱ ውኃውን እንደ ፍንጃል አጽንቶለት ።

፴ ወሶበ ርእየ ነፋሰ ኃያለ ።

፴ ጽኑ ነፋስ ሲነፍስ ባየ ጊዜ ፈራ ማለት ሃይማኖቱን ሰቀቀ ወአኃዘ ይስጠም ።

ውኃውም ጽንዑን ለቀቀው ይሰጥም ጀመር ።

ወአውየወ ሶቤሃ እንዘ ይብል እግዚእ አድኅነኒ ። ያን ጊዜ አቤቱ አድነኝ ብሎ አሰምቶ ተናገረ ።

፷፩ ወዕቤሃ ሰፍሐ እዴሁ እግዚእ ኢየሱስ ወእኀዞ ።

፷፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያን ጊዜ እጁን ዘርግቶ አወጣው ።
ወይቤሎ ዕውኀደ ሃይማኖት ለምንት ናፈቀ ፤ አንተ ሃይማኖት የሌለህ ለምን ትጠራጠራለህ ከሱ ጋራ ሳለሁ ጥፋት አያገኘኝም በሱ ስም አጸና ዋለሁ አትልም አለው ። ሐተታ ሃይማኖቱ ፍጹም ቢሆን የፍጹም ሥራ ሠራለት ሃይማኖቱ ወጣኒ ቢሆን የወጣኒ ሥራ ሠራበት ። እንደ ሦስቱ መነኰሳት ወደ አባ እንጦንስ ሲሄዱ አንዱ ከመንገድ ሞተ አንዱ ደከሞ ቀረ አንዱን እድ ብርሀት እየመራች ከሱ ዘንድ አድርሳዋለች ። አባ አሞን ይባላል ያንን ሰው ሰዶ አስመጥቶታል ፤ ይ የወጣኒ ይህ የፍጹም ፤

፷፪ ወአሪገ ውስተ ሐመር ውእተ ጊዜ ኀደገ ነፋስ ወኮነ ዛኀነ ።

፷፪ ወደ መርከብ በወጣ ጊዜ ነፋስ ጸጥ አለ ።

፷፫ ወእለሰ ውስተ ሐመር ሰገዱ ሎቱ እንዘ ይብሉ አማን ወልደ እግዚአብሔር አንተ ።

፷፫ በመርከብ ያሉት በውነት የእግዚአብሔር ልጅ ነህ ብለው ሰገዱለት ፤ አንድም ትስብእቱን በማመን ያሉ በውነት የአብ የባሕርይ ልጁ ነህ ብለው ሰገዱለት ።

ዘከመ ዓደወ ውስተ ጌንሴሬጥ ፤

፷፬ ወዓዲዎሙ በጽሑ ምድረ ጌንሴሬጥ ማር፤ ፮ ፤ ፶፫ ።

፷፬ ባሕሩን ተሻግረው ጌንሴሬጥ ደረሱ ። ጌንሴሬጥ ባሕሩ ምድር ወደቡ ነው ።

፷፭ ወአእመርዎ ሰብአ ውእቱ ብሔር ።

፷፭ የዚያ አገር ሰዎች አይተው አወቁት ። ወፈነው ኀበ ኵሉ አድያም ።
ወደ ሀገሩ ሁሉ ላኩ ። ድውይ ያለህ ምዘዝ አሉ ። ወአምጽኡ ሎቱ ኵሎ ሕሙማነ ።
ሕሙማኑን ሁሉ አመጡለት ።

፷፮ ወአስተብቍዕዎ ከመ ይግሥሡ ዘፈረ ልብሱ ።

፷፮ የልብሱን ዘርፍ ይዳሥሡ ዘንድ ማለዱት ። እስመ ኵሎሙ እለ ገሠሥዎ የሐይው ።
የልብሱን ዘርፍ የዳሰሱ ሁሉ ይድኑ ነበርና ።

በእንተ ፈሪሳውያን ወሥርዓቶሙ ።

ምዕራፍ ፲፭ ።

፩ ወእምዝ መጽኡ እምኢየሩሳሌም ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ማር ፯ ፤ ፩ ።

፩ ዝ ሲናገረው የመጣ ነው ። ከዚህ በኋላ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ከኢየሩሳሌም ወደ ጌታ መጡ ።

፪ እንዘ ይብሉ ለምንት ይትዓደው አርዳኢከ ሥርዓተ ረበናት ወትእዛዞሙ ለሊቃነ ካህናት ።

፪ ደቀ መዛሙርትህ የረበናትን ሥርዓት ያሊቃነ ካህናትን ትእዛዝ ለምን ይተላለፋሉ አሉት ። እስመ ኢይትሐፀቡ እደዊሆሙ ሶበ ኅብስተ ይበልዑ እንጀራ በሚበሉበት ጊዜ እጃቸውን አይታጠቡም ነበርና ይላል ጸሐፊው ። ለእመ በሕቁ ኢተሐጽቡ ይላል በማርቆስ ።
እነሱ መላልሰው ደም እስኪሰርበው እስኪመለጥ ካልታጠቡ አይበሉም ነበር ።

፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ለምንት አንትሙኒ ትትዓደው ትእዛዘ እግዚአብሔር በእንተ ሥርዓትክሙ ።

፫ እናንተስ የናንተን ሥራት ለማጽናት የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ለምን ታፈርሳላችሁ አላቸው

፬ ወእግዚአብሔር ይቤ አክብር አባከ ወእመከ ዘፀ ፤ ፳፤፲፪ ። ዘዳ ፭፤፲፮ ። ኤፌ ፮፤፪ ። ዘፀ ፳ ፤ ፳፤፲፯ ዘሌ ፳ ፤ ፱ ምሳ ፳ ፤ ፳ ።

፬ እግዚአብሔርስ እናት አባትህን አክብር ማለት እርዳ ብሏል ።
ወዘአሕሠመ ቃለ ላዕለ አቡሁ ወእሙ ሞተ ለይሙት ባባቱና በናቱ ክፉ ነገር የሚናገር ማለት አባት እናቱን አልረዳም ያለ ሰው ፈጽሞ ይሙት ብሏል ።

፭ ወአንትሙሰ ትብልዎ ዘይቤሎ ለአቡሁ ወለእሙ ሀብተ ቍርባን ዘረባኀከ እምኔየ ።

፭ እናንተ ግን ካኔ ይልቅ ይረባኛል ይጠቅመኛል ያልከው ይርዳህ ያጽባሕ ። አንድም ዘረበሐከ ዘበቍዓከ ይላል ። እኔን ከመውለድህ የተነሣ የበላኸው መሥዋዕት የረባህ የጠቀመህ ነው በለው ትሉታላችሁ ። ሐተታ አዕሩገ እሥራኤል የወለዱት የሚበሉት ያልወለዱት የሚበሉት መሥዕት አለና ፤ አንድም ዘረባሕኩከ ዘበቋዕኩከ ይላል ። እኔን ለቤተ እግዚአብሔር ከመስጠትህ የተነሣ እሰጥሃለሁ ያልኩህ ገንዘብ የቤተ እግዚአብሔር ነው በለው ብላችሁ ላባትና ለናቱ የሚመልሰውን ምላሽ ትነግሩታላችሁ ። ጌታ ሙሴን የግብጻውያንን በኵር እጥፍቼ አውጥቻችኋለሁና በኵር ለኔ ይገባል በኵሩን ለይልኝ አለው ቢያስቈጥር ሁለት እልፍ ከሁለት ሺህ ሁለት መቶ ሰባ ሦስት ሆኑ ። ሌዋውያንን ቈጠራቸው አለው ፤ ሁለት እልፍ ከሁለት ሺህ ሆኑ ፤ በሁለት እልፍ ከሁለት ሺህ በኵር እኒህን ተቀብ ያለሁ የሁለት መቶ ሰባ ሦስቱን ዋጋ አምስት አምስት ቀመት እየተቀበልህ ከቤተ እግዚአብሔር አግባ ገንዘብ ያለው ገንዘብ እየሰጠ ልጁን ይውሰድ ፤ ገንዘብ የሌለው ልጁን ይስጥ ብሎታል ገንዘብ ያለው እየሰጠ ልጁን አስቀርቷል ገንዘብ የሌለው ልጁን ሰጥቷል ፤ የመቶው አምስት መቶ የመቶው አምስት መቶ የስሳው ሦስት መቶ ያሥሩ አምሳ የሦስቱ አስራ

እምስት ሺህ ከሦስት መቶ ሰላሳ አምስት ይሆናል ። ከዚህ በኋላ አባት እየደከመ ገንዘቡ እያለቀበት ልጅ ገንዘብ እያገኘ ይሄዳል ምንቱ ለቤተ እግዚአብሔር ብሰጠው ልጄ አይደስምን ርዳኝ ልበለው ብሎ ይሄዳል እንዲህ ብለህ መልስለት ብለው ተንኰል ያስተምሩታልና ።

፬ ዘብሂል ኢያከብር አባሁ ወእሞ፤

፭ እንዲህ ማለት እናት አባቱን አይርዳ ማለት ነው ።

ወሠዓርክሙ ቃሉ ለእግዚአብሔር በእንተ ሥርዓትክሙ ።

የናንተን ሥርዓት ለማጽናት የእግዚአብሔርን ትእዛዝ አፈረሳችሁ ።

፯ ኦ መደልዋን ሠናየ ተነበየ ኢሳይያስ ላዕሌክሙ ።

፯ እናንት ግብዞች እሙነ ቢል ነው ኢሳይያስ በናንተ እውነት ነገርን ተናግሮባችኋል ።

፰ እንዘ ይብል ዝ ሕዝብ በከናፍሪሆሙ ያከብሩኒ ። ኢሳ ፳፱ ፥ ፲፫ ማር ፯ ፥ ፯ ።

፰ እነሀ ሕዝብ በአፋቸው እናከብርሃለን ይሉኛል ማለት እናምንብሃለን ይሉኛል ።
ወልቦሙሰ ነዋኃ ይርኅቀ እምኔየ ።
በልቡናቸው ግን አስረዝመው ይርቃሉ ማለት ዕሩቅ ብእሲ ይሉኛል ።

፱ ወከንቶ ያመልኩኒ ።

፱ በሐሰት ያመልኩኛል ።
እንዘ ይሜህሩ ትምህርተ ሥርዓታተ ሰብእ ።
የሰውን ሥርዓት እያስተማሩ ማለት ሰው መሬሽ ትምህርት እያስተማሩ ።

፲ ወጸውዖሙ ለሕዝብ ወይቤሎሙ ስምዑ ወለብው ከመ አኮ ዘይበውእ ውስተ አፍ ዘያረኵሶ ለሰብእ ። ማር ፥ ፯ ፥ ፲፬ ።

፲ ሕዝቡን ጠርቶ ሰውን የሚጎዳው ባፍ የሚገባው እንዳይደለ ስሙ ዕወቁ አላቸው ።

፲፩ አላ ዘይወፅእ እምውስተ አፍ ውእቱ ያረኵሶ ለሰብእ ።

፲፩ ካፍ የሚወጣው እሱ ይጎዳዋል እንጂ ።

፲፪ ወእምዝ ቀሪቦሙ አርዳኢሁ ይቤልዎ ኢተአምርሁ ከመ ፈሪሳውያን ሰሚዖሙ ቃለከ አንጐርጐሩ ።

፲፪ ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው ፈሪሳውያን ትምህርትህን ሰምተው እንዳዘኑ አታውቅምን አሉት ። እንደዚህማ ከሆነ ጅብም ቀበሮም ቢበሉ አይጐዳማ ብለው ነው ሐዋርያት በነገሩ እያሉበት ፈሪሳውያንን ጥግ አድርገው ይጠይቁታል ።

፲፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ኵላ ተክል እንተ ኢተከላ አቡየ ሰማያዊ ትሴረው ዮሐ፥ ፲፭ ፥ ፪ ።

፲፫ ሰማያዊ አባቴ ያልሠራት ሥራ ሁሉ ታልፋለች ትመር ትለፍ አላቸው ።

፲፬ ኅድግዎሙ እስመ ዕውራን እሙንቱ መምህርተ ዕውራን ። እምርህት እምህርት ይላል ።

፲፬ የዕውራን አእምሮ መሪዎች መምሮች ናቸውና ተዋቸው አለዕውር ዕውረ ለእመ መርሀ ክልኤሆሙ ይወድቁ ውስተ ግብ ። ዕውር ዕውሩን ቢመራው ሁለቱም ከጉድጓድ ይወድቃሉ ዕውር ዕውርን ቢስቶል ተያይዘው ገደል እንዲሉ ።

፲፭ ወአውሥአ ጴጥሮስ ወይቤሎ ንግረነ ዘንተ ምሳሌ ማር፥ ፯ ፥ ፲፯ ።

፲፭ ጴጥሮስ መሰለ ይሆነ ነገር ተርጉመህ ገልጸህ ንገረን አለው ፩ኛ ከመጽሐፈ ዲቤየ ሠለስቱ ምሳሌያት ካለው አንዱን ነገር እንዳለው ።

፲፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስን ዓዲሁ አንትሙኒ ኢለበውክሙኑ ዘንተ ።

፲፮ ጌታም እናንተም ገና ይህን አላወቃችሁትም አላቸው ።

፲፯ ኢተአምሩኑ ከመ ኵሉ ዘይበውእ ውስተ አፍ ውስተ ከርሥ ይትገመር ፤

፲፯ ባፍ የሚገባው ሁሉ በሆድ እንዲወሰን አታውቁምን ወጽመ ይትከዐው ።
ጥቂት ቀይቶም አትዲፈስ ወጽቡ ይትከዓው ይላል በማርቆስ ። እሥር እሥሩ እንዲፈስ ሐተታ የበላነውን የጠጣነውን መሬት ይሸከማል ውኃ ያረጥባል ። እሳት እንደ ገና ያበስላል ነፋስ አረቄ አረቄውን ወደ ላይ ይዞ ይወጣል የሰው አሥራው ፮ ፪፻፹ ነው ፳፬ ለስ ሳው ስሳው ለስድስት መቶው ያቀብላሉ በዚህ ጊዜ አሥር እሥሩ ቁልቁል ይወርዳልና ።

፲፰ ወዘሰ ይወፅእ እምውስተ አፍ እምልብ ይወፅእ ።

፲፰ በአፍ የሚያፈጣው ግን ከልብ ይወጣል ወውእቱ ያረኵሶ ለሰብእ ። ይህ ሰውን ይጎዳዋል ሰውን የሚጐዳው ይህ ነው ።

፲፱ እስመ እምውስተ ልብ ይወፅእ ሕሊና እኩይ

፲፱ ከልብ ክፉ አሳብ ይነቃልና ዘውእቱ ቀቲል እኩይ ያለውን ይተረትራል ያውም ነፍስ መግደል ነው ወዝሙት ፥ ዝሙት ነው ስርቅ ፤ መስረቅ ፤ ስምዕ በሐሰት ። በሐሰት መመስከር ነው ።

፳ ወፅርፈት

፳ ስድብ ነው ። እሉኬ ዘያረኵስዎ ለሰብእ ሰውን የሚጎዱት እሊህ ናቸው እሊህ ሰውን ይጐዱታል ። ወዘእንበለ ተሐፅቦ እድስ በሊዕ ኢያረኵሶ ለሰብእ ።
እጅ ሳይታፀቡ መብላትስ ሰውን አይጎዳውም በይውም መሬት ተበይውም መሬት ምን ይጎዳል ።

፳፩ ወወፂአ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ ተግኅሠ ውስተ ደወለ ጢሮስ ወሲዶና ።

፳፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚያ ወጥቶ ወደ ጢሮስና ወደ ሲዶና አውራጃ ገባ ።

በእንተ ከነናዊት ።

፳፪ ወናሁ መጽአት ብእሲት ከነናዊት እም ውእቱ አድዋል ፤

፳፪ ማር ፯፥፳፭ ። ከነናዊት ከነዓናዊት ይላል ከነናዊት ቢል የከናኔዎን ወገን ከነዓናዊት ቢል የከ ነዓን ወገን የምትሆን ሴት ከዚያ አውራጃ መጣች ።
እንዘ ትጸርኅ ወትብል መሀረኒ ወልደ ዳዊት ።
ወልደ ዳዊት አቤቱ እዘንልኝ እያለች እየጮኸች ።
እስመ ለወለትየ እኩይ ጋኔን አኃዛ ።
ልጄን ቢስ ጋኔን አድሮባታልና ፤ ወየዓብዳ አእምሮ ዋን ያሳጣታልና ፤

፳፫ ወኢያውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ቃለ ፤
፳፫ ጌታም ነገር አልመለሰላትም ወቀረቡ እርዳኢሁ አስተብቍዕዎ እንዘ ይብሉ ፈንዋ ለዛቲ ብእሲት ።
ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው ይህቺን ሴት አሰናብታት ብለው ማለዱት ።
እስመ ትጸርሕ በድኅሬነ። በኋላ በኋላችን ትጮሃለችና ሐተታ ፤ ትምህርት ታስፈታለች ብለው ። አንድም ወይ ተናግረው እያስደርጉ ወይ እያሰናብቱ ትላለች ብለው ብታሳዝናቸው ።
፳፬ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ኢተፈነውኩ ዘእ ንበለ ኀበ አባግዕ ዘተኃጕላ ለቤተ እስራኤል፤ ማቴ ፲፥፮ ።
፳፬ ትምርት መምህር አጥተው የተጎዱ እስራ ኤልን ሳስተምር ሰው ሁኜለሁ እንጂ ፤ ያለዚያ ሰው አልሆንኩም ብሎ መለሰላቸው ።
፳፭ ወተረብባ ሰገደት ሎቱ ። ማር ፯ ቍ. ፳፮ ።
፳፭ ቀርባ ሰገደችለት እንዘ ትብል እግዚእየ ርድአኒ አቤቱ ጌታዬ እዘንልኝ ብላ ።
፳፮ ወአውሥአ ወይቤላ ኢኮነ ሠናየ ነሚአ ኅብስተ ውሉድ ወወሂብ ለከለባት ።
፳፮ የልጆችን ዳቦ ለውሻ መስጠት አይገባም ማለት ለእስራኤል የማደርገውን ታምራት ለአሕዛብ አላደርገውም አላት ።
፳፯ ወትቤሎ እወ እግዚእ ።
፳፯ አቤቱ አዎን ውሻ ነኝ አለችው ከለባትኒ ን ይበልዑ እምፋርፋራት ዘይወድቅ እማዕደ አጋዕ ዝቲሆሙ ።
ውሾችም እንጂ ውሾችም እኮን ከጌታቸው ማዕድ የወደቀ ፍርፋሪን ይመገባሉ ። እንደዚህስ ሁሉ ለእስ ራኤል ደጋጉን ታምራት ብታደርግላቸው ለኔ ጥቃቅኑን ታምራት አታደርግልኝም አለችው ።
፳፰ ወእምዝ አውሥአ ።
፳፰ ከዚህ በኋላ መለሰ ።
ወይቤላ ብእሲቶ ዓቢይ ሃይማኖትኪ ።
አንቺ ሆይ ሃይማኖትሽ ታላቅ ነው ማለት ፍጹም ነው ።

ይኩንኪ በከመ ተአመንኪ ።
እንዳመንሽ ይደረግልሽ አላት ሐተታ ሦስት ነገር አግኝቶላታል ሃይማኖት ትሕትና ጥበብ ፤ ሃይማኖት ያድንልኛል ብሎ መምጣት ። ትሕትና በውሻ ቢመ ስላት አዎን ውሻ ነኝ ማለት ጥበብ መስሎ ቢነግራት መስሎ መናገር ነው ።
ወሐይወት ወለታ እምእይቲ ጊዜ ።
በዚያን ጊዜ ልጅዋ ዳነች ።

ዘከመ ተፈወሱ ካልአን ሕሙማን ።

፳፱ ወኃሊፈ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ በጽሐ ኀበ ሐይቀ ባሕር ዘገሊላ ፤

፳፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚያ አልፎ ከገሊላ ባሕር ወደብ ደረሰ ።
ወዓርገ ደብረ ነበረ ህየ ፤
ከዚያ ከተራራ ላይ ወጥቶ ተቀመጠ ።
፴ ወቀርቡ ኀቤሁ አሕዛብ ብዙኃን እንዘቦ ምስሌሆሙ ሐንካሳን ወጽዉራን ወጽሙማን ወዕው ሳን ። ኢሳ ፥ ፴፭ ፥ ፭ ።
፴ ብዙ ሰዎች ዕውራንን ሐንካሳንን ደንቆሮ ዎችን ልምሾ የሆኑትንም ይዘው መጡ ።
ወባዕዳንሂ ብዙኃነ ድውያነ ሌሎችን ብዙ ድውያንን አመጡ ።
ወገደፍዎሙ ታሕተ እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ። ከእግሩ አፈሰሷቸው ፤ ወፈወሶሙ ፤ አዳናቸው ።
፴፩ እስከ ሶበ አሕዛብ ያነክሩ እንዘ ይሬእዩ ከመ በሐማን ይትናገሩ ።
፴፩ በሐማን ሥጋ በታምራት በሐማን ነፍስ በትምህርት ሲናገሩ ።
ወሐንካሳን የሐውሩ ። ሐንካሳነ ነፍስ በትምህርት ሲሄዱ ወዕውራን ይሬእዩ ፤ ዕውራነ ሥጋ በታምራት ዕውራነ ነፍስ በትምርት ሲያዩ አይተው አሕዛብ አስኪያደንቁ ድረስ ፤
ወሰብሕዎ ለአምላከ እስራኤል ዘወሀበ ዘከመዝ ሥል ጣነ ለሰብእ ለሰው እንዲህ ያለ ሥልጣን የሰጠ ማሌት አላመኑም ቢሉ ደግ ነቢይ ያስነሣልን ብለው አምነ ዋል ቢሉ ሰራሱ ድኅነት ይሻ የነበረ ሥጋን ከባሕርይ ልጅህ ጋራ አዋሕደህ ድኅነትን እንዲያድል ያደረግ ኸው ብለው የእስራኤልን አምላክ አመሰገኑ ።
በእንተ ካልዕ አብዝኆተ ኅብስት ።
፴፪ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ወይቤሎሙ ያምህሩኒ እሉ ሕዝብ ማር፥ ፰ ፥ ፩ ።
፴፪ ደቀ መዛሙርቱን ጠርቶ እሊህ ሰዎች ያሳ ዝኑኛል አላቸው ። እስመናሁ ሠሉስ መዋዕል እምዘ በልዑ እከለ እህል ከበሉ ሦስት ቀናቸው ነውና ።
ወአልቦሙ ዘይበልዑ ።
የሚበሉት የላቸውምና ።

ወኢይፈቅድ እፈንዎሙ ርኁባኒሆሙ ።
እንደተራቡ ላሰናብታቸው አልወድም ።
ከመ ኢይመጽልው በፍኖት ።
ከጐዳና በስልት እንዳይወድቁ

፴፫ ወይቤልዎ አርዳኢሁ እምአይቴ እንከ ለነ በገዳም ኅብስት ዘያጸግብ ለዘመጠነዝ ሕዝብ ።

፴፫ ለዚህን ያህል ሰው የሚበቃ እንጀራ ከወዴት እናገኛለን አሉት ።

፴፬ ወይቤሎሙ ሚመጠን ሐባውዝ ብክሙ ።
፴፬ ምን ያህል እንጀራ አላችሁ አላቸው ።
ወይቤልዎ ሰብዑ ።
ሰባት እንጀራ ። ወኅዳጥ ዓሣ ። አንድ ዓሣ ሎምቢ ዓሣ አለ አሉት ። ወገባሩ ኅዳጥ እንዲል ።

፴፭ ወአዘዞሙ ለሕዝብ ይርፍቁ ዲበ ምድር ።
፴፭ ሕዝቡን ከምድር ተቀመጡ አላቸው ።
፴፮ ወነሥአ ሰቡዓ ኅብስተ ወዓሣኒ ።
፴፮ ሰባቱን ኅብስት ዓሣውንም ያዘ ።
ወይእቲ ጊዜ እእኰተ ።
ያን ጊዜ አመሰገነ ።
ባረከ ፤ ገመሰ ፤ ወፈተተ ፤ ቈረሰ። ወወሀቦሙ ለአዳርኢሁ ፤ ሰጡ ብሎ ለደቀ መዛሙርቱ ሰጣቸው ።

፴፯ ወበልዑ ኵሎሙ ወጸግቡ ።
፴፯ ሁሉም በልተው ጠገቡ ። ወዘተርፈ ፍተታተ አግኃሡ ሰብዓተ አስፈሬዳተ ምሉአ ።
መሳይምተ መዛርዓ አከፋፈ አስፈሬዳተ ይላል ።
የተረፈውን ፯ መሶብ ዕንቅብ ቅርጫት ማለት ነው መልተው አነሱ ።

፴፰ ወእለሰ በልዕዎ የአከሉ ፬ሺህ ዘእንበለ አንስት ወደቅ ።
፴፰ የበሉት ሰዎች ከሴቶችና ከሕፃናት በቀር አራት ሺህ ያህል ይሆናሉ ፤ ሐተታ እንዳለፈው ምዕራፍ ፲፬ ቍ ፳፩ ፤ ሰባት ማንሳታቸው ፀሰባቱ ዕለታት በ፯ ልዑካን ምሳሌ ፬ሺህ ሰዎች በልተውለት ፬ተረፈው በዘመነ ብሉይ ከተገለጸው ምሥጢር ከራቱ ባሕርያት የተፈጠረ ሰው የተቻለውን ያህል ኣሥቶለት የተረፈው በልበ ነቢያት እንደቀረ ያጠይቃል አምስተኛ አልጨመረላቸውም በግዕዘ እንስሳ ናችሁ ሲል እንጀራውም ገብስ ነው ገብስ ምግበ እንስሳ ነው በግዕዘ እንስሳ አላችሁ ሲል ። እንድም ገዳም በሄዳችሁ ጊዜ ምግብ አታሻሽሉ ለማለት ፤ ካምስቱ አሥራ ሁለት ከሰባቱ ሰባት አነሡ እሉ ጥቂቱን ብዙ ብዙውን ጥቂት የማደርግ እኔ ነኝ ሲል ።

፴፱ ወፈቲሖ እሕዛበ ዓርገ ውስተ ሐመር ወሖረ ውስተ ደወለ መጌዶል ።
፴፱ ሕዝቡን አሰናብቶ በመርከብ ተጭኖ ወደ መጌዶል ሄደ ።

ዘከመ ኀሠሡ ትእምርተ እምሰማይ ።

ምዕራፍ ፲፮ ።

፩ ወመጽኡ ኀቤሁ ፈሪሳውያን ወሰዱቃውያን እንዘ ያሜክርዎ ወይሴአልዎ ትእምርተ እምሰማይ ያርእዮሙ ማር ፰ ፥ ፲፮ ።

፩ ከዚህ በኋላ ሰዱቃውያንና ፈሪሳውያን ሲፈትኑት ከሰማይ ምልክት አሳየን ሲሉት መጡ ሐተታ እንዳለፈው ፥ ምዕ ፲፪ ቍ ፴፰ ።

፪ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እምከመ መስየ ወኮነ ሕዋየ ትብሉ ጽሕወ ብሔር ። ሉቃ ፲፪፡ ፶፬ ።

፪ የመሸ ድግዝግዝታም የሆነ እንደሆነ ብራ ያድራል ትላላችሁ ።
እስመ ያጥየሐይሕ ሰማይ ። ሰማይ አልፎ አልፎ በቀይ ሰብኳልና ።

፫ ወእምከ ጽሕወ ትብሉ ዮምሰኬ ይዘንም ።
የነጋ እንደሆነ ግን ዛሬ ይዘንማል ትላላችሁ ።
እስመ ያጥየሐይሕ ሰማይ ድሙነ ።
ደመና ዳር እስከ ዳር ገጥሞ ይፈልቃልና ።
አ መደልዋን ።
እናናት ግብዞች ።
፫ ገጸ ሰማይሰ ተአምሩ ፈኪሮ ማቴ ፲፪ ፥ ፴፱ ።
ዮሐ ፪ ፥ ፩ ።
፫ የሰማዩን ፊት ማለት የሰማይን ግብር እናውቃለን ትላላችሁ ወተአምረ መዋዕልሰ እፎ ኢተአምሩ በዘመናችሁ የተደረገውን ታምራት አለማወቃችሁ ስለምን ነው ። እንድም እምከመ መስየ ብሰሀ መልስ ሥጋ የለበስ ተስፋ የደረሰ እንደሆነ ። ጽሕወ ብሔር ሥጋ አለበሰም ተስፋ አልደረስም ትላላችሁ እስመ ያጥየሐይሕ ሰማይ ፤ የተነገረው ትንቢት የተቆጠረው ሱባዔ ገና ነውና ብላችሁ ። ወእምከመ ጽሕወ ሐሳዊ መሲሕ ግን የተወለደ እንደሆነ ገና ዛሬ ሥጋ ለበሰ ተስፋ ደረሰ ትላላችሁ ። በሐሰት ተጨፍና አምላክ ነኝ ብሏልና ። አመደልዋን ፥ እናንት ግብዞች ገጸ ሰማይሰ ፤ ሰማያዊ ልደቴን እናውቃለን ትላላችሁ ወተአምረ መዋዕልሰ ። በዘመናችሁ የተደረገውን ምድራዊ ልደቴን አለማወቃችሁ ስለምን ነው ። ወይቤሎሙ ትውልድ ዕሉት ወዘማ ትእምርተ ተኃሥሥ ። ዕምቢተኛ ሴሰኛ ቤተ አይሁድ ምልክትን ትሻለች ። ወትእምርትስ ኢተውህባ ዘእንበለ ትእምርተ ዮናስ ነቢይ ምልክት ግን ዮናስ ካደረገው ምልክት በቀር አይሰጣትም ። ም ፲፪ ቍ ፴፱ ተመልከት።
ወእምዝ ኃደጎሙ ወሖረ ።
ከዚህ በኋላ ትቷቸው ሄደ ።
በእንተ ብኁአ ፈሪሳውያን ወሰዱቃውያን ።
፭ ወበጺሖሙ አርዳኢሁ ማዕዶተ ረስዑ ነሢአ ኅብስተ ።

፭ ደቀ መዛሙርቱ ወንዙን ተሻግረው ከሄዱ
[illegible] እንጀራ ረሱ ማለት አለመያዛቸውን ዐወቁ ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ዑቁ ወተዓ
ቀቡ እምብሑአ ለፈሪሳውያን ።

፮ ጌታ ከፈሪሳውያን እርሾ ተጠበቁ አላቸው
[illegible] እንጋ ኅብ
[illegible] ።

፯ እርሱ በርሳቸው አስበው እንጀራ አልያዝን
ምና ተንተቡ ይለናል አሉ ።

፰ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ
ምንተ ትሔልዩ በበይናቲክሙ አ ሕጹፃነ ሃይማኖት ።
፰ ጌታም አውቆባቸው እናንት ሃይማኖት የሌ
ላችሁ እናንት በናንት ለምን ታስባላችሁ አላቸው ።
እስመሁ ኅብስት አልብክሙ ። እንጀራ አልያዛችሁ
ምና ተንተቡ እልኋችሁን ።

፱ ገዲሁ ኢትሌብዉኑ ወኢትዘከሩ ሀአመኃምስ
ኅብስት እለ ለ፭ ምእት ። ማቴ ፲፬ ፣ ፲፱ ዮሐ ፮ ፣ ፱ ።
፱ እምስት እንጀራ አበርክቼ ላምስት ሺህ ሰው
ባበላሁ ጊዜ የተደረገውን አታስተውሉም አታስቡ
ትምን ወሚመጠነ መዛርዓ አግኃሥክሙ ምን ያህል
ቅርጫት አነሣችሁ ።
ወይቤልዎ ፲ወ፪ተ ።
አሥራ ሁለት አነሣን አሉት ። አንድም ዘአግኃሥ
ክሙ ያነሣችሁት ምን ያህል ነው አላቸው ዐሥራ
ሁለት ነው አሉት ።

፲ ወአመ ሰብዑ ኅብስተ እለ ለ፬ ምእት ።
ማቴ ፲፭ ፣ ፴ ።
፲ ሰባቱን እንጀራ አበርክቼ ላራት ሺህ ሰው
ባበላሁ ጊዜ የተደረገውን አታስቡታውሉም ። ሚመ
ጠነ አስፈሬዳተ አግኃሥክሙ ። ምን ያህል እንቅብ
አነሣችሁ አላቸው ፯ አነሣን አሉት ዘአግኃሥክሙ
ያነሣችሁት ምን ያህል ነው ሰባት ነው አሉት ።

፲፩ እፎ ዘኢትሌብዉ ከመ አኮ በእንተ ኅብስት
ዘእቤለክሙ ተዓቀቡ እምብሑአሙ ለፈሪሳውያን ወሰ
ዱቃውን ።

፲፩ እንዲህ ከሆነ ተዓቀቡ ያልኋችሁ በቁሙ
ከፈሪሳውያን ከሰዱቃውያን እርሾ እንዳይደለ እንደ
ምን አታውቁ አላቸው ።

፲፪ ወእምዝ ለበዉ ከመ አኮ ዘይቤሎሙ ይት
ዓቀቡ እምነ ብኅዓተ ኅብስት ።

፲፪ ከዚሀ በኋላ ተጠበቁ ያላቸው ስለ እርሾ
እንዳይደለ ዐወቁ ።
አላ እምነ ትምህርተ ፈሪሳውያን ወሰዱቃውያን ።
ከፈሪሳውያን ከሰዱቃውያን ትምህርት ነው እንጂ ።

## በከመ ተአመነ ጴጥሮስ ።

፲፫ ወበጺሖ እግዚእ ኢየሱስ ብሔረ ቂሳርያ
ዘፊልጶስ ። ማር ፰ ፣ ፳፯ ሉቃ ፱ ፣ ፲፰ ።

፲፫ ጌታ የፊልጶስ ግዛት ከምትሆን ከቂሳርያ
አውራጃ በደረሰ ጊዜ በቂሳር ቂሳርያ ተብላለች በጢ
ባርዮስ ጥብርያዶስ በፊልጶስ ፊልጵስዩስ እንደተባ
ለች ። ይሀ ፊልጶስ የእስክንድር አባት የሄሮድስ
ወንድም ሐዋርያው ፊልጶስ ከሰባቱ ዲያቆናት አንዱ
ነው ።
ተስእሎሙ ለአርዳኢሁ እንዘ ይብል መነ ይብለኒ
ሰብእ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
ወልደ ዕጓለ እመሕያው እኔን ሰው ማን ይለኛል
ብሎ ደቀ መዛሙርቱን ጠየቃቸው ።

፲፬ ወይቤሉ ቦ እለ ይብሉከ ዮሐንስሃ መጥምቀ

፲፬ ዮሐንስ መጥምቅ ነው የሚሉህ ዮሐንስ
መጥምቅ እንደሆንክ የሚናገሩልህ አሉ ። ንጽሕና
ውን አይተው ።
ወካልዓን ይብሉከ ኤልያስሃ ። ኤልያስ ነው የሚሉህ
አሉ ኤልያስ እንደሆንክ የሚናገሩልህ አሉ ድንግል
ናውን አይተው ወመንፈቆሙ ይብሉከ ኤርምያስ ።
ኤርምያስ ነህ የሚሉህ አሉ ። ኤርምያስ እንደሆንክ
የሚናገሩልህ አሉ ። ቅድስናውን አይተው ።
ወእመ አኮ ፩ዱ እምነቢያት ቀደምት ።
ይህም ባይሆን ከቀደሙ ነቢያት ማለት ሙሴን ኢያ
ሱን ነው የሚሉህ አሉ አሉት ታምራቱን አይተው ።

፲፭ ወይቤሎሙ አንትሙኬ መነ ትብሉኒ ።

፲፭ እናንተስ ማን ትሉኛላችሁ ። ከዊን ይላል
አብነት በምን ሀልዎት አለ ትሉኛላችሁ አላቸው ።

፲፮ ወአውሥአ ስምዖን ጴጥሮስ ወይቤ አንተ
ውእቱ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ሕያው ። ዮሐ
፮ ፣ ፷፱—፸ ።

፲፮ ጴጥሮስ አስከ ክርስቶስ ተብሎ የተነገረልሀ
የሕያው የእግዚአብሔር ልጅ ነህ ብሎ መለሰ ፤

፲፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፤

፲፯ ጌታም መለሰ ።
ወይቤ ብፁዕ አንተ ስምዖን ወልደ ዮና ፤
የዮና ልጅ ስምዖን ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ ።
እስመ ኢከሠተ ለከ ዘሥጋ ወደም ፤
የኔን አምላክነት ሥጋዊ ደማዊ አእምሮ አልገለጸል
ሀም ። አላ አቡየ ዘበሰማያት ፤ ሰማያዊ አባቴ ገለጸ
ልህ እንጂ ፣ አንድም ሥጋዊ ደማዊ መምህር አላስተ
ማረህም ስማያዊ አባቴ አስተምሮሃል እንጂ ።

፲፰ ወአነኒ እብለከ ከመ አንተ ኰኵሕ ፤ ዮሐ
፩ ፣ ፵፪ ።

፲፰ እኔ መሠረት ነህ ብየ መሠረት እንደሆንህ
እናገርልሃለሁ፤ በጥንተ ስብከት አንተኬ ትሰመይ ኬፋ
ብሎት ነበርና ያ እንደተፈፀመለት ለማጠየቅ መሠ
ረትነቱ የሃይማኖት የሹመት ወዲበ ዛቲ ኰኵሕ አሐ
ንጽ ለቤተ ክርስቲያንየ ።
ባንተ መሠረትነት ምእመናን አንጻቻለሁ አጸናቻለሁ።

ወአናቅጸ ሲኦልኒ ኢይኄይልዋ አጋንንት አያናውጹ ዋትም ማለት ድል አይነሱዋትም ። ሐተታ አናቅጽ አላቸው በበር ይወጡበታል ይገቡበታል እንዲገቡ በት ጻድቃን ድል ነሥተው ይገቡባቸዋልና እንዲ ወጡበት ኃጥአን ድል ተነሥተው ይወጡባቸዋልና፡

፲፱ ወእሁበከ መራኁተ ዘመንግሥተ ሰማያት ኢሳ፡፳፪ ፤ ፳፪ ዮሐ ፳ ፡ ፳፫ ።

፲፱ የመንግሥተ ሰማያት መክፈቻ ማለት ከመ ንግሥት ሰማያት የምታወጣበት ወደ መንግሥተ ሰማ ያት የምታገባበት ሥልጣን እሰጥሃለሁ ፡ የኪዳን የሹ መት ፡ ዘአሰርከ በምድር ይኩን እሱረ በሰማያት ። በምድር ያሰርኸው በሰማይ የታሰረ ይሆን ዘንድ ። ወዘፈታሕከ በምድር ይኩን ፍቱሐ በሰማያት ። በምድር የፈታኸው በሰማይ የተፈታ ይሆን ዘንድ አንድም ዘአሰርከ በል ፡ በምድር አንድ ያደረግኸው በሰማይ አንድ ይሆን ዘንድ ። ወአሰረ ፪ተ ህላዌ ያተ እንዲል ወዘፈታሕከ በምድር የለየኸው በሰማይ የተለየ ይሆን ዘንድ ። አንድም ዘአሰርከ በል ፡ ኢደ ለዎሙ ለእለ አሰርናሆሙ እንዲል ፡ በምድር የቀጸ ርኸው በሰማይ የተቀጸረ ይሆን ዘንድ ። ወዘፈታሕከ ያሰናበትኸው በሰማይ የተሰናበተ ይሆን ዘንድ ። ይሁን ብየ እንዲሆን እሁበከ በል ።

፳ ወእምዝ አዘዞሙ ለአርዳኢሁ ከመ ኢይን ግሩ ወኢለመኑሂ ከመ ውእቱ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

፳ ከዚህ በኋላ ክርስቶስ እንደሆነ እንዳይናገሩ ለደቀ መዛሙርቱ ነገራቸው ።

ዘከመ ተነበየ ኢየሱስ ሕማሞ ።

፳፩ ወእሚሃ አኃዘ እግዚእ ኢየሱስ ይንግሮሙ ለአርዳኢሁ ፤ ከመ ሀለዎ ይሑር ኢየሩሳሌም ።

፳፩ ከዚያ ቀን ጀምሮ ከዚያ ቀን ወዲህ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ኢየሩሳሌም ይሄድ ዘንድ እንዳለው ለደቀ መዛሙርቱ ይነግራቸው ጀመር ።

ወብዙኀ የሐምምዎ ረበናት ሽማግሎች ብዙ መከራ እንዲያመጡበት ።

ወሊቃነ ካህናት ።

የካህናትም አለቆች ።

ወጸሐፍት ፤

ጸሐፍትም መከራ እንዲያመጡበት ፤

ወይትቀተል ፡ እንዲሞት ፤

ወበሣልስት ዕለት ይትነሣእ ።

በሦስተኛ ቀን እንዲነሣ ይነግራቸው ጀመር ።

፳፪ ወተሠጥዎ ጴጥሮስ ።

፳፪ ጴጥሮስም መለሰለት ።

ወይቤሎ ሐሰ ለከ እግዚኦ ይኩን ላዕሌከ ዝንቱ ። አቤቱ ይህ ሞት ባንተ ሊደረግ አይገባም አለው ። ።

፳፫ ወተመይጦ ይቤሎ ለጴጥሮስ ሑር እምድ ኅሬየ ሰይጣን ። ማርቆስ ፰ ፡ ፴፫ ።

፳፫ ወደ ጴጥሮስ ተመልሶ ሰይጣን ከኋላየ ወግድ አለው ። ጽኑ ባላጋራዬ ሲል ነው ራስ አይቶ የሚመጣ ጠላት ጽኑ ነውና ፡ ወአቀሞ ዓዴርሃ ሰይ ጣነ ላዕለ ሰሎሞን እንዲል ፡ አንድም የምእመናን የነቢያት ጽኑ ባላጋራቸው ሲል ፡ ጌታችን አይሙት ማለት ነቢያትን ሐሰተኞች ማድረግ ነውና ፡ ምእመ ናንም አይዳኑ ማለት ነውና አንድም ከብፅዓን ወደ ተግሣፅ ተመልሶ ሑር አለው ። ከዚያ አንደ ጊዜ ግብሩ ብፁዓን ሰጪው ከዚህም አንደ ጊዜ ግብሩ ሰይ ጣን አለው ። አንድም በጴጥሮስ እንጻር ሰይጣንን ሲገሥጽ እንዲህ አለ በአንጻረ በለስ ረገማ ለኃጢአት እንዲል ፡ እስመ ኮንከኒ ሊተ ዕቅፍተ ፡ መሰናክል ሆንህብኛልና ፡ እስመ ኢትሄሊ ዘእግዚአብሔር ዘእ ንበለ ዘሰብእ ።

ሙቶ ፈርሶ በስብሶ ይቀራል ፤

ትላለህ እንጂ ይነሣል አትለኝምና ፡ አንድም ከሰው ሹመት ሽልማት ትሻለህ እንጂ እግዚአብሔር የሚ ያወርስህን ክብር አትሻምና ።

ዘከመ ይደልዎ ለክርስቲያን ጎዲገ ርእሰ በእንተ ክርስቶስ ።

፳፬ ወእምዝ ይቤሎሙ እግዚእ ለአርዳኢሁ ዘይፈቅድ ይትልወኒ ይጽላዕ ነፍሶ ያጥብዕ ወይንሣእ መስቀሎ ሞቱ ወይትልወኒ ። ማቴ ፲ ፡ ፴፰ ሉቃ ፱ ፡ ፳ ፫ ፡ ፲፬ ።

፳፬ ከዚህ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሊከተለኝ ማለት ሊመስለኝ የሚወድ ሰውነቱን ለመከራ አሳልፎ ሰጥቶ ጨክኖ ነፍሱን ከሥጋው የሚለይበትን መከራ ተቀብሎ በመከራ ይምሰለኝ ብሎ ለደቀ መዛሙርቱ ነገራቸው ።

፳፭ ወዘሰ ይፈቅድ ያድኅና ለነፍሱ ለይግድፋ ሉቃ.፲፯ ፡ ፴፫ ።

፳፭ ዮሐ .፲፪፡ ፳፭ ። ሰውነቱን ሊያድናት የወ ደደ ይጣላት ።

ወዘገደፋ ለነፍሱ በእንቲአየ ይረክባ ፡ ስለኔ የጣላት ሰውነቱን ያገኛታል ። ትርጓሜ እንዳለፈው ም. ፲ ቍ፡ ፴፰ ።

፳፮ ወምንተ ይበቊዖ ለሰብእ ለእመ ኮሎ ዓለመ ረብሐ ወነፍሶ ኃጕለ ።

፳፮ ሰው ዓለሙን ሁሉ ቢያተርፍ ማለት ፡ ዓለሙን ሁሉ ቢገዛ በነፍሱ ከተጎዳ ምን ይረበዋል ወምንተ እምወሀበ ሰብእ ቤዛሃ ለነፍሱ ምረረ ገሃነምን ጣዕመ መንግሥተ ሰማይን ባያውቅ ነው እንጂ ። ቢያውቅማ ለነፍሱ ቤዛ ምን በሰጠ ነበር ፡ ምንተ እምኢወሀበ ምን አልሰጥ ባለ ነበር ።

፳፯ እስመ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ይምጻእ በስብሐተ አቡሁ ምስለ መላእክቲሁ ። ግብ. ሐዋ. ፲፯ ፡ ፴፩ ። ሮሜ ፪ ፡ ፯ ።

፳፯ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ለክርስቶስ መላእክትን አስከትሎ ባባቱ ጌትነት ይመጣ ዘንድ አለውና ።
ወእሜጌ የዓሥዮ ለዙሉ በከመ ምግባሩ ።
ለሁሉም እንደ ሥራው ይሰጠዋል ።

፳፰ አማን እብለክሙ ቦ እምእለ ሀለዉ ይቀውሙ ዝየ እለ ኢይጥዕምዋ ለሞት እስከ አመ ይሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በመንግሥቱ ። ማር ፱ ፡ ፩ ። ሉቃ ፱ ፡ ፳፯ ።

፳፰ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ በጌትነቱ መጥቶ እስኪያዩት ድረስ ከዚህ ቁመው ካሉት የማይሞቱ እንዳሉ በዕውነት እነግራችኋለሁ ሐተታ ደብረ ታቦር እላለፈም ቢሉ የተመቸ አልፋዋል ቢሉ ዮሐንስን ያያል ።

ዘከመ ተወለጠ ኢየሱስ በደብረ ታቦር ።

ምዕራፍ ፲፯ ።

፩ ወእምድኅረ ስሱ መዋዕል ፡ ነሥአሙ እግዚእ ኢየሱስ ለጴጥሮስ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ እኁሁ ወአዕረጎሙ ደብረ ነዋኅ እንተ ባሕቲቶሙ ማር ፱ ፡ ፩ ። ሉቃ ፱ ፡ ፳፰ ።

፩ ስለ ሦስት ነገር ያመጣዋል ። አማን እብለክሙ ቦ እምእለ ሀለዉ ይቀውሙ ዝየ እለ ኢይጥዕምዋ ለሞት እስከ አመ ይሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በመንግሥቱ ብሎ ነበርና ከዚያ ለማያያዝ ፡ እሞታለሁ ቢለው ቅዱስ ጴጥሮስ ሐስ ለከ ብሎት ነበርና ሎቱ ስምዕም ለማለት በባሪያ ቃል የተነገረውን በጌታ ቃል ለማስመስከር ፡ ከመ ፩ዱ እምነቢያት ብለውታልና፡ እግዚአ ነቢያት እንደሆነ ለማጠየቅ የስድስተኛው ድኅር ሰባት ነው ። በቂሳርያ መኑ ይብልዎ ሰብእ ለወልደ እመሕያው ባላቸው በሰባተኛው ቀን ሦስቱን ባለሟሎቹን ለብቻቸው ወደ ተራራ ይዟቸው ወጣ ። ሐተታ ዝቅ ብሎ ቢሆን በነቁ ነበር ። ከፍ ብሎ ቢሆን ባዘኑ ነበርና እመሀይ ቀን ሽቶ ። ባለሟሎቹስ እነማናቸው ቢሉ ጌታ እንደ ሰው ወረተኛ ነውን ዋንተ ባለሟሎቹ ናቸው ። እነዚህንስ ባለሟል ያደረገበት ምንድነው ቢሉ እልታወቀም ሙሴን ለምስፍና አሮንን ለክህነት የመረጠበት ግብር እንዳልታወቀ አንድም ታውቋል ክሀደት በኒህ ጸንቷልና ፡ ጴጥሮስ እሞታለሁ ቢለው ሐስ ማለቱ ሹመት ሽልማት ሽቶ አይደለምን ፡ እኒያስ አሐድን በየማንከ ወአሐድን በፀጋምከ ማስታቸው ሹመት ሽልማት ሽተው አይደለምን ።

አንድም ለፍቅሩ ይሳሳሉና በፍቅሩ ይናደዳሉና ጴጥሮስ እመውት ቢለው ሐስ ማለቱ ቢናደድ አይደለምን እኒያስ ትክሉኑ ሰትየ ጽዋዕ ዘአነ እስቴ ቢላቸው እወ ንክል ማለታቸው ቢናደዱ አይደለም ለፍቅሩ ይሳሳሉና በፍቅሩ ይናደዳሉና ፡ ስምንቱን ከእግረ ደብር ትቶ ሦስቱን ይዟቸው ወጥቷል ። ስለምን ቢሉ በይሁዳ ምክንያት ። ይዞት እንዳይወጣ ያእትትዎ ለኃጥእ ከመ ኢይርአይ ስብሐተ እግዚአብሔር ተብሎ ትንቢት ተነግሮበታል ፡ ለይቶም እንዳይተወው ከምሥጢረ መንግሥቱ ቢለየኝ ከሞቱ ከገባሁበት ባለ ነበርና ፡ ነገር ግን በርእሰ ደብር ለሦስቱ የተገለጠ ምሥጢር በእግረ ደብር ላሉ ለስምንቱም ተገልጧል ። በደብረ ሲና ለሰባ ሊቃናት የተገለጸ ምሥጢር በከተማ ላሉ ለኤልዳድ ለሙዳድ እንደተገለጸ ። ተራራ የወንጌል ምሳሌ ተራራ ሲወጡት ያጥራል ከወጡት በኋላ ግን ጭንጫውን ግጫውን ሲያሳይ ደስ ያሰኛል ። ወንጌልም ሲማሯት ታጽራለች ። ከተማሯት በኋላ ግን ጽድቅና ኃጢአት ለይታ ስታሳውቅ ደስ ታሰኛለችና ። አንድም ተራራ የመንግሥተ ሰማያት ተራራን በብዙ ጻዕር እንዲወጡት መንግሥተ ሰማይንም በብዙ መከራ ያገኟታልና ፡ እስመ በብዙኅ ጻማ ሀለወነ ንባእ ለመንግሥተ እግዚአብሔር እንዲል ፡ ተራራውንም ሐዋርያት በሲኖዶስ ታቦር ብለው እንሥተውታል ። በታቦር ያደረገው በሌላ ያላደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ትንቢት ታቦር ወአርሞንኤም በስመ ዚአከ ይትፌሥሑ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌ ባርቅ ሲሳራን ድል ነሥቶበታል ። ጌታም በልበ ሐዋርያት ያደረ ሰይጣንን ድል ይነሣበታልና ፡ በተራራ ያደረገው በመንደር ያላደረገው ስለምን ቢሉ በመንደር መካከል አድርጎት ቢሆን ምሥጢር አፈሳ በሆነ ነበርና ። ስለዚህ በተራራ አደረገው ።

፪ ወተወለጠ አርአያሁ በቅድሜሆሙ ።

፪ መልኩ በፊታቸው ተለወጠ ። ወእምድኅረ ውላጤ ይመጽእ ካልእ ውላጤ እንዳለው ያለ አይደለም ሦስቱ ከንድ ከስንዝር እካል ምሉእ ብርሃን ሁኖዋል ጽጌያት ከአዕጹቃቸው እንዲፈነዱ ።
ወአብርሃ ገጹ ከመ ፀሐይ ።
እንደ ፀሐይ ብሩህ ሆነ ።
ወአልባሲሁኒ ኮነ ጸዓዳ ከመ በረድ ።
ልብሱ እንደ በረድ ጸዓዳ ሆነ ። ይህ ሁሉ ጌትነቱን ገለጸ ማለት ነው ።

፫ ወናሁ አስተርአዩ ሙሴ ወኤልያስ እንዘ ይትናገሩ ምስሌሁ ።

፫ ሙሴ ኤልያስ ከሱ ጋራ ሲናገሩ ተሰሙ ። ሙሴ ኤልያስ መሆናቸው በምን ታውቋል ቢሉ ሙሴ በልቁትነቱ ኤልያስም በጸጉርነቱ ። በነፍስስ ልቁትነት የሌም ካባ ዕንጦንስ ዘንድ እንኳ ሲላክ ዘፍነው በነፍሱ ይለዋል በእካለ ነፍስ መጥቶ ተርጕሞላቸዋል፡

ብሎ ብሩህ ሁኖ ተወልዷል ይህ ጺጋው ነው አይኑ ማውምና ኤልያስን ዘጥብሉል በአጽርቅተ እሳት ይለዋል ይህ ጸጋው ነው አይነማውምና በዚህ ታውቋል ። አንድም በነጋገራቸው ታውቋል ። ሙሴ የኔን የሙሴን ጌታ ማን ሙሴ ይልሃል እግዚአ ሙሴ ይበሉህ እንጂ ፤ ኤልያስም የኔን የኤልያስን ጌታ ማን ኤልያስ ይልሃል እግዚአ ኤልያስ ይበሉህ እንጂ ሲሉ ተሰምተዋል ። እንድም ሙሴ እኔ ባሕር ብከፍል ጠላት ብገድል ደመና ብጋርድ መና ባወርድ እሥራኤልን ከከፋታቸው መልሶ ማዳን አልተቻለኝም ሳንተ ማን መልሶ ማዳን ይቻልሃል ። ኤልያስም እኔ ሰማይ ብለጉም እሳት ባዘንም እሥራኤልን ከከፋታቸው መልሶ ማዳን አልተቻለኝም ላንተ ግን መልሶ ማዳን ይቻልሃል ሲሉ ተሰምተዋል ። አንድም ሞውቱ ለሕያው ሕያው ለምውት ሲጸልዩ ተሰምተዋል ። ምውቱ ለሕያው አቤቱ ሁሉን ለንስሐ ሳታበቃ በሞት ባትጠራው የሚሻል ይመስለኛል ሲል ሕያው ለምውት የሰው ፍቅር አገብሮህ ልትሞት ወደዚህ ዓለም መጣህን ሲል ። እነዚህንስ ያመጣበት ምክንያት ምንድነው ቢሉ ሙሴ ፊትህን ሳየው እወዳለሁ ቢለው ገጽየስ ኢያስተርኢ ለከ ወድኅረስ ትሬኢ ። መሥዋዕት ሁኜ በምቀርብበት ጊዜ በደብረ ታቦር እገለጽልሃለሁ ብሎት ነበርና ፤ ኤልያስንም አንተስ ትከውነኒ ሰምዓ በደኃሪ መዋዕል ብሎት ነበርና ። ስለምን ሁለቱን ከነቢያት ሦስቱን ከሐዋርያት አመጣ ቢሉ ተራራ የቤተ ክርስቲያን ምሳሌ ፤ በቤተ ክርስቲያን ብሉይ ሐዲስ እንዲነገሩ ለማጠየቅ ፣ አንድም የመንግሥተ ሰማያት ምሳሌ፤ ነቢያትም ሐዋርያትም አንድ ሁነው እንዲወርሷት ለማጠየቅ ። ከመዓስባን ሙሴን ከደናግል ኤልያስን አመጣ ። ደናግል እንጅ መዓስባን አይወርሷትም ባሉ ነበርና ደናግልም መዓስባንም አንድ ሁነው እንዲወርሷት ለማጠየቅ ። ከምውታን ሙሴን ከሕያዋን ኤልያስን አመጣ ። ንሕነ ሕያዋን የተባሉና ኢንበጽሖሙ ለምውታን የተባሉ አንድ ሁነው እንዲወርሷት ለማጠየቅ ።

፬ ወአውሥአ ጴጥሮስ ወይቤሎ ለእግዚእ ኢየሱስ እግዚኦ ሠናይ ለነ ሀልዎ ዝየ ።

፬ ቅዱስ ጴጥሮስ ከዚህ መኖር ለኛ በጎችን ነው አለው ። አንተ የወትሮ ሥራህን እየሠራህ ብንራብ እያመሰኸን ብንታመም እየፈወስኸን ብንሞት እያነሣኸን ። ሙሴ የወትሮ ሥራውን እየሠራ ደመና እየጋረደ መና እያወረደ ባሕር እየከፈለ ጠላት እየገደለ ። ኤልያስ የወትሮ ሥራውን እየሠራ ሰማይ እየለጐመ እሳት እያዘነመ ዝናም እያቆመ በዚህ መኖር ለኛ በጐእችን ነው ወእመሰ ትፈቅድ ንግበር በዝየ ፫ተ ማኅደረ ።

ሐስ ለከ ቢለው ገሥጾት ነበርና ቢሆንስ የኔን ነገር አትወድልኝም እንጅ ብትወድልኝስ ከዚህ ሦስት አዳራሽ እንሥራ ። አሐደ ለከ ። አንዱን ላንተ ። ወአሐደ ለሙሴ ፣ አንዱም ለሙሴ ። ወአሐደ ለኤልያስ ፣ አንዱን ለኤልያስ ። ሐተታ እንዚህን ቀኛዝማችነት ግራዝማችነት ይሾሙ ያለ ይመስላል ። የሱን አልተናገረም ቢትወደድነት የለመነ ይመስላል ።

፭ ወእንዘ ይትናገሩ መጽአ ደመና ብሩህ ወጸለሎሙ ። ማቴ ፫፥፲፯ ፣ ፪ ጴጥ ፩፥፲፯ ።

፭ ይኽን ሲናገሩ ብሩህ ደመና መጥቶ ጋረዳቸው ወሰበ ቦኡ ውስተ ደመና ይላል በሉቃስ ንጉሥ በትርሽማ ድንኳን ሳለ በላይ መላጛ ድንኳን ቢተክሉበት ንጉሥ ከድንኳን ገባ እንዲባል ።
ወናሁ መጽአ ቃል እምውስተ ደመና ዘይብል ። ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ዘቦቱ ሠመርኩ ። ከደመናው ልመለከበት የወደድሁት ለተዋሕዶ የመረጥሁት ልጄ ይህ ነው የሚል ቃል ተሰማ ።
ወሎቱ ስምዕዎ እሞታለሁ ቢላችሁ አትሞትም አትበሉት ተቀበሉት ።

፮ ወሰሚዖሙ አርዳኢሁ ወድቁ በገጾሙ ።

፮ ደቀ መዛሙርቱ ይኽን ሰምተው ደነገፁ ። ወፈርሁ ጥቀ ።
ፈጽመው ፈሩ ። ሐተታ ዮሐንስን ደነገጠ አላለውም እነዚህን ደነገጡ አለ እንደምነው ቢሉ ።
ዮሐንስ ፣ አልተጠራጠረምና ደንገጠ እላለውም እኒህን ተጠራጥረዋልና ደነገጡ አለ ። አንድም አታስደንግጥ ያለው አያሸደነግጥምና ዮሐንስ አልደነገጠም አለ ። አታስደንግፅ ያላለው ያስደነግጣልና እኒህን ደነገፁ አለ ።

፯ ወቀርበ እግዚእ ኢየሱስ ወገሠሦሙ ።

፯ ጌታ ቀርቦ ያዛቸው ወይቤሎሙ ተንሥኡ ወኢትፍርሁ ።
አይዟችሁ ተነሡ አላቸው ።

፰ ወአንሥኡ አዕይንቲሆሙ ።

፰ ዓናቸውን አቅንተው አዩ ። ወአልቦ ዘርእዩ ወኢመነሂ ዘእንበለ እግዚእ ኢየሱስ ባሕቲቱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን አዩ እንጂ ማንንም ማን አላዩም ።

፱ ወእንዘ ይወርዱ እምደብር አዘዞሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይብል ኢትንግሩ ወኢለመኑሂ ዘርኢክሙ እስከ አመ ወልደ ዕጓለ እመሕያው እሙታን ይትነሣእ ።

፱ ጌታም ከተራራው ሲወርዱ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ከሙታን እስኪነሣ ድረስ ያያችሁትን የሰማችሁትን አትናገሩ አላቸው ። ሐተታ ውዳሴ ከንቱ አይሻምና የሚያምኑበት ጊዜ አልደረሰምና እስከ ትንሣኤ ፣ አንድም መከራን ወደ ኋላ አድርጎ ክብርን መናገር አይገባምና ። አንድም

ሰውን ሁሉ እየሰበሰበ መንግሥቴን ላሳያችሁ እያለ ምትሐት ያሳያል ሆን ባሉት ነበርና ።

፲ ወተስእልዎ አርዳኢሁ እንዘ ይብሉ እፎ ይብሉ ጸሐፍት ኤልያስ ሀለወ ይምጻእ ቅድመ ፤

፲ መውደቃቸው ሞት መነሣታቸው ትንሣኤ መስሏቸው ጸሐፍት ኤልያስ እስቀድሞ ይመጣ ዘንድ እንዳለው የሚናገሩት እንደምን ነው አሉት ።

፲፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።

፲፩ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ እወ ኤልያስ ይቀድሞ መጺአ ።
አዎን ኤልያስ አስቀድሞ ይመጣል ።
ወያስተራትዕ ኵሎ ።
ሁሉን ያከናውናል ።
፲፪ ወባሕቱ እብለክሙ ከመ ኤልያስ ወድአ መጽአ ።
፲፪ ነገር ግን ኤልያስ ፈጽሞ መጥቶ እንዳለ ወኢያእመርዎ ።
እንዳላወቁት ማለት እንዳልተቀበሉት እነግራችኋለሁ ወባሕቱ ገብሩ ላዕሌሁ ኵሎ ዘከመ ፈቀዱ ።
የወደዱትን አደረጉበት እንጂ ማለት ዓሰበ ዘማ አደረጉበት እንጂ ወከማሁ ሰወልደ ዕጓለ እመሕያውኒ ሀለዎ ይሕምም እምኔሆሙ ።
ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርቶስም እንደሱ ከሳቸው መከራ ይቀበል ዘንድ አለው ።
፲፫ ወእምዝ አእመሩ አርዳኢሁ ከመ በእንተ ዮሐንስ ይቤሎሙ ።
፲፫ ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ ገብሩ ላዕሌሁ የነገራቸው ስለ ዮሐንስ መጥምቅ እንደሆነ ዐወቁ ዮሐንስ መጥምቅ ነው አሉ ።

በእንተ ወርኃዊ ዘይጸዓር ።

፲፬ ወበጺሖ ኀበ አሕዛብ ይቤሎሙ ምንትኑ ትትኀሠሥዎሙ ማር.፱፥፲፯ ሉቃ ፱፥፴፰ ።
፲፬ ክሕዝቡ በደረሰ ጊዜ ለምን ታዳክሟቸዋላችሁ አላቸው ። ሐተታ ስምንቱን መምህራችሁ ወዴት ሄደ እያሉ ሲያደክሟቸው ቆይተዋል ። ወቀርበ ኀቤሁ ብእሲ ወሰገደ ሎቱ እንዘ ይትመሐለል ወይብል ተሣሃል ሊተ ወልድየ ።
ክነገር ያልገባ ሰው ነው ለብቻው ቆይቶ ሰገደለት እቤቱ ልጄን አድንልኝ አለው ።
እስመ እኩይ ጋኔን እኃዞ ቢስ ጋኔን አድሮበታልና ። ወበአርእስተ አውራኅ ይሣቅዮ ወርኅ እያየ ይጥለዋልና ምልአተ ወርኅ ሲሆን ደም ይመላል ብርድ ብርድ ይላል ደዌ ይቀሰቀሳልና ጨረቃ እንጂ ባታመልኩ ነው ለማለት ።
ወመብዝኅቶስ ያወድቆ ውስተ እሳት ወቦ እመ ያወድቆ ውስተ ማይ ።
ይልቁንም ብዙ ጊዜ ከእሳት ከወኃ ይጥለዋል ።

፲፮ ወአምጽእክዎ ኀበ አርዳኢከ ።
፲፮ ያድኑልኛል ብየ ወደ ደቀ መዛሙርትህ አመጣሁት ።
ወስዐኑ ፈውሶቶ ።
ማዳን ተሳናቸው ።

፲፯ ወእምዝ አውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፯ ከዚህ በኋላ ጌታችን መለሰ ፡ ወይቤ ኦ ትውልድ ኢአማኒት ወእሉት ።
እንቢተኛ አሉተኛ ትውልድ ሐዋርያት ፤
እስከ ማዕዜኑ እሄሉ ምስሌክሙ ።
እስከመቼ ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ።
ወእስከ ማዕዜኑ እትዔገሠክሙ እስከ መቼ ዝም እላችኋለሁ አላቸው ። ሐተታ ንጉሥ በሌለበት ጊዜ ከንቲባ መሥራት መቅጸት እንዲገባው ባያውቁ መምህራችን በሌለበት ጊዜ አይቻለንም ብለዋልና እስከ መቼ ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ንጉሥ ባለ ጊዜ ከንቲባ መሥራት መቅጻት እንዳይገባው ባያውቁ መምራሀችን ሳለ ነው እንጂ ብለዋልና እስከ መቼ ዝም እላችኋለሁ ሳለሁማ እኔ አደርገው የለ ምን ሲል እንዲህ አለ ።
አምጽእ ሊተ ዝየ ።
ወዲህ አምጣልኝ አለ ።

፲፰ ወገሠጾ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፰ ጌታ ገሠጸው ማለት ፃዕ መንፈስ ርኩስ አለው ።
ወወፅአ ጋኔኑ እምላዕሌሁ ፡ ጋኔኑ ከሱ ወጣ ።
ወሐይወ ወልዱ በይእቲ ሰዓት ልጁ በዚያች ሰዓት ዳነ ።

፲፱ ወእምዝ ቀረቡ አርዳኢሁ እንተ ባሕቲቶሙ ይቤልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ በእንተ ምንት ንሕነ ስዐነ አውፅኦቶ ።
፲፱ ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ ለብቻቸው ቀርበው እኛ ማስወጣት ስለምን ተሣነን አሉት ።

፳ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ በእንተ ሕጸተ ሃይማኖትክሙ ሉቃ ፲፯ ፥ ፯ ።
፳ ስለ ሃይማኖታችሁ ማነስ ማለት ሃይማኖት ባይኖራችሁ ነዋ አላቸው ።
አማን እብለክሙ እመ ብክሙ ሃይማኖት መጠነ ኅጠተ ሰናፔ ።
አካኋን አይሻም ፍጽምት ናት ፍጹም ሃይማኖት ቢኖራችሁ ወትብልዎ ለዝ ደብር ፍልስ እምዝየ ኀበ ከሀ ወይፈልስ ይህን ተራራ ክዚህ ተነሥተህ ወዲያ ሂድ ብትሉት እንዲሄድ ።
ወእልቦ ዘይሰአነክሙ ።
ቸግሯችሁ የሚቀር እንደሌለ በውነት እነግራችኋለሁ ። ሐተታ ሊጸፍ ባይቻል ነው እንጂ በሱ ጊዜ ተደርጓል በሱ ጊዜስ አልተደረገም በአብርሃም ሶር ያዊ ጊዜ የተደረገውን መናገር ነው ። ስሊቀ ጳጳሱ

አንድ አይሁዳዊ ወዳጅ ነበረው ከንጉሥ ተንባላት ወዳጆች ናቸው ያም ሲጠይቅ ያም ሲጠይቅ እየሄዱ ይገናኛሉ እየተከራከሩ ሊቀ ጳጳስ አይሁዳዊን ምላሽ ያሳጣዋል ከዕለታት አንድ ቀን ለብቻው ገብቶ ነገር ሠራ የኒህ የክርስቲያን ሃይማኖታቸው እንጂ ደካማ ነው አለው ። እንኪያ እየተከራከሩ ምላሽ ያሳጧችኋልሳ አለው ።

ለዚህማ ምልክት እንጅል የምትባል መጽሐፍ አለ ቻቸው ለእመ ብከሙ ትላለች ። አድርጉ ብትላቸው አይሆንላቸውም አለው እሱን ሲያገኘው ነገሩን ያጣ ዋል ነገሩ ትገዝ ሲለው እሱን ያጣዋል ከዕለታት ባንድ ቀን እሱ ባለበተ ነገሩ ትዝ አለው አባቴ የምጠይ ቅህ ኑሮኝ አንተን ሳገኝህ ነገሩን እያጣሁት ነገሩ ትዝ ሲለኝ አንተን እያጣሁህ ነበር ። አሁን ግን ነገሩም ትዝ ብሎኛል አንተም መጥተሃል አለው ። ምንድነው አለው እንጅል የምትባል መጣፍ አለቻ ችሁን አለው ። አዎን አለው እንዲህ ትላለች አለው እምን አለው ታደርጋላችሁን አለው ፤ አዎን አለው ሚመጠን አእላፍ ክርስቲያን የዚህ ሁሉ ክርስቲያን ንማ ሃይማኖት ተራራ አያህልምን እንኪያስ አድር ገህ አሳየኝ አለው ቀን ስጠኝ አለው ሦስት ቀን ስጠው ሂዶ ከእመቤታችን ሥዕል አመለከተ ልጂ እንዲህ ያለው ሳንተ አይደረግልህም የሚደረግልት ስምዖን ዘአሐቲ ዓይኑ አለ ተርታ ሰው መስሎ ከገቢያ ዕን ጨት ሲሸጥ ታገኘዋለህ ሂደህ ንገረው እኔን አለችህ በለው ያለዚያ በጅ አይልህም አለችው ቢሄድ እንደ ነገረችው አገኘው እየፈራ ሂዶ በስተኋላው ልብሱን ያዘው አወቀብኝ ብሎ ተቆጣው ምን አድ ርግ ትለኛለህ በሀገርህ ድኃ አይኖርምን አለው እመ ቤታችን ልካኝ ነው ብሎ ነገሩን ገልጦ ነገረው ። እንኪያስ እኔን አትግለጠኝ ክርስቲያንን ባንድ ወገን አሕዛብን ባንድ ወገን ሰብስበህ ካህናቱን ልብሰ ተክ ህኖ አልብሰህ ቆየኝ አንተ እኔ የምሠራውን ሥራ እያየህ ሥራ ሕዝቡ አንተ የምትሠራውን እያዩ ይሥሩ ፵፩ ኪርያላይሶን አድርሰው ሰግደው ሲነሡ ተራራው ተነሣ በውስጡ ተያዩ ሲሰግዱ ይመለ ሳል ሲነሡ ይነሣል ሦስት ጊዜ እንዲሁ አድርገው ባራተኛው እየወጣ የሚያውካቸው ውኃ ነበር ሂደህ ተጋረድላቸው ብሎት ቦታውን ለቆ ሂዶ ተጋርዶ ላቸዋል እንድም ለእመ ብከሙ ብለህ መልስ ፤ ሰመዮ ደብረ በእንተ ትዕቢቱ ምንትኑ ዝ ደብር ቅድመ ዘሩባቤል እንዲህ ፤ ደብር የተባለ ዲያብሎስ ነው ፍጹም ሃይማኖት ቢኖራችሁ ሰይጣንን ውጣ ብትሉት ይወጣል ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፳፩ ወዝንቱ ዘመድ ኢይመፅእ ዘእንበለ በጾም ወጸሎት ።

፳፩ ይህ አብሮ አደግ ጋኔን ካልጾሙ ካልጸለዩ አይወጣም ። እንድም ይህ ደካማ ባሕርያችሁ ካልጾመ ካይልጸለየ ጋኔን ሊያወጣም ። እንድም ወዘ መደ ፍጥረትኒ መስዎ ለአስሐትያ እንዲል ፤ ይህ የፍጥረት ወገን የሚሆን ሰይጣን ካልጾሙ ካልጸለዩ አይወጣም ።

፳፪ ወእንዘ ያንሶሱ ውስተ ገሊላ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ያግብእዎ ውስተ እደ ሰብእ። ማቴ ፳፥ ፲፰ ማር ፱፥ ፴፩። ሉቃ ፱ ፥ ፵፬ ።

፳፪ ጌታ በገሊላ ሲመላለስ የሰውን ልጅ ያሲዙት ዘንድ አላቸው ።

፳፫ ማለት እያዛለሁ ። ወይቀትልዎ ።

፳፫ እሞታለሁ ። ወአመ ሣልስት ዕለት ይት ነሣእ፤ በሦስት ቀን እነሣለሁ አላቸው ። ወተከዙ ጥቀ አርዳኢሁ ለሚየሙ ዘንተ ።
ደቀ መዛሙርቱ ይኸን ሰምተው ፈጽመው አዘኑ ።

በእንተ ውሂበ ጸባሕት ።

፳፬ ወበጺሖሙ ቅፍርናሆም መጽኡ እለ ጸባ ሕተ ዲናር ይነሥኡ እምኀበ ጴጥሮስ ።

፳፬ ቅፍርናሆም በደረሰ ጊዜ ከጴጥሮስ ግብር የሚቀበሉ ሰዎች መጡ ።
ወይቤልዎ ሊቅክሙሰ ኢይጸብሕኑ ጸባሕተ ።
መምህራችሁ አይገብርም አሉት ።

፳፭ ወይቤ እወ ።

፳፭ የኔ መምህር አዎን ይገብራል አዎን አይገ ብርም አላቸው ።
ወበዊአ ውስተ ቤት አቅደመ እግዚእ ኢየሱስ ብሂ ሎቶ ከቤት በገባ ጊዜ ጌታ አስቀድሞ ጠየቀው ።
ምንተ ትብል አ ስምዖን ።
ስምዖን ሆይ ምን ትፈርዳለህ ነገሥተ ምድር እምኀበ መኑ ይነሥኡ ጸባሕተ ወጋዳ ።
ነገሥታት ያመት ግብርና እጅ መንሻ ከማን ይቀበ ላሉ ።
እምኀበ ውሉዶሙኑ ወሚመ እምኀበ ነኪር ።
ከልጆቻቸው ነው ወይም ከሌላ አለው ።

፳፮ ወይቤ እምኀበ ነኪር ።

፳፮ ከሌላ ነው እንጅ ልጆቻቸውማ ይገብሩን ያስገብሩን አለው ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ውሉ ዶሙሰ እንጋ አግዓዝያንኑ እሙንቱ ።
እንኪያ ልጆቻቸው ነጻ ናቸዋ አለው እኔም ነፃ ነኝ ሲል ነው እንክስ ግዑዝ ውእቱ ወልድ ብሎታል ሊቁ ።

፳፯ ወባሕቱ ከመ ኢያንጐርጕሩ ሑር ውስተ ባሕር ወደይ መቃጥነ ።

፳፯ ነገር ግን እንዳያዝኑ ከባሕር ሂደህ መረብ ህን ጣል ።
ወዘቀዳሚ አሥገርከ ዓሣ ንሣእ ወክሥት አፉሁ ።
መጀመሪያ የያዝኸውን ዓሣ ወስደህ አፉን ክፈት ማለት ሆዱን ቅደደው ።

ወትረክብ ውስቴቱ ስጠ.ጥራስ ዘውእቱ ፩ቱ ድር ኅም ።
በውስጡም አራት ድሪም ታገኛለህ ። ኪያሁ ንሣእ ወሀቦሙ ሀየንቴየ ወህየንቴከ ፡
እሱን ወስደህ ፪ን ስለኔ ፪ን ስላንተ ስጣቸው እለው ሐተታ ቁመቱ ፳ ፳ እይደለም ቢሉ በዘመን ብዛት ቀርቷል ከገበረስ አጉድሎም አይገብር ብሎ የሚዛን ደገንት ነው ፡ ባሕር የዚህ ዓለም ሰጠ.ጥራስ የወን ጌል ምሳሌ ፪ ድርሀም ፪ ክፍል ሁና መጻፉን ያጠይቃል ወንጌልን ተገዘብ አድርገህ ሀየንቴየ አሕዛብን ሀየንቴከ እሥራኤልን አስተምር ሲል ነው ከዚህም እንደ ሰውነቱ ገበረ እንደ እምላክነቱ ባሕ ርን አስገበረ ።

በእንተ ክርስቲያናዊት ትሕትና ።

ምዕራፍ ፲፰ ።

፩ ወበይእቲ ሰዓት ቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ለእ ግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይብሉ መኑ እንጋ የዓቢ በመን ግሥተ ሰማያት ። ማር ፱፡ ፴፫ ። ሉቃ ፱፡ ፵፮። ማቴ ፡ ፲፱ ፡ ፲፩ ። ከዚያ ብፅዓን ሰጠው ከዚህ ገበረለት ሾመው እንጂ ሾመው ተባብለዋል ።

፪ በዚያች ሰዓት ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው በመንግሥት ሰማይ በላይ የሚሆን ማነው አሉት ፡

፫ ወጸውዓ ሕፃነ ወአቀመ ማእከሎሙ ።
ብላቴና ጠርቶ በመካከላቸው አቆመው ።

፬ ወይቤ እማን እብለከሙ እመ ኢተመየጥ ከሙ ከመ ዝንቱ ሕፃን ኢትበውኡ ውስተ መንግ ሥተ ሰማያት ። ፩. ቆሮ ፲፬ ፡ ፳ ።

፭ ተመልሳችሁ ከየውሃት ጠባይዓዊ ደርሳችሁ እንደዚህ ሕፃን ካልሆናችሁ መንግሥተ ሰማይ እንዳትገቡ በእውነት እነግራችኋለሁ ።

፮ ወዘአትሐተ ርእሶ ከመ ዝንቱ ሕፃን ውእቱ የዓቢ በመንግሥተ ሰማያት ።

፯ እንደዚህ ሕፃን ሁኖ ራሱን ያዋረደ የመን ግሥተ ሰማይ ባለቤት ይሆናል ። ይህም ትሕትና የሚያስተምርበት ሕፃን አግናጥዮስ ምጥው ለአንበሳ ነው ። በአንጾኪያ የጴጥሮስ ሦስተኛ ሁኖ ተሹሟል ።
፰ ወዘሂ ተወክፈ ፩ደ ሕፃነ ዘከመዝ በስምየ ኪያየ ተወክፈ ፤
፱ እንደዚህ ሕፃን የሆነውን በኔ ስም የተቀበለ እኔን ተቀበለ ማለት እኔ አድርባታለሁ ።
በእንተ ዘተናገረ ኢየሱስ በሳዕለ ዕቅፍት ።
፲ ወዘሂ አስሐቶ ለ፩ዱ እምእሉ ንኡሳን እለ የአምኑ ብየ ይኄይሶ ከመ ይእስሩ በከሣዱ ማኅረፀ አድግ ወያስጥምዎ ውስተ ልጐተ ባሕር ።

፲፩ በኔ ካመኑ ምእመናን አንዱን ያሳተ አህያ በመዘውር የሚፈጭበትን ወፍጮ ካንገቱ አስሮ ከጥልቅ ባሕር ቢያስጥሙት ይሻለዋል ። አንድም ጽኑ ቀኖና ሰጥተው በእንብዓ ንስሐ ቢያስጥሙት ይሻለዋል ።

፲፪ አሌ ሎቱ ለዓለም እመንሱት ዘይመጽእ ።
፲፫ ከሚመጣው መከራ የተነሣ ለሰው ሁሉ ወዮለት ።
እስመ ግብር ይመጽእ መንሱት መከራ ግድ ይመ ጣልና ።
ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ ዘያመጽእ ለመ ንሱት ።
ነገር ግን ዋዛ ፈዛዛ ተጫውቶ መከራን ለሚያመጣት ለይሁዳ ወዮለት ።

፲፬ ወእመኒ እዴከ አው እግርከ ታስሕተከ ምትራ ወግድፋ እምላዕሌከ ። ማቴ ፭.፴ ፡ ማር ፱፡፵፪

፲፭ እጅህም ብትሆን ወይም እግርህ ብታስትህ ካንተ ቆርጠህ ጣላት ።
እስመ ይኄይሰከ ትባእ ውስተ ሕይወት ሐንካስከ ወጽውስከ እምእንዘ ብከ ፪ እዕዳው ወ፪ እእጋር ትት ወደይ ውስተ እሳት ዘለዓለም ።
ሁለት እጅ ሁለት እግር ኑሮህ ወደ ዘለዓለም እሳት ስትገባ እንካሳ ልምሾ ሁነህ ወደ ሕይወት ብትገባ ይሻልሃልና ።

፲፮ ወእመሂ ዓይንከ ታስሕተከ ምልሓ ወእው ጽኣ እምላዕሌከ ።

፲፯ ዓይንህ ብታስትህ አውጥተህ ጣላት ።
እስመ ይኄይሰከ ነቋረከ ትባእ ውስተ ሕይወት እም ትባእ ምስለ ፪ሆን አዕይንቲከ ውስተ እሳተ ገሃነም ሁለት ዓይን ኑሮህ ወደ ገሃነመ እሳት ከምትገባ አንድ ዓይን ኑሮህ ወደ መንግሥተ ሰማያት ብትገባ ይሻልሃልና ፡ አንድም ወእመሂ ዓይንከ ብለህ መልስ ኤጲስ ቆጶስህን ብትነቅፈው ሻረው ፤ እስመ ይኄይ ሰከ የነቀፍኸውን ኤጲስቆጶስ ሹመህ ኑረህ ኋላ ገሃነመ እሳት ከምትገባ የነቀፍኸውን ኤጲስ ቆጶስ ሽረህ ኑረህ ኋላ መንግሥተ ሰማይ ብትገባ ይሻልሃ ልና ።

፲፰ ዑቁ ኢታስተኃቅርዎሙ ለ፩ እምእሉ ንኡ ሳን ። መዝ ፴፫ ፡ ፯ ።
፲፱ በኔ ካመኑ ምእመናን አንዱን እንዳትንቁ እንዳታቃልሉ አስተውሉ ።
እብለከሙ ከመ መላእክቲሆሙ በሰማያት ወትረ ይሬእዩ ገጾ ለአቡየ ዘበሰማያት ።
መላእክተ ዑቃቢዎቻቸው ያባቴን ፊት ዘወትር ያያሉ ማለት መላእክተ ዑቃቢዎቻቸው በባለሟል ነት እንዳሉ እነግራችኋለሁ እንዳይቀስፉችሁ ማለት ነው ። አንድም መላእክተ ዑቃቢዎቻቸው በባለሟ

ልነት እንዳሉ እሳቸውም በባለሟልነት እንዳሉ እነግራችኋለሁ እንዳያስፈርዱባችሁ ማለት ነው ።

በእንተ በግዕት ዘተሐጉለት ።

፲፩ እስመ መጽአ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ይኅሥሥ ወያድኅን ዘተኃጉለ ፤ ሉቃ ፲፱፥ ፲ ።

፲፩ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ የጠፋውን ሊሻ የተጐዳውን ሊያድን ሰው ሁኖዋልና ።

፲፪ ምንተ ትብሉ ። ሉቃ ፲፫፥፩ ።

፲፪ አንቀጸ ንስሐ ነው ምን ትፈርዳላችሁ ። እመቦ ብእሲ ዘቦቱ ፻ አባግዕ ፤ መቶ በግ ያለው ሰው ቢኖር ወእመ ተገድፈ ፩ እምኔሆሙ ፥ ከመቶው አንዱ ቢጠፋበት ፥ እኮሁ የኃድግ ፺ወ፱ተ ውስተ ገዳም ።
ዘጠና ዘጠኙን በበረሃ ትቶ ። ወየሐውር ይኅሥሥ ዘተገድፈ የጠፋበትን ሊፈልግ ይሄድ የለምን ።

፲፫ ወእምከመ ረከቦ አማን እብለክሙ ከመ ይትፌሣሕ በእንቲኣሁ ፈድፋደ እም ፺ወ፱ እለ ኢተገድፉ ።

፲፫ ያገኘው እንደሆነ ካልጠፉት ከዘጠና ዘጠኙ ይልቅ ጠፍቶ በተገኘው ደስ ይለዋል ብዬ ደስ እንዲ ሰው በእውነት እነግራችኋለሁ ።

፲፬ ከማሁኬ ኢይፈቅድ አቡየ ዘበሰማያት ከመ ይትኃጐል ፩ዱ እምእሉ ንኡሳን ።

፲፬ እንደዚህም ሁሉ ሰማያዊ አባቴ ከተነሣ ሕያን አንዱ ሊጐዳ አይወድም ። አንድም ምንተ ትብሉ ብለህ መልስ ። መቶ በጎች የተባሉ መቶ ነገደ መላእክት ናቸው ከመቶው አንዱ ዲያብሎስ ቢወጣ በሱ ሥፍራ አዳም ቢገባ አዳም ቢወጣ እኮሁ የኃ ድግ ፥ ባርሕየ መላእክትን ትቶ ባሕርየ አዳምን ገን ዘብ ማድረጉን መናገር ነው ። ኢነሥእ ለዘነሥእ እመላእክት ዘእንበለ ዳዕሙ እምዘርዓ አብርሃም እንዲል ፥ ወእምከመ ረከቦ ። አዳምን ንስሐ ገብቶ ቢያገኘው አማን እብለክሙ ንስሐ ከማያሻቸው ከመላእክት ይልቅ ንስሐ በሚያሻው በአዳም መመ ለስ ደስ ይለዋል ብዬ በእውነት እነግራችኋለሁ ። ከማሁኬ ኢይፈቅድ አቡየ ዘበሰማያት ከመ ይትኃ ጐል ፩ዱ እምእሉ ንኡሳን ።
አሁን እንደ ተናገርነው ሰማያዊ አባቴ ከተነሳሕያን አንዱ ሊጐዳ አይወድም ።

በእንተ ዘከመ ይደልዎሙ ለአኃው ተገሥጾ ።

፲፭ ወእመኒ አበሰ ለከ እኁከ ሑር ወገሥጾ ለባሕቲትከ ። ዘሌዋ ፲፱፥፲፯ ። ሲራ ፲፱፥፲፫ ። ሉቃ ፲፯፥፫ ። ያዕ ፭፥፲፱ ።

፲፭ ወንድምህ ቢበድልህ በብቻህ ሁነህ በብቻው አድርገህ ለባሕቲትከ ለባሕቲቱ ለብቻህ ሁነህ ለብቻው አድርገህ ብቻህን ሁነህ ብቻውን አድርገህ ምከረው ወእመ ሰምዓከ ረባሕከ ለእኁከ ።
የተቀበለህ እንደሆነ ረባኸው ጠቀምኸው ።

፲፮ ወእመሰ ኢሰምዓከ ንሣእ ምስሌከ በዳ ግም አሐደ ። ዘዳ ፲፯፥፲፭ ። ዮሐ ፰፥፲፯ ። ፪ቆሮ ፲፫፥፩ ። ዕብ ፲፥፳፰ ።

፲፮ ባይቀበልህ ግን በሁለተኛው አንድ ሰው ጨምረህ ምከረው ። አው ፪ተ ።
አናንተን ባይቀበል ሁለት ሰው ጨምረህ አንተ ሦስ ተኛ ሁነህ ምከረው ።
እስመ በአፈ ፪ቱ ወ፫ቱ ሰማዕት ይቀውም ኵሉ ነገር ፀሁለት ምስክር ነገር ይጸናልና ። ንሣእ አሐደ ፥ በሦስት ምስክር ነገር ይጸናልና ። ንሣእ ፪ተ ። አን ድም ባምስት ምስክር ነገር ይጸናልና ። ንሣእ ፪ተ አው ፫ተ ።

፲፯ ወእመሰ ኢሰምአሙ ሎሙሂ ንግራ ለቤተ ክርስቲያን ። ፩ ቆሮ· ፭፥፱ ። ፪ተሰሎ ፫፥፲፫ ።

፲፯ እሳቸውንም ባይቀበል ንገሩ ለጉባኤ ይላል የፍርድ መጣፍ ባንድ ደወል ለሚሰበሰቡ ንገሩ እኒያን ባይቀበል ለቤተ ክርስቲያን ንገሩበት ።
ወእመሰ ለቤተ ክርስቲያን ኢሰምዓ ይኩን ከመ አረማዊ ወመጸብሐዊ ። ቤተ ክርስቲያን ንም ባይሰማት እንደ አረማዊ እንደ መጸብሐዊ ይሁን ማለት ይለይ ። ሐተታ ወንድሙን ቢበድል እግዚአ ብሔርን የካደ ይመስል ይለይ ማለቱ ስለምነው ቢሉ ፥ ወንድሙን ከበደለ ከሥጋው ከደሙ ይከለከ ላል ከሥጋው ከደሙ ከተከለከለ እንደ አረማዊ እንደ መጸብሐዊ መሆኑ ነውና ፥ አንድም የሚያየውን ወንድሙን መበደሉ እግዚአብሔርን መበደሉ ነውና

፲፰ አማን እብለክሙ ዘአሰርክሙ በምድር ይኩን እሡረ በሰማያት ። ዮሐ ፳፥፳፫ ።

፲፰ ከምድራውያን ነገሥታት ከሌዋውያን ካህ ናት ወገን ያይደለን መለየቱ እንደምን ይሆናል ትሉኝ እንደሆነ በምድር ያሰራችሁት በሰማይ የ ታ ሰረ እንዲሆን ።
ወዘፈታሕክሙ በምድር ይኩን ፍቱሐ በሰማያት በምድር የፈታችሁት በሰማይ የተፈታ እንዲሆን በውነት እነግራችኋለሁ ። እንዳለፈው ፥ ም ፲፮ ቍ ፲፱

፲፱ ወዓዲ እብለክሙ ለእመ ኃብሩ ፪ እው ፫ እምኔክሙ በውስተ ምድር በእንተ ኵሉ ግብር ዘሰ አሉ ይትገበር ሎሙ በሀበ አቡየ ዘበሰማያት ።

፲፱ ያውስ ቢሆን ጥቂት ነን ብዙ አይደለን መለየቱ እንደምን ይሆንልናል ትሉኝ እንደሆነ ከና ንተ ወገን ስለሚሹት ነገር በዚህ ዓለም ሁለቱ ወይም ሦስቱ አንድ ቢሆኑ በሰማይ አባቴ ዘንድ የሚሹት ነገር ይደረግላቸውዋል ብዬ እነግራችኋለሁ ።

፳ እስመ ኀበ ሀለው ፪ቱ ወ፫ቱ ጉቡአን በስምየ ሀየ እሄሉ አነ ማእከሎሙ ።

፳ ሁለቱ ሦስቱ በስሜ አምነው አንድ ቢሆኑ አንድ በሆኑበት እኖራለሁ ማለት በአድሬባቸው እኖራለሁና ። ሐተታ ሠልስቱ የተባሉ እንባቢ ተር

ጓሜ መጽሐፍ ናቸው ። አንድም ናዛዚ ተናዛዚ ጌር ላእከ ናቸው ።አንድም ንጽሐ ሥጋ ንጽሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና ናቸው ። ሃይማኖት ትውክልት ተፋቅሮ ናቸው

፳፩ ወእምዝ ቀርበ ጴጥሮስ ወይቤሎ እግዚእ ሚመጠነ እመ አበሰ ሊተ እኁየ እኅድግ ሎቱ ሉቃ ፲፯፥፬ ።

**፳፩ ከዚህ በኋላ ጴጥሮስ አቤቱ ወንድሜ ምን ያህል ቢበድለኝ ይቅር** ልበለው ። እስከ ሰብዕኑ እስከ ሰባት ድረስ ነውን አለው ።

፳፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ኢይብለከ እስከ ሰብዕ ።

፳፪ እስከ ሰባት እልልህም ፤ አላ እስከ ሰብዓ በበስብዕ ሰባቱን አንድ ሺባቱን አንድ እያልክ እስከ ሰባ ነው እንጂ ፡ አንድም እስከ ሰብዕ በበሰብዓ ሰባውን አንድ እያልክ እስከ ሰባት ነው እንጂ አለው

በአንተ ምሳሌ አግብርት ወፈድዮተ ዕዳ ።

፳፫ ወበእንተዝ እብለክሙ ትመስል መንግሥሥተ ሰማያት ብእሴ ንጉሠ ዘፈቀደ ይትሀሰቦሙ ለአግብርቲሁ ።

፳፫ ንስሐ የሚገባ ስለሆነ መንግሥተ ሰማያት ሕገ ወንጌል ፡ ሕገ ወንጌል ተስፋ ፡ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ብላቴኖቹን ሊቈጣጠራቸው የወደደ ንጉሥን ትመስላለች ።

፳፬ ወሶበ አኃዘ ተሐስቦቶሙ አምጽኡ ሎቱ አሐደ ዘይፈድዮ እልፈ መካልየ ።

፳፬ በተቆጣጠራቸው ጊዜ የእልፍ ወቄት ባለዳ አመጡለት ።

፳፭ ወኃጢኦ ዘይፈድዮ አዘዘ እግዚኡ ይሢጥዎ ምስለ ብእሲቱ ወምስለ ውሉዱ ።

፳፭ የሚከፍለው ቢያጣ ከልጆቹና ከሚስቱ ጋራ ሽጡት ብሎ አዘዘ በወንጌልስ መሸጥም የለ ተገዝቶ ደሞዝ አውጥቶ ይከፈለኝ ሲል ነው ።
ወኵሎ ዘቦ እስከ ይፈዲ ።

፳፮ እልፍ ወቄት እስኪከፍል ድረስ ።

፳፮ ወወድቀ እንከ ውእቱ ገብር ወሰገደ ሎቱ ወአስተብቍዖ ። ያ ባሪያ ወድቆ ማለደው ፤ እንዘ ይብል እግዚኦ ተዓገሠኒ አቤቱ ታገሠኝ ። ወኵሎ አፈድየከ ። እልፍ ወቄት እከፍልሃለሁ ብሎ ።

፳፯ ወምሀሮ እግዚኡ ለውእቱ ገብር ወዕዳሁኒ ኀደገ ሎቱ ፤

፳፯ ለዚያ ባሪያ ጌታው አዘነለት ዕዳውን ሁሉ ተወለት ።

፳፰ ወወፂአ ውእቱ ገብር ረከበ አሐደ ገብረ እምነ አብያጺሁ ዘይፈድዮ እልፈ ዲናረ ።

፳፰ ያ ባሪያ ወጥቶ ከባልንጀሮቹ ወገን የመቶ ወቄት ባለዳ አገኘ ።
ወአኀዞ ወኀነቆ እንዘ ይብል ሀበኒ ዘትፈድየኒ።

ገንዘቤን ስጠኝ ብሎ አስጨንቆ ያዘው ።

፳፱ ወወድቀ ውእቱ ገብር ታሕተ እገሪሁ ወአስተብቍዖ እንዘ ይብል ተዓገሠኒ ።

፳፱ ያ የጌታ ባርያ ታገሠኝ ማለት ቀን ስጠኝ ብሎ ወድቆ ማለደው ፡ ወኵሎ አፈድየከ ።
ጥቂት ጥቂት እያልሁ ሁሉንም እከፍልሃለሁ ።

፴ ወዓበዮ ወሖረ ወሞቅሖ ፡

፴ ብትከፍለኝ ከፈለኝ ያለዚያ አይሆንም ብሎ አስሮ አጋዘው እስከ ይፈድዮ ፡
እስኪከፍለው ድረስ ።

፴፩ ወርእዮሙ አግብርተ እግዚኡ ዘገብረ ተከዙ ጥቀ ፡

፴፩ የጌታው ባሮች ባልንጀሮቹ ያደረገውን አይተው ፈጽመው አዘኑ ፡
ወሖሮሙ ነገርዎ ለእግዚኦሙ ኵሎ ዘገብረ ፡ ሄደው ያደረገውን ሁሉ ለጌታቸው ነገሩት ፡

፴፪ ወእምዝ ጸውዖ እግዚኡ ለ ገብር እኩይ ኵሎ ዕዳ ኀደጉ ለከ ።

፴፪ ከዚህ በኋላ ጌታው ጠርቶ አንት ክፉ ባርያ ዕዳህን ሁሉ ተውሁልህ ።
እስመ አስተብቋዕከኒ ።

፴፫ ማልደኸኛልና ስለ ማለድኸኝ አኮሁ መፍትው እንተሂ ትምህር ውእተ ገብረ ቢጸከ በከመ አነ መሀርኩከ ።

፴፫ እኔ እልፍ ወቄት እንደተውሁልህ አንተስ ልትተው አይገባህም ነበርን ።

፴፬ ወተምዓ እግዚኡ ወመጠዎሙ ለእለ ይሣቅይዎ ።

፴፬ ጌታው ተቈጥቶ እሱ ለሰው ካላዘነ ብሎ መከራ ሥቃይ ለሚያጸኑበት ሰጠው ።
እስከ አመ ይሜልጥ ኵሎ ዘይፈድዮ ።
እልፍ ወቄት እስኪከፍለው ድረስ ።

፴፭ ከማሁኬ አቡየኒ ሰማያዊ ይገብር ለክሙ እመ ኢኃደግሙ እበሳሆሙ ለቢጽክሙ እምኵሉ ልብክሙ ።

፴፭ እንደዚህም ሁሉ የወንድሞቻችሁን ኃጢአት በፍጹም ልቡናችሁ ይቅር ካላላችሁ ሰማያዊ አባቴም እንዲህ ያደርግባችኋል ። አንድም ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብለህ መልስ።መንግሥተሰማያት አብ መላእክትን ሊቈጣጠራቸው የወደደ ንጉሥን ትመስላለች አለ እሱ ነው ማለት ነው ። ወሶበ አኀዘ ተሀስቦቶሙ። በተቆጣጠራቸው ጊዜ ፍጹም ኃጢአት የሠራ አዳምን አመጡለት ። ወኃጢኦ ዘይፈድዮ ። ሃይማኖት ምግባር ቢያጣበት ። አዘዘ ይሢጥዎ በሱ በሔዋን በልጆቹ ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስን ፈረደባቸው። በአዳም ሁሉን መናገር ነው።አንድም መምህረ ንስሐ ነው ፡ አዘዘ ይሢጥዎ ፡ በሕዋሳቱ ደዌያትን ፈረደበት ፡ ወኵሎ ዘቦ፡ ቀናኖውን እስ

ኪፈጽም ድረስ ። ወወድቀ ወአስተብቊዖ፣ በድየሃለሁ ይቅር በለኝ።ወኵሎ እፈድየከ፣ ቀኖናየን እፈጽማለሁ አለው ። ወምሀሮ ፣ አዘነለት ፣ ኃጢአቱን አስተሰረ የለት ። ወወፅአ ፣ ኃጢአቱ ከተሰረየለት በኋላ ከሕዝቡ አንድ ተነሃሳሂ አገኘ ። ወአኀዞ ወሐነቆ ፣ መጽሐፍ ያዘዘውን ፈጽም ብሎ አስጨንቆ ያዘው ። ወወድቀ ወአስተብቊዖ ፤ ቀኖናየን ልፈጽም ብሎ ማለደው ። ወአበዮ ወሞቆሖ ። ብትፈጽም ፈጽም እስዚያ አይሆንም ብሎ አወገዘው ። እስከ ይፈድዮ ፤ ቀኖናውን እስኪፈጽም ድረስ ፤ ወርእዮሙ አብያጺሁ ፣ መላእክት አይተው ፈጽመው አዘኑ ሰው ለሰው እንዲህ ይጨክናል ብለው ፤ ወሐዊሮሙ ነገርዎ ፣ ሂደው የሠራውን ሥራ ሁሉ ለጌታቸው ነገሩት ሐተታ መንገሩስ የለም የነገሩት ዐውቆ ሥራ እንዲሠራ ዐውቆ ሥራ መሥራቱን መናገር ነው ። ወአምዝ ጸውዖ ፣ ከዚህ በኋላ በደዌ ጸራው ። ወይቤሎ ፤ አንተ ክፉ ቄስ እኔ ኃጢአትህን ሁሉ አስተሰረይኩልህ ፤ እስመ አስተብቋዕከኒ ፣ ማልደኸኛልና ስለማለድኸኝ ። አኮሁ መፍትው እኔ ይቅር እንዳልኩህ አንተስ የወንድምህን ኃጢአት ልታስተሰርይለት አይገባህምን ? ተመየጥ አንተ ወእኔ ተወከፍኩ ሀየንቴከ ሞተ በከመ ተወከፈ ክርስቶስ ሞተ ሀየንቴየ ወሀየንተ ኵሎሙ ልትለው አይገባህም ነበር አለው ። ወተምዓ ወመጠዎ ፣ ፈርዶ መከራ ለሚያጸኑበት ለደዌያት ሰጠው ። እስከ ይፈዲ ፣ ቀኖናውን እስኪፈጽም ድረስ ። ወከማሁኬ ፣ የወንድማችሁን ኃጢአት በፍጹም ልቡናችሁ ይቅር ከላላችሁ ሰማያዊ አባታችሁ አሁን እንደተናገርሁት ያደርግባችኋል ።

በእንተ ዘተግኅሠ ኢየሱስ እም ኢየሩሳሌም ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

፩ ወሶበ ፈጸመ እግዚእ ኢየሱስ ተንሥአ እምገሊላ ወሐረ ወበጽሐ ውስተ ብሔረ ይሁዳ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ። ማር ፲ ፣ ፩ ።

፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ይህን ነገር አስተምሮ ከፈጸመ በኋላ ከገሊላ ወጥቶ የዮርዳኖስ ማዶ ወደሚሆን ወደ ምድረ ይሁዳ ደረሰ ።

፪ ወተለውዎ አሕዛብ ብዙኃን ።
፪ ብዙ ሰዎች ተከተሉት ።
ወፈወሶሙ በሀየ ፣ በዚያም አዳናቸው ።
በእንተ ኪዳን ዘኢይትፈታሕ

፫ ወመጽኡ ኀቤሁ ፈሪሳውያን ያመክርዎ ወይበልዎ ። ማር ፲ ፣ ፪ ።

፫ ፈሪሳውያን ሊፈትኑት እንዲህ ሊሉት መጡ ይከውኖሁ ለብእሲ ኀዲገ ብእሲት በኵሉ ዘአበሰት ሎቱ ሳትስስንበት ደረቀች ሰትፈች ብሎ ለሰው ሚስቱን መፍታት ይገባዋልን አሉት ።

፬ ወአውሥአ መለሰ ፣ ወይቤሎሙ ኢያንበብክሙኑ በውስተ ኦሪት ዘከመ ፈጠሮሙ እምትካት ተባዕተ ወአንስተ ። ዘፍ ፩ ፣ ፳፯ ።

፬ ጥንቱን አዳምን ወንድ ሔዋንን ሴት አድርጎ እንደፈጠራቸው በኦሪት እንደተጻፈ አልተመለከታችሁም አላቸው ። ብእሴ ወብእሲተ ገብሮሙ ተባዕተ ያለውን ብእሴ አንስተ ያለውን ብእሲተ አለ ።

፭ ወይቤ ወበእንተዝ የኃድግ ብእሲ አባሁ ወእሞ ወይትልዋ ለብእሲቱ ዘፍ፪፣ ፳፬ ። ፩ ቆሮ ፮፣ ፲፮ ። ኤፌ ፭፣ ፴፩ ።

፭ ስለዚህ ነገር ሰው አባት እናቱን ትቶ ሚስቱን ተከትሎ ይሄዳል ። ሐተታ ፣ ቆላ ብትሆን ቆላ ይወርዳል ደጋ ብትሆን ደጋ ይወጣል ። አንድም እሱ ፈቃድ ቢነሣበት በናቴ ላድርገው አይልም እሷም ፈቃድ ቢነሣባት ባባቴ ላድርገው አትልምና አንድም በግብር አንድ ይሆናሉና ። ወይትለዋ አዓግዓ ቀርሜሎስ እንዲል ይትሳጸቃ ሲል ፤ ወይከውኑ ፪ ሆሙ አሐደ ሥጋ አንድ አካል ይሆናሉ በግብር አንድም ወንዶች ቢወልዱ ያንተ ናቸው ሴቶች ቢወልዱ ያንቺ ናቸው አይባባሉምና ። አንድም እሱን ቢመስሉ ያንተ ይሁኑ አትለውም እሷን ቢመስሉ ያንቺ ይሁኑ አይላትምና ፣ አንድም በዚህ ዓለም ሳሉ በሕጋቸው ጸንተው ዐሥራት በኩራት ቀዳምያት አውጥተው እንግዳ ተቀብለው ሥጋውን ደሙን በሚገባ ተቀብለው ቢኖሩ በወዲያውም አንድ ዓለም ወርሰው አንድ ፀሐይ ሞቀው ይኖራሉና ።

፮ ናሁኬ ኢኮኑ ፪ተ ።
፮ እነሆ ሁለት አይባሉም ።
አላ አሐዱ ሥጋ እሙንቱ ።
አንድ አካል ናቸው እንጂ ።
ዘእግዚአብሔር አስተፃመረ ሰብእ ኢይፈልጥ ።
እግዚአብሔር አንድ ያደረገውን ሰው አይለይም አትለይ ሲል ነው ።

፯ ለምንት እንከ አዘዘ ሙሴ የሀብዋ መጽሐፈ ኅዳጋቲሃ ወይድኃርዋ ፣ ዘዳ ፳፬ ፣ ፩ ።

፯ እንዲህ ከሆነ ሙሴ የምትፈታበትን ነውር የሚናገር ደብዳቤ ሰጥቶ ይፍታት ብሎ ለምን አዘዘን አሉት ።

፰ ወይቤሎሙ ሙሴሰ አዘዘክሙ በከመ እከየ ልብክሙ ትድኅሩ አንስቲያክሙ ።

፰ ሙሴስ እንደ ልቡናችሁ ክፋት ሚስቶቻችሁን ትፈቱ ዘንድ አዘዛችሁ ።
ወእምፍጥረትስ አኮ ከማሁ ዘተገብረ ።
ጥንቱን ግን የታዘዘው እንዲህ አይደለም አላቸው ሐተታ ። አንዲት ሴት ላንድ ወንድ አንድ ወንድ ላንዲት ሴት ነው እንጂ የሞተችበት የሞተባት በፈቲው ዖር የሚናደዱ ሆኑ ። ሙሴ ወደ እግ

ዘእግዚአብሔር ቢያመለክት የሞተበት ያግባ ብሎታል ሲጸላት ጊዜ ወንዱ ልጇን እያሸ የሚገድላት ሆነ ሴቲቱም መርዝ አጠጥታ ሥራይ አብልታ የምትገ ድለው ሁናለችና እንዲህ አለ ።
ወእንዘ እብለክሙ ኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ ለሊሁ ረሰያ ዘማ ማቴ·፭ ፡ ፴፪ ። ማር ፲ ፡ ፲፩። ሉቃ ፡ ፲፰ ፡ ፲፰ ፡ ፩·ቆሮ ፡ ፯ ፡ ፲ ።

፱ እኔም ሳትሰስንበት ደረቀች ሰነፈች ብሎ ሚስቱን የሚፈታ ሁሉ ዘማ አስኘት ብየ እነግራ ችኋለሁ ።
ወእንተ ደኃርዋ ዘእውሰበ ዘመወ ።
በነውር የተፈታቾቶቱንም ያገባ በደለ ።

፲ ወይቤልዎ አርዳኢሁ እመ ከመዝ ውእቱ ሥርዓተ ብእሲ ወብእሲት ኢይርቱዕ እውስቦ ።

፲ የባልና የሚስት ሥራት እንዲህ ከሆነ ማለት ሰነፈች ደረቀች ብሎ መፍታት የማይገባ ከሆነ ሊያገቡ አይገባም አሉት ።

፲፩ ወይቤሎሙ አኮ ለኵሉ ዘይትከሃል ዝንቱ።
፲፩ ይህ ንጽሕ ጠብቆ መኖር ለሁሉ አይቻልም ዘእንበለ ለዘተውህቦ ።

ሀብተ ንጽሕ ለተሰጠው ግዕዛኑ ለጸናለት እራቱ ባሕርያት ለተስማሙለት ነው እንጂ
፲፪ እስመቦ ሕፅዋን እለ ከማሁ ተወልዱ እም ከርሠ እሞሙ ።
፲፪ ከእናታቸው ማኅፀን ጀምሮ ሕፅዋን ሁነው የተወለዱ አሉና እንደ አባ ባይሉል ልጆች ሙጻዓ ስንት ብቻ ነበራቸው ።
ወቦ ሕፅዋን እለ ሐፀውዎሙ ሰብእ ።
ኃላ ሻንቅላ ሕፅዋን ያደረጋቸው አሉና ለኒያ ነው እንጂ ወቦ ሕፅዋን እለ ሐፀው ርእሶሙ በእንተ መንግሥተ ሰማያት ።
ከቤተ መንግሥት እንበላለን እንጠጣለን ብለው ሕፅዋን የሆኑ አሉ ለኒያ ነው እንጂ ።
ሐተታ ፤ ይህስ አይደነቅም እህያን አልተዋ ጋም በሬን አልተራገጠም ብሎ ። እስመ ቦ ሕፅ ሕን ከናታቸው ማኅፀን ሕፅዋን ሁነው የተወ ለዱ አሉና ለኒያ ነው እንጂ ፤ እለ ኤርምያስ ቀደስኩከ እምከርሠ እምከ እንዲል ፤ ወቦ እለ ሐፀ ውዎሙ ሰብእ ። መምህራን መክረው አስተምረው ንጹሐን ያደረጓቸው አሉና ለኒያ ነው እንጂ ። ሙሴ ኢያሱን ኤልያስ ኤልሳዕን ወቦ እለ ሐፀው ርእ ሶሙ በእንተ መንግሥተ ሰማያት ፤ ባሕርያቸው ደካማ ነውና አይችሉትም ብሎ ነው እንጂ ከሕገ ሥጋ ሕገ ነፍስ ከሕገ እንስሳ ሕገ መላእክት እንዲ በልጥ ታውቆ የለም መንግሥተ ሰማያትን እንወ ርሳለን ብለው ንጽሕ ጠብቀው ከሴት ርቀው የሚ ኖሩ አሉና ለኒያ ነው እንጂ ወዘሰ ይክል ተዓግሦ ለይትዓገሥ ።

መታገሥ የሚቻለው ማለት ንጽሕ ጠብቄ ከሴት ርቄ እኖራለሁ የሚል ግን ንጽሕ ጠብቆ ከሴት ርቆ ይኑር ።
በእንተ ሕፃናት እለ መጽኡ ኀበ ኢየሱስ ፤
፲፫ ወእምዝ አምጽኡ ሎቱ ሕፃናተ ከመ ያን ብር እዴሁ ላዕሌሆሙ ወይጸሊ ። ማር ፲ ፡ ፲፫ ሉቃ ፲፰ ፡ ፲፭ ።
፲፫ ከዚያ በኋላ እጁን ይጭንባቸው ዘንድ ማለት በአንብሮተ እድ ይባርካቸው ዘንድ ሕፃና ትን ይዘው መጡ ። በኤልሳዕ ልማድ ሕፃናት መጥ ተው ዕርግ በራህ ብለው ዘበቱበት ሁለት ድባት አስነስቶ ፵፪ ሕፃናት አስፈጀ የነቢየ እግዚአብሔር መርገሙ እንዲህ የጐዳ በረከቱ እንደምን ይጠቅም ብለው እያመጡ የሚያስባርኩ ሁነዋልና በዚያ ልማድ አመጡለት ።
ወገሠጽዎሙ አርዳኢሁ ለእለ አምጽእዎሙ ።
አባቶቻቸው ያመጧቸው ሕፃናትን ተቆጧቸው ይጠ ቀጥቁናል ብለው ፤ አንድም ሕፃናትን ያመጧቸው አባቶቻቸውን ተቆጧቸው ትምህርት ያስፈቱናል ብለው ።

፲፬ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኅድግዎሙ ለእሉ ሕፃናት ኢትክልእዎሙ ይምጽኡ ኀቤየ ማቴ ፲፰ ፡ ፫ ።

፲፬ ወደኔ ይመጡ ዘንድ ሕፃናትን ተዋቸው አትከልክሏቸው እለ እስመ ለዘከመ እሉ ይእቲ መንግሥተ ሰማያት ።
መንግሥተ ሰማያት ወንጌል የምትነገር እንደነዚህ ላሉ ነውና አንድም መንግሥተ ሰማያት የምትወ ረስ እንደነዚህ ላሉ ነውና ።

፲፭ ወአንበረ እዴሁ ላዕሌሆሙ ወኃለፈ እምህየ ።

፲፭ እጁን ጭኖ ባርኳቸው ከዚያ ሄደ እነዚህም ከ፸፪ የሚበዙ ናቸው ከነሀም ከፍጹምነት ያልደ ረሰ ሊቀ ጳጳስነት ጳጳስነት ኤጲስቆጶስነት ያልተ ሾመ የለም ከነዚህም አንዱ አግናጥዮስ ምጥው ለአንበሳ ነው ።

በእንተ ወሬዛ ባዕል ።

፲፮ ወናሁ መጽአ ፩ ብእሲ ወይቤሎ ሊቅ ኄር ምንተ እግበር እምሠናያት ከመ እረስ ሕይወተ ዘለዓለም ። ማር ፲ ፡ ፲፯ ሉቃ ፲፰ ፡ ፲፰ ።
፲፮ አንድ ሰው መጥቶ መምህር የማታልፍ መንግሥተ ሰማያትን እወርስ ዘንድ ከበጐ ነገር ወገን ምን ላድርግ አለው ።
፲፯ ወይቤሎ ምንተ ትብለኒ ኄር ።
፲፯ እላመንም ብሎ ሳታምንብኝ ለምን ኄር ትለኛለህ አለው ። አንድም ኄር ብለው ኄር ይለኛል ብሎ በተንኮል መጥቷልና የሕሊናውን

አውቆቤት ኄር ብለው ኄር ይለኛል ብለህ ለምን ኄር ትለኛለህ ።
አልቦ ኄር ዘእንበለ ፩ እግዚአብሔር ።
ካንድ ከእግዚአብሔር በቀር ቸር የለም አለው ።
ወእመሰ ትፈቅድ ትባእ ውስተ ሕይወት ዕቀብ ትእዛዛተ ። ወደ ሕይወት ማለት መንግሥተ ሰማያት ትገባ ዘንድ ከወደድህስ ሕግጋትን ጠብቅ ዘፀ ፳ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬ ፡ ፲፭ ፡ ፲፮ ።

፲፰ ወይቤሎ አይቴኑ ዕቀብ ።
፲፰ ማን ማን ልጠብቅ ። ዘአዓቅቦን የምጠብቃቸው ማን ማን ናቸው አለው ።
ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ኢትቅትል ነፍሰ ።
ጌታም ነፍስ አትግደል ።
ኢትዘሙ ። አትሰስን ።
ኢትስርቅ ። አትስረቅ ።
በሐሰት አትመስክር ።

፲፱ አክብር አባከ ወእመከ ።
፲፱ አክብር ማለት አባትህን እናትህን ርዳ ።
ወአፍቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ።
ባልንጀራህን እንደ ራስህ ውደድ አለው ።

፳ ወይቤሎ ወሬዛ ዘንተሰ ኵሎ ዓቀብኩ እምንዕስየ ።

፳ ይህንስ ሁሉ ከሕፃንነቴ ጀምሬ ጠብቄያለሁ ፤
ምንት እንከ ተርፈኒ ።
ምን ቀረኝ ዘተርፈኒ የቀረኝ ምንድነው አለው ።
ወነጸሮ እግዚእ ኢየሱስ ወአፍቀሮ ።
ጌታ አይቶ ወደደው ።

፳፩ ወይቤሎ አሐቲ ተርፈትከ ።
፳፩ አንዲት ቀርታሃለች አለው ።
እመሰ ፈቀድከ ፍጹመ ከመ ትኩን ሑር ወሢጥ ኵሎ ጥሪተከ ወሀብ ለነዳያን ።
ፍጹምነትስ ከወደድህ ሂደህ ገንዘብህን ሁሉ ሸጠህ ለነዳያን ስጥ አለው ።
ወታጠሪ መዝገበ ዘበሰማያት በሰማይ መዝገብ ታገኛለህ ማለት መንግሥተ ሰማያትን ትወርሳለህ ። ሐተታ እርድና ከምጽዋት ነገረው ሑር ሢጥ ብሎ እርድና ሀብ ብሎ ምጽዋትን ። አንድም ነዳያን ላም በሬ ፈረስ በቅሎ ቢሰጧቸው ወጥቶ ወርዶ መሸጥ አይሆንላቸውምና ፤ ዳግመኛ የከብቱን ዋጋ የሚያውቅ ባለቤቱ ነውና ፤ እንዳገኙ እንዳይጥሉት ። ወነዓ ትልወኒ ።
ለጊዜው በእግር ተከተለኝ ፍጻሜው በግብር ምሰለኝ አለው ።

፳፪ ወሰሚዖ ወሬዛ ዘንተ ነገረ ወሖረ እንዘ ይቴክዝ ።
፳፪ እሱም ይኸን ነገር ሰምቶ እያዘነ ሄደ ።
እስመ ብዙኅ ጥሪቱ ። ገንዘቡ ብዙ ነውና ። ሢጥ ቢለው ስንቱን ይሸጣል ብሎ አንድም እሴን መከተል ሸቶ ነበርና ሑር ቢለው ። አንድም ፍጹምነት ሸቶ ነበርና አሐቲ ተርፈተከ ቢለው ።

፳፫ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ አማን እብለከሙ ከመ ባዕል እምዕጹብ ይበውእ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ።

፳፫ ጌታ ለደቀ መዛሙርቱ ባለጸጋ ጨርሶ መጽውቶ በጭንቅ መንግሥተ ሰማያት ይገባል ብየ እንዲገባ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ።

፳፬ ወካዕበ ዕብለከሙ ይቀልል ይኅልፍ ገመል እንተ ሰቀረተ መርፍዕ እምባዕል ይባእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፬ ዳግመኛ ባለጸጋ መንግሥተ ሰማይ ከሚገባ ገመል በመርፌ ቀዳዳ ቢያልፍ ይቀላል ብየ እነግራችኋለሁ ፤ ሐተታ ባይጸፍ ነው እንጂ በሱ ጊዜ ተደርጓል ። በሱ ጊዜስ አልተደረገም ደቀ መዝሙሩ ታዴዎስ ያደረገውን መናገር ነው ይህን ቢያስተምር ነጋድያን ገመል ጭነው መጡ በቃል ያስተማርኸንን አድርገህ አሳየን አሉት አንጥረኛ ወዳጅ ነበረውና መርፌ ስደድልኝ አለው ነገሩን አስቀድሞ ሰምቷልና ቀዳዳውን አስፍቶ ሰደደለት ምን ቢሰፋ ገመል ያሳልፋል ያንተንም ዋጋ እግዚአብሔር አያስቀርብህ እንደጥንቱ አድርገህ ስደድልኝ አለው እንደጥንቱ አድርጎ ሰደደለት ሦስት ጊዜ እያመላለሰ አሳይቷቸዋል አንድም አይሁዳዊ አምኖ ተጠምቆ መንግሥተ ሰማያት ቢገባ አረማዊ አምኖ ተጠምቆ መንግሥተ ሰማያት ከገባ ይቀላል ብየ በውነት እነግራችኋለሁ አይሁዳዊ አያደርገውም አረማዊ ያደርገዋል ማለት ነው ።
፳፭ ወሰሚዖሙ አርዳኢሁ አንከሩ ጥቀ እንዘ ይብሉ መኑ እንጋ ይክል ድኅነ ።
፳፭ ደቀ መዛሙርቱ ይኸን ሰምተው ገንዘቡን ሁሉ ጨርሶ መጽውቶ መንግሥተ ሰማያት መግባት ለማን ይቻለዋል ብለው ፈጽመው አደነቁ ። አንድም ታምራት ማድረግ ለማን ይቻለዋል ብለው አደነቁ ።
፳፮ ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ በኀበ ሰብእ ኢይትከሀል ዝ ።
፳፮ ጌታ አይቷቸው ታምራት ማድረግ በሰው ዘንድ አይቻልም
ወበኀበ እግዚአብሔርሰ ኵሎ ይትከሃል ።
በእግዚአብሔር ዘንድ ግን ይህ ሁሉ ይቻላል ።
አንድም እግዚአብሔር ባላደረበት ሰው ዘንድ አይቻልም ። እግዚአብሔር ባደረበት ሰው ዘንድ ግን ይቻላል ። አንድም ገንዘቡን ጨርሶ መመጽወት እግዚአብሔር ላላደረበት ሰው አይቻልም እግዚአብሔር ላደረበት ሰው ግን ይቻላል ።

በእንተ ዘኪመ ይደልዎሙ ዕሤት ለእለ ይተልውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፯ ወእምዝ አውሥአ ጴጥሮስ ወይቤሎ ናሁ ንሕነ ኀደግነ ኵሎ ወተለውናከ ምንተ እንከ ንረክብ ።

፳፯ ጴጥሮስ መሰሰ እኛ ሁሉን ትተን ተከ ትለንሃል ምን እናገኝ ይሆን አለው ፤ ሐተታ ምን ነበረውና እንዲህ አለ ቢሉ አንድ አህያ አንድ በሬ መረቡን መርከቡን ትቶ ተከትሎታልና ይህ ሁሉ አይደለም እከብራለሁ ባይ ልቡናውን ትቶ ተከ ትሎታልና እንዲህ አለ ።

፳፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አንትሙ እለ ተለውክሙኒ አመ ዳግም ልደት አመ ይነብር ወልደ ዕጓለ እመሕያው ዲበ መንበረ ስብሐቲሁ ።

፳፰ ሰው በሆንኩ ጊዜ ያመናችሁብኝ እናንተ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ በዕርገት በየማነ አብ በዘባነ ኪሩብ በናረ ጊዜ ።
ወአንትሙኒ ትነብሩ ዲበ ፲ቱወ፪ቱ መናብርት ።
ባሥራሁለቱ ነገደ እሥራኤል በመምህርነት ትሾማላችሁ ፤
ወትኴንኑ ፲ተ ወ ፪ተ ሕዝበ እሥራኤል ።
ዐሥራ ሁለቱን ነገደ እሥራኤልን ታስተምራላችሁ አንድም አመ ይነብር ውስተ ዓለም ሐዲስ ይላል ያመናችሁብኝ እናንተ በፅለቱ ምጽአት ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ በንጉሥነት በቀኘ ጊዜ ባሥራ ሁለቱ ወንበር ትቀመጣላችሁ ዐሥራሁለቱ ነገደ እሥራኤል ትፈርዳላችሁ ። ያን ጊዜስ መቀመ ጥም መፍረድም የለም ዛሬ የፈረዱት ፍርድ የማ ይንቀፍባቸው ስለሆነ እንዲህ አለ ፤

፳፱ ወኵሉ ዘኃደገ አብያተ ወአኃወ ወአኃተ አበ ወእመ ወብእሲተ ወውሉደ ወገራውኃ በእንተ ስምየ ምእተ ምክዕቢተ ይነሥእ ፤
፳፱ በኔ ስም አምኖ በኔ ስም ስላመነ አባቱን እናቱን እኅቱን ሚስቱን ቤቱን ንብረቱን ርስቱን የተወ ሁሉ መቶ ዕጥፍ ያገኛል አለ ሐተታ መቶ እናት አባት መቶ እኅት ወንድም መቶ ሚስት ያገኛል ማለት አይደለም በዚህ ዓለም ያባትነትየናትነትየወንድምነት የእኅትነት የሚስትነት ሥራ ይሠራለታል ሲል ነው ።
ወሕይወተ ዘለዓለም ይወርስ ። በወዲያው የዘለዓ ዓም ሕይወት መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል ፤

፴ ወብዙኃን ቀደምት ይከውኑ ደኃርተ ወደ ኃርት ይከውኑ ቀደምተ ። ማቴ ፳ ፣ ፲፮ ማር ፣ ፲ ፣ ፴፩ ሉቃ ፣ ፲፫ ፣ ፴ ።

፴ ኋለኞች ፊተኞችን ፊተኞች ኋለኞችን ይሆ ናሉ ማለት ቀደምት ጸሐፍት ፈሪሳውያን ደኃርት ሐዋርያትን ይሆናሉ አለ ዓሥራቱን በዠራቱን እጥ ተው ደኃርት ሐዋርያት ቀደሞት ጸሐፍት ፈሪሳ ውያንን ይሆናሉ አለ አግኝተው ፤ አንድም ቀደምት ሐዋርያት ደኃርት ሠለስቱ ምእትን ደኃርት ሠለስቱ ምእት ቀደምት ሐዋርያትን ይሆናሉ ኋላ በሥራ ያስፋታል እንጂ በጥምቀት በሚገኘው ክብር አንድ ናቸውና ።

በእንተ ምሳሌ ዘዓቀብተ ወይን ።

ምዕራፍ ፳ ።

፩ እስመ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብእሴ በዓለ ቤት ዘወፅአ ነግሃ ይትዓሰብ ገባእተ ለዐጸደ ወይኑ ።

፩ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ሕገ ወን ጌል ተስፋ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ለወይኑ ቦታ ምንደኞችን ሊስማማ ማለዳ የወጣ ባለ ቤትን ትመስላለችና ቀደምት ወይከውኑ ደኃርተ ደኃርት ይከውኑ ቀደምተ ላለው ። አንድም ትመስላለች እኮን ።

፪ ወተከሃሎሙ በበዲናር ለለዕለት ።
፪ በቀን ድሪም ድሪም እሰጣችኋለሁ ብሎ የተስማማቸውን ወፈነዎሙ ውስተ ዐጸደ ወይኑ ይትቀነዩ ።
ወይን ጨብቂ ብሎ ወደ ወይኑ ቦታ የላካቸውን ባለቤት ትመስላለች ፤ ሐተታ ነግህ የተባለ ከተወ ለዱ ጀምሮ እስከ ሰባት ዓመት ያለው ዘመን ነው እስከዚያ ሥራት አይሠራባቸውም መምህረ ንስሐ የሚይዙ ጾም የሚጀምሩ ከዚያ በኋላ ነውና ።

፫ ወወፂኦ ጊዜ ፫ቱ ሰዓት ርእየ ካልዓነ እንዘ ይቀውሙ ውስተ ምሥያጥ ጽሩዓነ ።
፫ በሦስት ሰዓት ቢወጣ ሌሎችን ሥራ ፈተው ካደባባይ ቆመው አገኘ ።

፬ ወሎሙኒ ይቤሎሙ ሑሩ አንትሙኒ ውስተ ዓጸደ ወይንየ ወተቀነዩ ወዘረትዓኒ እሁበክሙ ።
፬ እናንተም ከወይኔ ቦታ ሂዱችሁ ወይኔን ጠብቁ የቀናኝን እሰጣችኋለሁ አላቸው ።
በኋላ የመጣን የቀናኝን እሰጥሃለሁ ማለት ልማድ ነው ።
ወእሙንቱ ሖሩ ።
እነርሱም ሔዱ ።

፭ ወወፂኦ ጊዜ ስሱ ወተሱዓት ሰዓት ገብረ ከማሁ ።
፭ ዳግመኛም በቀትር በተሣት ወጥቶ ሥራ ፈትተው ካደባባይ ቆመው አገኘ ፤ እናንተም ሂዳችሁ ወይኔን ጠብቁ የቀናኝን እሰጣችኋለሁ አላቸው ።

፮ ወጊዜ አሠሩ ወ፩ ሰዓት ወጺአ ረከበ ካል ዓነ እንዘ ይቀውሙ ።
፮ በሠርክ ወጥቶ ሌሎችን ሥራ ፈተው ካደ ባባይ ቆመው አገኘ ።
ወይቤሎሙ ለምንት ቆምክሙ ዝየ ኵሎ ዕለተ ጽሩዓኒክሙ ።

ቀኑን ሁሉ ሥራ ፈታችሁ ለምን ቆማችኋል አላቸው ፤ ከዚያው ገብቶ ከተቀጠረ ብሎ ዠሎ ዕለተ እለ ። እንድም ዠሎ ሰዓተ ሲል ነው ። ዐሥራ ሁለቱን ሰዓተ መዓልት ሥራ ፈታችሁ ለምን ቆማችኋል አላቸው ።

፯ ወይቤልዎ እስመ አልቦ ዘተዓሰበነ ።

፯ የተስማማን የለምና የተስማማን ባይኖር ነው እሉ ።
ወይቤሎሙ ሑሩ አንትሙኒ ውስተ አጸደ ወይንየ ተቀነዩ ወዘረትዓኒ እሁበክሙ ።
እናንተም ሄዳችሁ ወይኔን ጠብቁ የቀናኝን እሰጣችኋለሁ አላቸው ። ሠለስት የተባለ ከሰባት ዓመት እስከ ሃያ ዓመት ያለው ዘመን ነው ። ቀትር ከሃያ እስከ አርባ ያለው ነው ።
ተሳት ካርባ እስከ ስሳ ያለው ዘመን ነው ። ሠርክ ከስሳ እስከ ሰማንያ ያለው ዘመን ነው እስከዚያ ድረስ ሃይማኖት ሳይማሩ ምግባር ሳይሠሩ ኑረው ከዚህ በኋላ በመምህራን አድሮ አስተምሮ በቃለ መጻሕፍት ገሥጾ ምግባር እንዲሠሩ ሃይማኖት እን ዲይዙ ማድረግ ነው ።

፰ ወሶበ መስየ ይቤሎ በዓለ ዓጸደ ወይን ለመጋቢሁ ጸውዖሙ ለገባእት ወሀቦሙ ዓስቦሙ

፰ ሲመሽ የወይን ባለቤት ሹሙን ጠርቶ ለም ንደኞች ዋጋቸውን ስጣቸው አለው ።
ወእኀዝ ቅድመ እምቀደምት እስከ ደኃርት ።
ከገባእተ ሠርክ ጀምረህ እስከ ገባእተ ነግህ ስጥ አለው

፱ ወመጽኡ እለ ዐሠርቱ ወ፩ ሰዓት ።

፱ ገባዕተ ሠርክ መጡ ።
ወነሥኡ በበዲናር ።
ድሪም ድሪም ሰጣቸው ።

፲ ወመጽኡ ቀደምት ።

፲ ገባዕተ ነግህ መጡ ።
ወመሰሎሙ ዘያበዝኅ ሎሙ ውሂበ ።
አብዝቶ የሚሰጣቸው መሰላቸው ነበር ።
ወወሀቦሙ ሎሙኒ በበዲናር ።
ለሳቸውም ዲሪም ዲሪም ሰጣቸው ።

፲፩ ወነሢኦሙ አንጐርጐሩ ላዕሌሁ ለበዓለ ቤት ።

፲፩ ተቀብለው በባለቤቱ አዘኑበት ።

፲፪ እንዘ ይብሉ እሉ ደኃርት አሐተ ሰዓተ ተቀንዩ ወአስተዓረይኮሙ ምስሌነ ለእለ ጾርነ ክበዳ ወላህባ ለዕለት ።

፲፪ የዕለት ጻሯን ጋሯን ትኩሳቷን ማለት ጧት ጀምረን እስከ ማታ ስንደክም ከዋልን ከኛ ጋራ ገባ እተ ሠርክን አስተካከልሃቸው ብለው አዘኑ ።

፲፫ ወይቤሎ ለ፩ እምኔሆሙ ዓርክየ ኢዓመፅኩከ

፲፫ ከገባእተ ነግህ አንዱን ወዳጄ አልበደ ልሁህም አለው ።
አኮኑ በበዲናር ተከሃልኩከ በድሪም ተስማምቸህ አልነበረም ።

፲፬ ወንሣእ ዘይረከበከ ወሑር ።

፲፬ የሚገባህን ይዘህ ሂድ አለው ።
ወፈቀድኩ ለዝ ደኃራዊ እሀብ ከማከ ።
በኋላ ለመጣው ለዚህ እንዳንተ ልሰጠው ወድጄ ለሁና ።

፲፭ ወሚመ ኢይደልወኒኑ ዘፈቀድኩ እግበር በንዋይየ ።

፲፭ ወይም በገንዘቤ የወደድሁትን ማድረግ አይገባኝምን ።
አው ዓይንከኑ ሐማሚ ውእቱ ዓይንህ ምቀኛ ናት ማለት አንተስ ምቀኛ ነህን ።
ወአንሰ ኄር ።
እኔ ግን ቸር ነኝ ማለት ምቀኛ አይደለሁም ።

፲፮ ከማሁ ይከውኑ ደኃርት ቀደምተ ወቀደ ምት ደኃርተ ።

፲፮ እንደዚሁም ሁሉ ገባእተ ሠርክ ገባእተ ነግህን ገባዕተ ነግህ ገባዕተ ሠርክን ይሆናሉ ።
እስመ ብዙኃን ጽውዓን ወኅዳጣን ኅሩያን ።
ጥቂትም ሁነው ብዙም ሁነው የተጠሩ የተመረጡ ናቸውና ካጠገቡ ሳለው ቀደምት ይከውኑ ደኃርት ወደኃርት ይከውኑ ቀደምተ ሳለው አርእስት ሰጥ እንድም ወሶበ መስየ ብለህ መልስ ፣ ምጽአት በደ ረሰ ጊዜ እምጻኤ ዓለማት ፈጣሬ ዓለማት አብ መጋ ቢሁ ወልድን እምጻኤ ዓለማት ፈጣሬ ዓለማት ወልድ መጋቢሁ መልአኩን ምእመናንን ጠርተህ ከኋለ ኞች ጀምረህ እስከ ፊተኞች ስጥ አለው ። ወመጽኡ እለ ዐሠርቱ ወ፩ዱ ሰዓት ፤ ኋለኞች መጡ ወነሥኡ በበዲናር ። እንደ ሥራቸው ሰጣቸው ወመጽኡ ቀደምት ፊተኞች መጡ ወመሰሎሙ በቀዲመ እቅ ማናት በአብዝኆ ገድላት የሚያበልጥላቸው መሰ ላቸው ነበር ። ወወሀቦሙ ሎሙኒ ለሳቸውም እንደ ሥራቸው ሰጣቸው ። ወነሢኦሙ አን ጐር ጐሩ ማዘን የለም ነገሩ የሚያሰኝ ስለሆነ ነው እንጂ ዋጋ ቸውን ተቀብለው ፍርዱን አደነቁ ። እሉ ደኃርት አሐተ ሰዓተ ተቀንዩ ጥቂት ሰዓት መከራ የተቀበሉ እሊህን ብዙ ዘመን መከራ ከተቀበልን ከኛ ጋራ አስተካከላቸው ብለው አደ ነቁ ። ፤ ወይቤሎ ለ፩ እምኔሆሙ ዓርክየ ፤ ከደኃርት ጻድቃን አንዱን ወዳጄ አልበደልሁህም አለው ።
መፍቀሬ ሰብእ ነውና ዓርክየ ይለዋል ወፈ ቀድኩ ለዝ ደኃራዊ እሀብ ከማከ ወሚመ ኢይደል ወኒኑ እግበር ዘፈቀድኩ በንዋይየ ። እንዲህ ማለት ይህን ተናግሮ ዕንጦንስን ከአስካፍ መቃሪን ከከል

ሎቱ እንስት አዮጺን ከፍላዊ ትሩፍ ቤበኑዳን ከፈያ ታይ መዓንዝር መስደዱን መናገር ነው ።

አው ዓይንከኑ ሐማሚ እስመ አነ ኄር እንዲህ ማለት ገባእተ ሠርክን ከገባእተ ነግህ ገባእተ ነግህ ገባእተ ነግህን ከገባእተ ሠርክ ማለት ኋለኞችን ከፊተኞች ፊተኞችን ከኋለኞች ያስተካከለበትን ፍርዱን ክሱ በቀር የሚያውቀው ሌላ መናሩን መናገር ነው ፤ ክማሁኬ አሁን እንደ ተናገርኩት ገባእተ ሠርክ ገባእተ ነግህን ገባእተ ነግህ ገባእተ ሠርክን ይሆናሉ ። እስመ ብዙኃን ፣ ብዙም ሁነው ጥቂትም ሁነው የተጠሩ የተመረጡ ናቸውና ቀደምት ይከውኑ ደኃርተ ደኃርት ይከውኑ ቀደምት ላለው ለላይኛው ስጥ ። ም ፡ ፲፱ ፡ ቍ ፡ ፴ ።

ሐተታ ፣ ነግህ የተባለ ዘመነ አበው ነው ሠለስት ዘመነ መሳፍንት ቀትር ዘመነ ነገሥት ተሰዓት ዘመነ ካህናት ሠርክ ዘመነ ሥጋዌ ነው ። አንድም ነግህ የተባሉ ዘመነ አዳም ። ሠለስት የተባለ ዘመነ አብርሃም ቀትር ዘመነ ሙሴ ተሰዓት ዘመነ ዳዊት፡ ሠርክ ፡ ዘመነ ክርስቶስ ቀደምት ይከውኑ ደኃርተ ደኃርት ይከውኑ ቀደምት አለ ። በአቤል ጊዜ የነበሩ በዕለተ ዓርብ ያሉትን በዕለተ ዓርብ ያሉት በአቤል ጊዜ የነበሩትን ይሆናሉ ። አንድም በዓጸደ ነፍስ ያሉት ባዓጸደ ሥጋ ያሉትን በዓጸደ ሥጋ ያሉት በዓጸደ ነፍስ ያሉትን ይሆናሉ ። አንድም ነግህ ዘመነ ክርስቶስ ፣ ሠለስት ዘመነ ሐዋርያት ቀትር ዘመነ ሰማዕታት ተሰዓት ዘመነ ሊቃውንት ሠርክ ዘመነ መነኮሳት ዘመነ ሐዋርያትና ዘመነ ክርስቶስ አንድ ወገን ነው ብሎ ፣ ሠለስት ዘመነ ሰማዕታት ቀትር ዘመነ ሊቃውንት ስዓት ዘመነመነኮሳት ሠርክ ዘመነ ደኃርት ጻድቃን ባዕለተ ዓርብ ያሉት በዕለተ ምጽአት ያሉትን በዕለተ ምጽአት ያሉት በዕለተ ዓርብ ያሉትን ይሆናሉ ። አንድም ንሕነ ሕያዋን የተባሉት ኢንበጽሖሙ ለምውታን የተባሉት ንሕነ ሕያዋን የተባሉትን ይሆናሉ ።

በእንተ ትንቢት ሣልሲት ዘሕማማት ።

፲፯ ወእንዘ የዓርግ ኢየሩሳሌም ነሥአሙ ለ፲ወ፪ቱ አርዳኢሁ እንተ ባሕቲቶሙ ። ማር ፡ ፲ ፡ ፴፪ ሉቃ ፡ ፲፰ ፡ ፴፩ ።

፲፯ ወደ ኢየሩሳሌም ሲወጣ ዐሥራ ሁለቱን ደቀ መዛሙርቱን አስከትሏቸው ሄደ ።
ወአግኃሶሙ እምፍኖት ።
ከመንገድ ፈቀቅ አደረጋቸው ፣ሐቀታ ፣ ወቀደሞሙ በፍኖት ይላል በማርቆስ ፣ በፊት ያሉት በኋላ ነው በኋላ ያሉት በፊት ነው ሲሉ ቀድሟቸው ተገኝቷል እንዲህ ሲሆን እሞታለሁ ይላል ብለውታል ።
፲፰ ወይቤሎሙ ናሁ ንዓርግ ኢየሩሳሌም ።
፲፰ ኢየሩሳሌም እወጣለሁ ።
ወይእኅዝዎ ለወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ።
ወልደ ዕጓለ እመሕያውን ይይዙታል ማለት እያዛለሁ ።
ወያገብእዎ ኀበ ሊቃናት ወጸሐፍት ።
ለሊቃናት ለጸሐፍት አሳልፈው ይሰጡኛል ።
ወይኴንንዎ በሞት ።
ይሙት በቃ ይፈርዱብኛል ።

፲፱ ወይሜጥውዎ ለሕዝብ ።
፲፱ ለሕዝብ አሳልፈው ይሰጡኛል ወይሳለቁ ላዕሌሁ ።
ይዘብቱብኛል ።
ወይቀሰፍዎ ።
እገረፋለሁ ።
ወይሰቅልዎ ። እሰቀላለሁ ።
ወይቀትልዎ ።
እሞታለሁ ።
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛው ቀን እነሣለሁ አላቸው ።

በእንተ ደቂቀ ዘብዴዎስ ።

፳ ወእምዝ መጽአት ኀቤሁ እሞሙ ለደቂቀ ዘብዴዎስ ምስለ ደቂቃ ማር ፡ ፲ ፡ ፴፭ ።

፳ ከዚህ በኋላ የዘብዴዎስ ልጆች እናት ማርያም ባውፍልያ ልጆችዋን አስከትላ መጣች ።
ወሰገደት ሎቱ እንዘ ትስእሎ እየማለደች ሰገደችለት ። ሐተታ ፣ እንዲያው አይደለም ኢየሩሳሌም ሊወጣ ሆነ የሹመት ነገር አንድ ጊዜ ከተደሳደለ በኋላ ያስቸግራልና ሂደሽ ተናገሪልን ለዘመድሽ ብለዋታል ፣ ወይቤላ ምንተ ትፈቅዲ እግበር ለኪ. ምን ላደርግልሽ ትወጃለሽ አላት ።

፳፩ ወትቤሎ ረሲ ሊተ ከመ ይንበሩ እሉ ደቂቅየ ፩ዱ በየማንከ ወ፩ዱ በፀጋምከ በመንግሥትከ

፳፩ በመንግሥህ ጊዜ እኒህ ልጆቼ አንዱ በቀኝህ አንዱ በግራህ እንዲቀመጡ አድርግልኝ ማለት አንዱን ቀኝዝማች አንዱን ግራዝማች በልልኝ አለችው ።

፳፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤላ ኢተእምሩ ዘትስእሉ ፤

፳፪ የምትለምኑትን አታውቁም ማለት የባለጸጋ ልጅ ኃዘን ቢነግሩት አደን እንዲሉ እሞታለሁ እሰቀላለሁ ብላችሁ ሹመት ሽልማት ትለምናላችሁ አለ ትክሉኑ ሰትየ ጽዋዕ ዘአነ እስቲ ወጥምቀተኒ ዘአነ እጠመቅ ትጠመቁኑ ።
በዚያውስ ላይ የኔን ጽዋ ትጠጣላችሁ የኔን ጥምቀት ትጠመቃላችሁ ማለት እኔ የምሞተውን ሞት ትሞታላችሁ ኦላቸው ። ሐተታ ጽዋዕ ጥምቀት አለው ሞቱን ። ጽዋ በተራ እንደሆነ ሞትም በተራ ነውና ጽዋ እንዲያፋቅር ሞቱም ያፋቅራልና ጽዋ

ፈጥኖ እንዲጨለጥ ፈጥኖ ተነሥቷልና ወአሕጸረ ፡ ዕድሜ ለርእሱ እንዲል ።

ጥምቀት እንዲያነጻ ሞቱም መንጽሒ ነውና ወይቤልዎ እወ ንክል ፡
አዎን ይቻለናል አሉት ሐተታ ፡ ለጌታ የሚያደርጋ ሰው ሞትህን ሞት ሕይወትህን ሕይወት አደርጋ ለሁ ማለት ልማድ ነውና ። አንድም ለፍቅሩ ይሳሳሉ በፍቅሩ ይናደዳሉና ።

፳፫ ወይቤሎሙ ጽዋዕየሰ ትሰትዩ ወጥምቀት የኒ ትጠመቁ ።

፳፫ ጽዋየን ትጠጣላችሁ ጥምቀቴን ትጠመ ቃላችሁ ማለት ሞቴንስ ትሞታላችሁ ። ወነቢረሰ በየ ማንየ ወበፀጋምየ አኮ እነ ዘእሁብ ። በግራና በቀኝ መቀመጥ ግን የምሰጥ እኔ አይደለሁም ማለት ቀኛ ዝማችነት ግራዝማችነት የምሾም እኔ አይደለሁም ዘእንበለ ዘአስተዳለወ ሎሙ አቡየ ዘበሰማያት ሰማያዊ አባቴ ላዘጋጀላቸው ለነገሥታት ነው እንጂ አእምር ከመ ልዑል ይኬንን መንግሥተ ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው ወዘፈቀደ ይሁብ እስመ ኢይሠ የም መኰንን ዘእንበለ እምኀበ እግዚአብሔር ይል የለም ቢሉ አልመጣሁበትም ሲል እንዲህ አለ ። አንድም በቀኝ በግራ ሁነን እንሰቀል ትላላችሁን በቀኝ በግራ መሰቀል ለናንተ አይደለም ሰማያዊ አባቴ በትንቢት ላዘጋጀላቸው ለፈያታዊ ዘየማን ለፈያታይ ዘፀጋም ነው እንጂ ። አንድም ትክልኑ ብለህ መልስ ። በክብር እንኑር ትላላችሁን እንግዲ ህሰ ወጼሀ በክብር መኖር ለናንተ ብቻ አይደለም ለምእመናን ሁሉ ነው እንጂ ወለዲያቆናትኒ በፀ ጋሙ እንዲል ።

፳፬ ወሰሚዖሙ ፲ቱ አንጐርጐሩ ላዕለ ፪ቱ አኃው ።

፳፬ ዐሥሩ ይኸን ሰምተው በሁለቱ ወንድ ማማቾች አዘኑ ዛሬስ ከዚህ አኑረውን ሹመት ይካ ሰሱብን ጀመር ብለው ።

፳፭ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኢተአምሩኑ ከመ መኳንንቶሙ ለአሕዛብ ይኴንን ዎሙ ወዓበይቶሙ ይቀንይዎሙ ።

፳፭ ጌታ ጠርቶ አሕዛብን ነገሥታቱ እንዲገዟ ቸው ሹማምንቱ እንዲያዟቸው አታውቁምን አላቸው ፤
፳፮ ወለከሙሰ አኮ ከማሁ ።
፳፮ ለናንተ ግን እንዲህ አይደለም ።
፳፯ ወባሕቱ ዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ዓቢየ ይኩንክሙ ገብረ ወዘሂ ይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ ይኩንክሙ ላዕከ ።
፳፯ ከናንተ ወገን ገዥ ሊሆን የወደደ ሰው ተገዥ ይሁናችሁ በላይ ሊሆን የወደደም አገልጋይ ይሁ ናችሁ እንጂ ።

፳፰ እስመ ኢመጽአ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ከመ ይትለአክዎ ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ ይትላአክ ወየሀብ ነፍሶ ቤዛ ብዙኃን ።

፳፰ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ሊያ ገለግል እንጂ ሊያገለግሉት ቤዛ ሊሆን እንጂ ቤዛ ሊሆኑት አልመጣምና ፤ እንዲህም ባለ ጊዜ ፍቅረ ሢመትን አጥፍቶላቸዋል ሁለቱ እኛ የምንገዛቸው መስሎን ነው አንጂ የማንገዛቸው ከሆነ ሹመት ሰምናችን ብለዋል ፀሥሩም የሚገዙን መስሎን ነው እንጂ የማይገዙንማ ከሆነ ቢሾሙ ምንዳችን ብለዋል ።

፳፱ ወእንዘ ይወፅእ እምኢያሪኮ ተለውዎ ሰብእ ብዙኃን ።
፳፱ ከኢያሪኮ ወጥቶ ሲሄድ ብዙ ሰዎች ተከ ተሉት ።

በእንተ ዕውራን ዘኢያሪሆ ።

፴ ወናሁ ፪ቱ ዕውራን ይነብሩ ጥቃ ፍኖት ።
፴ ሁለት ዕውራን እነሆ ከመንገድ ባጠገብ ተቀምጠው ነበር ። ወሰሚዖሙ ከመ እግዚእ ኢየ ሱስ የኃልፍ ጸርሑ ።
ጌታ ሲያልፍ ሰምተው አሰምተው ተናገሩ ።
ወይቤልዎ ተሣሃለነ እግዚእ ወልደ ዳዊት ።
የዳዊት ልጅ አቤቱ እዘንልን አሉት ።
፴፩ ወሰብእሰ ይጌሥጽዎሙ ከመ ያርምሙ።
፴፩ ሰዎች ግን ዝም በሉ ይሏቸው ነበር ። ታምራት ይደረጋል ሰው ይሰባል ወንጌል ትሰፋ ለች አሪት ትጠፋለች ብለው ።
ወአዕበዩ ጸሪሐ እንዘ ይብሉ ተሣሃለነ እግዚእ ወልደ ዳዊት ባይን ዋዛ ብለው የዳዊት ልጅ አቤቱ እዘን ልን ብለው አሰምተው ተናገሩ ።
፴፪ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ወጸውዖሙ ።
፴፪ ለዕውር ርቆ መሄድ አይሆንለትምና ቆሞ ጸራቸው ።
ወይቤሎሙ ምንተ ትፈቅዱ እግበር ለክሙ ።
ምን ላደርግላችሁ ትወዳላችሁ አላቸው ።
፴፫ ወይቤልዎ ከመ ይትከሠታ አዕይንቲነ ።
፴፫ ዕውር ምን ይሻል ቢሉት ብርሃን እንዲሉ አቤቱ ዓይናችን ይበራልን ዘንድ እንወዳለን አሉት።
፴፬ ወእምሐርዎ ለእግዚእ ኢየሱስ
፴፬ ጌታችንን አሳዘኑት ።
ወገሠሦሙ አዕይንቲሆሙ ።
ዓይናቸውን ዳሰሳቸው ።
ወበጊዜሃ ነጸሩ ።
በዳሰሳቸውም ጊዜ አዩ ።
ወተለውዎ ።
ሰጊዜው በእግር ተከተሉት ፍጻሜው በግብር መሰ ሉት ከቋ አርድዕት ገብተው ተቈጠሩ ። አንድም ወእንዘ ይወፅእ እምኢያሪኮ ብለህ መልስ ከልዕ

ልና ወደ ትሕትና በመጣ ጊዜ ነቢያት በግብር መስ ሉት ወናሁ ፪ቱ ዕውራን ይነብሩ ጥቃ ፍኖት ፣ ባሕ ታውያን ክህሁ ዓለም እፍኦ በምትህግ በበረሃ አሉ ። ፍኖት ሐተታ እንዳለፈው ምዕ ፳ ፣ ቍ ፣ ፳፭ ባሕታውያንን ዕውራን አላቸው ከማየት ተከልክ ለዋልና ። ምሥጢር ገና አልተገለጸላቸውምና ፣ ወሰሚያሙ ጊታ በኢጋ እንዲገለጥ ምሥጢር እንዲ ገለጥ ዕውቀው ።

ወይቤልዎ ተሣሃለነ ምሥጢር ገለጥልን አሉት ወሰብአስ ፣ አጋንንት ግን ገድላቸውን ያስተዋቸው ፍጹምመከራ ያጸኑባቸው ነበር በማደሪያቸው ሰብእ እላቸው ። ወአዕበዩ ጽራሐ ፡ ዲያጋንንቱ ፍር ታግ ሠው አመለከቱ ። ወቆመ በጸጋ ተገለጠላቸው ።

ወይቤሎሙ ምን ላደርግላችሁ ትወዳላችሁ አላ ቸው ከመ ይትከሠታ ፣ ምሥጢር ሊገለጥልን እንወዳለን አሉት ። ወገሠሦሙ ምሥጢር ገለጠላ ቸው ወበጊዜሃ ፣ ያን ጊዜ ዐወቁ ። ወተለውዎ ፣ ባሕታውያን በግብር መሰሉት ።

ዘከመ ቦአ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም

ምዕራፍ ፳፩ ።

፩ ወቀረቡ ኢየሩሳሌም በጽሑ ቤተ ፋጌ እንተ ገቦ ደብረ ዘይት ፣ ማር ፲፩፡፩ ፡ ሉቃ ፲፱ ፡ ፩ ፡ ፱ ።
፩ ወደ ኢየሩሳሌም ሊገባ በቀረበ ጊዜ የደ ብረ ዘይት አጠገብ ከምትሆን ቤተ ፋጌ ደረሰ ። ገቦ ይላል ትግሬ አጠገብ ሲል ፋጌ ፎናና የተመሳቀለ ጐዳና ማለት ነው ።
ወሶበሃ ፈነወ እግዚእ ኢየሱስ ፪ተ እምአርዳኢሁ ያን ጊዜ ጌታ ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ላከ ።

፪ ወይቤሎሙ ሑሩ ሀገረ ዘቅድሜክሙ ።
፪ በፊታችሁ ወዳለ ሀገር ሂዱ ። ወይእተ ጊዜ ትረክቡ ዕድግተ ዕሥርተ ምስለ ዕዋላ ።
ያን ጊዜ እህያ ከውርንጭላዋ ጋራ ታስራ ታገኛ ላችሁ ።
ፍትሕዎን ወአምጽእዎን ሊተ ። ፈታችሁ አምጡ ልኝ አላቸው ሐተታ ፣ ሰው ሁሉ ከማእሰረ ኃጢ አት የሚፈታበት ጊዜ እንደደረሰ ለማጠየቅ ።

፫ ወእመቦ ዘይቤለክሙ ምንተ ትገብሩ ።
፫ ምን ታደርጋላችሁ የሚላችሁ ሰው ቢኖር በሉ እግዚእሙ ይፈቅዶሙ ። ጌታቸው ይሻቸዋል በሉ በተፈጥሮ ጌታቸው ነውና እንዲህ አለ ።
ወበጊዜሃ ይፈንውክሙ ።
ያን ጊዜ ያሰናብቷችኋል ።

፬ ወዝ ኵሉ ዘኮነ ከመ ይትፈጸም ዘተብህለ
፬ በነቢይ በልዋ ለወለተ ጽዮን ነዋ ንጉሥኪ ጻድቅ ወየዋህ ይመጽእ ኀቤኪ እንዘ ይጼዐን ዲበ ዕድ ግት ወዲበ ዕዋላ ።

፬ ይህ ሁሉ የተደረገ ጻድቅ
፭ የባሕርይ አምላክ የዋህ ኃዳጌ በቀል ንጉሥሽ በዕዋል በዕድግት ተቀምጦ ይመጣል ብላችሁ ለጽ ዮን ልጅ ንገሯት ብሎ ነቢዩ የተናገረው ቃል ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ።

ሐተታ ፣ ወለተ እሥራኤል ናቸው ጽዮን ኢየ ሩሳሌም ናት ፣ በሀገሪቱ ሰዎቹን መናገር ነው ልጅ ያግሬ ልጅ የጎጃም እንዲሉ እንድም ወለት አይ ለወጥም ጽዮን ሕግ ናት እናት ልጆቹዋን ሠርታ ቀጥታ እንድታሳድግ ሕግም ሕዝቡን ሠርታ ቀጥታ ታኖራለችና ። ቃለ ነቢያት ያለ እንደሆነ አያሳት ትም በልዋ ለወለተ ጽዮን ያለ ኢሳይያስ ይመጽእ ንጉሥኪ ያለ ዘካርያስ ነውና፣ ቃለ ነቢይ ያለ እንደ ሆነ የሁሉ ስም ነውና ፤ ቃ ለኢሳይያስ ይላል አብ ነት ኢሳይያስ እንደ አባት እንደ መምህር ዘካርያስ እንደ ልጅ እንደ ደቀ መዝሙር ናቸውና ።

፮ ወሖሩ አርዳኢሁ ገብሩ በከመ አዘ ዞሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

፯ ወአምጽኡ ሎቱ ዕድግተ ምስለ ዕዋላ ።

፮ ደቀ መዛሙርቱ ሄደው እንደ አዘዛቸው
፯ አደረጉ እህያ ከውርንጭላዋ ጋራ አመ ጡለት ።
ወረሰዩ አልባሲሆሙ ላዕሌሆን ።
ልብሳቸውን ጐዘጐዙለት ። ሐተታ ፣ ኮርቻ ይቀረ ቁራል ልብስ አይቀረ ቁርጥና የማትቀረቁር ሕግ ሠራሁላችሁ ሲል ፣ እንድም ልብስ በአካል ያለውን ነውር ይሰውራል ። አንተም ከባቴ አበሳ ነህ ሲሉ ፣ ወተጽዕነ እግዚእ ኢየሱስ ዲቤሆን ።
በሁለቱም ጌታ በጥበብ ፩ ጊዜ ተቀመጠባቸው ።

ሐተታ ፣ ከኢየሩሳሌም እስከ ቤተ መቅደስ ፣ ፲፫ ምዕራፍ ነው ። ፲፪ቱን በእግሩ ሄዶ ሁለቱን በዕ ድግት ሄዷል በዕዋል ሁና ቤተ መቅደስን ፫ ጊዜ ዞሯል ። የምስትንት ምሳሌ ፣ ዐሥራራቱን በእግሩ መሄዱ ፲ ቃላት ፪ቱ ኪዳናት ኪዳኑ ኖኅ ከሀንተ መልክ ጸዴቅ ግዝረተ አብርሃም ጥምቀተ የሐንስ ነው ። እንድም ፭ቱን ሽህ ካምስት መቶ ዘመን ባራት ባራት መቶ ዘመን ቢቈጽሩት ዐሥራ አራት ሊሆን መቶ ይጐድለዋል ። ይህ ሲፈጸም ሰው እንደሆነ ለማጠየቅ ባህያ መቀመጡ ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ፣ ትንቢት አጠፍዕ ሠረገላ እም ኤፍሬም ወአፍራሰ እምይሁዳ ተብሎ ተነግሯል።

ምሳሌም ቀድሞ አባቶቹ ነቢያት ዘመነ ጸብእ የሆነ እንድ ሆነ በፈረስ ተቀምጠው ዘገር ነጥቀው ይታያሉ ዘመነ ሰላም ቢሆን እንደሆነ ባህያ ተቀም ጠው መነሳንስ ይዘው ይታያሉና ዘመነ ሰላም ደረሰ ሲል ትንቢቱን ባወቀ አናግሯል ምሳሌውንም እንጅ ባወቀ አስመስሏል ምሥጢሩ እንደምነው ቢሉ

ባህያ የተቀመጠ ሸኽቶ እያመለጥም አሳዶም አይ
ዝም እሰም ካልኸኝ አልገኝም ከኸኝም አሊታጣም
ቢል ፡ አንድም እለ ከመ እንተ አድግ ነፍስቶሙ
እንዲል ፡ በንጹሐን መሐይምናን አድሬባቸው እና
ራለሁ ሲል ፡ ዕድግት የእስራኤል ምሳሌ የሠረገላ
ቀንበር መሸከም የለመደች እንደሆነች እስራኤልም
ሕግ መጠበቅ ለምደዋልና ዕዋል የአሕዛብ ቀን
በር መሸከም ያለመደች እንደሆነች አሕዛብም ሕግ
መጠበቅ ያለመዱ ናቸውና ፡ አንድም ዕድግት የኦሪት
ዕዋል የወንጌል ምሳሌ ፡ ዕድግት ቀንበር መሸከም
የለመደች እንደሆን ኦሪትም የተለመደች ሕግ ናትና
ዕዋል ቀንበር መሸከም ያለመደች እንደሆነች ወን
ጌልም ያልተለመደች ሕግ ናትና ።

፰ ወዘይበዝኁ ሕዝብ ነጸፉ አልባሲሆሙ ውስተ
ፍኖት ።

፰ የሚበዙት ሕዝብ ልብሳቸውን በጐዳና አነጠፉ
ሐተታ፡ስንኳን ላንተ ለተቀመጥክባት ለህያ መሬት
መርገጥ አይገባትም ሲሉ ፡ አንድም በኢዩ ልማድ
ኤልሳዕ ከደቂቀ ነቢያት አንዱን ቀርነ ቅብዑን ይዘህ
ሂደህ ኢዩን ቀብተህ አንግሠሽው ፈጥነህ ና ከሰው
ጋራ አትጫወት ብሎ ላከው ። ቢሄድ ኢዩን ከባል
ንጀሮቹ ጋራ ሲጫወት ቢደባባይ ተቀምጦ አገኘው
ብየ መልእክት አለው ። እምኔነኑ እምኀበ መኑ
አለው ከኛን ነው ከሌለ ቢለው ኀቤከ መልአክ
ከንቶ ተልኬ መጥቻለሁ አለው ፡ ከእልፍኝ ይዞት
ገባ ከመዝ ይቤ እግዚአብሔር እስራኤል ቀባዕኩከ ትን
ግሥ ላዕለ ሕዝብየ እስራኤል ብሎ ቀብቶት ሩጦ ሄደ።
ኋላ ኢዩ ወጣ ምን አለህ ንገረን አሉት ። ኢትአ
ምሩኑ ከመ በከ ይዋዋዕ ዝ ብእሲ ፡ ይህ ሰው ዋዛ
ፈዛዛ እንዲናገር አታውቁምን አላቸው ። እውቀን
ንገረን አሉት ፡ ንገረንማ ካላችሁኝ ትነግሣለህ
ብሎ ቀብቶኝ ሄደ አላቸው እኛስ ሌላ ምን እንሻለን
ብለው አኩሌቶቹ አነጸፉዋል አኩሌቶቹ ጋርደዋ
ልና በዚያ ልማድ ።

ወካልዓንኒ ይመትሩ አዕጹቀ እምውስተ ዕፀው
ወይነጽፉ ውስተ ፍኖት ።

ሌሎችም ቅጠል እየቆረጡ ከመንገድ ያነጥፉ ነበር
ሐተታ ፡ ሰሌን ነው ያሉ እንደሆን አብርሃም ይስ
ሐቅን ይስሐቅ ያዕቆብን በወለዱ ጊዜ ፡ እሥራኤል
ከግብጽ በወጡ ጊዜ ፡ የዲት ሆሎፎርኒስን በገደለች
ጊዜ ፡ ሰሌን ቆርጠው ይዘው አመስግነዋልና በዚያ
ልማድ ። አንድም ሰሌን እሾሀም ነው ትእምርተ
ኃይል ትእምርተ መዊእ አለህ ሲሉ ፡ እሱት አይብ
ላውም ለብልዐ ይተወዋል።ባሕርይህ አይመረመርም
ሲሉ ተምር ነው ያሉ እንደሆን ተምር ልዑል ነው ፡
ልዑለ ባሕርይ ነህ ሲሉ ፍሬው አንድ ነው ።
ዋሕደ ባሕርይ ነህ ሲሉ ፍሬው በእሾህ የተከበበ
ነው ባሕርይህ አይመረመርም ሲሉ ዘይት ነው
ያሉ እንደሆን ዘይት ጽኑዕ ነው ጽኑዓ ባሕርይ ነህ
ሲሉ ፡ብሩህ ነው ብሩሃ ባሕርይ ነህ ሲሉ ፡ መሥዋ
ዕት ነው ። መሥዋዕት ትሆናለህ ሲሉ ።

፱ ወሕዝብሰ እለ ይመርሁ ወእለሂ ይተልው
ይጸርኁ ወይብሉ ሆሣዕና ለወልደ ዳዊት ። መዝ፡
፻፲፯ ፡ ፳፯ ። ማር ፡ ፲፩ ፡ ፩ ፡ ሉቃ ፡ ፲፱ ፡ ፴፰ ።

፱ በፊት በኋላ ያሉ ሕዝቡም ለዳዊት ልጅ
መድኃኒት መባል ይገባዋል ። አሉ ።

ሐተታ ፡ ይተልው አዕሩግ ይመርሑ ሕፃናት
ይተልው ሕፃናት ይመርሑ አዕሩግ ይተልው ሐዋ
ርያት ይመርሑ ነቢያት አልፍ ቅድሜሁ አልፍ
ድኅሬሁ ። ጻድቃን በየማኑ ተነሣሕያን በፀጋሙ
እነዚህ ሁሉ ለዳዊት ልጅ መድኃኒት መባል ይገባ
ዋል እያሉ አመስግነዋል ።
ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር ።
በእግዚአብሔር ስም ማለት እግዚአብሔር ነኝ
ብሎ እግዚአብሔር ባወጣለት ስም በስምዓ እግ
ዚአብሔር ፡ እግዚአብሔር ፡ መሰከረለት ፡ የመጣ እሱ
መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌለበት በረከተ
ሥጋ በረከተ ነፍስ የሚያድል ነው አሉ ።
ሆሣዕና በአርያም ።
በሰማይ ያለ መድኃኒት ነው ።

፲ ወበዊአ ኢየሩሳሌም ተሀውከት ኵላ ሀገር
እንዘ ትብል መኑ ውእቱ ።

፲ በኢየሩሳሌም ከተማ በገባ ጊዜ ይህ ማነው
ብለው ከተማዋ ተደሰሰች የሱ ብርሃን ፀሐይን
ሲበዘብዛት አይታ የሕፃናትን ምስጋና ሰምታ ።

፲፩ ወይቤሉ ሕዝብ ዝንቱ ውእቱ ኢየሱስ
ዘእምናዝሬት ዘገሊላ ። ማር ፲፩ ፡ ፲፩ ። ሉቃ ፡ ፲፱ ፡
፵፭ ። ዮሐ ፡ ፪ ፡ ፲፭ ።

፲፩ ሕዝቡ የገሊላ ክፍል በምትሆን በናዝሬት
ያደገ ኢየሱስ ነው አሉ ።
ዘከመ ሰደዶሙ ኢየሱስ ለእለ ያረኵሱ ቤተ መቅ
ደስ ።

፲፪ ወቦአ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ቤተ
መቅደስ ።

፲፪ ጌታ ከቤተ መቅደስ በገባ ጊዜ ።
ወሰደደ ኵሎ እለ ይሰይጡ ወይሳየጡ ውስተ ቤተ
መቅደስ የሚሸጡትን ሁሉ አስወጣ ማለት ገበ
ያውን ፈታ ።
ወገፍትዓ ማዕዳቲሆሙ ለመወልጣን ።
ብሩን ለወርቅ ወርቁን ለብር የሚለውጡበትን ሰፍ
ራቸውን አፈረሰባቸው ።
ወመናብርቲሆሙ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ፡ ንግዳ ።
ርግብ የሚሸጡትንም ወንበራቸውን ገለበጠባቸው።

ሐተታ ፡ የከተማ ቅሬ በወንበር ተቀምጣ ዶሮ እን ድትሸጥ እንሱ ቋንጤ ወምበር አላቸው ከዚያው ላይ ሁነው ርግብ ይሸጣሉና ።

፲፫ ወይቤሎሙ ጽሑፍ ቤትየሰ ቤተ ጸሎት ይሰመይ ። ኢሳ ፶፯ ፡ ፯ ፡ ኤር ፡ ፯ ፡ ፲፩ ፡ ሉቃ ፡ ፲፱ ፡ ፵፯ ።

**፲፫ ቤቴ ቤተ መቅደስ የጸሎት ቤት ይባላል የሚል ጽሑፍ አለ ። ወአንትሙሰ ረሰይክምዎ በአተ ፈያት ወሰረቅት ።**

**እናንተ ግን የሌባ ዋሻ የወንበዴ ጋሻ አደረጋችሁት። ግዚያ ከሆን ግን የተሰረቀውን የተቀማውን ይሸ ጡበታል ይለውጡበታልና እንዲህ አለ ። አንድም ግብያው የሕዝቡ ነው ያሉ እንደሆነ ሁለቱን ቅጽር ወደ ውስጥ አንዱን ቅጽር ወደ ውጭ አድርገው ግብያ አድርገዋል ስለምን ቢሉ ቀረጥ ፈርተው ።**

**ግብያ ገብተው አይተርጉሟቸውም** ቢሉ አይ **ገባቸውም** እንደ ሕጋቸው ይገዟቸዋል እያወጡ ይሸጣሉ እንድም ድል ገበያ ሲሆን እጅም ያስፈራ ነበርና ዘግቶ ለመዋጋት ። የካህናት ክልክል መስክ አለ ከካህናት አንዱ የሚያስወገሽ ልብስ ለብሶ ወደ ክብቱ ሂዶ ይቆማል ወግሽቶ ይገባል አውጥቼ ልውሰድ ያለ እንደሆነ ከሊ የገባ አይነጣ ቤተ መቅ ደስ የገባ አይወጣ እያሉ በምክንያት ያስቀሩባቸዋልና እንዲህ አለ ። ገበያው የካህናቱ ነው ያሉ እንደሆነ ካምስተኛው ቆመ ብእሲ አድርገውታል ። ለመሥ ዋዕት ይሆናል ብሎ የሰባውን ከሩቅ አገር ነድቶ ይዞ ይመጣል ፣ ከመንገድ ይከሳበታል እመቦ ዘቦ ዝክር ሙናይ ዘያበውእ በግዓ ንውረ ርጉም ውእቱ ትላለች ኦሪት ይኸን ለምን አመጣኸው ይሉታል እኔስ የሰባውን ነበር ያመጣሁት ከመንገድ ከሳብኝ እንጂ ይላል ቅንነቱማ ካለ የሰባ የኛ አለ ባንድ ሁለት ለውጠህ አትሠዋም ይሉታል እሺ ብሎ ለውጦ ይሠዋልና ።

ቀይ ወርቅ ያጣ እንደሆነ ነጭ ወርቅ ይዞ ይመጣል ፣ ለምን ይኸን አመጣህ ይሉታል ቀይ ወርቅ ባጣ ነው እንጂ ይላል ቅንነቱማ ካለ ከኛ ቀይ ወርቅ አለ ባንድ ሁለት አትሰጥም ይሉታል እንዲህ እያሉ ሁለተኛ ይቀበሉታልና እንዲህ አለ።

፲፬ ወመጽኡ ኀቤሁ ዕውራን ወሐንካሳን በቤተ መቅደስ ።

፲፬ ጌታ በቤተ መቅደስ ሳለ ዕውራን ሐንካሳን መጡ ።

ወአሕየዎሙ ።

አዳናቸው ።

፲፭ ወሶበ ርእዩ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት መን ክረ ዘገብረ ወደቂቅኒ እንዘ ይጸርኁ በቤተ መቅ ደስ ወይብሉ ሆሣዕና ለወልደ ዳዊት ።

፲፭ ሊቃነ ካህናት ጸሐፍትም ያደረገውን ታም ራት አይተው ለዳዊት ልጅ መድኃኒት መባል ይገ ባዋል ብለው ሲያመሰግኑ የሕፃናቱንም ምስጋና ሰምተው ኢሐወዘሙ ።

ደስ አላሰኛቸውም ። ኢሐወዘኒ ሰበ ሞቱ ፣ ኢሐወዘኒ ሰዕማኤ አፉክሙ እንዲል ።

፲፮ አሳ አንጐርጐሩ ።

አዘኑ እንጂ ።

ወይቤልዎ ኢትሰምዕኑ ዘይብሉ ፣

እሉ ሕፃናት ። መዝ ፡ ፰ ፡ ፪ ።

፲፮ እሊህ ሕፃናት የሚሉትን አትሰማምን አሉት ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እወ ።

እምን እሰማለሁ ይገባኛል ብየ ነው እንጂ አላቸው ፣ አልቦሁ አመ አንበብክሙ ዘይቤ እምአፈ ደቂቅ ወሕፃናት አስተዳሎከ ስብሐተ ።

እንዲገባኝማ ለማጠየቅ ከልጆች ከሕፃናት አፍ ምሥጋና አዘጋጅ ያለውን የተመለከታችሁበት ጊዜ የለም አልተመለከታችሁም አላቸው ። ሐተታ ፣ ደቂቅ የመንፈቅ ያመት ሕፃናት ያመት ከመን ፈቅ የሁለት ዓመት ። አንድም ደቂቅ ያርባ የሰማንያ ቀን ሕፃናት የመንፈቅ ያመት ናቸው ። ስንዚህ መሥዋዕት ሊሰውላቸው ዕጐለ ርግብ ዘወግ ማዕነቅ ይዘውላቸው ወጥተዋል ሕፃናትም እናት አባታቸውን ተከትለው ወጥተዋል እዕ ባን ሲያመሰግኑ አይተው ከናቶቻቸው ትከሻ እየወረዱ ሰሌን እየቆረጡ ይዘው አመሰግነዋል ።

፲፯ ወኃደጎሙ ወወፅአ አፍአ እም ሀገር ወቦአ ቢታንያ ወቤተ ህየ ።

፲፯ ትቷቸው ከከተማ ወጥቶ ቢታንያ ገብቶ አደረ ።

በእንተ በለስ ዘተረግመት ።

፲፰ ወጸቢሖ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ የዓርግ ሀገረ ርኀበ ፣

፲፰ ማለዳ ወደ ከተማ ሲወጣ ተራበ

፲፱ ወርእየ ዕፀ በለስ በፍኖት ፣ ማር ፲፩ ፡ ፲፫ ።

፲፱ በመንገድ ዕፀ በለስን አየ ፣

ወሖረ ኀቤሃ ይንግእ ፍሬ እምኔሃ ።

ፍሬ ጥገኝባት ብሎ ወደሷ ሄደ ወኢልቦ ዘረከበ ውስቴታ ዘእንበለ ቆጽል ባሕቲቱ ።

ከቅጠል ብቻ በቀር ፍሬ አላገኘባትም ።

ወይቤላ ኢይኩን ፍሬ እምውስቴትኪ ለዓለም ፣ እንግዲህ ወዲህ ለዘላለም ፍሬ አይገኝብሽ ብሎ ረገማት ፣ ወየብሰት በጊዜሃ ይእቲ በለስ ያን ጊዜ ፈጥና እንድም በምትለመልምበት ጊዜ ደረቀች

ሐተታ ፣ በማርቆስ እስመ ኢኮነ ጊዜሁ ለበለስ ይላል ሊቁም እስመ ሙዋዕለ ክረምት ውእቱ ይላል እንደሌለ ያውቅ የለም ቢሉ አንዳንድ በዘረ በለስ አይታጣም ብሎ ያው ቅሉ እንደሌለ ያውቅ የለም

ቢሉ አላዋቂ ሥጋን እንደ ተዋሐደ ለማጠየቅ ፡ እኮ ኢያእምሮ ኀቡአተ እላ ከመ የሀብ ሙከነ ለጥንተ ትስብእቱ ዘኢየአምር ኅቡአተ እንዲል ፡ አንድም አውቃለሁ ብሎ ሥራውን አይተውምና በዚያው ሥራውን ለመሥራት ፡ እንድም ወጸቢሖ ብለህ መልስ ሰው በሆነ ጊዜ ሰው ሁኖ ሲያስተምር ከሰው ፍቅር ተራብ ወርእየ ዕፀ በለስ እሥራኤልን በኢየሩሳሌም አገኘ በለስ ዘይቤ ቤተ እሥራኤል እሙንቱ እንዲል ወሖረ ህቤሃ ፡ ሃይማኖት ምግባር ባገኘባቸው ብሎ ሄደ አላገኘባቸውም ዘእንበለ ቆጽል ባሕቲቱ እሥራኤል ከመባል በቀር እሥራኤል መባል ብቻ ነው እንጂ ወይቤላ ኢይኩን እንከ ፍሬ ደግ ሰው እንዳ ይገኝብሽ ብሎ ረገማት ወየብሰት ፡ ያን ጊዜ ደግ ሰው ጠፋ ። ምነው እስጢፋኖስ ጳውሎስ ኤጲፋን ዮስ ፲፬ አልፍ ካራት ሽህ ሰማዕታት ሕፃናት የተ ገኙ ከእሥራኤል አይደለም ቢሉ ከነሆ በቀር ቢል ነው አንድም መልስ አሪትን በዚህ ዓለም ሰፍና አገኛት ፡ ወሖረ ኀቤሃ ፡ ፈጻሚ ሕግ ተባለ ። ወአልቦ ዘረከበ ዘእንበለ ቆጽል ፡ ፈጻሚ ሕግ ከመባል በቀር ድኅነትን አላደረገባትም ።

ወይቤላ ኢይኩን ፍሬ ባንቺ ድኅነት አይደረግ አላት ። ወየብሰት ፡ አሪት ፈጥና ዐረፈች ። አንድም ወርእየ ዕፀ በለስ ብለህ መልስ የበለስ ቅጠል ስፌ እንደሆነ ኃጢአትን በዚህ ዓለም ሰፍና አገኛት ። እንድም በለስ ሲበሉት ያጣፍጣል ቆይቶ ይኮመ ጥጣል ። ኃጢአትም ሲሠሩት ደስ ያሰኛል ኋላ ያሳዝ ናልና ፡ ወሖረ ኀቤሃ ኃጥእ ተባለ ወአልቦ ዘረከበ ፡ ኃጥእ ተመባል በቀር ኃጢአት አልሠራም ። ወይ ቤላ ኢይኩን እንከ ፍሬ ፡ ባንቺ በመጣ ፍዳ የሚ ያዝ አይኑር አላት ወየብሰት ፡ ኃጢአትም ፈጥና ጠፋች ። በአንጻረ በለስ ረገማ ለኃጢአት እንዲል።

በእንተ ትውክልት ኀበ እግዚአብሔር ።

፳ ወርእዮሙ አርዳኢሁ አንከሩ ወይቤሉ እፎ በጊዜሃ የብሰት በለስ ። ማር ፲፩ ፡ ፳ ።

፳ ደቀ መዛሙርቱ አይተው በምትሰመልም በት ጊዜ ፈጥና እንደ፯ምን ደረቀች ብለው አደነቁ ።

፳፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እማን እብለክሙ ከመ እመ ብክሙ ሃይማኖት ወኢትናፍቁ አኮ ከመ ዕፀ ባሕቲቶ ዘትገብሩ ማቴ ፡ ፲፯ ፡ ፲፱ ።

፳፩ ሃይማኖት ቢኖራችሁ ባትጠራጠሩ ዕን ጨት ብቻ አድርቃችሁ እትቀሩም ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ።

አላ ለዝንቱኒ ደብር እመ ትብልዎ ፍልስ ወተ ወረው ውስተ ባሕር ይትገበር ለክሙ ። ይኸንም ተራራ ከዚህ ተነሥተህ ከባሕር ግባ ብትሉት ይደረ ግላችኋል እንጂ ታሪክ እንዳለፈው ም፡ ፲፯ ፡ ቍ፡ ፩ ።

፳፪ ወኵሎ ዘሰአልክሙ በጸሎት እንዘ ትት አመኑ ትነሥኡ ።

ማቴ ፡ ፯ ፡ ፯ ፡ ማር ፡ ፲፩ ፡ ፳፬ ፡ ዮሐ ፡ ፲፬ ፡ ፲፫ ፡ ፲፮ ፡ ፳፫

፳፪ በሃይማኖት ጸንታችሁ የለመናችሁትን ሁሉ ታገኛላችሁ ።

ዘከመ ተስእሎሙ እግዚእ ኢየሱስ በእንተ ጥምቀተ ዮሐንስ

፳፫ ወበዊአ ቤተ መቅደስ እንዘ ይሜህር መጽኡ ኀቤሁ ሊቃነ ካህናት ወመላህቅተ ሕዝብ ወይቤልዎ በመባሕተ መኑ ትገብር ዘንተ ።
ማር ፲፩ ፡ ፳፰ ። ሉቃ ፡ ፳፡፪ ።

፳፫ ከቤተ መቅደስ ገብቶ ሲያስተምር ሊቃነ ካህናት የሕዝቡም አለቆች መጥተው ይህን የምታ ደርግ ከምድራውያን ነገሥታት ከሌዋውያን ካህ ናት ወገን ያይደለህ ገበያውን መፍታትህ ማን እስ ናብቶህ ነው ። ወመኑ ወሀበከ ዘንተ ሥልጣነ በማን ሥልጣን ነው አሉት ።

፳፬ ወአውሥአ ። መለሰ ወይቤሎሙ እሴ አለክሙ አነሂ አሐተ ቃለ ።

፳፬ እኔም አንድ ነገር እጠይቃችኋለሁ አላ ቸው ። ሐተታ ቢጠይቁት መመለስ ነው እንጂ መጠ የቅ ይገባልን ቢሉ ቅድሚያ አለኝ ቢል ነው ምሳሌ በግዕን ጠይቋቸው አልመለሱለትም ነበርና ። አንድም እንደ ምላሽ ያለ ጥያቄ ነው ። እምከመ ነገርክሙኒ አነሂ እየድዓክሙ በአይ ሥልጣን እገ ብር ዘንተ ።
የነገራችሁኝ እንደሆነ ገበያውን የምፈታ በማንም ሥልጣን እንደሆነ እኔም እነግራችኋለሁ ።

፳፭ ጥምቀቱ ለዮሐንስ እምአይቴ ውእቱ ፡
፳፭ የዮሐንስ ጥምቀት ከወዴት ነው ማለት ዮሐንስ ማስተማሩ በማን ፈቃድ ነው ።
እምሰማይኑ ወሚመ እምሰብእ ከሰማይ ነውን ማለት በእግዚአብሔር ፈቃድ ነውን ፡ ወይስ በሰው ፈቃድ ነው አላቸው ወሐለዩ በበይናቲሆሙ ወይቤሉ ። እርስበርሳቸው እንዲህ አሉ ።
፳፮ እመ ንብሎ እምሰማይ ይብለነ በእፎ ዘኢ አመንክምዎ ፡ ማቴ ፡ ፲፬ ፡ ፲፭ ።
፳፮ በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው ብንለው ምነው ያላመናችሁበት ይለናል ።
ወእመ ንብሎ እምሰብእ ንፈርሆሙ ለሕዝብ ፡
በሰው ፈቃድ ነው ብንለው ሕዝቡን እንፈራለን ። እስመ ከመ ነቢይ ይሬስይዎ ለዮሐንስ በኀቤሆሙ ዮሐንስን እንደ አባት ያከብሩታል እንደ መምህር ያፍሩታልና ወእውሥኡ መለሱ ።

፳፯ ወይቤልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ኢነአምር።
፳፯ አናውቅም አሉት ።
አነሂ ኢያየድዓክሙ በአይ ሥልጣን እገብር ዘንተ።
ገበያውን በማንም ሥልጣን እንደ ፈታሁት እኔም አልነግራችሁም አላቸው ።
፳፰ ወምንተ ትብሉ ።

፳፰ ምን ትፈርዳላችሁ ። ብእሲ ቦቱ ፪ቱ ደቂቅ እኅው ፤ ላንድ ሰው ሁለት ልጆች አሉት ። ወይቤሎ ለቀዳማዊ ሑር ወወልድየ ተቀንይ የም ውስተ ዐፀደ ወይንየ ።
ታላቁን ልጁን ልጄ ዛሬ ሂደህ ወይን ጠብቅ አለው

፳፱ ወአውሥአ ወይቤ እሆ እግዚእየ ።
እሺ አለው ።
ወኢሖረ ።
ሳይሄድ ቀረ ።

፴ ወለካልኡኒ ይቤሎ ከማሁ ፤
፴ ታናሹን ሂደህ ወይኑን ጠብቅ አለው ።
ወይቤ እንብየ ።
አይቻለኝም አለ ።
ወእምድኅረዝ ነስሐ ወሖረ ።
ከዚህ በኋላ ያባቴን ትእዛዝ አፈረስሁን ብሎ ሄደ ።

፴፩ መኑ እንከ እምክልኤሆሙ ዘገብረ ፈቃደ አቡሁ ።
፴፩ እሄዳለሁ ብሎ ከቀረውና አልሄድም ብሎ ከሄደው ያባቱን ፈቃድ የፈጸመ ማነው አላቸው ።
ወይቤልዎ ደኃራዊ ።
ታናሹ ነዋ ታላቁማ ዘበተበት እንጂ አደረገስትን አሉት ።

ሐተታ ፤ ታላቅ ልጅ የተባሉ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ። ታናሽ ልጅ የተባሉ ኃጥአን መጸብሐን ናቸው ። እሄዳለሁ ብሎ እንደ ቀረ ኦሪትን ተቀብለው በወንጌል ሳያምኑ ቀርተዋል ። አልሄድም ብሎ እንደሄደ ኃጥአን መጸብሐንም ሕጉን ካፈረሱ በኋላ በወንጌል አምነዋልና ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለክሙ ከመ መጸብሐን ወዘማውያን ይቀድሙክሙ በዊአ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
ኃጥአን መጸብሐን ቀድመዋችሁ መንግሥተ ሰማይ ይገባሉ ብየ እንዲገቡ በውነት እነግራችኋለሁ ። መከተሉስ አለና እንዲህ አለ ቢሉ ቢያምኑ እንዲ ያገባቸው ለማጠየቅ ፤

፴፪ እስመ መጽአ ኀቤክሙ ዮሐንስ በፍኖተ ጽድቅ ወኢ አመንክምዎ ።
፴፪ ዮሐንስ ወንጌልን ቢያስተምር አንቀበልህም ብላችሁታልና ወመጸብሐንሰ ወዘማውያን አምንዎ ።
ኃጥአን መጸብሐን ግን አምነውታልና ።
ወአንትሙሰ ርኢክሙሂ ኢነሳሕክሙ ።
እናንተ ግን አይታችሁ አላመናችሁም ።
ድኅረ ለአሚን ቦቱ ።
ኋላ ለማመን ፤ አንድም ድኅረ ከመ ትእመኑ ቦቱ ኋላ ታምኑበት ዘንድ ። አንድም ነሳሕክሙ ድኅሬሁ ለአሚን ከማመን ወደኋላ አፈገፈጋችሁ ። አንድም ድኅሬሁ ፤ ኋላ ታምኑበታላችሁን ። ድኅረሰ ተአምኑ ቦቱ ኋላ ግን ታምኑበታላችሁ እርሱ ርእይ ታመጽእ አሚነ ፤ እንዲል ፤ እርሱ ኮነ ወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ይሉታልና ።

በእንተ አኩያን ገባዕት ።

፴፫ ወይቤሎሙ ካልዕተ ምሳሌ ስምዑ ።
ኢሳ ፤ ፭ ፤ ፩ ፤ ኤር ፤ ፪ ፤ ፳፩ ። ማር ፤ ፲፪ ፤ ፩ ፤ ሉቃ ፤ ፳ ፤ ፱ ።

፴፫ ፪ኛ ምሳሌ ስሙ ፤ ብእሲ በዓለ ቤት ተከለ ዐጸደ ወይን ። ባለቤት ወይን ተከለ ፤ ዐጸድ ወይን አፍለስከ እምግብጽ እንዲል ፤ ዐጸደ ወይን ሐረገ ወይን ጕንደ ወይን ምንዳደ ወይን ይላል አብነት ።
ወገብረ ሎቱ ጸቆነ ።
ቅጽር ቀጠረለት ።
ወአክረየ ሎቱ ምክያደ ።
የዘቢብ ማስጫ ውድማ አበጀለት ።
ወሐነጸ ማኅፈደ ።
ለጠባቂ ማንብ ሠራ ።
ወሤመ ዓቀብተ ።
ጠባቂ ሾመ ።
ወወሀቦሙ ለዓቀብት ወነገደ ።
ጠባቂ ሹሞ ሄደ ።

፴፬ ወአመ በጽሐ ጊዜ ፍሬሁ ፈነወ አግብርቲሁ ኀበ ዓቀብቶ ወይን ፤
፴፬ የሚያፈራበት ጊዜ ቢደርስ ብላቴኖቹን ከጠባቆች ላከ ።
ከመ ያምጽኡ ሎቱ እምፍሬ ወይኑ ።
ከወይኑ ፍሬ ያመጡለት ዘንድ አምጡ ብሎ ፤

፴፭ ወአኃዝዎሙ ዓቀብት ለአግብርቲሁ ።
፴፭ ጠባቆች ብላቴኖችን ይዘው ፀ ዘቀተሉ።
የገደሉት አለ ።
ወቦ ዘወገሩ ።
በደንጊያ የመቱት አለ ።
ወቦ ዘቀሠፉ ።
የገረፉት አለ ።

፴፮ ወእምዝ ፈነወ ካልዓነ አግብርተ ዘይበዝኁ እምቀደምት ።
፴፮ ከዚህ በኋላ ከቀደሙት የሚበዙ ሌሎች ብላቴኖች ላከ ። ወኪያሆሙኒ ከማሁ ረሰይዎሙ እላቸውንም እንደዚሁ አደረጓቸው የገደሉት በደንጊያ የመቱት የገረፉት አለ ።

፴፯ ወድኅረ ፈነወ ኀቤሆሙ ወልዶ እንዘ ይብል የኀፍርዎ ለወልድየሰ ።
፴፯ ከዚህ በኋላ ልጁንስ ቢሆን ያከብሩታል ባይሆንም ያፍሩታል ብሎ ልጁን ላከ ።

፴፰ ወሶበ ርእይዎ ዓቀብት ለወልዱ ወይቤሉ በበይናቲሆሙ ነዋ ዝንቱ ውእቱ ወራሲሁ ንዑ ንቅትሎ ወንርከብ ርስቶ ። ማቴ ፤ ፳፯ ፤ ፬ ፤ ፳፯፡፩።

፴፰ ጠባቆች ባዩት ጊዜ ርስቱ ይገባኛል የሚል እነሆ ይህ ነው እሱን ገድለን ርስቱን እጅ እናድርግ አሉ ፤

፴፱ ወነሥእዎ ወአውፅእዎ አፍአ እምዓጸደ ወይን ወቀተልዎ ። ዮሐ ፤ ፲፩ ፤ ፶፫ ።

፴፱ ይዘው ከወይኑ ቦታ አውጥተው ገደሉት የሰው ደም ተክል የደርቃል ይባላልና ።

፵ ወሶበ መጽአ በዓለ ዓጸደ ወይን ምንተ ይሬስዮሙ ለእሉ ዓቀብት ።

፵ የወይኑ ባለቤት በመጣ ጊዜ ምን ያደርጋ ቸዋል እነዚህን ጠባቆች አላቸው ።

፵፩ ወይቤልዎ በእኪት ለእኩያን ያጠፍዖሙ

፵፩ እንደመሰለባቸው ያወቁት እንዲህ የሚያ ደርግ የለም ብለዋል ፤ ያላወቁት ግን ይሙት በቃ ፈርዶ ይገላቸዋል አሉ ፤

ወወይናኒ ይሁብ ለካልዓን ዓቀብት ።

ወይኑንም ለሌሎች ሰዎች ያስጠብቃል ።

ለእለ ይሁብዎ ፍሬሁ በበጊዜሁ ፍሬውን በየጊዜው ለሚያቀርቡለት ።

ወበበእግዋሊሁ ።

በየዘለላው ፤ ካንዱ ዘለላ ቀይ ጥቁር ነጭ ያፈራልና እንድም ብእሲ በዓለ ቤት ብለህ መልስ ፤ እምጺኤ ዓለማት ፈጣሬ ዓለማት አብ ሕገ ኦሪትን ሠራ፤ ወገብረ ሎቱ ጸቆነ ፤ በኦሪት ረድኤት እንዲገኝ ማድረጉን መናገር ነው ፤ ወአከረየ ምሥዋዓ ብር ትን ፤ ወሐነጸ ቤተ መቅደስን ሠራ ፤ እንድም ወአከ ረየ ልቡናን ፤ ወሐነጸ ማኅፈደ ተልዕሎተ ትን ቢትን ፤ እንድም እምጺኤ ዓለማት ፈጣሬ ዓለማት አብ በልጁ ህልው ሁኖ ወንጌልን ሠራ ወገብረ ሎቱ፤ በወንጌል ልጅነት እንዲገኝ አደረገ ።

ወአከረየ ፤ ንዋየ ቅድሳትን ፤ ወሐነጸ ቤተ ክር ስቲያንን ሠራ ። እንድም ወአከረየ ስፍሐ አእምሮን ወሐነጸ ተልዕሎተ ፤ ሃይማኖትን ሠራ ፤ ወወሀቦሙ ለዓቀብት ። ጠብቁ ብሎ ሕግ መሥራቱን መናገር ነው ወአመ በጽሐ ። ሃይማኖት የሚይዙበት ምግ ባር የሚሠሩበት ጊዜ ቢደርስ ፈነወ አግብርቲሁ ፤ ሃይማኖት ምግባር ያሠሩለት ዘንድ ዓበይተ ነቢ ያትን ላከ ፤ ወነሥእዎሙ ሕግ መጠበቅ የሚገባ ቸው ሕዝቡ ዓበይተ ነቢያትን ደቂቀ ነቢያትን ይዘው ቦ ዘቀተሉ ፤ የገደሉት አለ እነ ኢሳይያስን ወቦ ዘወገሩ እነኤርምያስን ። ወቦ ዘቀሠፉ ፤ እለ እሞጽን ሠያጤ በለስ ብለው ገርፈውታል ። ወእምዝ ፈነወ ከዚህ በኋላ ከዐበይተ ነቢያት የሚበዙ ደቂቀ ነቢያትን አስተምሩ ብሎ ላከ ። ወኪያሆሙኒ ከማሁ እሳቸውንም እንደነዚያ አደረጓቸው ። ወእ ምዝ ፈነወ ከነዚህ ሁሉ በኋላ ልጁን በሥጋ ላከ ።

ልጄንስ ቢሆን ያከብሩታል ባይሆን ያፍሩታል ብሎ ፤ ወሶበ ርእይዎ ፤ ሕግ መጠበቅ የሚገባቸው ሕዝቡ ሰው ሁኖ ባዩት ጊዜ መምህርነት ይገባኛል የሚል እነሆ መጣ ንዑ ንቅትሎ እሱን ገድለን መም ህርነቱን ገንዘብ እናድርግ አሉ ። ወአውፅእዎ ከከ ተማው አፍአ አውጥተው በቀራንዮ ሰቅለው ገደ ሉት ። እንድም ሕግ መጠብቅ ከሚገባው ከል ቡናቸው አውጥተው ጠልተው ተመቅኝተው ሰቅ ለው ገደሉት ።

ወሶበ መጽአ ምንተ ይሬስዮሙ ሲል ነው ። የሕጉ ባለቤት ጌታ በመጣ ጊዜ ምን ያደርጋችኋል አላ ቸው ፤ ወይቤልዎ በእኩይ ለእኩያን ይቀትሎሙ ። ፈርዶ ያጠፋቸዋል አሉት ። ወወይናኒ ይሁብ ፤ ሕጉንም ለሌሎች ያስጠብቃል ። ለእለ ይሁብዎ ።

በዓሉን በየጊዜው ለሚያከብሩ መጸለት ሰዊት ፋሲካ ነው ። ወበበእግዋሊሁ በየእገባቡ ።

፵፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አልቦሁ አመ አንበብክሙ ውስተ መጻሕፍት እብን እንተ መነ ንዋ ነደቅት ይእቲ ኮነት ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ።መዝ ፻፲፯፥፳፩ ። ግብ፡፬፡፲፩። ሮሜ፡፱፡፴፫ ። ፩፡ጴጥ፡፪፡፯ ።

፵፪ እናጢዎች የናቋት ደንጊያ የማዕዘን መሰ ብሰቢያ ሆነች ፤እምኀበ እግዚአብሔር ኮነት ዛቲ ። ይህች በእግዚአብሔር ፈቃድ ሆነች ።

ወነካር ይእቲ ለአዕይንቲነ ።

ለዓይነ ልቡናችን ድንቅ ናት ብሎ መጽሐፍ የተናገረውን የተመለከታችሁበት ጊዜ የለምን አላ ቸው ። እንድም እንተ መነንዋ ብለህ መልስ አሕ ዛብ የናቋት አሪት በ፬ ማዕዘን መከበሪያ መጽደቂያ ሆነች ። እምኀበ እግዚአብሔር ። መናቋም መከ በሪያ መጽደቂያ መሆንዋም በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው ። ነቋም እግዚአብሔር እብ ነው ወነካር ለዓይነ ልቡናችን ድንቅ ናት ። እንድም እብን እንተ መነንዋ አሕዛብ የናቁት ዘሩባቤል ንጉሠ ነገሥት ሆነ ። መናቁም ንጉሠ ነገሥት ። መሆኑም በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው ወመንከር በል ለዓይነ ልቡናችን ድንቅ ነው ወያዕቆብስ ያስተኤሪ ንጉሠ እንዲል ሁለቱ ካሥሩ ነገድ ከተለዩ በኋላ አንድ አድርጎ ነግሷልና ። እንድም እብን እንተ መነንዋ ሐና ቀያፋ የካዱት ክርስቶስ ንጉሠ ነገ ሥት በሥረ ምእመናን ሆነ ሐተታ ። ነደቅት አላ ቸው የሰውን ልቡና በትምህርት እናንጻለን ይላሉና እምኀበ እግዚአብሔር ኮነት ።

መናቁም በሥረ ምእመናን ንጉሠ ነገሥት መሆኑም በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው ነቁም እግዚአብ ሔር ነው ወመንከር ፤ ለዓይነ ልቡናችን ድንቅ ነው ። እንድም እብን እንተ መነንዋ ፤ ጸሐፍት ፈሪሳውያን የናቋት ወንጌል ፤ በአራት ማዕዘን መከበሪያ መጽደቂያ ሆነች ፤ እም ኀበ እግዚአብሔር ። መና ቋም መከበሪያ መጽደቂያ መሆንዋም በእግዚአብ

ሐር ፈቃድ ነው ነቋም እግዚአብሔር ወልድ ነው።
ወነካር ፤ ለዓይነ ልቡናችንም ድንቅ ናት ።

፵፫ ወበእንተዝ እብለክሙ ከመ ይነሥእዋ እም
ኔክሙ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ወይሁብዋ ለሕ
ዝብ ዘይገብሩ ፍሬሃ ።

፵፫ ስለዚህ ነገር ማሰት አንቀበልም ስላችሁ
ወንጌልን ከናንተ ነሥተው ሥራቷን ለሚሠሩ ለሌ
ሎች ሰዎች ያስጠብቋታል ብየ እነግራችኋለሁ ፤
እንዲሁም ባለ ጊዜ ክህነትንም መንግሥትንም ከላ
ቸው እንዳሳለፈባቸው ያጠይቃል ።

**፵፬ ዘሰ ወድቀ ዲበ ይእቲ እብን ይትቀጠቀጥ ።**

፵፬ ከደንጊያ ላይ የወደቀ ይሰበራል ወለዘሂ
ወድቀት ዲቤሁ ተሐርያ የወደቀችበትም ይሰበ
ራል ። ሐተታ ፤ በላይም ሆነ በታችም ሆነ ደን
ጊያ ሰባሪ ሰው ተሰባሪ ነው ። አንድም ዘሰ ወድቀ
በዕለተ ዓርብ በጌታ በጠላትነት የተነሣበት አይ
ሁዳዊ ፤ ይትቀጠቀጥ ፤ በታምራት ይጠፋል ወዘሂ
ወድቀት ። ጌታ በታምራት የተነሣበት አይሁዳዊ
የሐርያ ። በአርባ ዘመን በጥጦስ ይጠፋል ።
አንድም ዘሰ ወድቀ ዲበ ዕብን በዕለተ ዓርብ በጌታ
በጸላትነት የተነሣበት አይሁዳዊ በ፵ ዘመን በጥ
ጦስ ይጠፋል ። ወለዘሂ ወድቀት ዲቤሁ ። ጌታ
በአርባ ዘመን በጥጦስ በጠላትነት የተነሣበት አይ
ሁዳዊ ተሐርያ ፤ በምጽአት ይጠፋል አንድም በመ
ባሕተ መኑ ትገብር ዘንተ በማለት በጌታ በጠላትነት
የተነሣ አይሁዳዊ ይትቀጠቀጥ ። ጥምቀቱ ለዮሐ
ንስ እምኀበ አይቴ ባለው ይረታል ። ክርስቶስ ወልደ
መኑ በማለት ጌታ በጠላትነት የተነሣበት አይሁ
ዳዊ ዘለሊሁ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ በእፎ ይከውኖ
ወልዶ ባለው ይረታል ።

፵፭ ወሰሚዖሙ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን
ምሳሌያቲሁ እንከሩ ወአእመሩ ከመ በእንቲአሆሙ
ይብል ።

፵፭ ፈሪሳውያን ሊቃነ ካህናት ምሳሌውን ሰም
ተው አደነቁ በሳቸው እንደመሰለባቸው ዐወቁ

፵፮ ወፈቀዱ የእኀዝዎ ።

፵፮ ሊይዙት ወደዱ ።
ወፈርሁ ሕዝበ ።
ነገር ግን ሕዝቡን ፈሩ ።
እስመ ከመ ነቢይ ይሬእይዎ ሕዝቡ ጌታን እንዳባት
ያከብሩታል እንደ መምህር ያፍሩታልና ።

በእንተ ምሳሌ ንጉሥ ዘገብረ ከብካበ ለወልዱ ።

## ምዕራፍ ፳፪ ።

፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ዳግመ ወነገረ
በምሳሌ ።

፩ ጌታ ሁለተኛ በምሳሌ ነገራቸው

፪ እንዘ ይብል ትመስል መንግሥተ ሰማያት
ብእሴ ንጉሠ ዘገብረ ከብካበ ለወልዱ ሉቃ ፲፬፡ ፪
፲፮ ፤ ራዕ ፤ ፲፱ ፤ ፱ ።

፪ መንግሥተ ሰማያት ሕገ ወንጌል ሕገ ወን
ጌል ተስፋ ተሰፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ለልጁ ሰርግ
ያዘጋጀ ንጉሥን ትመስላለች ።

፫ ወፈነወ አግብርቲሁ ይጸውዕዎሙ ለእለ
ተዓሥሩ ውስተ ከብካብ ።

፫ የታደሙትን ወደ ሰርግ ጥሯቸው ብሎ ብላ
ቴኖቹን የላከን ወዓበዩ መጺአ ፤ አንመጣም
ያሉትን ።

፬ ወዳግመ ፈነወ ካልዓነ አግብርተ ።

፬ ሁለተኛ ሌሎችን ላከ ።
እንዘ ይብል በልዎሙ ለእለ ዓሠርናሆሙ ።
ያደምናቸውን እንዲህ በሏቸው ብሎ ።
ናሁ ምሳሀየ አስተዳሎኩ እነሆ ሰርግ አዘጋጅቻለሁ
ወጠባሕኩ መጋዝዕትየ ወአስዋርየ ።
ሜል ገች አርጃለሁ ።
ወኵሉ ድልው ።
ሁሉ ተዘጋጅቷል ።
ንዑ ውስተ ከብካብየ ።
ወደ ሰርግ ኑ ብሎ ላከ ።

፭ ወእሙንቱሰ ተሐየዩ ወኃለፉ

፭ እሳቸው ግን ቸል ብለው ሄዱ
ቦ ዘሖረ ውስተ ገራኅቱ ፤
ወደ እርሻው የሄደ አለ ።
ወቦ ዘሖረ ውስተ ንግዱ ።
ወደ ንግዱ የሄደ አለ ።
ወቦ ዘሖረ ውስተ ዓጸደ ወይኑ
ወደ ወይን ጥበቃው የሄደ አለ

፮ ወእለ ተርፉ እኀዙ አግብርቲሁ ወቀተልዎሙ

፮ የቀሩት ግን ብላቴኖቹን ይዘው ገደሏቸው ።
ወኪያሁኒ እግዚእሙ ጸአሉ ። እሱንም ነቀፉት ።

፯ ወተምዓ ንጉሥ ወፈነወ ሐራሁ ይቅትል
ዎሙ ለእልክቱ ቀተልት ።

፯ ንጉሥ ተቆጥቶ ግደሏቸው ብሎ ጭፍራ ላከ
ወቀተልዎሙ ።
ገደሏቸው ።
ወሀገሮሙኒ አውዓዩ በእሳት ።
ሀገራቸውን አቃጠሉ ።

፰ ወእምዝ ይቤሎሙ ለአግብርቲሁ ከብካብ
የሰ ድልው ውእቱ ።

፰ ከዚህ በኋላ ለብላቴኖቹ ሰርጉስ ተዘጋ
ጅቷል ።
ወባሕቱ ኢደለዎሙ ለእለ ዓሠርናሆሙ ።
ነገር ግን ላደምናቸው አላደላቸውም አላቸው ።

፱ ሑሩኬ እንከ ውስተ መራህብት ወአናቅጽ
ወኵሎ ዘረከብክሙ ጸውዑ ሊተ ውስተ ከብካብ

፱ እኒያ አይሆንም ካሉ ወደ ዐደባባይ ወጥታችሁ ከፉውንም በጎውንም ጠርታችሁ ይዛችሁ ኑ አላቸው ።

፲ ወወፂአሙ አሙንቱ አግብርት ውስተ ፍናው አስተጋብኡ ኵሎ ዘረከቡ እኩያነ ወኄራነ

፲ ወደ ዐደባባይ ወጥተው ከፉውንም በጐውንም ያገኙትን ጠርተው ይዘው መጡ ።
ወመልአ ቤተ በዓል እምአለ ይረፍቁ ።
ከተቀመጡት የተነሣ የሰርግ ቤት መላ ።

፲፩ ወበዊአ ንጉሥ ይርአዮሙ ለእለ ይረፍቁ ረከበ በህየ ዘኢለብሰ ልብሰ መርዓ ።

፲፩ ንጉሥ ከሰርግ ቤት ገብተው የተቀመጡትን ሊያያቸው በገባ ጊዜ የሰርግ ልብስ ያለ በሰ አንድ ሰው አገኘ ።

፲፪ ወይቤሎ አርከየ ለምንት ቦእከ ዝየ ዘኢለበስከ ልብሰ መርዓ ።

፲፪ ወዳጄ የሰርግ ልብስ ያለበስህ ከሰርግ ቤት ለምን ገባህ አለው ።
ወተፈጸመ ውእቱ ብእሲ ።
ያሰው ምላሽ አጣ ። ሐተታ ፣ ባጣ ቢቸግረኝ አይ ለውም ቢሉ ያነኑ ከውኃ ባደረስከው ይለዋልና ።

፲፫ ወእምዝ አዘዞሙ ንጉሥ ለአግብርቲሁ ይእ ስርዎ እደዊሁ ወእገሪሁ ወያውፅእዎ ውስተ ጸናፌ ጽልመት ። ማቴ ፰ ፲፪ ፲ ፫ ፴፪ ፳፭ ፴ ።

፲፫ ከዚህ በኋላ እጁን እግሩን አስራችሁ ወደ ጽኑ ጨለማ አውጡት ።
ኀበ ሀሎ ብካይ ወሐቅየ ስነን ።
ልቅሶ ጥርስ ቁርጥማት ወዳለበት ቦታ ብሎ ብላ ቴኖቹን አዘዛቸው ።
፲፬ እስመ ብዙኃን እሙንቱ ጸውዓን ።
፲፬ የተጠሩ የቀሩ ብዙ ናቸውና
ለምንት ቦእከ ዝየ ።
ወኅዳጣን ኅሩያን የተጠሩ የተመረጡ ጥቂት ናቸውና ፣ እሰሩ እደዊሁ ወእገሪሁ በል ። አንድም ትመስል መንግሥተ ሰማያት ብለህ መልስ መን ግሥተ ሰማይ አብ ለልጁ ሥጋዌን ያደረገ ንጉሥን ይመስላል ማለት እሱ ነው ። ወፈነወ አግብርቲሁ ፣ ትንቢት የተነገረላቸውን በአሪት ፣ ተስፋ መስቀል የተነገረላቸውን በወንጌል ያሰምኑ ዘንድ አስተምሩ ብሎ ዓበይተ ነቢያትን ሐዋርያትን ላከ ። ወአበዩ ፣ እናምንም አሉ ። ወዳግመ ፈነወ ካልዓነ አግብርተ ፣ ለዓበይተ ነቢያት ካልዓን የሚሆኑ ደቂቀ ነቢያትን ለሐዋርያት ካልዓን የሚሆኑ ፸ አርድእትን ፣ ትን ቢት የተነገረላቸውን በአሪት ተስፋ መስቀል የተነ ገረላቸውን በወንጌል አሳምኑ ብሎ ላከ ። ናሁ ምሳ ህየ አስተዳሎኩ ኦሪትን ወንጌልን ሠርቻለሁ ፣ ወዘሎ ድልው ፣ በኦሪት በወንጌል ጥቃቅኑ ደጋጉ ታምራት ይደረጋል ። ንዑ ውስተ ከብካብየ ፣ በኦ ሪት በወንጌል እመኑ ብላችሁ አስተምሩ ብሎ ላካ ቸው ወእሙንቱሰ ተሐየዩ ፣ አላቸው ግን ቸል ብለው ሄደው ቦ ዘሐረ ውስተ ገራኅቱ ፣ እርሻችሁን ተው የምትል ሕግ አንሻም ብሎ ወደ እርሻው የሄደ አለ። ቦ ዘሐረ ውስተ ተግባሩ ፣ ንግዳችሁን ተው የም ትል ሕግ አንሻም ብሎ ወደ ንግዱ የሔደ አለ ወቦ ዘሐረ ወ ስተ ዐጸደ ወይኑ ወይናችሁን ተው የምትል ሕግ አንሻም ብሎ ወደ ወይኑ ጥበቃው የሄደ አለ የቀሩት ግን ዓበይተ ነቢያትን ደቂቀ ነቢያትን ሐዋርያትን ፸ አርድእትን ይዘው ገደ ሏቸው ወኪያሁኒ ጸዓሉ ፣ እሱንም እሩቅ ብእሲ አሉት ። ወተምዓ ንጉሥ ፣ ጌታ ፈርዶ ነቢያትን በገደሉ ነገሥተ ፋርስን ሐዋርያትን ፸ አርድእትን በገደሉ ነገሥተ ሮምን አስነሥቶ አጠፋቸው ወሀገሮሙኒ አውዐዩ ፣ ሀገራቸውንም በእሳት አቃጠለ።

ወእምዝ ይቤሎሙ ከብካብየስ ፣ ድልው ሕንስ ተሠርቷል ወባሕቱ ኢደለዎሙ ለእለ ዓሠርናሆሙ ትንቢት ተስፋ መስቀል ላናገርንላቸው አልሆንላቸ ውም እንጅ ፣ ሑሩኬ ውስተ መራህብት ፣ በአራቱ መዓዝን ዙራችሁ አስተምራችሁ ያገኛችሁትን በኦ ሪት በወንጌል አሳምኑ ። ወወፂአሙ ውስተ ፍናው ባራቱ መዓዝን ዙረው አስተምረው በኦሪት በወ ንጌል አሳመኑ ። እኩያነ ወኄራነ ፣ እኩያን አምነው ተጠምቀው ሥራ ያልሠሩ ናቸው ኄራን አምነው ተጠምቀው ሥራ የሠሩ ናቸው ። ወመልአ ቤተ በዓል እምአለ ይረፍቁ ፣ ከምእመናን ብዛት የተነሣ መን ግሥተ ሰማያት መላች ። መምላትስ የለም ብዛታ ቸውን መናገር ነው እንጅ ወበዊአ ንጉሥ ያመኑ ትን የተጠመቁትን በተመራመራቸው ጊዜ ረከበ ብእሲ ዘኢለብሰ ልብሰ መርዓ ፣ አምኖ ተጠምቆ የክርስቲያን ሥራ ያልሠራ ሰው አገኘ ። ወይቤሎ አርከየ ለምንት ቦእከ ዘኢለበስከ ልብሰ መርዓ መፍቀሬ ሰብእ ነውና አርከየ ይለዋል ወዳጄ የክ ርስቲያን ሥራ ላትሠራ ሰምን አመንከ ተጠመ ቅሁ አልህ አሰው ።

ወተፈጸመ ምላሽ አጣ ባሕርየ ደካማ ቢሆን ባይቻለኝ አይለውም ቢሉ ያኑ ከመምህረ ንስሐህ ባደረስኸው ይለዋልና ፣ ወእምዝ አዘዞሙ ንጉሥ ለአግብርቲሁ ። ከዚህ በኋላ መላእክትን ከመንግ ሥተ ሰማይ በአፍአ ጽኑ ፍዳ ወዳለበት ወደ ገሃ ነም አውጡት አላቸው ። እስመ ብዙኃን ጸውዓን፣ እንዳለፈው በል ።

፲፭ ወእምዝ ሖሩ ፈሪሳውያን ወተማከሩ ከመ ያስሕትዎ በቃሉ ማር ፲፪ ፲፫ ። ሉቃ ፳ ፳ ።

፲፭ ከዚህ በኋላ ፈሪሳውያን ሄደው በነገር ሊያስቱት መከሩ ።

በእንተ ዘከመ ይደሉ ውሂበ ጸባሕት ለቄሣር።

፲፮ ወፈነዉ ኀቤሁ አርዳኢሆሙ ምስለ ሰብአ ሄሮድስ ።

፲፮ ብላቴኖቻቸውን ከሄሮድስ ብላቴኖች ጋራ ላኩ በሀገር የሊቀ መጣኔ ወምበር እንዲኖር ያገር ምዝክር ሹማምት አሉና ፤ እንድም ብላቴኖቻቸውን የሄሮድስ ብላቴኖች ነን በሉ ብለው ላኩ ።
ወይቤልዎ ሊቅ ነአምር ከመ ራትዕ አንተ ።
መምህር ዐዋቂ ቅን እንደሆንህ እናውቃለን ።
ወበጽድቅ ትሜህር ፍኖተ እግዚአብሔር ።
በውነት ወንጌልን እንድታስተምር ።
ወኢተሐስብ መነሂ ።
ማንንም ማንን እንዳትፈራ ፡ ወኢየኃዝነከ መኑሂ ይላል ማንም ማን እንዳያሳፍርህ ።
ወኢታደሉ ለገጸ ሰብእ ።
ፊት አይተህ እንዳታደላ እናውቃለን ።

፲፯ ንግረነኬ ዘይረትዕ ።

፲፯ የሚገባውን ንገረን ።
ይከውነነሁ ነሀበ ጸባሕተ ለንጉሥ ፡
ለቄሣር ግብር መስጠት ይገባናል ።
አው አልቦ ።
ወይም አይገባንም አሉት ፡ ሐተታ ፡ ይገባል ቢላቸው የእግዚአብሔር ወገን ነኝ ይላል ለእግዚአብሔር የሚገባውን ለቄሣር ስጡ አለን ለማለት ፡ አይገባም ቢላቸው ከቄሣር ለማጣላት ነው ።
፲፰ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ እከዮሙ
፲፰ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ተንኰላቸውን ዐውቆባቸው ፡ ሚናሙ ይላል አብነት እከዮሙ ማለት ነው ።
ወይቤሎሙ ምንተ ታሜክሩኒ አ መደልዋን ።
እናንት ግብዞች ለምን ትፈትኑኛላችሁ ።
፲፱ አርእዩኒ አላደ ዲናሩ ።
፲፱ ቅርጹን አሳዩኝ አላቸው ።
ወአምጽኡ ሎቱ ዲናረ ።
፳ አመጡለት ።
፳ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ዘመኑ ዝንቱ መልክኡ ወመጽሐፉ ።
ቅርጹ መጽሐፉ የማነው አላቸው ።
፳፩ ወይቤልዎ ዘቄሣር ።
የቄሣር ነው አሉት ። ሮሜ ፲፫ ፡ ፯ ።
፳፩ ወይቤሎሙ ዘቄሣር ሀቡ ለቄሣር ።
የቄሣርን ለቄሣር ስጡ ።
ወዘእግዚአብሔር ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር ስጡ አላቸው ምልአተ ንባብ ነው ። እንድም የንጉሥ የሆነ እንደሆነ ስመ ንጉሥ ይጸፍበታል ሥዕለ አንበሳ ይቀርጹበታልና የቄሣርን ለቄሣር ስጡ አለ የእግዚአብሔር የሆነ እንደሆነ ስመ አምላክ ይጸ ፍበታል ሥዕለ ኪሩብ ይቀረጽበታልና የእግዚአብ ሔርን ለእግዚአብሔር ስጡ አለ እንድም በተን ኮል መጥተዋል መጠን አራት አድ ይላታል ብር የምታህል ናት ባንድ ወገን ስመ ንጉሥ ጽፈው ሥዕለ አንበሳ ቀርጸው ባንድ ወገን ስመ እግዚአብ ሔር ጽፈው ሥዕለ ኪሩብ ቀርጸው ይዘው መጡ ፤ ዘቄሣር ያለን እንደሆነ ዘእግዚአብሔር ይላልሳ፥ ዘእግዚአብሔር ያለን እንደሆነ ዘቄሣር ይላልሳ ብለን ምላሽ እናሳጣዋለን ብለው ነው ። እሱም በመ ጡበት ይጨነቁበት ብሎ የግራ የቀኙን እንድ ጊዜ ተናገረው ፤ እንዳይለዩት የማይለይ ነው ከእ ሳትም ቢያገቡት ሁሉም ይጠፋል ። እንድም አር አያ ቄሣር ሰውነታችሁን ለቄሣር አስገዙ አርአያ እግዚአብሔር ሰውነታችሁን ለእግዚአብሔር አስ ገዙ እንድም አፍአዊ ሰውነታችሁን ለቄሣር አስ ገዙ ውሳጣዊ ሰውነታችሁን ለእግዚአብሔር አስገዙ.
፳፪ ወሰሚዖሙ አንከሩ ወኃደግዎ ወኃለፉ።

፳፪ ምላሹን ሰምተው አድንቀው ትተውት ሄዱ ።

በእንተ ሰዱቃውያን ወትንሣኤ ምውታን።

፳፫ ወበይእቲ ዕለት መጽኡ ኀቤሁ ሰዱቃ ውያን እለ ይብሉ አልቦ ትንሣኤ ሙታን ግብ ፳፫ ፡ ፰ ።

፳፫ በዚያች ቀን ትንሣኤ ሙታን የለም የሚሉ ሰዱቃውያን መጡ ።

፳፬ ወተስእልዎ እንዘ ይብሉ ።
ዘዳግም ፡ ፳፭ ፡ ፭ ። ማር ፡ ፲፪ ፡ ፲፱ ፡ ሉቃስ ፡ ፳፡፳፰

፳፬ እንዲህ ብለው ጠየቁት ።
አ ሊቅ ሙሴ ጸሐፈ ለነ ለእመ ሞተ እኁሁ እንዘ አልቦ ውሉድ ያውስብ ብእሲተ እኁሁ ወያቅም ዘርዓ ለእኁሁ ።
መምር ሆይ ወንድሙ ልጅ ሳይወልድ ቢሞት ታናሽ ወንድሙ አግብቶ ስሙን የሚያስጠራ ልጅ ይው ለድለት ብሎ ሙሴ ጽፎልናል ።
፳፭ ወሀለዉ ኀቤነ ፯ቱ አኀው ።
፳፭ ሰባት ወንድማማች ከኛ ዘንድ ነበሩ ።
ወዘይልሕቅ አውሰበ ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።
ታላቁ ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ሞተ ።
ወኃደገ ብእሲቶ ለእኁሁ ። ሚስቱን ለወንድሙ ተወለት ። ሐተታ ፤ የምትገባው ስለ ሆነ እንዲህ አለ ።
፳፮ ወከማሁ ካዕበ ካልዑኒ ወሣልሱኒ እስከ ፯ቲሆሙ አውሰብዋ ።
፳፮ እንደዚሁም ሁሉ አንዱ እየሞተ አንዱ እየተተካ ሰባቱ ሁሉ አገቧት ።
ወኢኃደጉ ውሉደ ።
ሁሉም ልጅ ሳይወልዱ ሞቱ ።

፳፯ ወድኅረ ኵሎሙ ሞተት ይእቲ ብእሲት፣
፳፯ ከእሳቸው በኋላ እሱዋም ሞተች ።
፳፰ ወአመ ይትነሣኡ እንከ ምውታን ለመኑ እምኔቲሆሙ ትከውን ብእሲተ ፣

፳፰ ሙታን በሚነሡበት ጊዜ ከሰባቱ ለማን ትሆናለች ።
እስመ ኵሎሙ አውሰብዋ መላው አግብተዋታልና

ሐተታ ፣ ሰዱቃውያን ትንሣኤ ሙታን የለም ይላሉ ፤ ፈሪሳውያን ግን ትንሣኤ ሙታን አለ እንድ ገና ከሚስቶቻችን ከልጆቻችን ጋራ እንኖራለን ይላሉ ፣ ትንሣኤ ሙታን ካለ ለማናቸው ትገባለች ይሏቸዋል ለመላው ያሏቸው እንደሆን ዓለመ ዝሙት ናታ ይሏቸዋል ላንዱ ያሏቸው እንደሆን ዓለመ ማፍዕ ናታ በወዴሁ ሥራት ይሠራባቸው በወዲያው ይከለከልባቸው እያሉ ምላሽ ያሳጧቸዋል እንደነዚያ መስሏቸው ጌታን ይጠይቁታል እሱም ይመልስ ላቸዋል ። እንድም ብእሲት ይህቺ ዓለም ሰባት እሰከምጽአት የሚነሡት ነገሥታት ናቸው ፣ በፍ ጹም ተናገራቸው ። እስመ ኵልኰ ሰብእ በኀበ እብ ራያውን ፍጹም ውእቱ እንዲል ።

፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፳፱ ጌታ መለሰ ።
ወይቤሎሙ ስሕትክሙ በኢያእምሮ መጻሕፍት ።
የሥነ ፍጥረትን ነገር የሚናገር መጽሐፍን ባለማወቅ
ወኢኃይለ እግዚአብሔር ።
እምጻኤ ዓለማትነቱን ባለማወቅ በደላችሁ ።

ሐተታ፣ እያሥነሣም ይሉታል እንጂ አልፈጠ ረም ይሉታል ቢሉ ጥንቱን አካል ያለውን አካል ሰጥቶ እያስነሣም ካሉት ይህን ዓለም እምኀበ አልቦ አምጥቶ አልፈጠረም ያሰኝባቸዋልና ፤ እንድም ስሕትክሙ ብለህ መልስ የትንሣኤ ሙታንን ነገር የሚናገሩ መጻሕፍትን ባለማወቅ ፣ ወኢኃይለ እግ ዚአብሔር የጌታችንን ትንሣኤ ባለማወቅ በደላችሁ ሐተታ ፣ ሙታን አይነሡም ብለዋል እንጂ ጌታን አልተነሣም ብለዋልን ቢሉ ሙታን አይነሡም ካሉ ጌታ አልተነሣም ማለት ነውና ።

፴ አመሰ የሐይው ምውታን ኢያወስቡ ወኢ ይትዋሰቡ ።
፴ ሙታን በሚነሡበት ጊዜ አያገቡም አይ ጋቡም ። አላ ከመ መላእክተ እግዚአብሔር ይከውኑ እሙንቱ በሰማያት እንደ መላእክት አንድ ወገን ሆነው በመንግሥተ ሰማይ ይኖራሉ እንጂ ፣

፴፩ ወበእንተ ትንሣኤ ሙታንሰ ኢያንበብ ክሙኑ ዘተብህለ ለክሙ እምኀበ እግዚአብሔር ዘይቤ

፴፪ አነ እግዚአብሔር አምላከ አብርሃም ወአ ምላከ ይስሐቅ ወአምላከ ያዕቆብ ።

፴፪ ትንሣኤ ሙታንማ እንዳለ ለማጠየቅ የአ ብርሃም የይስሐቅ የያዕቆብ አምላክ እኔ ነኝ ብሎ

፴፪ እግዚአብሔር ለሙሴ የነገረውን አልተመ ለከታችሁምን አላወቃችሁምን ፣ ወእግዚአ ብሔርሰ ኢኮነ አምላከ ምውታን አላ አምላከ ሕያዋን እግዚአብሔር ግን የሕያዋን አምላክ ነው እንጂ ነበሩኝ ሞቱብኝ ለማለት የአብርሃም የይስሐቅ የያ ዕቆብ አምላክ ነኝ አላለም ። በነፍስ ሕያዋን ናቸ ውና ። ይቀድሱታልና እንዲያስነሣቸው ያውቃልና እንዲህ አለ ። ሐተታ ይህች ዓለም ዛሬ በሰባቱ ዕለታት ትመገባለች ኋላ እንደምን ናት ቢሉት ኋላስ መዓልትና ሌሊት ክረምትና በጋ ብርሃንና ጨለማ የለም እንደ መላእክት አንድ ወገን ሁነው ይኖራሉ ብሏቸዋል ። ዛሬ ሥጋና ነፍስ ይሳሳባሉ ኋላ እንደምን ይሆናሉ አሉት ኋላስ መሳሳብ የለም ዓለሙም ዓለመ ነፍስ ነው ሥጋም ነፍስን መስላ እንደ መላእክት ሁነው ይኖራሉ አላቸው ። ዛሬ ሥጋዊውን ከንጉሥ እስከ ኳደሬ እስከ አቅራሪ መንፈሳዊውን ከሊቀ ጳጳስ እስከ ዓፃዌ ኆኅት ባለው አድር ይመግባል ። ኋላ እንደምነው ቢሉት ። ኋላስ ገዢና ተገዢ የለም፤ወአስኩብዎ ለውእቱ ሰይፍ ውስተ መካኑ እንዲል ። ገዢው አንድ እሱ ነው ። እንደ መላእክት አንድ ወገን ሁነው ይኖራሉ አላቸው ።
፴፫ ወሰሚዖሙ ሕዝብ እንከሩ ምሕሮቶ ።
፴፫ ሕዝቡ ሰምተው ትምህርቱን አደነቁ ።

### በእንተ ዓቢይ ትእዛዝ እግዚአብሔር

፴፬ ወሰሚዖሙ ፈሪሳውያን ከመ ፈጸሞሙ አፉ ሆሙ ለሰዱቃውያን ተጋብኡ ኅቤሁ ኵሎሙ ኅቡረ
፴፬ ሰዱቃውያንን ምላሽ እንዳሳጣቸው ፈሪሳው ያን ሰምተው ደስ ብሏቸው ባንድነት ወደሱ ተሰበ ሰቡ ። ሐተታ ቢስ የቢስ ቀን ከፉ የከፉ ቀን ብለው።

፴፭ ወተስእሎ ፩ ጸሐፊ እምኔሆሙ ።
፴፭ ከሳቸው ወገን አንድ ጸሐፊ ማለት ዐዋቂ ነኝ የሚል ጠየቀው ። እንዘ ያሜክሮ ሲፈትነው

፴፮ ኦሊቅ ዓይኑ ትእዛዝ ዓባይ በውስተ ኦሪት
፴፮ መምህር ደገኛው ትእዛዝ ማናቸው ነው ። አንድም በኦሪት ማናቸው ትእዛዝ ይበልጣል አለው
፴፯ ወይቤሎ አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አም ላክከ በኵሉ ልብከ ፣

፴፯ እግዚአብሔርን በፍጹም ልቡናህ ውደ ደው ያለው ነው ።
ወበኵሉ ነፍስከ ።
በፍጹም ሰውነትህ ።
ወበኵሉ ኃይልከ ።
በፍጹም ዕውቀትህ
ወበኵሉ ሕሊናከ ።
በፍጹም ሕሊናህ ።

፴፰ ዛቲ ትእዛዝ ዓባይ ወቀዳሚት

፴፰ ደገኛዪቱ መጀመሪያይቱ ትእዛዝ ይህች ናት ። እንድም ቀዳሚሆሙ ለአሕዛብ አግሌቅ እን ዲል ፤ ፈጽሞ ደገኛይቱ ትእዛዝ ይህች ናት ።

፴፱ ወካልዕታኒ እንተ ትመስላ አፍቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ።

፴፱ ሁለተኛይቱም አፍቅር በማለት ዋጋ በማ ሰጠት የምትመስላት ፍቅረ ቢጽ ናት ።

፵ ወበእላ ክልኤቲ ትእዛዝ ተሰቅሉ አሪት ወነቢያት
፵ በነዚህ በሁለቱ በፍቅረ ቢጽና በፍቅረ እግ ዚአብሔር አሪት ነቢያት ተጠብቀው ይኖራሉ ።
ሐተታ ፤ ሁለቱ እንደ ሁለቱ ፍንጅ በምንቱ እንደ ሰምንቱ ጠንግ ሁነው ።

በእንተ ሠሙሙ ወልደ ዳዊት ።
ማቴ ፳፪ ፵፩
፵፩ ወእንዘ ጉቡአን ፈሪሳውያን ተስእሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ።
፵፩ ፈሪሳውያን ባንድነት ተሰብስበው ሳሉ ጌታ ጠየቃቸው
፵፪ እንዘ ይብል ምንተ ትብሉ በእንተ ክርስቶስ
፵፪ የክርስቶስን ነገር ምን ትናገራላችሁ ብሎ ወልደ መኑ ውእቱ ።
የማን ልጅ ነው ።
፵፫ ወይቤልዎ ወልደ ዳዊት ።
፵፫ የዳዊት ልጅ ነው አሉት ።
፵፬ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ በእፎ እንከ ለሊሁ ዳዊት በመንፈስ ቅዱስ ይቤ ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ ።
፵፬ ልጅማ ከሆነ ዳዊት በመንፈስ ቅዱስ እግ ዚአየ አብ እግዚእየ ወልድን በቀኝ ማለት በዕሪናዊ ኑሮ እለው እንዴምን ቻለ ። እስከ እገብሮሙ ለጸላ እትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ።
ጠላቶችህን በእጅህ ጭብጥ በእግርህ እርግጥ አድ ርጌ እስካስገዛልህ ድረስ ጸላዕት አይሁድ አጋንንት መናፍቃን ናቸው ። መከየደ እግር ያለው ሕዋርያት ሥልጣኑ መለኮት መሸቀል ሂድኤቱ ነው ።
፵፭ ዘለሊሁ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ እፎ እንከ ይከውኖ ወልዶ ።
፵፭ ዳዊት ጌታዬ ያለው እንዴምን ልጁ ይሆ ነዋል ። ይህንም ሊቁ በዝቋ አክህዶ ልደተ ሥጋሁ ዘእምዘርዓ ዳዊት ብሎታል ። የአምላክነቱን ነገር ሲናገር ነው እንጂ በሥጋ ከዳዊት መወለዱን አሉ ብሎት አይደለም ብሏል ።
፵፮ ወአልቦ ዘክህለ አውሥኦት ቃለ ወአልቦ ዘተሀበለ ተሰእሎቶ ምንተኒ እምይእቲ ዕለት ።
፵፮ ከዚያች ቀን ጀምሮ ከዚያች ቀን ወዲህ ማንም ማን ሊጠይቀው ሊመልስለት የወደደ የደ ፈረ የለም ።

በእንተ መደልዋን ፈሪሳውያን ።

ምዕራፍ ፤ ፳፫ ።

፩ ወእምዝ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለሕ ዝብ ወለአርዳኢሁ ።
፩ ከዚህ በኋላ ጌታ ለሕዝቡ ነገራቸው ።
፪ እንዘ ይብል ዲበ መንበረ ሙሴ ነበሩ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ። እዝራ ፰ ፤ ፬ ።
፪ ጸሐፍት ፈሪሳውያን በሙሴ ወንበር ማለት በሙሴ መምህርነት አሉላችሁ ።
፫ ኵሎ ዘይቤሉክሙ ግበሩ ።
፫ ያዘዟችሁን ፤ ሁሉ ሥሩ ።
ወዘመሐሩክሙ ዕቀቡ ።
ያስተማሯችሁንም ጠብቁ ።
ወዘከመ ምግባሮሙሰ ኢትግበሩ ።
እንደ ሥራቸው ግን አትሥሩ
እስመ እሙንቱ ይሜህሩ ለባዕድ ።
ለሌላ ያስተምራሉና ግበሩ ዕቀቡ ።
ወኢይገብሩ ።
እሳቸው አይሠሩትምና ኢትግበሩ ፤ እንድም ንግሩ እንጂ ግበሩ የለምና ኢትግበሩ ብል
፬ ወየአስሩ ጾረ ዓቢየ ወክቡደ ወያሰክምዎ ለሰብእ ዲበ መትከፍቱ ። ሉቃ ፤ ፲፩ ፤ ፵፮፤ ግብ ፲፭ ፲
፬ ጽኑ ሸክም አስረው ሰውን ተሸከም ይሉታል ወለሊሆሙሰ ኢይለክፍዎ በአፅባዕቶሙ ጥቀ ። እሳቸው ግን ስንኳ ሊሸከሙት በጣታቸው አይዳ ስሱትም ። እንድም ወየአስሩ ፤ ጽኑ ሥርዓት ሠር ተው ሰውን ጠብቅ ይሉታል ። ወለሊሆሙሰ እሳ ቸው ግን ስንኳን ሊሠሩት እንሠራዋለን ብለው አያ ስቡም ።
፭ ወኵሎ ምግባሮሙ ይገብሩ ለዓይነ ሰብእ ይግበሩ ። ዘኍል ፤ ፲፭ ፤ ፴፰ ። ዘዳ ፤ ፳፪ ፤ ፲፪ ። ማር ፲፪ ፤ ፴፱ ። ሉቃ ፤ ፲፩ ፤ ፵፫ ፤ ፵፮ ።
፭ የሚሠሩት ሁሉ ለሰው ይምሰል ነው ። ወይሰፍሑ ክርበታቲሆሙ ።
እንደጎልጎታ ያለ አላቸው ያን ባደባባይ ዘርግተው ይታያሉ ወየዓብዩ አዝፋረ አልባሲሆሙ የልብሳቸ ውን ዘርፍ አስፍተው ያስጥሉታል ፤ ሐተታ ፤ ጌታ ሙሴን በልብሳችሁ ሰማያዊ ሐር አስጥሉ ብሎታል ለጊዜው ሰማይ የሚመስል ባሕር ከፍሎ አሻገር ኋችሁ ሲል ነው ፍጻሜው ግን ሰማያዊ ሕግን ጠብቁ ሲል ነው ፤ ከሕዝቡ ይልቅ እኛ እንጠብቃ ለን ለማለት እሳቸው እያሰፉ የሚያስጥሉ ሁነ ዋል ፤ እንድም አልፈው አልፈው ያስጥሉባታል እንደ ሉሲ ፣ ጠብር እንደቀሽ መሪ መታጠቂያ እንደ መረሻት ፤ እንድም ፲ቱ ቃላትን በልብሳቸው ይጽፉ ነበር ከሰውነታችን የተረፈው በልብሳችን

አለ ለማለት ቱስ ዐ፮ ምህርካ ድንግል ኢየሱስ ናዝ
ራዊ ብለው በልብሳቸው ጽፈው እንደነበረ ፥

፮ ወያፈቅሩ ርእሰ ምርፋቃት በውስተ ምሳሐት
፮ በምሳም ጊዜ በላይ መቀመጥን ይወዳሉ
ምንጣፍ መጨጊያ ካለበት ወጥ ከተደፋረበበት
እንጀራ ከበዛበት ጽዋ ከሚጀመርበት ይህ ለጊዜው
ጥቅም ያለበት ነው ፥
ወንቢረ ፍጽም በውስተ አዕዋዳት ።
ባደባባይ ፊት ለፊት መቀመጥን ይወዳሉና

፯ ወተአምኆ በውስተ ምሥያጣት
፯ ባደባባይ እጅ ሊነሷቸው ሊያከብሯቸው
ይወዳሉ ፥
ወይበልዎሙ ስብእ መምህራን ፥
መምህራን ይሏቸው ዘንድ

፰ አንትሙሰኬ ኢትሰምዩ መምህረ በዲበ
ምድር ፥ ያዕ ፥ ፫ ፥ ፩ ።

፰ እናንተስ ምድራዊ መምህር አይኑራችሁ ፥
እስመ ፩ዱ ውእቱ መምህርክሙ ፥
መምህራችሁ አንድ ሰማያዊ ክርስቶስ ነውና ፥
ሐተታ ፥ ዲበ መንበረ ሙሴ ነበሩ ያለውን ማፍረሱ
ነው ቢሉ ያንም እንጂ ወዘከመ ምግባርሙሰ ኢት
ግበሩ ባለው አፍርሶታል እንድም ለጣዖት ስገዱ
ሃይማኖታችሁን ካዱ የሚል መምር አይኑራችሁ
ሲል ነው

፱ ወኢትረስዩ ለክሙ አበ በዲበ ምድር ።
ሚልክ ፩ ፥ ፮ ።

፱ ምድራዊ አባት አይኑራችሁ ፥ እስመ
ውእቱ አቡክሙ ሰማያዊ ።
አባታችሁ አንዱ ሰማያዊ ክርስቶስ ነውና ፥ ሐተታ
አክብር አባከ ወእመከ ይል የለም ቢሉ ከአክብ
ሮተ አብ ወእምአክብሮተ እግዚአብሔር እንዲ
በልጥ ለማጠየቅ ፥ እንድም ለጣዖት ስገዱ የሚል
አባት አይኑራችሁ ሲል ነው ፥ ዘኢኃደገ አባሁ ወእሞ
ኢይከል ይፀመደኒ እንዲል ፥
አንትሙሰ አኃው ኵልክሙ እናንተስ ወንድማማች
ናችሁ ።

፲ ወኢትሰምዩ እግዚእ በዲበ ምድር ።
፲ ምድራዊ ጌታ አይኑራችሁ ፥ ሐተታ ዘቄሣር
ሀቡ ለቄሣር ብሎ የለም ቢሉ ፥ ያንም እንጂ ወዘ
እግዚአብሔር ለእግዚአብሔር ባለው አፍርሶታል
እንድም ለጣዖት ስገዱ ሃይማኖታችሁን ካዱ የሚል
ጌታ አይኑራችሁ ሲል ነው ፥
እስመ ፩ዱ ውእቱ እግዚእክሙ ክርስቶስ ፥
ሰማያዊ ጌታችሁ አንድ ክርስቶስ ነውና ።

፲፩ ወባሕቱ ዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን
ዓቢየ ይኩንክሙ ገብረ ።

፲፩ ከናንተ ወገን በላይ ሊሆን የወደደ አገል
ጋይ ይሁናችሁ ወዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ
ይኩንክሙ ላዕከ ።
ገዢ ሊሆን የወደደ ተገዢ ይሁናችሁ ።

፲፪ እስመ ዘአዕበየ ርእሶ የኃሥር ሉቃ፥ ፲፬፥ ፲፩
፲፪ ራሱን ያከበረ ይዋረዳልና ።
ወዘአትሐተ ርእሶ ይከብር
ራሱን ያዋረደ ይከብራልና ።

፲፫ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ።
፲፫ ጸሐፍት ፈሪሳውያን እናንተ ግብዞች ወዮ
ላችሁ።
እለ ትበልዑ አብያተ መበለታት በምክንያተ አንኖ
ጸሎትክሙ ። አብዝተን እንጸልያለን በማለት ምክ
ንያት የድሆችን ገንዘብ የምትበሉባቸው ። ማዕ
ዜመ አገብር ቤተ ለርእስየ ያጠርያ ቤተ እምጽድቀ
ዘአሆን እንዲል ፥ አብዝተው ሲጸልዩ ያዩዋቸው
እንደሆነ የባሎቻችንን ነፍስ ያስምሩልናል ልጆ
ቻችንን ያሳድጉልናል እያሉ ይሰጧቸዋልና ።
ወበእንተ ዝንቱ ትረክቡ ኵነኔ ፈድፋደ ።
ስለዚህ ጽኑ ፍዳ ትቀበላላችሁ

፲፬ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደ
ልዋን ።

፲፬ እናንት ግብዞች ወዮላችሁ
እስመ ተዓፅው መንግሥተ ሰማያት ቅድመ ገጹ
ለሰብእ በሰው ፊት መንግሥተ ሰማይን ትዘጉብ
ታላችሁና ፥ አብነት ሁናችሁ እንዳይገቡ ታደ
ርጓቸዋላችሁ ማለት ነው ።
አንትሙኒ ኢትበውዑ ፥
እናንተም አትገቡ ።
ወለእለኒ ይበውዑ ትከልዕዎሙ በዊእ ።
የሚገቡትንም አብነት ሁናችሁ እንዳይገቡ ታደር
ጓቸዋላችሁ ።
፲፭ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደ
ልዋን ።
እናንተ ግብዞች ወዮላችሁ ።
እስመ ተዓውዱ ባሕረ ወየብሰ ከመ ታግምዑ አሐደ
ፈላሴ
፲፭ ትገዝሩ ሲል ነው ከጣዖት ከኃጢአት
ፈልሶ የመጣውን ትገዝሩ ዘንድ የብሱን በእግር
ባሕሩን በሐመር ትዞራላችሁና ወተጠሚቆ ትሬሰ
ይዎ ወልደ ገሃነም ።
የገሃነም ልጅ ማሰት ከተገዘረም በኋላ ተግልታችሁት
ገሃነም ትወርዳላችሁ ።
፲፮ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እም
ሀርተ ዕውራን ።
፲፮ እምርሁት ይላል የዕውራን እእምሮ መሪ
ዎች መምሮች ወዮላችሁ ።
እለ ትብሉ ዘመሀለ በቤተ መቅደስ ይጊጊ ።

በቤተ መቅደስ ዉስጥ ልዩ አይሆንበትም የምትሉ።
ወዘሰ መሀለ በወርቅ ቤተ መቅደስ አይጌጊ ።
በመብው ቢምል ግን ዕዳ ይሆንበታል የምትሉ ።

፲፯ ዓብዳን ወዕውራን ።
፲፯ እናንተ ዐላዋቆች ሰነፎች ።
ጎይ የዓቢ ።
ግን ይበልጣል ።
ወርቅኑ ፤ ወርቅ ይበልጣልን ወሚመ ቤተ መቅደስ ዘይቄድሶ ለወርቅ ።
ወይም ወርቁን የሚያከብረው ቤተ መቅደስ ይበልጣልን አኮኑ ቤተ መቅደስ ዘይቄድሶ ለወርቅ ።
ወርቁን የሚያከብረው ቤተ መቅደስ ይበልጥ የለምን

፲፰ ወዘመሐለ በምሥዋዕ ኢይጌጊ ።
፲፰ በምሥዋዑ ባሉ በታቦቱ የማለ ዕዳ አይሆንበትም ትላላችሁ ወዘሰ መሐለ በጽንሐሕ ዘላዕሌሁ ይጌጊ ትብሉ ።
በመሥዋዕቱ የማለ ግን ዕዳ ይሆንበታል ትላላችሁ

፲፱ አ ዓብዳን ወዕውራን ።
፲፱ እናንተ ዐላዋቆች ሰነፎች ።
መኑ የዓቢ ።
ግን ይበልጣል ።
ጽንሐሕኑ ወሚመ ምሥዋዕ ።
መሥዋዕቱ ይበልጣልን ወይስ ታቦቱ ይበልጣል ።
አኮኑ ምሥዋዕ ዘይቄድሶ ለጽንሐሕ ።
መሥዋዕቱን የሚያከብረው ታቦቱ ይበልጥ የለምን ፤ ከታቦትና ከመሥዋዕት ግን ይበልጣል ቢሉ እስኪለወጥ ታቦት ይበልጣል ከተለወጠ በኋላ ግን አንድ ነው ከደሙ ደሙ አይበልጥም ከታቦትና ከመስቀል ግን ይበልጣል ቢሉ በሀገራቸው ሜሮን ይቀባሉና ሁሉም እኩል ነው ። በሀገራችን ግን ሜሮን አይቀቡምና ታቦት ይበልጣል ፤ መስቀል ያንሳል ።

፳ ዘኬ መሐለ በምሥዋዕ መሐለ ቦቱ ።
፳ ቢታቦቱ የማለ በታቦቱ ማለ
ወበኵሉ ዘዲነብር ዲቤሁ ።
በታቦቱ ላይ ባለው ሁሉ ማለ ።
፳፩ ወዘሂ መሐለ በቤተ መቅደስ መሐለ ቦቱ
፳፩ በቤተ መቅደስ የማለ በቤተ መቅደስ ማለ
ወመሐለ በኵሉ ዘይኅብር ውስቴቱ ።
በቤተ መቅደስ ውስጥ ባለው ሁሉ ማለ ።
፳፪ ወዘሂ መሐለ በሰማይ መሐለ መንበር ለእግዚአብሔር ።
፳፪ በሰማይ የማለ በዙፋኑ ማለ ።
ወበዘይነብር ዲቤሁ ።
በሰማይም ባለው ማለ ።
እንዲሁም ዘሂ መሐለ ብለህ መልስ በትሰብእት የማለ በትሰብእት ማለ ወበዘይነብር ዲቤሁ ተዋሕዶትም ባለው በመለኮት ማለ ። ወዘሂ መሐለ በሰማይ ፣ በመለኮት የማለ በመለኮት ማለ ወበዘይነብር ዲቤሁ ፣ ተዋሕዶትም ባለ በትሰብእት ማለ ።

፳፫ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደልዋን እለ ታዐሥሩ ዐሥራተ ጼጋሁ ለአሕዛብ ሉቃ ፲፩ ፡ ፵፪ ።
፳፫ ያብሽ ፣

ወሰፊላን ፣ የድንብላል ወለከሙን ።
ፌጦ ። እንድም የባሕር ከሙን ካሥር አንድ የምትሰጡ ። ወኀደግሙ ዘየዓቢ ትእዛዛተ ኦሪት ።
በኦሪት የታዘዘውን ደገኛውን ትእዛዝ የምታስቀሩ ፍትሐ ። ፍርድን ማለት ዘቈማር ሀቡ ለቄማር ያለውን ወጽድቀ ። ምጽዋተ አበደሮ እመሥዋዕት ያለውን ፣ ወሃይማኖተ ። ወዘእግዚአብሔር ለእግዚአብሔር ያለውን የምታስቀሩ ።
ዘኒ መፍትው ትግበሩ ።
ይህንስ ልታደርጉ ይገባል ማለት ደጋጉን ልትሰጡ ይገባል ወዝክተኒ ኢትኅድጉ ።
ያንንም አትተው ማለት ጥቃቅኑንም አታስቀሩ ።

፳፬ አምርሀተ ዕውራን እለ ጸጹተ ትነጥፉ ።
፳፬ ጥቃቅኑን ካሥር አንድ አጥርታችሁ የምትሰጡ ። ወይነጥፎሙ ለደቂቀ ሌዊ እንዲሉ ወገመለስ ትውኅጡ ።
ታላላቁን ስውራችሁ የምታስቀሩ መሪዎች ፤

፳፭ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደልዋን እለ ተሐፅቡ ለጽዋዕ ወለጻሕል እንተ አፍኣሁ ።
፳፭ ፃሕል ጽዋውን ውጭውን የምታጥቡት ግብዞች ወዮላችሁ ወእንተ ውስጡሰ ምሉእ ሐይደ ወትዕግልተ ፤
በውስጥ ግን ቅሚያን የተመላ ነው ፣ በአሰበ ደነሰ በመማለጃ ሰርቀው ቀምተው ያመጡታልና ፤ እንድም በዚህ የመጣውን ይበሉበታልና ።
፳፮ ፈሪሳዊ ዕውር ቅድመ ሕጽብ ለጽዋዕ ወለፃሕል እንተ ውስጡ
፳፮ አንት ዐላዋቂ ፈሪሳዊ ጻሕል ጽዋውን አስቀድመህ ውስጡን እጠበው ።
ከመ ይኩን ንጹሐ እንተ አፍአሁኒ ።
በአፍአም ንጹሕ ይሆን ዘንድ እንድም እለ ጸጹተ ትነጥፉ ብለህ መልስ ጥቃቅኑን ኃጢአት አጥርታችሁ የምትናገሩ ። ወገመለሰ ። ታላላቁን ሰውራችሁ የምታስቀሩ ። እለ ተሐፅቡ ጻህል ጽዋ ሰውነታችሁን በአፍአ ንጹሕ የምታደርጉ ። ወእንተ ውስጡሰ ። በውስጥ ግን ኃጢአትን የተመላ ነው ቅድመ ሕፅበ ፣ አስቀድመህ ፃሕል ጽዋ ሰውነትህን በውስጥ ንጹሕ አድርገው ። ከመ ይኩን በአፍአም ንጹሕ ይሆን ዘንድ የሥጋ ንጽሕ ስንፍስ አይሆንም ነፍስ የነፃች እንደሆነ ግን ለሥጋም ይተርፈዋል ቅዱሳን የበቁ እንደሆኑ የነፍሳቸው ለሥ

ጋቸው ፣ የሥጋቸው ለልብሳቸው ተርፎት በልብሳ ቸው በመቋሚያቸው በጭራቸው ከመፈወስ ይደ ርሳሉና ።

፳፯ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደ ልዋን እስ ትመስሉ መቃብረ ግብሱሳነ እለ እም አፍአሆሙ ያስተርእዩ ሠናያነ

፳፯ በአፍአ አጊጠው የሚታዩ የተለሰኑ መቃ ብራትን የምትመስሉ ግብዞች ወዮላችሁ ።
ወእንተ ውስጦሙሰ ምሉአን አዕፅምተ ወኵሉ ርኩስ ።
ርኩስ ነገር ማለት በውስጥ ግን እዠት ፈሶ ኹርማቱ ተፀጣጥሶ አጥንቱ ተከስክሶ ሥጋው ተልከስክሶ ለዓይን የሚያስከፋ ለፍንጫ የሚከረፋ ነገር ያለባ ቸውን መቃብራት የምትመስሉ ።

፳፰ ከማሁ አንትሙኒ ትጼደቁ ለዓይነ ሰብእ

፳፰ እንደ በአፍአ አጊጠው እንዲታዩ እናን ተም በአፍአ ደጋግ መስላችሁ ትታያላችሁ ።
ወእንተ ውስጥክሙሰ ምሉአን አንትሙ ዓመፃ ወአድልዎ በውስጥ ግን ኃጢአትን የተመላችሁ ናችሁ ።

፳፱ አሌለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደ ልዋን እስ ተሐንጹ መቃብሪሆሙ ለነቢያት ወቻ ሜንዩ ዝጎሮሙ ለጻድቃን ።

፳፱ ደጋግሞ ካልሆኑ የነቢያትን መቃብር ያን ጹሉ ይበሉን ብላችሁ የነቢያትን መቃብር የምታንጹ የጻድቃንን መቃብር የምታስጌጡ ግብዞች ወዮላችሁ
፴ ወትብሉ ሶበሰ ሀሎነ በመዋዕለ አበዊነ እም ኢተሳተፍነ ምስሌሆሙ በከዒወ ደመ ነቢያት ።
፴ ባቤቶቻችን ዘመን ኑረንስ ቢሆን የነቢያ ትን ደም በማፍሰስ ከላቸው ጋራ አንድ ባልሆነም ነበር ትላላችሁ ።
፴፩ ናሁ ሰኬ ለሊክሙ ትከውኑ ስምዓ ከመ ደቂ ቆሙ አንትሙ ለቀተልተ ነቢያት ።
፴፩ ነቢያትን ለገደሉ ሰዎች ልጆቻቸው እን ደሆናችሁ እነሆ ትመሰክራላችሁ ።
፴፪ አንትሙሂ ፈጽሙ መሥፈርተ አበዊክሙ
፴፪ እናንተም ካባቶቻችሁ የቀረውን ፈጽሙ አጸንሆ ለአምሬምን እስከ አመ ይትፈጸም ኃጢአቱ እንዲል ፤ እሱስ እይዛቸውም እንዳይተውት ያውቃ ልና እንዲህ አለ እንጂ ። የጌታ ሞት ለነቢያት ሞት ምልእት እንደሆን የውሉድም ኃጢአት ለአ በው ኃጢአት መልእት ይሆናል ።
፴፫ አ ትውልደ አራዊተ ምድር አፎ ትክሉ አምስጠ እምዙነኔ ገሃነም ። ማቴ ፫ ፣ ፯ ።
፴፫ እናንት የምድር አባብ ልጆች በገሃነም ከሚመጣው ፍዳ መዳን እንደምን ይቻላችኋል ።
፴፬ ወበእንተዝ እነ እፌኑ ኀቤክሙ

፴፬ ስለዚህ ሁሉን የምትሉ ስለሆነ ስለዚህ ነገር ወደናንተ እልካለሁ ነቢያት ፤

| | | |
|---|---|---|
| ነቢያት ፣ | ፫ | አርድዕትን |
| ወሐዋርያተ | | ሐዋርያትን |
| ወጠቢባተ ። | | ሹማምንትን |
| ወጸሐፍተ | | መምህራንን |

መተርጓማንን እልካለሁ ።
ፀ እምኔሆሙ ፀትቀትሉ ፣ ከባቸው ወገን የምትገድሉት አለ
ወፀ እምኔሆሙ ዘትሰቅሉ ።
የምትሰቅሉት አለ ።
ወፀ እምኔሆሙ ዘትቀሥፉ በምኵራባቲክሙ ።
በምኵራባችሁ አግብታችሁ የምትገርፉት አለ ።
ወትስድድዎሙ እምሀገር ውስተ ሀገር ።
ካንዱ አገር ወዳንዱ አገር አስወጥታችሁ የምት ሰዱት አለ ።

፴፭ ከመ ይብጻሕ ላዕሌክሙ ደመ ኵሉሙ ጻድቃን እምደመ አቤል ጻድቅ እስከ ደመ ዘካርያስ ወልደ በራክዩ ዘቀተልክምዎ በማእከለ ቤተ መቅ ደስ ወምሥዋዕ ። ዘፍ ፣ ፬ ፣ ፰ ፣ ዕብ ፣ ፩ ፣ ፬ ፣ ፪ ፣ ሕጹጸ ፳፬ ፣ ፳፪ ።

፴፭ ከአቤል ደም ጀምሮ በዕቃ ቤትና በቤተ መቅደስ መካከል በገደላችሁት እስከ ዘካርያስ ደም ድረስ በዓለም የፈሰስ የጻድቃን ደም ፍዳ ሊደረግባ ችሁ ንድ ፣ ሐተታ ፣ ጠርዙንና ጠርዙን ይዞ ቲናገረ ። ለበማዕታተ ብሊት ጥንታቸው አቤል ፍጻሜያቸው ዘካርያስ ነውና ፤ አንድም ግፍ ለግፍ ሲያነጻጽር አቤል የሞተ በግፍ ነው ዘካርያስም የሞተ በግፍ ነውና ። አንድም ደመ ስክየትንና ደመ ስክየትን ሲያነጻጽር መልአኩ ለሄኖክ ማኀደረ ኃጥአንን አያ ዞረ ሲያሳየው እንዲት ነፍስ እየተንጻረጻረች ስታ ካስስ ስታሳጣ አይቶ ዘመንፈስ ዘመኑ ብሎ ጠየቀው ዘአቤል ዘቀተሎ እኁሁ ። ይሰኪ ኪያሁ እስከ አመ ይትኃጎሉ ደቂቁ እምገጸ ምድር በማየ አይኅ ብሎ ታል ። የዘካርያስም ደም ፫ ዘመን ሲፈላ ኑሯል ። ጥጦስ አይቶ ምንድነው ብሎ ጠየቀ ። ደግ ሰው ነበረ በግፍ አስገድለውት ነው አሉት ከንጉሮቹ ወገን ሰባት ሰዎች አስመጥቶ ቢያሳርድ መፍላቱን ትቷል፤ ከዕቃቤትና ከቤተ መቅደስ መካከል ያስገደላችሁት አለ ፣ የምትሻው ሕፃን ከዘካርያስ ቤት አለ ሲፀንስ ያባቱን እንደበቅ የዘጋ ሲወለድ የፈታ ብለው ነገ ሩት ። አስጠርቶ እንዲህ ያለ ብላቴና አለ ብሎ ጠየ ቀው ። አዎን ምነው ጠየቅኸኝ አለው ይህን ልት ነግረኝ ነው ሂድ አለው ። ይህ ዓላዊ አለ ነገር እል ጠየቀኝም ልጄን ሊያስገድለው ነው ሁሉት ሳላሳ ድርበት ብሎ ከቤተ መቅደስ አግብቶ ሲጸልይለት ግደሉ ብሎ ጭፍራ ላከ ። ከቤት ቢሄዱ አጡት ኋላ መልአኩ ለኤልሳቤጥ ይህ ዓላዊ ልጅሽን ሊያስ

ገድልብሽ ነው ገዳም ይዘሽ ሂጂ አላት ገዳም ይዛ ሂዳለች ከቤተ መቅደስ ቢሄዱ እሱን አገኙት ከዚያ ገድለውታል ። አንድም የምትሻት ሴት ከልጅዋ ጋራ ከዘካርያስ ቤት ትገባለች ትወጣለች ብለው ነገሩት አስጠርቶ ወስዶ አኔ የምሻት ሴት ካንተ ቤት አስችን አለው እዎን አለው ። ምነው ያልነገርከኝ አለው እመቤቴን የሷን ሞት ለኔ ያድርገው አለው ። እንዳየህ ውጋው አለው ወጉት ደም ተኩሶት ሂዶ ከቤተ መቅደስና ከዕቃቤት መካከል ወድቋል ።

፴፮ እማን እብለክሙ ከመ ዝንቱ ኵሉ ይበጽሐ ለዛቲ ትውልድ ።

፴፮ በቤተ እይሁድ ይህ ሁሉ እንዲደረግባት በውነት እነግራችኋለሁ ።

ዘከመ ኄሳ ለኢየሩሳሌም ።

፴፯ ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም እንተ ትቀትሎሙ ለነቢያት ወትዌግሮሙ ለሐዋርያት እለ ተፈነው ኀቤሃ ። ሉቃ. ፲፫ ፡ ፴፬ ።

፴፯ በመምህርነት ወዳንች የተላኩ ነቢያትን ያጠፋሻቸው ሐዋርያትን የተጣላሻቸው ቤተ አይሁድ ሚመጠነ ፈቀድኩ አስተጋብኦሙ ለውሉድኪ ከመ እንተ ታስተጋብእ ዶርሆ ዕጕሊሃ ታሕተ ክነፊሃ ። ዶሮ ልጆቿን በክንፏ እንድትሰበስብ ማለት ነቢያት ሕዝቡን አንድ ያደርጓቸው እንደ ነበረ ልጆችሽን በትምህርት አንድ አደርጋቸው ዘንድ ምን ያህል ወደድኩ ።
ሐተታ ፡ ዶርሆ አላቸው ነቢያትን ፡ ዶሮ ወተት የላትም ልጆቿዋን የምታሳድግ ስው በጸረበት ነው ነቢያትም በጻዕር የተገኘውን ነውና ሲያስተምሩ የነበረ መልአክ የነገራቸውን መንፈስ ቅዱስ የገለጣላቸውን ።ወአበይክሙ እናምን አላችሁ ።

፴፰ ናሁ ይትኀደግ ለክሙ ቤትክሙ በድወ ።

፴፰ እነሆ ቤተ መቅደስ ትፈርሳለች ።

፴፱ እማን እብለክሙ ኢትሬእዩኒ እምይእዜ እስከ ሶበ ትብሉ ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር ።

፴፱ በእግዚአብሐር ስም የሚመጣ የተባረከ ነው እስክትሉ ድረስ ከእንግዲህ ወዲህ አታዩኝም ብየ በእውነት እነግራችኋለሁ ። ሆሣዕና አላለፈም ቢሉ የተመቸ ፡ አልፏል ቢሉ ምጽአትን ያያል ።

በእንተ ዘአቅደመ ነጊረ ሙስናሃ ለቤተ መቅደስ

ምዕራፍ ፡ ፳፬ ።

፩ ወወፂአ እግዚእ ኢየሱስ እምቤተ መቅደስ ሖረ ።

፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከቤተ መቅደስ ወጥቶ ሄደ ።
ወቀርቡ አርዳኢሁ ወአርአይዎ ንድቀ ሕንጻሁ ለቤተ መቅደስ ደቀ መዛሙርቱ ቀርበው የቤተ መቅደስን ሥራ አሳዩት ማለት እንዲህ ሲያምር ይፈርሳል ትላለህ አሉት ፡ የጧት ፀሐይ ወድቆበት ሲያሸበርቅ አይተው

፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ መለሰ ፤

፪ ወይቤሎሙ ትሬእዩኑ ዘንተ ኵሎ ፤
ይህን ሁሉ ታያላችሁን ማለት ይህን ይደንቃችኋልን እማን እብለክሙ ኢይትኀደግ ዝየ እብን ዲበ እብን ዘኢይትነሠት ።
የማይፈርስ ሁኖ ደንጊያ በደንጊያ ላይ አይቀርም ብየ እንዳይቀር በውነት እነግራችኋለሁ ሐተታ ፡ ከጥጦስ ሠራዊት አንዱ ደንጊያ ቢፈነቅል ድስት ሙሉ ወርቅ አገኘ እንደዚያ እናገኛለን እያሉ ቤተ መቅደስን ሲያፈርሷት ፩ ፡ ፩ ደንጊያ አልደረሳቸውም አንድም ትሬእዩኑ ብለህ መልስ ይህን ይደንቃችኋልን ይህስ የሰው ሕንጻ ነው እማን እብለክሙ ሕንጻ እግዚአብሔር ሰው ይፈርሳል ይበሰብሳል ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፫ ወእንዘ ይነብር እግዚእነ ውስተ ደብረ ዘይት ቀርቡ ኀቤሁ አርዳኢሁ ።

፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በደብረ ዘይት ተቀምጦ ሳለ ደቀ መዛሙርቱ ወደሱ ቀረቡ ወይቤልዎ እንተ ባሕቲቶሙ ለብቻቸው ጠየቁት ሦስቱ ባለሟሎቹ እንድርያስን ጨምረው ይጠይቁታል ።
ንግረነ ማእዜ ይከውን ዝንቱ ወናሁ ይትኀደግ ለክሙ ቤትክሙ በድወ ብሎ ነበርና ቤተ መቅደስ የሚፈርስበት ምን ጊዜ ይሆናል ።
ወምንትኑ ተአምሪሁ ለምጽአትከ ።
እማን እብለክሙ ኢትሬእዩኒ ብሎ ነበርና የምጻትህስ ወለኀልፈተ ዓለም ።
የኀልፈተ ዓለምስ ምልክቱ ምንድነው አሉት ።

፬ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ዑቁ ኢያስሕትክሙ ኤፌ ፡ ፭ ፡ ፮ ።

፬ እንዳያስቷችሁ አስተውሉ አላቸው ።

፭ እስመ ብዙኃን ይመጽኡ በስምየ እንዘ ይብሉ አነ ውእቱ ክርስቶስ ።

፭ እኔ ክርስቶስ ነኝ እያሉ ብዙ ሰዎች በኔ ስም ይነሣሉና ፡ ታሪክ ባማራ መንግሥት ጊዜ ዘክርስቶስ ይሉኛል ብሎ ተነሥቶ እንደነበረ ሰቅለው ገድለውታል ከሱ ጋራ ፯ መቶ ሰዎች ሙተዋል ሰማዕታተ ዘክርስቶስ ተብለዋል ።
ወያስሕትዎሙ ለብዙኃን ፡ ብዙ ሰዎችን ያስታሉ ።

፮ ወሶበ ሰማዕክሙ ።
ዶር ሲሰበሰብ ፡

፮ ወአጽባዕተ ።
ጋሻ ለጋሻ ሲጋጕድ ፡
ወድምፀ ጸባኢት ፡
ገድሎ ስልቦ ሲያገር ብትሰሙ
ዑቁ ኢትደንግፁ ።
እንዳትደነግጡ አስተውሉ ፤

እስመ ግብተ ሀለዎ ይኩን ዝንቱ ኵሉ ።
ይህ ሁሉ ፈጥኖ ይደረግ ዘንድ አለውና ።
ወባሕቱ አኮ በጊዜሃ ዘየኃልቅ፤ነገር ግን ያን ጊዜ
የሚፈጸም አይደለም ።

፯ ወይትነሥኡ ሕዝብ ዲበ ሕዝብ ።
፯ ሕዝበ ሮም በሕዝበ እሥራኤል ላይ በጸላ
ትነት ይነሡባቸዋል ። እንድም ወይትነሥኡ ሕዝብ
ብስህ መልስ ሕዝበ እሥራኤል በሕዝበ እሥራኤል
ላይ ፤ ነገሥተ እሥራኤል በነገሥተ እሥራኤል ላይ
በጸላትነት ይነሡባቸዋል ።

ሐተታ ፤ ቀን ከጥጦስ ሠራዊት ጋራ ሲዋጉ ይውላሉ ።
ማታ ከኔ ወገን አንግሥ ከኔ ወገን አንግሥ እያሉ
ስንዝር ስንዝር ሙሉ ሾተል አልፎ ሲሄድ አበጅተው
አንዱ ባንዱ እየሸጐጠበት ይሄዳል ገዳዩ ስላልታ
ወቀ ሞተ ዕውር ተብሏል፤እንድም ሕዝበ ሮም በሕ
ዝበ እሥራኤል ላይ በጸላትነት ይነሡባቸዋል
ሕዝበ ሮም ያላቸው ቅሉ ከአርዳሚስ ጋራ የሄዱ
የአርዳሚስ ወገን ናቸው ።
ወነገሥት ላዕለ ነገሥት ።
ነገሥተ ሮም በነገሥተ እሥራኤል ላይ በጸላትነት
ይነሣሉ ። ነገሥተ ሮም ያላቸው ቅሉ የአር
ዳሚስ ልጆች ናቸው ።
ወይመጽእ ረኃብ ወብድብድ ፤
ወድልቅልቅ ውስተ ኵሉ በሐውርት ።
በየሀገሩ ረኃብ ቸነፈር ሽብር ይደረጋል ።
፰ ወዝንቱ ኵሉ ቀዳሚሁ ለሕማም ውእቱ።
፰ ይህ ሁሉ የመከራው መጀመሪያ ነው ማለት
በጥጦስ ለሚደረገው መከራ ፊት አውራሪ ነው ።
ቀዳሚሁ የጥጦስ ሕማም የሐሳዊ መሲሕ ቀዳሚሁ
የሐሳዊ መሲሕ ፤ ሕማም የምጽአት ።
፱ አሜሃ ይትባጽሑክሙ ወይሜጥውክሙ ለም
ንዳቤ ። ማቴ.፲ ፡ ፲ ፡ ፯ ። ሉቃ ፡ ፳፩ ፡ ፲፪ ። ዮሐ ፡
፲፭ ፡ ፳ ፡ ፲፮ ፡ ፪ ።
፱ ያን ጊዜ ስጸዋትወ መከራ አሳልፈው ይሰ
ጧችኋል ።
ወይቀሥፉክሙ ።
ከምኲራባቸው አግብተው ይገርፏችኋል ። ወይ
ቀትሉክሙ ይጸኗችኋል ።
ወትከውኑ ጽሉዓነ በኀበ ኵሉ ሰብእ በእንተ ስምየ።
ስለስሜ ማለት በኔ ስም ስላመናችሁ በኔ ስም ስላስ
ተማራችሁ በኔ ስም ስለተጸራችሁ ሁሉ ይጸላችኋል
፲ ወይእተ አሚረ የዓልዉ ብዙኃን ሃይማ
ኖቶሙ ።
፲ በዚያን ጊዜ ብዙ ሰዎች ሃይማኖታቸውን
ይለውጣሉ ።
ወይጸልዑ በበይናቲሆሙ ።
እርስበርሳቸው ይጣላሉ ።
ወያገብኡ ቢጾሙ ለሞት ይትቃተሉ ።
አንዱ አንዱን ይጸላዋል ።

፲፩ ወብዙኃን ሐሳውያን ነቢያት ይመጽኡ ።
፲፩ በመምህራን የሚያብሉ መምህራንን የሚ
ያሳብሉ ሐሰተኞች መምህራን ይነሣሉ ።
ወያስሕትዎሙ ለብዙኃን ።
ብዙ ሰዎችን ያስቷቸዋል ።

፲፪ ወእምብዝኃ ዓመፃ ወእከይ ተሐጽጽ ፍቅር
እምብዙኃን ።

፲፪ ከሐሰትና ከኃጢአት ብዛት የተነሣ ፍቅር
ከብዙ ሰዎች ታንሳለች። ትቈኩስ ፍቅር ይላል አብነት
የሐጽጽ ሲል ነው። ወይሴኩሱ ከመ ይቅብዑ መል
አከ ወንጉሠ እንዲል ። የአክስን ባነገሡ ጊዜ በእ
ልፍ በእልፍ ይቈጠሩ የነበሩ እሥራኤል ዐሥር ሠረ
ገላ አምሳ ፈረሰኛ ሺህ እግረኛ ሁነው ተገኝተዋል ።
ወብዙኃን የዓልዉ ሃይማኖቶሙ ወፍቅሮሙ ።
ብዙ ሰዎች ሃይማኖታቸውን ምግባራቸውን ይለው
ውጣሉ ።

፲፫ ወዘሰ አዝለፈ ትዕግሥቶ ውእቱ ይድኅን።
፲፫ ፈጽሞ መከራውን የታገሠ ከፍዳ የሚ
ድን እሱ ነው ። እስከ ፍጻሜ ይላል አብነት እስከ
ዕለተ ሞቱ ታግሦ መከራ የተቀበለ ከፍዳ የሚድን
እሱ ነው ።

፲፬ ወይሰበክ ዝ ወንጌለ መንግሥት ውስተ
ኵሉ ዓለም ።

፲፬ የመንግሥት ወንጌል ማለት ጌትነቱን የም
ትናገር ወንጌል ባ፷ቱ ማዕዘን ትነገራለች በእስላም
ቤት ስንኳ ሳይቀር ትገኛለች ። ታሪክ በሀገራ
ችን ቴዎድሮስ በሀገራቸው ዮሐንስ የሚባል ይነግ
ሣል የኛም ሄዶ ያም መጥቶ በእስክንድርያ ሦስት
ቀን ይዋጋሉ አራቱ ሊቃነ ጳጳሳት የክርስቲያን ደም
ለምን ይፈሳል መሥዋዕት ሠውተን በመሥዋዕቱ ምል
ክት ባታየለት ሃይማኖት ይጽና ይሏቸዋል ሁሉም በያ
ሉበት መሥዋዕት ያቀርባሉ ። የእስክንድርያ ሊቀ
ጳጳሳት በሠዋው እነ ውእቱ ክርስቶስ ብሎ በርግብ
አምሳል ወርዶ ይመስክራል ከዚህ በኋላ በሃይማኖት
አንድ ይሆናሉ በግቢ ይገናኛሉ እንደዚህ የሚል ከምን
አለ ቢሉ ከገድለ ፊቅጦር ከራእየ ሲኖዳ ።
ከመ ይኩን ስምዓ በላዕለ አሕዛብ ።
ባላመኑ በአሕዛብ መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ።
ወይእተ አሚረ ይበጽሕ ሕልቀት ።
ያልተያያዘ ይእተ አሚረ ነው የሐሳዊ መሲሕን
ሲናገር መጥቶ የጥጦስን ይእተ አሚረ አለ ነቢይ
ኢሳይያስ የዲዋዊን ነገር ሲናገር መጥቶ የሚጠትን
ይእተ አሚረ እንዳለ ።

፲፭ ወእምከመ ርኢክሙ ትእምርተ ርኩስ ዘም
ዝባሬ ዘተብህለ በዳንኤል ነቢይ ዘይቀውም ውስተ
መካን ቅዱስ ወዘያነብብ ለይለቡ ። ዳን ፱ ፡ ፳፯ ።
ማር ፲፫ ፡ ፲፬ ።

፲፮ ሉቃ ፳፩፡፳ ። በቅዱስ ቦታ የሚቆም ማለት ለቤተ መቅደስ አንባቢነት የሚሾም ያስተ ውል ተብሎ የተነገረውን ቤተ መቅደስ በሚፈርስ በት ጊዜ የሚሆን የጥጦስን ጣዖቱን ያያችሁ እንደ ሆን ያን ጊዜ ፍጻሜው ይመጣል ማለት የአይሁድ ጥፋት ይሆናል ትእምርተ በላየር እንዲል። አንድም ቤተ መቅደስ በሚፈርስበት ጊዜ የሚሆን የጥጦስን ጣዖት ያያችሁ እንደሆን ያን ጊዜ የአይሁድ ጥፋት ይሆናል ። ወዘተብህለ በዳንኤልም ለቤተ መቅደስ አንባቢነት የሚሾመው ለይለቡ ያለውን ያስተውል፤

አንድም ወይእተ አሚረ ያን ጊዜ የአይሁድ ጥፋት ይሆናል ። ወእምከመ ርኢክሙ ፣ ቤተ መቅደስ በሚፈርስበት ጊዜ የሚሆነን የጥጦስን ጣዖቱን ያያችሁ እንደሆነ ወዘተብህለ ። አሜሃ ይትኀተም ራእየ ነቢያት ወይትቀባዕ ቅዱስ ቅዱሳን ወየዓርፍ ሙስና ዲበ መትከፈ ርኩሳን ተብሎ በዳ ንኤል የተነገረውን ይወቅ።አንድም የተያያዘ ይእተ አሚረ ነው ሐሳዊ መሲሕን ሲናገር መጥቶ ምጽ አትን ይእተ አሚረ አለ ለቤተ መቅደስ አንባቢነት የሚሾም ለይለቡ ተብሎ በዳንኤል የተነገረለትን ይህ ዓለም በሚያልፍበት ጊዜ የሚሆን የሐሳዊ መሲ ሕን ጣዖቱን ጣዖትነቱን ያያችሁ እንደሆን ያን ጊዜ ኀልፈተ ዓለም ይሆናል ። አንድም ይህ ዓለም በሚ ያልፍበት ጊዜ የሚሆን የሐሳዊ መሲሕን ጣዖትነቱን ጣዖቱን ያያችሁ እንደሆነ ኀልፈተ ዓለም ይሆናል፤ ወዘተብህለ በዳንኤልም ለይለቡ ተብሎ የተነገረለ ትን ያስተውል ። አንድም ወይእተ አሚረ ያን ጊዜ ኀልፈተ ዓለም ይሆናል ። ወእምከመ ርኢክሙ ፣ ይህዓለም በሚያልፍበት ጊዜ የሚሆን የሐሳዊመሲሕ ጣዖቱን ጣዖትነቱን ያያችሁ እንደሆነ ዘተብህለ ፣ አሜሃ ይትኀተም ራእየ ነቢያት ወይትቀባዕ ቅዱስ ቅዱሳን ወየዐርፍ ሙስና ዲበ መትከፈ ርኩሳን ተብሎ በዳንኤል የተነገረውን ያስተውል ። ወእም ከመ ርኢክሙ ኃሣር ለሙስና ይላል በማርቆስ ።

፲፮ አሜሃ እለ ውስተ ይሁዳ ይጉዩ ውስተ አድባር ።

፲፮ ያን ጊዜ በይሁዳ ዕፃ ያሉ ወደ ተራራ ይሽሹ ።

፲፯ ወዘሂ ሀሎ ውስተ ናህስ ኢይረድ ይን ሣእ ዘውስተ ቤቱ ።

፲፯ ከሰገነት የወጣም ከምድር ቤት ያለውን ያነሣ ዘንድ ወደ ምድር ቤት አይወርድም ።

፲፰ ወዘሂ ገዳመ ሀሎ ኢይትመየጥ ድኅ ሬሁ ይንሣእ ልብሶ ።

፲፰ በበረሀም ያለ ልብሱን ያነሣ ዘንድ ወደ ኋላው አይመለስም እንደ ወጣ ይቀራል ማለት ነው ።

፲፱ ወባሕቱ አሌሎን ለጽንሳት ወለእለ የሐፅና በውእቱ መዋዕል ።

፲፱ ነገር ግን በዚያ ወራት ለፀነሱ ወልደው ለሚያሳድጉ ሴቶች ወዮላቸው ። ሐተታ የፀነሱት ከመንገድ ይወልዳሉ የወለዱት ወተት ፍትፍት አምጡ ብለው ያስቸግሯቸዋልና ።

፳ ወጸልዩ ባሕቱ ከመ ኢይኩን ጉየይክሙ በክረምት ወበሰንበት ግብ ፩፡፲፬ ።

፳ ነገር ግን ስደታችሁ በክረምት በሰንበት እን ዳይሆንባችሁ ለምኑ ። ሐተታ ፣ ክረምት ላዩ ውኃ ታቹ ውኃ ነው እያሸጋግርምና በሰንበትም ዕለተ ጽርዓት ነው ። መንገድ ቅሉ የሚያሳይ አይገኝምና ። አንድም ሦስት ወር ክረምት ዐርፋለሁ ብሎ ዘጠኝ ወር ምግ ቡን ሲሰበስብ ይባጃል በ፯ኛው ቀን አርፋለሁ ብሎ ፮ቱን ቀን በተግብሮ ይሰነብታል ዐርፋለሁ ባለበት ጊዜ ስደት የመጣ እንደሆን ከቀቢጸ ተስፋ ይደርሳ ልና አንድም አሜሃ እለ ውስተ ይሁዳ ብለህ መልስ በሃይማኖት ያሉ ሰዎች ረድኤተ እግዚአብሔርን ጥግ ያደርጋሉ ወዘሂ ውስተ ናሕስ ልዕልና ነፍስ ያለ ውም ወደ ትሕትና አይወርድም ይንሣእ ዘውስተ ቤቱ ሥጋዊ ሥራ ይሠራ ዘንድ ፣ ወዘሂ ሀሎ ገዳመ ፣ የመን ነም ወደ ዓለም አይመለስም ይንሣእ ልብሶ ፣ ዓለ ማዊ ሥራ ይሠራ ዘንድ ፣ ወባሕቱ አሌሎን ለፅኑሳት ነገር ግን በዚያ ወራት ኃጢአትን በሐልዮ ፀንሰው በነቢብ ወልደው በገቢር ለሚያሳድጉ ሰዎች ወዮ ላቸው መከራ ነፍስ አለባቸውና አንድም ምእመናንን በትምህርት ፀንሰው በትምህርት ወልደው በትም ህርት የሚያሳድጉ መምህራን ወዮላቸው መከራ ሥጋ አለባቸውና ፣ ወጸልዩ ባሕቱ ፣ ነገር ግን በሃ ይማኖት ብቻ ሳላችሁ ምግባር ሳትሠሩ ሞት እን ዳይታዘዝባችሁ ለምኑ ። ክረምት ወርኃ ልምላሜ ነው ፍሬ የለውም ሰንበትም ዕለተ ጽርዓት ናትና በጽርዓት ሳላችሁ ሲል ነው ።

፳፩ እስመ ይከውን ይእተ አሚረ ዓቢይ ሕማም ወምንዳቤ ዘኢኮነ ከማሁ እምፍጥረተ ዓለም እስከ ዮም ።

፳፩ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ ተደርጎ የማያውቅ ። ወኢይከውንሂ ። ከእንግዲህም ወዲህ የማይደረግ መከራ ጽዋትወ መከራ ያን ጊዜ ያደረጋልና ።

፳፪ ወሶበ ኢሐፀራ ንጉሥ መዋዕል እምኢ ድኅነ መኑሂ ዘሥጋ ።

፳፪ ቀንስ ባያጥር ሥጋዊ ደማዊ ሰው ሁሉ ከመከራ ከክህደት ባልዳነም ነበር ።

ወባሕቱ በእንተ ኅሩያኒሁ የሐፅራ እማንቱ መዋዕል ነገር ግን ስለ ምእመናን ቀኑ ያጥራል ። ከመዓልቱ አራት ከሌሊቱ አራት ስምንት ሰዓት ይነሣለታል።

፳፫ አሜሃ እመቦ ዘይቤለክሙ ነዋ ዝየ ሀሎ
ክርስቶስ ። ማር.፲፫ ፣ ፳፩ ። ሉቃ ፣ ፲፯ ፣ ፳፫ ።

፳፫ ያን ጊዜ ክርስቶስ ከወዲህ አለ ከወዲያ
የለም ከወዲህ ወዲያ ይሄዳል ።
ወነዋ ከሀከ ፣

ከወዲያ አለ ከወዲህ የለም ከወዲያ ወዲህ ይመጣል
ቢሏችሁ ።
ኢትእመኑ ።
በጅ አትበሉ ።

፳፬ እስመ ይትነሥኡ ሐሳውያን መሲሕ ፣
፳፬ መሲሕ ክርስቶስን የሚያሳብሉ በመሲሕ
በክርስቶስ የሚያብሉ ሐሰተኞች መምህራን ይነ
ሣሉና ።
ወሐሳውያን ነቢያት ፣
መምህራንን የሚያሳብሉ በመምህራን የሚያብሉ
ሐሰተኞች መምህራን ይነሣሉና ወይገብሩ ተአ
ምራተ ወመንከራተ ዓበይተ ለአስሕቶ ፤ ሰውን ለማ
ሳት በምትሐት ድንግ ተአምራት ያደርጋሉ ፣ አን
ድም ከመ ያስሕቱ ይሳል ፣ ያስቱ ዘንድ ፤
ሶበሰ ይትክሀሎሙ ለኅሩያንሂ እምአስሀትዎሙ ፣
አይቻላቸውም እንጂ ቢቻላቸውስ ምእመናንንም
ባሳቷቸው ነበር ።

፳፭ ወናሁ አቅደምኩ ነጊሮትክሙ ፤
፳፭ እነሆ አስቀድሞ ነገርኋችሁ ፤
፳፮ እመቦ ዘይቤለክሙ ነዋ ገዳመ ሀሎ ኢትፃዑ፤
፳፮ ክርስቶስ በገዳም ኅብስት አበርክቶ ያበ
ላል ቢሏችሁ አትውጡ ማለት በጅ አትበሉ ።
ወነዋ ውስተ እብያት ኢትእመኑ ።
እነሆ በምዝራብ ያስተምራል ቢሏችሁ በጅ አትበሉ

፳፯ እስመ ከመ መብረቅ ዘይወፅእ እምጽባሕ
ወያስተርኢ እስከ ዓረብ ።

፳፯ ፀሐይ በወጣ ጊዜ ከምሥራቅ እስከ ምዕራብ
እንዲታይ ።
ከማሁኬ ይከውን ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው
የወልደ ዕጓለ እመሕያው የክርስቶስ ምጽአቱ እን
ዲህ ነውና ማለት ሁሉ ያየዋልና ።
፳፰ ሀበ ሀሎ ገደላ ህየ ይትጋብኡ አንስርት።
ሉቃ.፲፯ ፣ ፴፫ ።
፳፰ በአይቴ ንትራከብ ብለውታል በሉቃስ
ያቀናዋል ምግብ ካለበት አንስርት ይሰበሰባሉ አለ
እኔ ካለሁበት እናንተ ትሰበሰባላችሁ ። ሐተታ ፣
ግደላ አለው ራሱን ነፍስ የተለየችውን መለኮት
የተዋሐደውን ሥጋውን ነውና የምንቀበለው ።
አንስርት አላቸው ሐዋርያትን አንስርት ክንፍ አላ
ቸው ። ሐዋርየትም ክንፈ ጸጋ አላቸውና ። አን
ስርት ተመስጦ እንዳላቸው ሐዋርያትም ተመስጦ
አላቸውና ።

በእንተ ካልዓዊት ምጽአት ፤
ዘወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
፳፱ ወእምድኅረ ሕማሞን ለእማንቱ መዋዕል
ፀሐይኒ ይፀልም ። ኢሳ.፲፫፣፲ ። ሕዝ.፴፪ ፣ ፯ ። ኢዮ
፪ ፣ ፲፫ ፣ ፲፩ ፣ ማር.፲፫ ፣ ፳፬ ። ሉቃ ፳፩ ፣ ፳፭ ።
ራዕ.፩ ፣ ፯ ።

፳፱ በሐሳዊ መሲሕ የሚደረገውን መናገር ነው
ይህ ሁሉ መከራ ከተደረገ በኋላ ፀሐይ ያልፋል ።
ወወርኅኒ ኢይሁብ ብርሃና ፤ ጨረቃም ብርሃኑን
አይሰጥም ማለት ያልፋል ።
ወከዋክብትኒ ይወድቁ እምሰማይ ። ከዋክብትም
ያልፋሉ ወያንቀለቅል ኃይለ ሰማያት ፣ አድማስ ድን
ዑን ይለቃል ።

፴ ወይእተ አሚረ ያስተርኢ ትእምርቱ ለወ
ልደ ዕጓለ እመሕያው ውስተ ሰማይ ።

፴ ያን ጊዜ የወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስ
ቶስ ምልክቱ በሰማይ ይታያል አሥረ ርግዘቱን አሥረ
ቅንዋቱን እስራቱን ሳያጠፉ ይመጣልና ። ታሪክ
ሳባ ጳኩሚስ እንደታየው ሲሰግድ ወዙ ወርዶ
መሬቱን ጭቃ አደረገው ወዲያው ጌታ ተገለጸ
ለት አንተን አገኝ ብየ እንዲህ እደክማለሁ አለው
እኔም እንጂ ሳንተ ብየ እንዲህ ሁኜ ተሰቅያለሁ።
ብሎ በዕለተ ዓርብ እንደ ተሰቀለ ሁኖ ጐኑን እንደ
ተወጋ ደሙ እንደፈሰሰ ሁኖ ታይቶታል ። አንድም
ወእምድኅረ ሕማሞን ብለህ መልስ ። በጥጦስ የሚ
ደረገው መከራ ነው ። ይህ ሁሉ መከራ ካለፈ በኋላ
ፀሐይ ይጨልማል ።

ወወርህኒ ኢይሁብ ብርሃና ወከዋክብትኒ ይወድቁ
እምሰማይ ። ጨረቃ ይጨልማል ከዋክብትም ይወ
ድቃሉ ፤ በዕለተ ዓርብ በሠሩት ኃጢአት እንደ
ተፈረደባቸው ለማጠየቅ በዕለተ ዓርብ የተደረገው
ሁሉ ተደርጓል ። ወይእተ አሚረ ያን ጊዜ የወልደ
ዕጓለ እመሕያው የክርስቶስ ምልክቱ በሰማይ ይታ
ያል ። ታሪክ ፣ በሮም አንጻርና በኢየሩሳሌም አን
ጻር ያሉ ከዋክብት ሠልፍ ሰርተው ሲዋጉ በሮም
አንጻር ያሉት በኢየሩሳሌም አንጻር ያሉትን ድል
ሲያደርጓቸው ታይተዋል ። ሮማውያን አይሁድን
ድል ለማድረጋቸው ምሳሌ ነው ።
አሜሃ ይበክዩ ኵሎሙ አሕዛበ ምድር ሶበ ይሬእይዎ
ለወልደ ዕጓለ ዕመሕያው እንዘ ይመጽእ በደመና
ሰማይ ።
በሰማይ ደመና ማለት በባሕርይ ክብሩ ሲመጣ
ባዩት ጊዜ ያን ጊዜ አሕዛብ ሁሉ ያዝናሉ ። ሐተታ
የዕርገት የደብረ ታቦር የምጽአት ደመና የባሕርይ
ክብር ነው ። አንድም በሥጋ ማርያም መጥቶ ባዩት
ጊዜ ፣ ሰማይ ዳግሚት እንዲል አንድም በክበበ
ትስብእት መጥቶ ባዩት ጊዜ ያዝናሉ ።
ምስለ ኃይል ።

ከኃይል ጋራ ማለት ዓለምን ከማሳለፍ ጋራ ።
ወስብሐት ብዙኅ ።
ቅዱስ እግዚአብሔር ዘያነቅሖሙ ለምውታን ተብሎ ከመመስገን ጋራ ሲመጣ ባዩት ጊዜ ።

፴፩ ወይፌንዎሙ ለመላእክቲሁ ምስለ ቃለ ቀርን ። ፩፡ቆሮ.፲፭ ፡ ፶፪ ። ፩፡ ተሰ ፡ ፬ ፡ ፲፮ ።

፴፪ ዐዋፎ ከመንገር ጋራ መላእክትን ያዛቸዋል ።
ወስብሐት ዓቢይ ።
ብርሃኑ መለኮቱን ገልጾ በመጣ ጊዜ ።
ወያስተጋብእዎሙ ለኅሩያኒሁ እምዐቅ ነፋሳት እም አጽናፈ ሰማይ እስከ አጽናፊሃ ።
ሙታንን ከራቱ ማዕዘን ይሰበስቧቸዋል ። ይመ ጽኡ ወያስተጋብእሙ ይፈኑዎሙ ወያስተጋብእዎሙ ይላል ።
፴፪ ቈጽለሰ በለስ አእምሩ እምሳሊሁ ፤
፴፪ ንገሩን በበለስ ዕወቁ ።
እምከመ ለምለመ አዕጹቂሁ ወሠረጸ ቈጽሉ ተአ ምሩ ከመ ቀርበ ማዕረር ።
በለስ ቅጠሉ የለመለመ ዓጽቅ ያወጣ እንደሆነ መከር እንደ ደረሰ ዕወቁ ። ሐተታ ፡ የጥጦስን በቅ ጠል የሐሳዊ መሲሕን በአበባ የምጽአትን በፍሬ መስሎ ይናገራል ። አንድም እንደ ቅጠሉ ሐሳዊ መሲሕ ነግሦላቸው ቤተ አይሁድ ደስ ብሏቸዋል። እንደ አበባው የምእመናን መከራቸው እንደ ፍሬው ሞታቸው ፡ አንድም እንደ ፍሬ ሞታቸው እንደ አበባ ክብራቸው ። አንድም ቆጽል አይለወጥም ። እንደ አበባው የአይሁድ መከራቸው እንደ ፍሬው ሞታቸው ፡ አንድም እንዳበባው ሞታቸው እንደ ፍሬው ፍዳቸው ።

፴፫ ከማሁ አንትሙኒ እምከመ ርኢክሙ ዘንተ ኵሎ አእምሩ ከመ ቀርበ ኀበ ኆኅት ።

፴፫ እናንተም ይህን ሁሉ ያያችሁ እንደሆነ እንደቀረበ ከደጅ እንዳለ ዕወቁ ከደጅ የቆመ ፈጥኖ እንዲገባ ፈጥኖ እንዲደረግ ዕወቁ ማለት ነው ።

፴፬ አማን እብለክሙ ከመ ኢተኃልፍ ዛቲ ትውልድ እስከዝ ኵሉ ይትገበር ።
፴፬ ይህ ሁሉ እስኪፈጸም ድረስ ቤተ አይሁድ አታልፍም ብየ እንዳታልፍ እነግራችኋለሁ ።
፴፭ ሰማይ ወምድር የኃልፍ ማር. ፲፫ ፡ ፴፩ ።
፴፭ ሰማይና ምድር ያልፋል ። ወቃልየሰ ኢየኃልፍ ።
ሕጌ ግን አያልፍም ። አንድም አለፍ ያልሁት ያልፋል አለፍ ያላልሁት አያልፍም ። አንድም ሕጌን የያዘ አያልፍም ሕጌን ያልያዘ ግን ያልፋል ።
ዘከመ ይደልዎ ተጊሀ ለክርስቲያን እስመ ኢየ አምር ሰዓተ ሞቱ ።

፴፮ ወበእንተሰ ይእቲ ዕለት ወይእቲ ሰዓት አልቦ ዘየአምራ ።

፴፮ ያችን ዕለት ያችን ሰዓት የሚያውቃት የለም ። ይእቲ ባለው ወኪያሃ ይላል አብነት ወይ እቲ ማለት ነው።ወሰምዓት ዮዲት በኪያሆን መዋ ዕል እንዲል ። ሐተታ ፡ ዘመኑ ዘመነ ዮሐንስ ወርኁ ወርኃ መጋቢት ዕለቱ ዕለተ እሑድ ሰዓቱ መንፈቀ ሌሊት አይደለም ቢሉ ብዙ ዘመነ ዮሐንስ ብዙ ወርኃ መጋቢት ብዙ ዕለተ እሑድ ብዙ መንፈቀ ሌሊት አለና ።
ኢመላእክተ ሰማይ ።
መላእክትም ሆነው ።
ወኢወልድ ።
ደቂቀ አዳምም ሁነው አያውቋትም ። ኦሪት ዘል ደት እንዲል ዘእንበለ አብ ባሕቲቱ ።
ክብቻው ከአብ በቀር አብ ብቻ ያውቃታል እንጂ ሐተታ ከፍጡራን ሲለየው ነው እንጂ ከወልድ ከመንፈስ ቅዱስ ሲለየው አይደለም ። አንድም ወልድ ቅድመ ተዋሕዶ የነበረ ዐላዋቂ ሥጋን እንደ ተዋሐደ ለማጠየቅ ። አኮ ኢያእሚሮ ኀቡእተ እላ ከመ የሀብ መካነ ለጥንተ ትስብእቱ ዘኢየአምር ኀቡእተ እንዲል ። አንድም አብ ለልጁ በመስጠት ዐውቋታል ፡ ወልድ ግን በሥራ ዐላወቃትም ሲል እንዲህ አለ ፡ አንድም ፡ ኢወልድ ባሕቲቱ ዘእንበለ አብ ፡ ወልድ ብቻ ያለ አብ አያውቃትም ።

፴፯ ወበከመ ኮነ በመዋዕሊሁ ለኖኅ ከማሁ ይከውን ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ዘፍ ፡ ፯፡ ፯ ሉቃ ፡ ፲፯ ፡ ፳፯ ።

፴፯ በኖኅ ዘመን እንደተደረገው የወልደ ዕጓለ እመሕያው የክርስቶስ ምጽአቱ እንዲህ ይደረጋል።

፴፰ እስመ በከመ ኮነ በመዋዕለ ኖኅ እምቅድመ ማየ አይህ ይበልዑ ወይሰትዩ ።

፴፰ ከማየ አይህ አስቀድሞ ሲበሉ ሲጠጡ ያወስቡ ወይትዋሰቡ ።
ሲያገቡ ሲጋቡ እንደነበረ ።
እስከ አመ ቦአ ኖኅ ውስተ ንፍቀ ታቦት ።
ንፍቀ ታቦተ ሲል ነው ስጠተ ልብሰ ጠፈረ ቤት እንዲል ስጡጠ ልብሰ ጥፉረ ቤተ ሲል ኖኅ ክፍል ክፍል ካለው መርከብ እስቲገባ ድረስ ።

፴፱ ወኢያእመሩ እስከ አመ መጽአ ማየ አይኅ ወአጥፍአ ኵሎ ፤
፴፱ የጥፋት ውኃም መጥቶ ሁሉን እስኪያ ጠፋ ድረስ እንዳላወቁ ከማሁ ይከውን ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

የክርስቶስ ምጽአቱ እንዲህ ነውና በኖኅ ጊዜ እንደ ተደረገ ይደረጋል ።

፵ አሜሃ ፪ቱ ይሄልዉ ውስተ ፩ዱ ገራኅት ።
፵ ያን ጊዜ ሁለት ሰዎች ባንድ እርሻ ይኖራሉ
፵፩ ፩ደ ይነሥኡ ።
፵፩ አንዱን በሞት ይወስዳሉ ።
ወካልዖ የኃድጉ ።
አንዱን በሕይወት ይተዋሉ ።
ወ፪ቲ የሐርፃ በ፩ዱ ማኅረፅ ሁለት ሴቶች ባንድ
ወፍጮ ይፈጫሉ ። ሐተታ ተራ አንድም ሽሮም
አንድም መቀበያውን አንድ አድርገው ።
አሐተ ይነሥኡ ።
አንዲቱን በሞት ይወስዳሉ ።
ወካልዕታ የኃድጉ ።
አንዲቱን ይተዋሉ ።
፪ቱ ይስክቡ ውስተ ፩ዱ አራት ባልና ሚስት ባንድ
አልጋ ይተኛሉ ።
፩ደ ይነሥኡ ።
አንዳቸውን በሞት ይወስዳሉ ።
ወካልዖ የኃድጉ ።

አንዳቸውን በሕይወት ይተዋሉ አንድም ፪ቱ ይሄልዉ ብለህ መልስ ለያርኅብ እግዚአብሔር ምድሮ ለያፌት እንዲል ። በያፌት ዕፃ ፪ ሰዎች ይኖራሉ ምግባር ሃይማኖት የያዘውን ይነሥኡ ወደ ገነት ። ምግባር ሃይማኖት ያልያዘውን የኅድጉ በገሃነም ። ወ፪ቱ ይስክቡ ውስተ ፩ዱ አራት ። ለይኅድር እግዚአብሔር ውስተ ቤቱ ለሴም እንዲል በሴም ዕፃ ፪ ሰዎች ይኖራሉ፤ምግባር ሃይማኖት የያዘውን ወደገነት ያልያዘውን ወደ ገሃነም ይተዋሉ ። አንድም ፪ቱ ይሄልው ብለህ መልስ ባሕታውያን በበረሃ ይኖራሉ እንደ እንጦንስ እንደ መቃርስ እንደ አቡነ ተክለሃይማኖት ያሉትን ይነሥኡ ወደ ገነት ። እንደ ሡናየ ዝክር እንደ በዓለ መቅጹት ያሉትን የኃድጉ በገሃነም ።
ወ፪ቲ የሐርጻ ።

ነዳያን በዚህ ዓለም ይኖራሉ እንደ አልዓዛር እንደ ሐዋርያት ያሉትን ወደገነት ። እንደ ይሁዳ እንደ አይሁድ ያሉትን በገሃነም ። ወ፪ቱ ይስክቡ ውስተ ፩ዱ አራት ፣ ባለጸጎች በዚህ ዓለም ይኖራሉ ፣ እንደ ኢዮብ እንደ አብርሃም ያሉትን ይነሥኡ ወደገነት፥ እንደ ነዌ እንደ ኪራም ያሉትን የኅድጉ በገሃነም።

፵፪ ትግሁ እንከ እስመ ኢተአምሩ በዓይ ሰዓት ይመጽእ እግዚአክሙ ማር ፡ ፲፫ ፡ ፴፫ ።
ሉቃ ፡ ፲፪ ፡ ፴፱

፵፪ ጌታችሁ በማናቸውም ሰዓት እንዲመጣ እታውቁምና ለትጉፋት ተግታችሁ ኑሩ ።
፵፫ ወዘንተ ባሕቱ አእምሩ ወኢትርስዑ ።
፵፫ ባሕቱ ዋዌ ነው ይህንም ዕወቁ ሰበሁ የእምር በዓለ ቤት ጊዜ ይመጽእ ሠራቂ እምተግሀ ወእምሀለወ ።

ባለቤት ሌባ የሚመጣበትን ጊዜ ቢያውቅ ተግቶ በጠበቀ ነበር ።
ወእምኢኃደገ ይክርዩ ቤቶ ።
ግድግዳውን ምሰው ናሱን አፍርሰው ይሰርቁት ዘንድ ቸል ባላለም ነበር ።

፵፬ ወበእንተዝ እንትሙኒ ድልዋኒክሙ ሀልዉ እስመ በጊዜ ኢተኃዘብክሙ ይመጽእ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፵፬ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ባልጠረጠራችሁት ዕለት ባላወቃችሁት ሰዓት ይመጣልና እንደዚህ እናንተም ተዘጋጅታችሁ ኑሩ ።

፵፭ መኑ እንጋ ውእቱ ገብር ምእመን ጠቢብ ዘይሠይሞ እግዚኡ ውስተ ኵሉ ቤቱ ።

፵፭ ቅዱስ ጴጥሮስ ለነሁ ትሜህረነ ወሚመ ለኵሉ ብሎታል በሉቃስ ፣ ምን እናንተን ብቻ እና ንተን ለመሰለ ሁሉ ነው እንጂ ብሎ አያይዞ በዚያ ውስ ላይ ጌታው አምኖ የሚሾመው ብልህ በጐባሪያ ማነው ።
ከመ የሀቦሙ ሲሳዮሙ በበጊዜሁ ።
በየጊዜው ምግባቸውን ይሰጣቸው ዘንድ የዕለት የሳምንት የወር ያመት ምግቡን የሚቀበል አለና፤

፵፮ ብፁዕ ውእቱ ገብር ዘመጺኦ እግዚኡ ይረክቦ እንዘ ከመዝ ይገብር ። ራዕ ፡ ፲፮ ፡ ፲፭ ።

፵፮ ጌታው በመጣ ጊዜ እንዲህ ሲያደርግ ማለት ምግባቸውን ሲሰጣቸው የሚያገኘው ባሪያን ዑድ ክቡር ነው ።

፵፯ አማን እብለክሙ ከመ ዲበ ኵሉ ጥሪቱ ይሠይሞ ።

፵፯ በገንዘቡ ሁሉ ይሾመዋል ብየ እንዲሾመው በውነት እነግራችኋለሁ ።

፵፰ ወእመሰ ይቤ ውእቱ ገብር እኩይ ይጐነዲ እቲወ እግዚእየ ።

፵፰ ያ ክፉ ባሪያ ግንጌታዬ የሚመጣበት ጊዜ ገና ነው ብሎ ።
፵፱ ወይዘብጥ አብያጺሁ አግብርተ ይበልዕ ወይስቲ ምስለ ሰካርያን ።
፵፱ የጌታውን ባሮች ባልንጀሮቹን ቢመታ ማለት በበትረ ረኃብ ቢመቱ ካዝማሪ ከዘዋሪ ጋራ እየበላ እየጠጣ ምግባቸውን አልሰጥም ቢል ።
፶ ወይመጽእ እግዚኡ ለውእቱ ገብር በዕለተ ኢተሀዘበ ወበጊዜ ኢያእመረ ወይሠጥቆ እማእከሉ
፶ ባላወቀው ዕለት ባልጠረጠረው ሰዓት መጥቶ ጌታው ከሹመቱ ይሽረዋል ።
፶፩ ወይሬሲ መክፈልቶ ምስለ መደልዋን ኀበ ሀሎ ብካይ ወሐቅየ ስነን ። ማቴ ፡ ፲፫ ፡ ፵፪፡፳፭፡፴።

፶፩ ዕድል ፈንታውን ጽዋ ተራውንም ልቅሶ ጥርስ ቁርጥማት ካለበት ቦታ ከግብዞች ጋራ ያደርግ በታል ። አንድም መኑ ውእቱ ብለህ መልስ ። ጌታው እምኖ በነዳያን ላይ የሚሾመው ባለጸጋ ማነው ጌታ ለሰው ብዕል መስጠቱ ለነዳያን መሾሙ ነውና ከመ የሀቦሙ ስጠን ባሉት ጊዜ ለነዳያን ሲሰጣቸው ። ብፁዕ ውእቱ ጌታው በመጣ ጊዜ ለነዳያን ምግባቸ ውን ሲሰጣቸው የሚገኝ ባለጸጋ ንዑድ ክቡር ነው ። አማን እብለክሙ በወዲያውም ዓለም ብዕል ይሾ መዋል ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ። ወእመሰ ይቤ ያ ክፉ ባለጸጋ ግን የምሞትበት ጊዜ ገና ነው ብሎ ከዘማሪ ከዘዋሪ ጋራ እየበላ እየጠጣ ነዳያን በበትረ ረኃብ ሲሞቱ አልሰጥም ቢል ዘሰ ይዳደቅ በእናቅጽ ውእቱኬ ያመነድብ ነፍሳተ እንዲል ወይመጽእ እግዚኡ ፡ ባልጠረጠረው ዕለት ባላወቀው ሰዓት ጌታው መጥቶ በማእከለ ዘመኑ ነፍሱን ከሥጋው ይለያታል እድል ፈንታውን ጽዋ ተራውን ከኃጥአን ጋራ ጽኑዕ ሥቃይ ባለበት ቦታ በገሃነም ያደርግበ ታል ። አንድም መኑ ውእቱ ብለህ መልስ ፡ ጌታው እምኖ በምእመናን የሚሾመው ቄስ መምር ማነው ። ከመ የሀቦሙ ሲሳዮሙ ፡ ያስተምራቸው ዘንድ ንስ ሐን ሥጋውን ደሙን ይሰጣቸው ዘንድ ። ብፁዕ ውእቱ ጌታው በመጣ ጊዜ ሲያስተምራቸው የሚ ገኝ መምህር ንስሐን ሥጋውን ደሙን ሊሰጣቸው የሚገኝ ቄስ ንዑድ ክቡር ነው ። አማን ዕብለክሙ በወዲያው ዓለም ምሥጢር ክብር ይሾመዋል ብዬ እንዲሾመው በውነት እነግራችኋለሁ ። ወእመሰ ይቤ ውእቱ ገብር እኩይ ። ያ ክፉ መምር ቄስ ግን የምሞትበት ጊዜ ገና ነው ብሎ ። ወይዘብጥ አብያ ጺሁ ምእመናን በበትረ ክህደት ሲሞቱ አላስተ ምርም ቢል በበትረ ኃጢአት ሲሞቱ ንስሐን ሥጋ ውን ደሙን አልሰጥም ቢል ። ኢትዘበጥ አንተ ከመ ኢይላሁ አነ ዛቲ ምጽንጋዕ ምዕረ ትዘብጠከ ወምዕረ ትዘብጠኒ እንዲል። ወይመጽእ እግዚኡ።ባላወቀው ዕለት ባልጠረጠረው ሰዓት ጌታው መጥቶ ነፍሱን ከሥጋው ይለያታል ። ወይሬሲ መክፈልቶ ፡ እድል ፈንታውን ጽዋ ተራውንም ከኃጥአን ጋራ ጽኑ ሥቃይ ባለበት በገሃነም ያደርግበታል ።

በእንተ ደናግል ጠባባት ወአብዳት ።

ምዕራፍ ፳፭ ።

፩ አሜሃ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ዐሥ ሮን ደናግለ እለ ነሥአ መኃትዊሆን ወወፅአ ውስተ ቀበላ መርዓዊ ።

፩ አብነት አሜሃ ይእተ አሚረ ይላል ያን ጊዜ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ። ሕገ ወንጌል ተስፋ ተስፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ፋና ይዘው ዐሥሩ ደናግል ሊቀበሉት የወጡ ሙሽራን ትመስላለች ። አንድም መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ትመስል መኃትወ መርዓዊን ሲቀበሉ ፲ ደናግል ይዘውት የወጡ ፋናን ትመስላለች ። አንድም መንግሥተ ሰማይ ምእመናን ትመስል ዐሥሮን ደናግለ ። ሙሽራውን ለመቀበል ፋና ይዘው የወጡ ደናግልን ትመስላለች ሐተታ ደናግል አላቸው ምእመናንን ፡ ድንግል ባባት በናቷ ቤት ሳለች ኋላ ከባሏ ጋራ አንድ የምትሆንበትን ሥራ ስትማር እንድታድግ ምእመናንም በዚህ ዓለም ሳሉ ኋላ ከክርስቶስ ጋራ አንድ የሚሆኑበትን ሥራ ሲሠሩ ይኖራሉ።አንድም በተፈጥሮ ደናግል ናቸውና አንድም ድንግልና ሥጋ አላቸውና ይህስ ለሁሉ አይቻልም ብሎ ድንግልና ነፍስ አላቸውና ።

፪ ወኃምስ እምኔሆን አብዳት አማንቱ ።

፪ ካሥሩ አምስቱ ሰነፎች ናቸው ወኃምስ ጠባባት ።
አምስቱ ልባሞች ናቸው ።

፫ ወዓብዳትሰ ነሢኦን መኃትዊሆን ኢነሥአ ቅብዓ ምስሌሆን ።

፫ ሰነፎች ፋና ይዘው በማሰሮቻቸዉ ዘይት አልያዙም ።

፬ ወጠባባትሰ ነሥአ ቅብዓ ምስለ መኃትዊ ሆን በንማዕዊሆን ።

፬ ልባሞች ግን ከፋናቸው ጋራ በማሰሮቻቸው ዘይት ይዘዋል ሐተታ፤ ዓብዳት የሚላቸው ሃይማኖት ጾም ጸሎት ትሕትና ኃፈረ ገጽን ይዘው ፮ኛ በል ቡናቸው ፍቅርን ያልያዙ ናቸው።ኃፈረና ገጽና ትሕ ትናስ አንድ ወገን ናቸው ብሎ ሃይማኖት ጾም ጸሎት ትሕትና ኃፈረ ገጽ አንድ ወገን ንጽሕናን ይዘው ፮ኛ በልቡናቸው ፍቅርን ያልያዙ ናቸው ። ጠባባት የሚላቸው አምስቱን ይዘው ስድስተኛ በልቡናቸው ፍቅርን የያዙ ናቸው ። ቅብዕ ኢይርኅቅ ቅብዕሰ ፍቅረ ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው እንዲል ። አምስቱን ይዛችሁ ስድስተኛ በልቡናችሁ ፍቅርን ካልያዛችሁ አይሆንም ይሏቸዋል ከነግህ ከሠለስትእንይዛለን ሲሉ ሞት ይመጣባቸዋል ። እኒያ አለመጠቀማቸውን እነዚህ መጠቀማቸውን መናገር ነው ።

፭ ወጐንድዮ መርዓዊ ደቀሳ ኵሎን ወኖማ ።
፭ ሙሽራው በዘገየ ጊዜ ዓብዳትም ጠባባ ትም ተኙ ።
፮ ወከዊኖ መንፈቀ ሌሊት ውውዓ ኮነ ናሁ መርዓዊ መጽአየሁ ተቀበሉ ።
፮ መንፈቀ ሌሊት ሲሆን ሙሽራው መጥቷ ልና ወጥታችሁ ተቀበሉ ተብሎ ተነገረ ። ሐተታ ፡ በሀገራቸው ሙሽራ የሚመጣ በመንፈቀ ሌሊት ነውና ።
፯ ወእምዝ ነቅሐ እልኩ ደናግል ኵሎን ወአ ሠነያ መኃትዊሆን ወወፅአ ውስተ ቀበላ መርዓዊ
፯ ከዚህ በኋላ ልባሞች ተነሥተው ፋናቸውን አዘጋጅተው ሙሽራውን ሊቀበሉ ወጡ ።

፰ ወእልኩ ዓብዳት ይቤላሆን ለጠባባት ሀባነ ቅብዓ እምቅብዕክን ።

፰ ሰነፎች ልባሞችን ከዘይታችሁ ዘይት ስጡን አሏቸው ።
እስመ መኅትዊነ ጠፍአነ ፤ ዘይት አልቆብናልና ።

፱ ወአውሥአሆን ጠባባት እንዘ ይብላ አልቦ ዘየአክል ለነ ወለክን ።

፱ ልባሞች ለኛና ለናንተ የሚበቃ ዘይት አል ያዝንምና ፡ አላ ሑራ ወተሣየጣ ለከን እምኀበ እለ ይሠይጡ ።

፲ ሄዳችሁ ዘይት ከሚሸጡ ግዙ እንጂ አሏቸው ወሐዊሮን ይሣየጣ በጽሐ መርዓዊ ።
፲ ለጊዜው ሂደው ሳሉ ሙሽራው መጣ ።
ወቦአ ምስሌሁ እልኩ እለ ድልዋት ውስተ ከብካብ ። የተዘጋጁ ከሱ ጋራ እንደሱ ወደሰርግ ገቡ ።
ወተዐፅወ ኆኅት ፤ ደጅ ተዘጋ ፤
፲፩ ወድኅረ መጽአ እልኩሂ ደናግል ወይ ቤላ እግዚኦ እግዚኦ አርኅወነ ።
፲፩ እነዚያ ከገቡ ደጅ ከተዘጋ በኋላ ሰነፎች መጥተው ክፈትልን ማለት እንድንገባ አድርገን አሉት ።
፲፪ ወአውሥኦን ፤ መለሰላቸው ወይቤሎን አማን እብለክን ከመ ኢየአምረክን ።
፲፪ ዐላውቃችሁም ብየ እንዳላውቃችሁ በውነት እነግራችኋለሁ እስመ ስእንክን ተጊሃ ወእምስዮ አሐተ ሰዓተ ምስሌየ ። ተግታችሁ ሥራ አልሠራ ችሁም ከኔ ጋራ አንዲት ሰዓት መቆ ምመቆየት አል ተቻላችሁምና ።
፲፫ ትግሁኬ እስመ ኢተአምሩ ዕለታ ወሰዓታ እንተ ባቲ ይመጽእ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ማር. ፲፫ ፡ ፴፫ ።
፲፫ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ የሚመጣበትን ዕለት ሰዓት አታውቁምና ለትሩፋት ተግታችሁ ኑሩ ። አንድም ወኮንድዮ መርዓዊ ብለህ መልስ ምጽአት በዘገየ ጊዜ ምእመናን ሁሉ መሞታቸውን መናገር ነው ። ወከዊና መንፈቀ ሌሊት በማእከለ ዘመን መርዓዊ ክርስቶስ መጥቷልና ለተዋሕዶ የሚ ያበቃ ሥራ ሥሩ ተብሎ ተነገረ ። ሐተታ ያልተካ ከለ መንፈቅ ነው ወንፍቃ ለሌሊት ወመንፈቆሙ ናፈቁ እንዲል ። ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ እስከ ዕለተ ምጽአት ያለውን አንድ ወገን ፡ ከምጽአት በኋላ ያለውን አንድ ወገን አድርጎ መንፈቅ አለ ። አንድም የተካከለ መንፈቅ ነው ዓለም ሳይፈጠር ያለውንና ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ያለውን አንድ ወገን ከም ጽአት በኋላ ያለውን አንድ ወገን አድርጎ ተናገረ የዚያ ጥንቱ እንዳይታወቅ የዚህም ፍጻሜው አይታ ወቅምና ፡ የቍጥር መጽሐፍ ክፍል ዳግም መንፈቅ ይላል ተአምረ ኢየሱስ ወበ፮ ሰዓተ ሌሊት ተንሥአ እግዚእ ኢየሱስ ይላልሳ ቢሉ ሦስት ሰዓት አሳልፎ ነው መከራ መቀበል የጀመረ ፡ ከዚያ ተነሥቶ ቈጥሮ ፮ አለ እንጂ ፡ ልደቱም ጥምቀቱም ትንሣኤ ውም ምጽአቱም ባሥረኛው ሰዓት ነው ። ወእምዝ ተንሥኣ ለተዋሕዶ የሚያበቃ ሠርተው ሀባነ ቅብዓ ከሥራችሁ አትርፉልን እስመ መኅትዊነ ጠፍአነ ለተዋሕዶ የሚያበቃ ሥራ አልሠራንምና ማለት ባንዱ ሥራ እንዱ የሚጠቀም እንደመሰላቸው መና ገር ነው ፡ ወአውሥኣሆን እንዘ ይብላ አልቦ ዘየአ ክል ለነ ወለክን ፡ ለኛና ለናንተ የሚያበቃ ሥራ የለ ንም አሏቸው ማለት ፡ ባንዱ ሥራ እንዱ እንዳይጠ ቀም ማወቃቸውን መናገር ነው ፡ አላ ሑራ ፡ ምሕ ረትን ከሚያድሉ ክሥላሴ ምሕረትን ከሚያሰጡ ከነዳያን ለምኑ እንጂ አሏቸው ፤ ወሐዊሮን ይሣ የጣ ፡ ነግ ሠልስት ሥራ እንሠራለን ሲሉ ምጽአት ደረሰ ። ወቦአ ምስሌሁ ፡ ሥራ ሠርተው የተገኙት ቈዋሐዱት ተዋሐዷቸው ። ወተዐፅወ ኆኅት ምሕረት ተከለከለ ፡ ወድኅረ መጽአ ወይቤላ አርኅወነ የሚ ገቡ እንደመሰላቸው መናገር ነው ወአውሥኦን አላው ቃችሁም ብየ እንዳላውቃችሁ በውነት እነግራችኋ ለሁ ፡ ፈጥሮስ ዐላውቃችሁም ማለት አይመችም ብሎ ወለድኋችሁ ካድኋችሁ አላቸዋለሁ ። እስመ ስእ ንክን ተጊሃ ፡ ለተዋሕዶ የሚያበቃ ሥራ አልሠራ ችሁምና ትግሁኬ እንዳለፈው ፡ ሐተታ ዓብዳት የሚላ ቸው ሃይማኖት እንበለ ምግባር ንጽሐ ሥጋ እንበለ ንጽሐ ነፍስ ፍቅር እንበለ ተስፋ ምሕረት እንበለ ትዕግሥት ጸሎት ዘምስለ ትምክህት የያዙ ናቸው ። ጠባባት የሚላቸው ሃይማኖት ዘምስለ ምግባር ንጽሐ ሥጋ ዘምስለ ንጽሐ ነፍስ ፡ ምሕረት ዘምስለ ትዕግ ሥት ፍቅር ዘምስለ ተስፋ ጸሎት እንበለ ትምክህት የያዙ ናቸው ይህን ይዛችሁ ይህን ካልያዛችሁ አይ ሆንም ይሏቸዋል ። ከነግ ከሠልስት እንይዛለን ሲሉ ሞት ይመጣባቸዋል እኒህ መጠቀማቸውን እኒያ አለመጠቀማቸውን መናገር ነው ። አንድም ዓብዳት የሚላቸው አእምሮ ለብዎ ለሚዕ ምሕረት ትዕግሥት እኒህን ኃምስቱን ይዘው አሚን ተስፋ ፍሥሐ ሰላም ፍቅርን ያልያዙ ናቸው ጠባባት የሚላቸው ዓሥሩ ንም የያዙ ናቸው ይኸን ይዛችሁ ይኸን ካልያዛ ችሁ አይሆንም ይሏቸዋል ። ከነግ ከሠልስት እንይዛለን ሲ ሉ ሞት ይመጣባቸዋል እኒህ መጠቀማቸውን እኒያ አለመጠቀማቸውን መና ገር ነው ። አንድም ዓብዳት የሚላቸው አይሁድ ተንባላት ናቸው ፡ ጠባባት የሚላቸው ክርስቲ ያን ናቸው ካላመናችሁ ካልተጠመቃችሁ አይሆንም ይሏቸዋል ከነግ ከሠልስት እንጠመቃለን ሲሉ ሞት ይመጣባቸዋል እኒህ መጠቀማቸውን እኒያ አለመጠ ቀማቸውን መናገር ነው ።
አንድም ዓብዳት የሚላቸው አምነው ተጠምቀው የክርስቲያን ሥራ የማይሠሩ ናቸው ጠባባት የሚላ

ቸው አምነው ተጠምቀው ሥራ የሚሠሩ ናቸው
አምናችሁ ተጠምቃችሁ ሥራ ካልሠራችሁ አይሆ
ንም ይሏቸዋል ከንግ ከሠልስት እንሠራለን ሲሉ
ዋት ይመጣባቸዋል እኒህ መጠቀማቸውን እኒያ
አለመጠቀማቸውን መናገር ነው ።

በእንተ ምሳሌ ዘመካልይ ።

፲፬ እስመ ከመ ብእሲ ዘይነግድ ወጸውዓ አግ
ብርቲሁ ወመጠዎሙ ንዋዮ ይትገበሩ በቱ፣ ሉቃ ፲፱
፲፪ ።

፲፬ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ፡ ሕገ ወን
ጌል ተሰፋ ተሰፋ ኢየሱስ ክርስቶስ ብላቴኖችን ጠርቶ
ወጥተው ወርደው ያተርፉበት ዘንድ ገንዘቡን የሰ
ጣቸውን ነጋዴን ትመስላለችና ትገሁ ፡ እንድም
ትመስላለችኮን ።

፲፭ ፡ ወለ ዘወሀበ ኀምስተ መክሊተ ።
፲፭ አምስት መክሊትን ለሰጠው ሰው አም
ስት መክሊት አለው አምስት መክሊትን ለሰጠው
ሰው ስጦታ አለው ለሰጠው አምስት መክሊት አለው
አምሰት መክሊት የሰጠው ሰው አለ ።
ወለ ለዘወሀበ ፪ተ መክሊተ ። ሁለት መክሊት
የሰጠው ሰው አለ እንዳለፈው በል ።
ወለ ለዘወሀበ አሐደ መክሊተ ፡ አንድ መክሊት የሰ
ጠው ሰው አለ ።
ወለለ፩ዱ እምኔሆሙ በአምጣነ ይከሉ ።
ከሳቸው ወገን ላንዱም ላንዱ እንደሚቻላቸው መጠን
ወነገደ በጊዜሃ ። ሰጥቷቸው ሄደ ፤
፲፮ ወሖረ ዝኩ ዘኀምስ መክሊተ ነሥአ ወተ
ገበረ ቦቱ ፤
፲፮ አምስት መክሊት የተቀበለው ወጥቶ ወርዶ
አተረፈ ፤ ወረብኃ ካልዓተ ፭ተ መካልየ ፤ አምስት
አተረፈ ዐሥር አደረገ ።
፲፯ ወከማሁ ዘሂ ፪ተ መካልየ ረብኃ ካልዓተ
መካልየ ።
፲፯ እንደዚሁ ሁሉ ሁለት መክሊት የተቀበለ
ውም ወጥቶ ወርዶ አተረፈ አራት አደረገ ።
፲፰ ወዘአሐደሰ መክሊተ ነሥአ ሖረ ወኃ
ለፈ ወከረየ ምድረ ወኃብአ ወርቀ እግዚኡ ።
፲፰ አንድ መክሊት የተቀበለው ግን ሌባ ቢሰ
ርቀኝ ወንበዴ ቢቀማኝ ቀማፊ ቢያታልለኝ ብሎ
ፈርቶ ሄዶ ምድር ቆፍሮ የጌታውን ወርቅ ቀበረ ።
፲፱ ወእምድኅረ ብዙኅ መዋዕል አተወ እግዚ
እሙ ለእሉ አግብርት ።
፲፱ ከብዙ ዘመን በኋላ የነዚያ የባሮች ጌታቸው
መጣ ፤ ወአኀዘ ይትሐሰቦሙ ፤ ተቈጣጠራቸው ።
፳ ወቀርበ ዘኀምስ መካልየ ነሥአ
፳ ወአምጽአ ካልዓተ ኃምሰ መካልየ ።
፳ አምስት መክሊት የተቀበለው ወጥቶ
ወርዶ ያተረፈውን አምስቱን ደርቦ አመጣ ።

እንዘ ይብል እግዚኦ ኃምሰ መካልየ ወሀብከኒ ።
አቤቱ አምስት መክሊት ሰጥተኸኝ ነበር ። አንድም
ዘወሀብከኒ የሰጠኸኝ አምስት መክሊት ነበር አኮሁ
ኃምሰ መካልየ ወሀብከኒ አምስት መክሊት ሰጥተ
ኸኝ አልነበረምን ፡ አንድም ዘወሀብከኒ የሰጠኸኝ
አምስት አልነበረምን ።
ወናሁ ኃምሰ መካልይ ዘረባሕኩ ዲቤሆን ።
እነሆ ወጥቼ ወርጄ አምስት አትርፌአለሁ ዐሥር
አድርጌአለሁ አለው ።

፳፩ ወይቤሎ እግዚኡ አ ገብር ኄር ወምእመን
ዘበኀዳጥ ምእመነ ኮንከ ዲበ ብዙኅ እሰይመከ ።

፳፩ አንተ በጐ ባሪያ በጥቂቱ ከታመንክ በብ
ዙው እሾምሃለሁ ።
ባእ ውስተ ፍሥሐሁ ለእግዚእከ ።
ጌታህ ተድላ ከሚያደርግበት ግባ ማለት ተሾም
ተሸለም አለው ።

፳፪ ወመጽአ ዘ፪ተ መክሊተ ነሥአ ።
፳፪ ሁለት መክሊት የተቀበለውም መጣ ።
ወይቤ እግዚኦ አኮሁ ፪ተ መካልየ ወሀብከኒ ።
አቤቱ ሁለት መክሊት ሰጥተኸኝ አልነበረምን ።
ወናሁ ፪ተ ካልዓተ መካልየ ረባሕኩ ።
እነሆ ወጥቼ ወርጄ ሁለት አተረፍኩ አራት አደረግሁ
አለው ።

፳፫ ወይቤሎ እግዚኡ አ ገብር ኄር ወምእመን
ዘበውኁድ ምእመነ ኮንከ ዲበ ብዙኅ እሠይመከ
ባእ ውስተ ፍሥሐሁ ለእግዚእከ ።

፳፫ አንተ በጐ ባሪያ በጥቂቱ ከታመንክ በብዙ
ወገን እሾምሃለሁ ጌታህ ተድላ ከሚያደርግበት ግባ
ማለት ተሾም ተሸለም አለው ።

፳፬ ወመጽአ ዘሂ ዘ፩ኒ መክሊተ ነሥአ ።
፳፬ አንድ መክሊት የተቀበለውም መጣ ።
ወይቤ እግዚኦ አእምረከ ከመ ብእሲ ድሩክ አንተ
ተአርር ዘኢዘራእከ ወታስተጋብእ ዘኢዘረውከ ።
አቤቱ ያልዘራኸውን የምታጭድ ያልበተንኸውን
የምትሰበስብ ትነሥእ ዘኢያንበርከ ይላል በሉቃስ
ያላኖርኸውን የምታነሣ ጽኑ ጨካኝ መሆንክን እው
ቃለሁና ።
፳፭ ወፈሪሃየ ሖርኩ ወከረይኩ ምድረ ወኀ
ፈንኩ መክሊተከ ውስተ ምድር ።
፳፭ ሌባ ቢሰርቀኝ ወምበዴ ቢቀማኝ ቀማፊ
ቢያታልለኝ ብየ ፈርቼ ምድር ቆፍሬ ቀብሬ አኑሬ
አለሁ ። ጠብለልክዋ ውስተ ሰበንየ ይላል በሉቃስ
በመጠምጠሚያየ ቋጥሬ ይዠለሁ ። ናሁ ንግእ
ንዋየከ ።
እነሆ ገንዘብህን ተቀበለኝ አለው ።
፳፮ ወአውሥአ እግዚኡ ።
ጌታው መለሰ ።

ወይቤሎ ኦ እኩይ ገብር ወሀካይ ተአምረኒኑ ከመ ብእሲ ድሩክ አነ አዓርር ዘኢዘራዕኩ ወአስተጋብእ ዘኢዘረውኩ ።

፳፯ ያልዘራሁትን የማጭድ ያልበተንሁትን የምሰበስብ ጽኑ ጨካኝ መሆኔን ታውቃለህን ።

፳፯ ወእምደለወከ ትገብእ ወርቅየ ውስተ ማዕድዮ ።

፳፯ ይኸን ካወቅህ ገንዘቤን ልትሰጠኝ የተገባህ ነበር ።
ወመጺእየ አነ ለልየ እምአስተገበርክዎ በርዱ ።
ወጥቶ ወርዶ ለሚያተርፍልኝ በሰጠሁት ነበር ።
አንድም እኔ ወጥቼ ወርጄ ባተረፍኩበት ነበር ።

፳፰ ወይቤሎሙ ለእለ ይቀውሙ ህየ ንሥኡ እምኔሁ ዘንተ መክሊተ ወሀብዎ ለዘቦ ፲ቱ መክሊት ማቴ.፲፫ ፣ ፲፪ ማር.፬ ፣ ፳፭ ሉቃ ፰ ፣ ፲፰ ፲፱ ፣ ፳፯
፳፰ ይህን መክሊት ከሱ ተቀብላችሁ ዐሥር መክሊት ላለው ስጡት ።
፳፱ እስመ ለዘቦ ይሁብዎ ።
፳፱ ላለው ይሰጡታልና ማለት አምስት ላለው አምስት ይሰጡታልና ።
ወይዌስክዎ ።
ይደርቡለታል እለ አንዱን ።
ወለዘሰ አልቦ ዘሂ ቦ የሀይድዎ ።
የሌለውን ግን ያኑ ያለውን ቅሉ ይወስዱበታልና ንሥኡ ፤

፴ ወለገብርሰ እኩይ ወሀካይ አውፅእዎ እፍአ ወደይዎ ውስተ ጽልመት ጸናፊ ኃበ ሀሎ ብካይ ወሐቅየ ስነን ።

፴ ያን ሐኬተኛ ባሪያ ግን ልቅሶ ጥርስ ቍርጥማት ወዳለበት ወደ ጽኑ ጨለማ አግዙት አለ ። አንድም ቦ ለዘወሀቦ ፳ተ መክሊተ ብለህ መልስ ። ባለ ፳ የተባለ ፍጹም ትምህርት ተምሮ መክሮ አስተምሮ ራሱን አስመስሎ ያወጣ ነው ። ባለ ሁለት የተባለ ፍጹም ትምህርት ተምሮ መክሮ አስተምሮ ራሱን አስመስሎ ያወጣ ነው ፥ ቅዱስ ጴጥሮስ ቀሌምንጦስን ጳውሎስ ጢሞቴዎስን እንዳወጡ ባሳንድ የተባለ ተምሮ ሳያስተምር የቀረ ነው ።
ወሖረ ዝኩ ዘኃምስ መክሊተ ነሥአ ፥ ፍጹም ትምህርት የተማረው ወጥቶ ወርዶ መክሮ አስተምሮ ራሱን አስመስሎ አወጣ ። ወዘ፩ሰ መክሊተ ነሥአ ባለ አንድ ዓሳውያን እሳት ስለት አሳይተው ቢያስክዱኝ መናፍቃን ተከራክረው ምላሽ ቢያሳጡኝ ብሎ ፈርቶ ሃይማኖቱን በልቡ የያዘ ፥ ወይቤሎ አአምረከ ከመ ብእሲ ድሩክ አንተ ። ሕግ ሳትሠራ በአእምሮ ጠባይዕ ዐውቃችሁ መምር ሳትሰጥ በሰነ ፍጥረት ተመራምራችሁ በሠራችሁ ብለህ የምትፈርድ ጽኑ ጨካኝ መሆንህን አውቃለሁና አሳውያን እሳት ስለት አሳይተው ቢያስክዱኝ መናፍቃን ተከራክረው ምላሽ ቢያሳጡኝ ብየ ፈርቼ ደፈንኩ ውስተ ምድር በልቡናዬ ይዠዋለሁ ። ጠብለልከዋ ውስተ ሰበንየ ባለው በአእምሮዬ ጠብቄአለሁ አለ ገብር ሐካይ ተአምረኒኑ ። ሕግ ሳልሠራ በአእምሮ ጠባይዕ ዐውቃችሁ መምህር ሳልሰጥ በሥነ ፍጥረት ተመራምራችሁ በሠራችሁ ብየ የምፈርድ ጽኑ ጨካኝ መሆኔን ታውቃለህን ፥ ወእምደለወከ አንዲህስ ካወቅህ ሹመትከን ልታበረክተኝ ይገባኝ ነበር ። ለልየ እምአስተገበርክዎ ። ወጥቶ ወርዶ ለሚያስተምር በሰጠሁት ነበር ። አንድም ከሁለት ከሦስት ጆሮ ባደረሰከው እኔ ተራድቼ ባስፋፋሁት ነበር ፥ ንሥኡ እምኔሁ የሱን መምህርነት ነሥታችሁ ለዚያ ደርቡለት ። ወለገብርሰ እኩይ አውፅእዎ ፤ እሱን ግን አውጡት አለ ። ከመንግሥተ ሰማይ አይወጣም በመሀርነት መግባት ቢቀርበት በሕዝባዊነት ይገባል ። ታሪክ ይህም ባባ መልክአ ክርስቶስ ታውቋል ፍጹም ትምህርት ሳያስተምሩ ቀርተዋል በተባሕትዎ ፈጽመውታል በሚሞቱበት ጊዜ መልአክ ገሠጻቸው ቀለሙ አካል እየገዛ ሲወጣ ታይቷል ። አንድም ባሳምስት ሙሴ ነው አምስቱ መጻሕፍት አሉትና ፤ ባለ ሁለት ቅዱስ ጴጥሮስ እንዲህ ግን ስለሆነ ቅዱስ ጴጥሮስ ይበልጣል ሁለት የተባሉ ብሉይና ሐዲስ ናቸውና ፥ ባሳንድ ይሁዳ አውፅእዎ አሁን የተመቸ ፥ አንድም ባላምስት ሊቀ ጳጳሳት እንብሮተ እድ ሳዕለ ጳጳስ ፤ ሠይመ ቀቢስ ሠይመ ዲያቆን ማጥመቅ ማቍረብ ባለሁለት ቄስ ማጥመቅ ማቍረብ ባሳንድ ዲያቆን ተልእኮ ፥ አንድም ባላምስት እሚን ፍሥሐ ምሕረት ትዕግሥት ተስፋ ባለሁለት እሚን ፍሥሐ ባሳንድ እሚን አንድም ባላምስት ጥምቀት ተአምኖ ኃጢአት ከዊነ ሰማዕት ተባሕትዎ ምንኩስና ፤ ባለሁለት ጥምቀት ተአምኖ ኃጢአት ፥ ባላንድ ጥምቀት ። አንድም ባላምስት ፍጹም ባለጸጋ ፤ ባስሁለት እንደመጠኑ ባለጸጋ ፤ ባላንድ ፍጹም ድኃ ።

በእንተ ኅልቀተ ዓለም ።

፴፩ ወአመ ይመጽእ ወልደ ዕጓለ እመሕያው በስብሐቲሁ ወኵሎሙ መላእክቲሁ ቅዱሳን ምስሌሁ ።

የቀደሙ መምህራን ትመስልን ለምእመናን መክሊትን ለመምህራን ፥ ወአመ ይመጽእን ለባለጸጎች ሰጥተው ይተረጕሙ ነበር ። ዛሬ ሁሉም በሁሉ አሉ ብሎ ትመስልን ለምእመናን ለመምህራን ለባለጸጎች መክሊትን ለምእመናን ለመምህራን ለባለጸጎች ወአመ ይመጽእን ለምእመናን ለመምህራን ለባለጸጎች ሰጥተው ይተረጕማሉ ።

፴፩ ወልደ ዕጓለ እመሕያው መላእክትን አስከትሎ በጌትነት በመጣ ጊዜ ።

አሜሃ ይነብር ዲበ መንበረ ስብሐቲሁ ። በሚመሰገን ዙፋን ማለት በጌትነት ይገኛል ።

፴፪ ወይትጋበኡ ኀቤሁ አሕዛብ ቅድሜሁ ።

፴፪ ሙታን ሁሉ ከሱ ዘንድ ይሰበሰባሉ ።
ወይፈልጦሙ ዘዘዚአሆሙ ።
እየራስ እየራሳቸው ይለያቸዋል ።
ከመ እንተ ይፈልጥ ኖላዊ አባግዐ እምአጣሊ ። እረኛ በጎችን ከፍየሎች እንዲለይ ጻድቃንን ከኃጥአን ይለያቸዋል ።

፴፫ ወያቀውም አባግዐ በየማኑ ።

፴፫ ጻድቃንን በቀኙ ያቆማቸዋል ።
ወአጣሌ በጸጋሙ ።
ኃጥአንንም በግራው ያቆማቸዋል ። ሐተታ ጻድቃንን አባግዕ አላቸው በግ ትሑት ነው ወደ ምድር እያየ ይሄዳል ። ጻድቃንም ዕለተ ሞታቸውን እያሰቡ ይኖራሉና ፣ ግብድ ውእቱ ዘይሄሊ ዘእንበለ መቃብሩ ዘውእቱ ርስቱ እንዲል ፣ በግ ሐፍረቷን በላቷ ትሰውራለች ፤ ጻድቃንም የራሳቸውን ኃጢአት በንስሐ የወንድማቸውን ኃጢአት በትዕግሥት ይሰውራሉና ፣ እንድም በግ ጭቃውን አይጸየፈውም ጻድቃንም መከራውን አይሰቀቁትምና ። እንድም በግ ከዋለበት አይታወቅም ፤ ጻድቃንም ካሉበት አይታወቁምና ፣ እንድም ከበግ አውሬ አንዱን የነጠቀለት እንደሆነ ይሸሻል ከሸሸም በኋላ አይመለስም በግ ከበረረ የሰው ልጅ ከተመረረ እንዲሉ ፣ ጻድቃንም ከባልንጀራቸው አንዱ የሞተ እንደሆነ ይመንናሉ ከመነኑም በኋላ አይመለሱምና ፣ እንድም በግ ኑሮው በደጋ ነው ጻድቃንም ኑሯቸው በደጋ መንግሥተ ሰማይ ነውና ፣ በቀኝ ያቆማቸዋል አለ የሚመጣው በክበበ ትስብእት ነውና ፣ እንድም ቀኝ ኃያል ነው ጻድቃንም ለበጎ ሥራ ኃያላን ናቸውና እንድም ቀኝ ፈጣን ነው ፈጣኖች ናቸውና ቅን ነው ቅኖች ናቸውና ፣ እንድም በክብርም ሲል ነው ። ኃጥአንን አጣሊ አላቸው ፍየል ትዕቢተኛ ናት ሽቅብ ሽቅብ ትመለከታለች ። ኃጥአንም ትዕቢተኞች ናቸውና እንድም ፍየል ኃፍረቷን በላቷ አትሰውርም ኃጥአንም የወንድማቸውን ኃጢአት በትዕግሥት የራሳቸውን ኃጢአት በንስሐ አይሰውሩትምና ። እንድም ፍየል ጭቃውን ይጸየፈዋል ። ኃጥአንም መከራውን ይሰቀቁታልና ። እንድም ፍየል ከዋለበት ሁሉ ከእሀል ከተክል እየገባ ሰው ሲያሳዝን ይውላል ፤ ኃጥአንም ሰው ሲያሳዝኑ ይኖራሉና ።
እንድም ፍየል አንዱን አውሬ የነጠቀበት እንደሆነ ለጊዜው ይሸሻል ኋላ ችፍ እያለ ይቀርባል እየነጠቀ ይፈጀዋል ኃጥአንም ከወገናቸው አንድ የሞተ እንደሆነ መነንን ይላሉ ተመልሰው በርስቱ በጉልበቱ በቤቱ በንብረቱ ሲጣሉ ይገኛሉና ፣ እንድም ፍየል ኑሮው ቆላ ነው ኃጥአንም ኑሯቸው ቆላ ገሃነም ነውና ፣ በግራው ያቆማቸዋል አለ የሚመጣ በክበበ ትስብእት ነውና እንድም ፣ ግራ ደካማ ነው ኃጥአንም በ ጎ ሥራ ለመሥራት ደካሞች ናቸውና ። ግራ ጎዶሎ ነው በጎ ሥራ ከመሥራት ጎዶሎን ናቸውና ። ጠማማ ነው ጠማሞች ናቸውና ፣ በኃሣርም ሲል ነው፤

፴፬ አሜሃ ይቤሎሙ ንጉሥ ለእለ በየማኑ ንዑ ኅቡረ ቡሩካኑ ለአቡየ ትረሱ መንግሥተ ሰማያት ዘድልው ለክሙ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ።

፴፬ ያን ጊዜ ንጉሥ ክርስቶስ በቀኙ ያሉ ጻድቃንን ቡረኩት ገሪዛን ያደረባችሁ በረከተ ነፍስ ያላችሁ ዓለም ሳይፈጠር በጣዕም በመዓዛ በስን በብርሃን ያዘጋጀላችሁ መንግሥተ ሰማይን ትወርሱ ዘንድ ወደኔ ኑ ይላቸዋል ። ወአስተዳሉኩ እምቅድመ ይኩን ዓለምሙ ለእለ ይነብሩ ውስቴታ እንዲል የሚመጣ በክበበ ትስብእት ነውና ወደኔ ኑ አለ ። እንድም ትእምርተ ፍቅር ነው ።

፴፭ እስመ ርኅብኩ ወአብላእክሙኒ ኢሳ.፶፰ ፣ ፯ ። ሕዝ ፲፰ ፣ ፯-፲፮ ።

፴፭ ብራብ አብልታችሁኛል ።
ጸማዕኩ ወአስተይክሙኒ ።
ብጠማ አጠጥታችሁኛልና ።
ነግደ ኮንኩ ወተወከፍክሙኒ
እንግዳ ብሆን ተቀብላችሁኛልና ።

፴፮ ዕሩቀ ወአልበስክሙኒ መክ. ፯ ፣ ፴፮ ።

፴፮ ብታረዝ አልብሳችሁኛልና ።
ደወይኩ ወሐወጽክሙኒ
ብታመም ጠይቃችሁኛልና ።
ተሞቃሕኩ ወመጻእክሙ ኀቤየ ወነበብክሙኒ ።
ብታሰር ወደኔ መጥታችሁ ጠይቃችሁኛልና ።
ሐተታ ፤ ካልጀመሩት አይሆንምና አብላዕክሙኒ አስተይክሙኒ ተወከፍክሙኒ አልበስክሙኒ ሐወጽክሙኒ ነበብክሙኒ አለ የመንግሥተ ሰማይ ዋጋ አይሆንምና አጠገባችሁኝ አኖራችሁኝ አስጌጣችሁኝ አዳናችሁኝ አስፈታችሁኝ አላለም ይህም ሦስቱ የባለጠጎች ሦስቱ የነዳያን ነው ። ርኅብኩ ዕሩቀ ተሞቃሕኩ የባለጠጎች ጸማዕኩ ነግደ ኮንኩ ደወይኩ የነዳያን ፤ አልብኩኑ ጽዋዓ ማይ ቀሪር ለአስትዮ ጽሙዕ አልብኩኑ ጠፈር ለአጎድሮ ነግድ አልብኩኑ እግር ለሐውጾ ድውይ እንዲል ። እንድም ለመምህራን በክህደት ምክንያት ብራብ ብጠማ አስተምራችሁኛልና በክህደት እንግዳ ብሆን በትምህርት ተቀብላችሁኛልና በክህደት ምክንያት ልጅነት ባይሰጠኝ በሃይማኖት እንዲሰጠኝ አድርጋችኋልና፤ በክህደት ብታመም በትምህርት ጠይቃችሁኛልና በማእሰረ ክህደት ብታሰር በትምህርት አስፈትታችሁኛልና ። እንድም ለቀሳውስት

በኃጢአት ከሥጋው ከደሙ ብከለከል በንስሐ ሥጋውን ደሙን ሰጥታችሁኛልና በኃጢአት እንግዳ ብሆን በንስሐ ተቀብላችሁኛልና ልጅነት በኃጢአት ቢነሣኝ በንስሐ እንዲመለስልኝ አድርጋችሁኛልና ። በማእሰረ ኃጢአት ብታሰር በንስሐ አስፈትታችሁኛልና ። አንድም አንድ ወገን ለባሕታውያን ተባሕትዎ ብይዝ በተባሕትዎ መስላችኛልሁና ።

፴፯ አሚሃ ያወሥኡ ጻድቃን እንዘ ይብሉ እግዚኦ ማዕዜኑ ርኢናከ ርኁበከ ወአብላዕናከ ።

፴፯ ጻድቃንም ሠርተውት ያልሠሩት ይመስላቸዋል
ከትሕትና ወደ ትሕትና ይሄዳሉና
አቤቱ መቼ ተርበህ አይተንህ አብልተንህ ።

፴፰ ወጽሙዓከ ወአስተይናከ ።
፴፰ መቼ ተጠምተህ አይተንህ አጠጥተንህ ወማዕዜ ርኢናከ እንግዳከ ወተወከፍናከ ።
ምን ጊዜ እንግዳ ሆነህ አይተንህ ተቀብለንህ ።
ወዕሩቀከ ወአልበስናከ ።
ምን ጊዜ ታርዘህ አይተንህ አልብሰንህ ።

፴፱ ወድውየከኒ ወሐወፅናከ ።
፴፱ ምን ጊዜ ታመህ አይተንህ ጠይቀንህ ።
ወሙቁሐከኒ ወመጻእነ ኀቤከ ወነበብናከ ።
መቼ ታስረህ አስፈታንህ ጠየቅንህ ይሉታል ።

፵ ወእምዝ ያወሥእሙ ንጉሥ ወይቤሎሙ አማን እብለከሙ ኵሎ ዘገበርክሙ ለ፩ዱ እምእሉ ንኡሳን አኃውየ እለ የአምኑ ብየ ሊተ ገበርክሙ ።

፵ በኔ ካመኑ ምእመናን ላንዱ ያደረጋችሁ ለኔ አደረጋችሁልኝ ላንዱ ያደረጋችሁ ለኔ ማድረጋችሁ ነው ብሎ በውነት ይመልስላቸዋል ።
፵፩ ወእምዝ ይብሎሙ ለእለ በፀጋሙ ሑሩ እምኔየ ውስተ እሳት ዘለዓለም ዘድልው ለሰይጣን ወለመላእክቲሁ ። መዝ. ፮ ፡ ፰ ። ማቴ. ፯ ፡ ፳፫ ። ሉቃ ፡ ፲፫ ፡ ፳፯ ።
፵፩ ከዚህ በኋላ በግራው ያሉ ኃጥአንን መርገመ ጌባል ያደረባችሁ መርገመ ነፍስ ያለባችሁ ለሰይጣን ለሠራዊቱ ወደ ተዘጋጀ ማለት ተፈርዶ ወዳለ ወደማያልፍ ሥቃይ ሂዱ ይላቸዋል ። ሐተታ ፤ የሚመጣ በከበበ ትስብእት ነውና ሑሩ እምኔየ ይላል ። አንድም ትምርተ ፀብ ነው ።
፵፪ እስመ ርኁብኩ ወኢያብላዕክሙኒ ።
፵፪ ብራብ አላበላችሁኝምና ።
ጸማዕኩ ወኢያስተይክሙኒ ፤ ብጠማ አላጠጣችሁኝምና ።

፵፫ ነግደ ኮንኩ ወኢተወከፍክሙኒ ።
፵፫ እንግዳ ብሆን አልተቀበላችሁኝምና ።
ዓረቁ ወኢያልበስክሙኒ ፤ ብታረዝ አላለበሳችሁኝምና ፡ ደወይኩ ወኢሐወፅክሙኒ ፤ ብታመም አልጠየቃችሁኝምና ፤ ተሞቃሕኩ ወኢመጻእክሙ ኀቤየ ወኢነበብክሙኒ ።
ብታሰር መጥታችሁ አልጠየቃችሁኝምና ።

፵፬ አሚሃ ያወሥኡ እለ በጸጋሙ ፤
፵፬ ያን ጊዜ በግራ ቆመው የነበሩ ኃጥአን ይመልሳሉ ።
እንዘ ይብሉ እግዚኦ ማዕዜ ርኢናከ ርኁበከ ወኢያብላዕናከ ከትዕቢት ወደ ትዕቢት መኼድ ልማዳቸው ነውና ፡ ምን ጊዜ ተርበህ አይተንህ አናበላህ ብለን ። ወማዕዜ ርኢናከ ጽሙዓከ ወኢያስተይናከ ።
ምን ጊዜ ተጠምተህ አይተንህ እናጠጣህ ብለን ።
ወእንግዳከ ወኢተወከፍናከ ፤ ምን ጊዜ እንግዳ ሁነህ አይተንህ አንቀበልህ ብለን ።
ወዕሩቀከ ወኢያልበስናከ ፤ ምን ጊዜ ታርዘህ አይተንህ አናለብስህ ብለን ።
ወድውየከኒ ወኢሐወፅናከ ፤ ምን ጊዜ ታመህ አይተንህ አንጠይቅህ ብለን ።
ወሙቁሐከኒ ወኢነበብናከ ፤ ምን ጊዜ ታስረህ አይተንህ አንጠይቅህ ብለን ብለው ይመልሱለታል ።

፵፭ ወእምዝ ያወሥእሙ ንጉሥ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ ኵሎ ዘኢገበርክሙ ለ፩ዱ እምእሉ ንኡሳን አኃውየ ሊተ ኢገበርክሙ ።

፵፭ በኔ ካመኑ ምእመናን ላንዱ አለማድረጋችሁ ለኔ አለማድረጋችሁ ነው ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ብሎ ይመልስላቸዋል ።

፵፮ ወየሐውሩ እሉሂ ውስተ ኵነኔ ዘለዓለም ዮሐ. ፭ ፡ ፳፱ ። ዳን. ፲፪ ፡ ፪ ።
፵፮ ኃጥአን ወደ ማያልፍ ሥቃይ ይሄዳሉ ሲ○ርዱ ይኖራሉ ። ወጻድቃንሰ ውስተ ሕይወት ዘለዓለም ።
ጻድቃን ግን ወደ ማያልፍ ክብር ይሄዳሉ ። ሲወጡ ሲወጡ ይኖራሉ ። ሐተታ ይህ ሁሉ መነጋገር አለ ቢሉ አዎን ይላሉ ይህማ እንዳይሆን ንቃሕ መዋቲ ባለ ጊዜ ጻድቃን ከፀሐይ ሰባት እጅ አብርተው ጌታቸውን ኢየሱስ ክርስቶስን መስለው ይነሣሉ ። ኃጥአንም ከቁራ ሰባት እጅ ጸልመው አለቃቸውን ዲያብሎስን መስለው ይነሣሉ ጽድቁም ይህ ፍጻሜውም ይህ ነው ። ፍርድ በፊት ወቅሳ ወደኋላ ይሆን የለም ቢሉ የለም ነገሩ የሚያሰኝ ስለሆነ ለሰው በሚረዳ መናገር ነው እንጂ የለም ።

ምዕራፍ ፳፮ ።

፩ ወሶበ ፈጸመ እግዚእ ኢየሱስ ዘንተ ኵሎ ነገረ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ።

፩ ተአምሩ ከመ እምድኀረ ሰኑይ መዋዕል ይከውን ፋሲካ ። ማር ፡ ፲፬ ፡ ፩ ፡ ሉቃ ፡ ፳፪ ፡ ፩ ።

፪ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ይህን አስተምሮ ከፈጸመ በኋላ እስከ ሁለት ቀን ድረስ ፋሲካ እንዲ ሆን ታውቃላችሁን አላቸው ። ሐተታ የሚያስተምረው ረቡዕ ነው ብሎ እስከ ወደቀበት ሐሙስ ነው ። አንድም ድኅረ ክልኤ ይላል ከሁለት ቀን በኋላ ፋሲካ እንዲሆን ታውቃላችሁ የሚያስተምርበት ማክሰኞ ነው ብሎ ድኅሩ ሐሙስ ነው ፋሲካ ከሐሙስ አይ ወጣም ። ወይእኅዝዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ፤ ወል ደ ዕጓለ እመሕያውን ይይዙታል ማለት እያዛለሁ ወይሰቅልዎ ። እሰቀላለሁ ።

፫ ወእምዝ ተጋብኡ ሊቃነ ካህናት ወሊቃናተ ሕዝብ ውስተ ዓጸደ ሊቀ ካህናት ዘስሙ ቀያፋ ።

፫ ከዚህ በኋላ የሕዝቡ አለቆችና የካህናቱ አለቆች ቀያፋ ከሚባለው ከካህናቱ አለቃ ቦታ ተሰበሰቡ ።

፬ ወተማከሩ ከመ በሁብል የአኀዝዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወይቅትልዎ ።

፬ በሐሰት አንድ ፡ በህብል ብለህ አጥብቀህ በድፍረት ይዘው ጌታን ይገሉት ዘንድ መከሩ ።

፭ ወይቤሉ አኮኬ በበዓል ከመ ኢይትሀወኩ ሕዝብ ።

፭ ነገር ግን ሕዝቡ እንዳይታወኩ በበዓል አይሁን አሉ ።

ዘከመ ረፈቀ ኢየሱስ ለድራር በቢታንያ

ወበእንተ ተካይዶቱ ለይሁዳ ።

፮ ወበጺሖ እግዚእ ኢየሱሰ ቢታንያ ቦአ ቤተ ስምዖን ዘለምጽ ። ዮሐ፡፲፩፥፪ ። ፲፪፥፫ ፡ ማር፡፲፬ ፫ ።

፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቢታንያ በደረሰ ጊዜ ከስምዖን ዘለምጽ ቤት ገባ ።

፯ ወመጽአት ኀቤሁ ብእሲት እንተ ባቲ ቢረሌ ዘምሉእ ዕፍረተ ዘአልባስጥሮስ ዘብዙኀ ሤጡ ።

፯ ዋጋው ብዙ የሚሆን የደቀቀ የጣፈጠ ሽቱ ይዛ ፤ አንድም ዘአልባሰ ጢሮስ ይላል በጢሮሳዊ ግማጃ ዋጋ ልክ በሦስት መቶ ወቄት የተገዛ ሽቱ የያዘች ሴት መጣች ።

ወሦጠት ዲበ ርእሱ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይረፍቅ ጌታችን ከስምዖን ቤት ተቀምጦ ሳለ በራሱ ላይ አፈሰሰችበት ።

፰ ወርእዮሙ አርዳኢሁ አንጐርጐሩ በእንተ ዝንቱ ነገር ።

፰ ደቀ መዛሙርቱ ይህን አይተው አዘኑ ። ወይቤሉ ለምንትኑ ዘመጠነዝ ዕፍረተ አኅጐለት ዛቲ ብእሲት፤ይህች ሴት ይህን ያህል ሽቱ ለምን አበላሸች ።

፱ እምኢተሠይጠኑ በብዙኀ ንዋይ ይትወሀብ ለነዳያን ።

፱ ለነዳያን ይመጸወት ዘንድ የሁብዎ ይላል ለነዳያን ይመጸውቱት ዘንድ ለብዙ ዋጋ ባልተሸጠም ነበር አሉ ።

፲ ወአእሚሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ለምንት ታስርኅዋ ለዛቲ ብእሲት ።

፲ ጌታችን እንዲህ ማለታቸውን ዐውቆባቸው ይህችን ሴት ለምን ታዳክሟታላችሁ አላቸው ሠናየ ግብረ ገብረት ላዕሌየ ሊተ ሲል ለኔ በጐ ሥራ ሠርታ ልኛለችና ።

፲፩ ወለነዳያንሰ ዘልፈ ትረከብዎሙ ።
፲፩ ነዳያንንስ ዘወትር ታገኙዋቸዋላችሁ፤
ወጊዜ ፈቀድክሙ ታሤንዩ ሎሙ ።
በወደዳችሁ ጊዜ ታደርጉላቸዋላችሁ ።
ወኪያየሰ አኮ ዘልፈ ዘትረክቡኒ ።
እኔን ግን ዘወትር አታገኙኝም ።

፲፪ ወዘንተሰ ዕፍረተ ዘሦጠት ዲበ ርእስየ ለቀበርየ ገብረት ።

፲፪ ይህንም ራሴን የቀባችኝ ሽቱ ለምቀበርበት ቀን አስጠብቃዋለች ። ሐተታ ዕለቱን እንዳትቀባው አይሁድ አያስደርሷትም እንደ ሕጋቸው በሦስተኛው እንዳትቀባው ፈጥኖ ይነሣባታልና ፤ ዛሬም እጸድ ቅበታለሁ ብሎ ከሥራው በኋላ ግዳከም አይገ ባም አስቀድሞ ግን ቤተ እግዚአብሔር ልንጽበትን ለነዳያን ልሰጣቸውን ብሎ ያግከረ እንደሆነ ሕንጻ እግዚአብሔር ሰው በረኃብ ሲፈርስ ሲበሰብስ ለነ ዳያን ስጥ እንጂ ማሰት ይገባል ከሥራ በኋላ ግን እንዲህ ማሰት አይገባም ያኑ ከሙተው ያደርሰዋልና ፤ ታሪክ አባ ኢዮብ አባ ጴሜን የሚባሉ ፍጹማን መነ ኰሳት ነበሩ ገባረ ሪፍ የሚባል በዓለም የሚኖር ደግ ሰው ነበረ እየመጣ ይጠይቃቸዋል ሊጠይቃቸው መጥቶ ሳለ አባ ጴሜን እንደምን ሁነህ ትኖራለህ አለው ተክል ተክየ ራሴን ረድቼ እንግዳ ተቀብዬ ቢቻለኝ ለነዳያን ተርፌ እኖራለሁ አለው መልካም ይዘሃል ብሎ አሰናበተው ከዚህ በኋላ አባ ኢዮብ መጣ ገባረ ሪፍ መጥቶ ነበር አለው ምን ብለህ አሰ ናበትከው አለው እንዲህ ቢለኝ መልካም ይዘሃል አልሁት አለው፡መልካም አላደረግህ ምእኛን መስለህ ኑር እንዳትለው አለው አጥፍቻለሁ ጠርቼ ላመጣው ብሎ ጠርቶ አመጣው እኛን መስለህ ኑር አለው ከነ ሁሉም አይቻለኝም ብሏል አባ ኢዮብ አላበጀሁም ማረኝ ብሏል ፡ ይህች ሴት ከራስ ጸጕሯ እስከ እግር ጽፍሯ ይህ ቀራት የማትባል መልከ መልካም ናት መባ አካሏን የሚያሳይ መስታወት አሳት ልብሷን አትራ መልኳን አይታ መፍረስ መበስበስ ሳይቀር እንዲህ ማማር ምን ይረባል የዚያስ የዚያስ ኃጢአት የሚያስተሰርይ ኢየሱስ ክርስቶስ መጥቷል አሉ ለሱ የምቀባው ሽቱ ገዝቼ እሄዳለሁ ብላ በዝሙት

የሰበሰበችው ሦስት መቶ ወቄት ወርቅ አላት ይዛ ሄደች ።

ዲያብሎስ ታመልጠኛለች ይሆን ጊዜ ላስታት ብሎ ቀድሞ ከምታውቀው አንዱን መስሎ በአምሳለ ወሬዛ ሠናየ ላህይ ከመንገድ ቆያት ወዴት ትሄጂለሽ አላት ዝም አለችው አንች ባትነግሪኝ እኔ እነግርሽ የለም እንግዳ ወንድ መጥቶብሽ ለሱ ልትቀቢው ሽቱ ልትገዢ ትሄጂለሽ አላት አዎን አለችው ። ይህም አይደለም ፍቅሩ ያላለቀለት ወንድ መጥቶብሽ ለዚያ የምትቀቢው ሽቱ ልትገዥ ትሄጂለሽ አላት አዎን አለችው ይህም አይደለም በጥቂት ገንዘብ ብዙ ገንዘብ የሚሸጥ ነጋዴ መጥቶብሽ ለሱ የምትቀቢው ሽቱ ልትገዥ ትሄጂለሽ አላት አዎን አለችው ሁሉ ንም አዎን አዎን ትያለሽ ማናቸው ነው አላት እንግዳ ወንድ መጥቶብሽ አልከኝ ከዚህ ዓለም ልዩ የሚሆን ጌታ መጥቷል ፍቅር ያላለቀለት ወንድ መጥቶብሻል ላልከኝ ፍቅር ሰሐቦ ለወልድ ኃያል እመንበሩ ወአብጽሖ እስከ ለሞት እንዲል ። የሰው ፍቅር አገብሮት ሊሞት መጥቷል በጥቂት ገንዘብ ብዙ ገንዘብ የሚሸጥ ባለጸጋ ነጋዴ መጥ ቶብሻል ላልከኝ አዎን በጥቂት ትሩፋት ብዙ ክብር የሚሰጥ ኢየሱስ ክርስቶስ መጥቷልና ለሱ የምቀባው ሽቱ ልገዛ እሄዳለሁ ብላ ስሙን ብትጸራበት እንደ ትቢያ በኖ እንደ ጢስ ተኖ ጠፍቶላታል ። ከዚህ በኋላ ሃድኖክ የሚባል ባለጸጋ ነጋዴ አለ ሄዳ ለነገ ሥታት የሚገባ ሽቱ አምጣ ብላ ሦስት መቶ ወርቅ ሰጠችው በሀገራቸው ሐሰት የለምና ይሆን ያሀልስ የሚያወጣ የለኝም አላት ኢሉ የማያውቀው እናቱ የምታውቀው ዳዊት ሰሎሞን ተቀብተውለት የተረፈ ነበር ከእንዲህ ያለ ቦታ አለ ሽጥላት ብላው ሽጦላት አምጥታ ቀብታዋለች ። ይህ ብቻም አይደለ ጌታ ግብጽ ሲወርድ ሰሎሜም ፈያታይ ዘየማን ይዘውት ሳለ ከልብሱ ላይ ወዛ ቢያጥቡት ሰፈፈ ይህን በዕቃ አትረውታል ይህም ተጨምሮበታል ።

፲፫ አማን እብለክሙ በኀበ ሰበክዋ ለዛቲ ወን ጌል ይንግሩ ውስተ ኵሉ ዓለም ዘገብረት ዛቲ ብእ ሲት ተዝካረ ላቲ ወይዝክርዋ ።

፲፫ ወንጌል በተነገረችበት ቦታ ሁሉ ይህች ሴት የሠራችውን ሊነግሩላት ይገባል ብዬ እንዲገባ በው ነት እነግራችኋለሁ ። ይህንም ይዘው አራቱ ሁሉ ጽፈዋታል ።

፲፬ ወእምዝ ሖረ ፩ዱ እም፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ዘስሙ ይሁዳ አስቆሮታዊ ኀበ ሊቃነ ካህናት ። ማር፡፲፬ ፥ ፲ ሉቃ፡ ፳፪ ፥ ፫ ።

፲፬ ከዚህ በኋላ ካሥራ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱ አንዱ የአስቆሮት ሰው የሚሆን ይሁዳ ወደ ሊቃነ ካህናት ሄደ ። ሐተታ እንዲያው አይደለም በደብረ ዘይት ሲበሉ አማን እብለክሙ ከመ ፩ዱ እምኔክሙ ያገብአኒ አላቸው ። ወአነኑ እንጋ እግዚእ አነኑ እንጋ ። የማሲዝህ እኔ ነኝ እኔ ነኝ ይባባሉ ጀመሩ ታሪክ በደብረ ዘይት ከነበሩ አእባን አንዱን መጥ ተህ መስክርበት አለው መጥቶ በይሁዳ ራስ ላይ ሦስት ጊዜ ዙሮ ንጹሕ ደም የምታሰፈስስ ይሁዳ ወዮልህ ብሎ መስክሮበታል ዛሬስ አለ እስና ይህ መሠርይ ደንጊያ ያናግርብኝ ጀመር እንኪያስ በማኘ ያገኘኝ ብሎ ወጥቶ ሄዷል ።

፲፭ ወይቤሎሙ ሚመጠነ ትሁቡኒ እመ አገ ብእ ለክሙ ።

፲፭ ባሲዛችሁ ምን ያሀል ትሰጡኛላችሁ አላ ቸው ።

ወተናገርዎ ምስሌሁ ወተሰነአው ከመ የሀብዎ ፴ ብሩረ ።

ሠላሳ ብር እንሰጥሃለን አሉት ። ወአስተሐለቁ ነገረ ይላል በሉቃስ ነገር ቆረጹ ነገር አቆሙ ነገር ወሰኑ ።

፲፮ ወእምይእቲ ዕለት አኀዘ ይኅሥሥ ሳሕተ ከመ ያግብኦ ሎሙ ።

፲፮ ከዚያ ቀን ጀምሮ ከዚያ ቀን ወዲህ ሊያ ሲዘው ምግላል ቦታ ይሻ ነበር ።

በእንተ ደኃሪት ድራር ።

፲፯ ወበቀዳሚት ዕለተ ፍሥሕ መጽኡ አርዳ ኢሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ወይቤልዎ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ ለከ ትብላዕ ፍሥሐ ። ማር፡ ፲፬ ፥ ፳፪ ሉቃ፡ ፳ ፥ ፱-፲ ።

፲፯ ፋሲካ ከሚውልባቸው ከ፯ቱ ዕለታት በመ ጀመሪያዪቱ ቀን ፤ አንድም ወአመ ቀዳሚት ዕለተ ፍሥሕ ይላል በመጀመሪያዪቱ ፋሲካ ደቀ መዛሙርቱ ወደ ጌታ ቀርበው በጉን ትበላ ዘንድ በወዴት ልና ዘጋጅልህ ትወዳለህ አሉት ፤ ሑሩ ወአስተዳልው ዘንበልዕ ፍሥሐ ብሏቸዋል በሉቃስ ።

፲፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሑሩ ውስተ ሀገር ኀበ እገሌ ።

፲፰ ጌታም ወደእገሌ ሀገር ሂዱ አላቸው ። እንደ ማርቆስ ምልክት ነግሮ ይሰዳቸዋል ። ወበልዎ ይቤለከ ሊቅ ጊዜየ በጽሐ በኀቤከ አገብር ፋሲካ ምስለ አርዳእየ።መምህር ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ባንተ ዘንድ በዓል የማከብርበት ቀን ደርሷል አለህ በሉት አላቸው ።

፲፱ ወገብሩ አርዳኢሁ በከመ አዘዞሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

፲፱ ደቀ መዛሙርቱ ጌታ እንዳዘዛቸው አደረጉ። አስተዳለው ሎቱ ፍሥሐ ።

በጉን የሚያርዱበት ወቅለምት ደሙን የሚቀበሉ በት ብርት ሥጋውን የሚቀቅሉበት ድስት አዘ ጋጅተዋል ።

ዘከመ ከሠተ ሎሙ ለዘያገብኦ ።

፳ ወምሴተ ከዊኖ ረፈቀ ምስለ ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ። ማር.፲፬ ፡ ፲፯ ሉቃ.፳፪ ፡ ፲፬ ሉቃ. ፲፫ ፡ ፳፩ ።

፳ ሲመሽ በመሽ ጊዜ ካሥራ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱ ጋራ ተቀመጠ ።

፳፩ ወእንዘ ይበልዑ ይቤሎሙ አማን እብለክሙ ከመ ፩ዱ እምኔክሙ ያገብአኒ ።

፳፩ ሲበሉ ከናንተ አንዱ ያሲዘኛል ብሎ እንዲያሲዘኝ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ።

፳፪ ወተከዙ ጥቀ ።

፳፪ ፈጽመው አዘኑ ።

ወአኃዙ ይበልዎ በበ፩ዱ አነኑ እንጋ እግዚኦ ።
እያንዳንዳቸው አቤቱ የሚያሲዝህ እኔ ነኝ እኔ ነኝ ይባባሉ ጀመር ።

፳፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ዘያወርድ እዴሁ ምስሌየ ውስተ መጸብሕየ ውእቱ ያገብአኒ ።

፳፫ ከኔ ጋራ ወጥ የሚያወጣው እሱ ያሲዘኛል አላቸው ። ሐተታ ለልማዱ ጌታ ስድስቱን አቁሞ ስድስቱን አስቀምጦ ይዞ ይበላሉ ይመገባሉ ። ዛሬ የተቀመጡ ነገ ይቆማሉ ወጥ የሚያወጣው በተራ ነው ጌታ እያወጣ ይበላል አውጡልኝ አይልም ስድስተኛው ላምስቱ ለራሱም እያወጣ ይበላል በዚያ ቀን ከተቀመጡት አንዱ ይሁዳ ነበር ወጥ ማውጣትም ተራው የይሁዳ ነበርና እንዲህ አለ ።

፳፬ ወልደ ዕጓለ እመሕያሰ የሐውር በከመ ተሠርዓ በእንቲአሁ ። መዝ.፵፣፲ ።

፳፬ ተጽሕፈ ሲል ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስም ስለሱ እንደተጻፈ ይሄዳል ማለት ይሞታል ወባሕቱ እሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ ዘያገብኦ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
ነገር ግን ምክንያት ሁኖ ለሚያሲዘው ለዚያ ሰው ወዮለት እምኃየሰ ሶበ ኢተወልደ ለውእቱ ብእሲ ። ባልተወለደ በተሻለው ነበር ፣ ሐተታ ። እናቱን ይዳፋት ማለት ነው ቢሉ ኢተፈጥረ ሲል ነው ባልተፈጠረ በተሻለው ነበር አሪት ዘልደት እንዲል ዘፍጥረት ሲል ። ይህስ ፍጠረኝ ብሎ ፈጥሮታልን ቢሉ ቢፈጥረውስ ግዕዛኑን ነሥቶ ፈጥሮታልን ።

፳፭ ወአውሥአ ይሁዳ ዘያገብኦ ወይቤ አነኑ እንጋ ውእቱ ረቢ ።

፳፭ የሚያሲዘው ይሁዳም የሚያሲዝህ እኔ ነኝ አለው ተለይቼ ብቀር ይታወቅብኛል ብሎ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንተ ትቤ ።
አንተ ትላለህ አለው ። መሰወር እንድም በፈቃዱ የምሞተውን ሞት በግድ አስገድለዋለሁ ትላለህ ። ታሪክ ጌታ ሙሴን በግብጻውያን ሞተ በኵር አምጥቼ አወጣችኋለሁ አለው እንዲህማ ከሆነ የእሥራኤልስ በኵር ሊሞት አይደለምን አለው ፤ እንዲህስ እንዳይሆን የሚያዝያ ጨረቃ ሠርቅ ባደረገች ባሥር ቀን ቀንዱ ያልከረከረ ጥፍሩ ያልዘረዘረ ጠጉሩ ያላረረ ዓመት የሆነው ጠቦት ያለው ከመንጋው ። የሌለው ገዝታችሁ እስከ ፲፬ ቀን እሰራችሁ ባ፲፬ኛው ቀን ፩ዱን ሰዓት ከ፲ ከፍላችሁ ፭ዱን እጅ ትታችሁ በ፮ እጅ ብርሃን ከሌሊቱም ፩ዱን ሰዓት ከ፲ ከፍላችሁ ባንዱ እጅ ጨለማ ሠውት።ስትሠውትም ፯ ዐሥር ፲፪ ሁናችሁ ። ያለው ቤተሰቡን ይዞ የሌለው ጐረቤቱን ጠርቶ አንድ በግ እንድትጨርሱ ሁናችሁ ደሙን መቃን መድረኩን እርጩት ያን እያየ ሞተ በኵር ይከለክልላችኋል ፡ ዝግኑን ቅቅሉን ብርንዶውን አትብሉ ጥብሱን ብሉ ኢታትርፉ እስከ ደግደግ እንዲል ። አትርፋችሁ አታሳድሩ ካንዱ ወዳንዱ አትውሰዱት የበላችሁትን በልታችሁ የተረፋችሁን ከእሳት ጨምሩት ሐምለ ብኂእ ረብርቡበት ብሎታል በሀገራቸው አራት ነገር ያመጣል የወይን ቅጥራን የበለስ ቅጥራን የሥንዴ ቅጥራን አዞ ከል ። በዚያ ወራት የሚበሉት ቂጣ ነውና እንዳረቄ እንዲበትንላቸው ። ስትበሉትም ጫማችሁን አዝባችሁ ዝናራችሁን ታጥቃችሁ ኩፌታችሁን ደፍታችሁ ቦሎታችሁን ይዛችሁ እየቸኮላችሁ ብሉት አጥንቱን አትስበሩት ብሏቸዋል ይህ ሁሉ ምሳሌ ነው ። በግዕ የጌታ ምሳሌ ዓመት የሆነው ጠቦት ወርድ እንጂ ቁመት አያክልም ። ጌታም ፍጹም የሠላሳ ዓመት ጐልማሳ ሲሆን ነውና የተሰቀለ ዓመት የሆነው ጠቦት ቀንዱ ያልከረከረ ጥፍሩ ያልዘረዘረ ጠጉሩ ያላረረ ማለቱ ምክንያተ ኃጢአት የለበትምና ። የሚያዝያ ጨረቃ ሠርቅ ባደረገች ባሥር ቀን ዋጅታችሁ እስከ ዐሥራ አራት እሰራችሁ ባሥራ አራት ቀን ሠውት ማለቱ የጌታም ምክረ ሞቱ ባሥር ተጀምሮ ባሥራ አራተኛው ቀን ተፈጽሟል ። በሁለት እጅ ብርሃን ባንድ እጅ ጨለማ ሠው ማለቱ ከነግህ እስከ ቀትር ብርሃን ሁኖዋል ። ከቀትር እስከ ሰዓት ጨለማ ሁኖዋል ። ወጸልመ ኵሉ ዓለም እንዲል ። በሠርክ ብርሃን ሁኖዋል ። ወፍና ሠርክ ይበርህ እንዲል ፥ ስትሠዉትም ስባት ዐሥር አሥራ ሁለት ሁናችሁ ሠዉት ማለቱ ሰባት በሳቸው ፍጹም ነው ዐሥርም በኛ ፍጹም ነው ፍጹማን ሁናችሁ ተቀበሉ ሲል ፲፪ ማለቱ ለጊዜው የሚቀበሉት ዐሥራ ሁለቱ ነገደ እሥራኤል ናቸው ፍጻሜው ግን ዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ናቸውና ፥ ደሙን መቃን መድረኩን እርጩት ማለቱ ለጊዜው ያን እያየ ቸነፈር ይከለክልላቸዋል ። ዛሬም ሥጋውን ደሙን ከሚቀበሉ ምእመናን አጋንንት ላለመቅረባቸው ምሳሌ ። ዝግኑን ቅቅሉን አትብሉ ማለት ሙስና መቃብር አገኘው አትበሉ ሲል ነው ። ብርንዶውን አትብሉ ማለቱ ደም ካለ ነፍስ አትለይም ። እስመ ነፍስ ተኃድር በደም እንዲል ነፍስ ያልተለየውን ሥጋውን እንበላለን አትበሉ ሲል ጥብሱን ብሉ ማለቱ መለኮት

የተዋሐደውን ነፍስ የተለየችውን ሥጋውን እን በላለን በሉ ሲል ነው አታሳድሩ አለ ካሣ ሳይፈጸም አላደረምና ካንዱ ወደ አንዱ አትውሰዱት አለ ለጊዜው መካነ መስቀሉ ለመካነ መቃብሩ ቅርብ ነው ፍጻሜው ግን ዛሬም መሥዋዕት ካንዱ ሠርቶ ወዳንዱ ወስዶ መሠዋት አይገባምና የበላችሁትን በልታችሁ የተረፋችሁን ከእሳት ጨምሩት ማለቱ የተቻላችሁን ያህል ምሥጢር መርምራችሁ የቀረውን መንፈስ ቅዱስ ያውቃል በሉ አትጋፉ ሲል ነው ። እሳት የመንፈስ ቅዱስ ምሳሌ ፤ ሐምለ ብኂእ ረብርቡብት ማለቱ ለጊዜው ቢዚያ ወራት የሚበሉት ቂጣ ነበርና እንደ አረቄ አንዲበትንላቸው ነው ዛሬም ሥጋውን ደሙን መቀበል የሚገባ የበሉት የጠጡት ከሆድ ሲጠፋ ላፍ ምሬት ሲሰማ ነውና ፤ ጫማችሁን አዝባችሁ አለ ምግባረ ወንጌልን ሠርታችሁ ዝናራችሁን ታጥ ቃችሁ አለ ንጽሕና ይዛችሁ ኩፌታችሁን ደፍታ ችሁ አለ አክሊለ ሦከን እያሰባችሁ በትራችሁን ይዛችሁ አለ ነገረ መስቀሉን እያሰባችሁ ሲል ነው እየቸኮላችሁ ብሉት ማለቱ ለጊዜው መንገደኞች ናቸው ፍጻሜው ግን ሞት አለብን እያላችሁ ኑሩ ሲል ነው ። አረጋዊ መንፈሳዊ ፤ ድርሳን ፤ ዓብድ ውእቱ ዘይሄሊ ዘእንበለ መቃብሩ ዘውእቱ ርስቱ እንዲል አጥንቱን አትሰበሩት ማለቱ ለጊዜው ግብ ጻውያን ሲጎዱ እሥራኤል አለመጐዳታቸውን መናገር ነው ፤ ፍጻሜው ግን ኃጥአን ሲጐዱ ጻድቃን ላለመጐዳታቸው ምሳሌ ነው በቁሙም የሁለቱን ወንበዶች ጭንና ጭናቸውን እየሰበሩ ሲያወርዷቸው የሱን አልሰበሩትምና ፀፅሞ ኢትስብሩ እንዲል ፤ እንደ አርዮስ ፍጡር በመለኮቱ አትበሉ ሲል ነው ከዚህም ኦሪትን ሠርቶ አሳልፏታል ፤ ንጉሥ ቀድሞ ሹሞት የነበረውንና ኋላ የሚሾመውን አቅርቦ ያን ወቅሶ ሽሮ ይህን እንዲሾም እሱም ወንጌልን የሚ ሠራ ነውና ።

ዘከመ ሠርዓ ኢየሱስ አኰቴተ ቍርባን ።

፳፮ ወእንዘ ይበልዑ ነሥአ ኅብስተ እግዚእ ኢየሱስ ባረከ ። ፩፡ ቆሮ ፲፩ ፡ ፳፫ ።

፳፮ ሲበሉ ጌታ ዳቦውን አንሥቶ ይዞ ባረከ አከበረ ለወጠ ።

ወፈተተ ። ገመሰ ቆረሰ ። እንድም ባረከ ገመሰ ፈተተ አጠቃቀነ ዐሥራ ሦስት አደረገ ፤ ጌዴዎን ዓሥራ ሦስት ሁኖ ሠውቷልና አንድም ባሥራ ሦስቱ ዕፀወ ዕጣን ምሳሌ እንድም ዐሥራ ሦስቱን ጸዋትወ መከራ እቀበልላችኋለሁ ሲል አክሊለ ሦክ ተኰርዖ ርእሰ ተጸፍዖ መልታሕት ተወክፎ ምራቅ ሰትየ ሐሞት ተአስሮ ድኅሪት ተቀስፎ ዘባን ርግዘተ ገቦ ርግዘተ ገቦ ከሞት በኋላ ነው አይሰማውም ብሎ ጸዊረ መስቀል ኃምስቱ ቅንዋት እግሩን እየራሱ ቸንከረውታል ያሉ እንደሆነ የተመቸ ነው ። ደርበው ቸንከረውታል ያሉ እንደሆነ ብሱን ያያል ። አንዱን እሱ ተቀብሎታል ፲፪ን ለሐዋርያት ሰጥቷቸዋል ዝ ሥጋየ ዝ ደምየ ብሏቸ ዋልና ለማስደፈር ጥዒሞ አጥዓሞሙ እንዲል ። አንድም ሳይቀበል አቀብሏቸው ቢሆን ቄሱ አቀብ ሏቸው ሳይቀበል በወጣ ነበርና ተቀብሎ ያቀብል ለማለት አብነት ለመሆን ወወሀቦሙ ለአርዳኢሁ ። ወይቤሎሙ ንሥኡ ብልዑ ዝ ውእቱ ሥጋየ ። ነገ በመልዕልተ መስቀል የሚሠዋው ሥጋየ ይህ ነው ብሎ ።

፳፯ ወነሥአ ጽዋዐ ወአእኰተ ።
፳፯ ጽዋውንም ይዞ አክብሮ ለውጦ ትኩስ ደም አድርጎ ።

፳፰ ወወሀቦሙ እንዘ ይብል ሰትዩ እምኔሁ ኵልክሙ ዝ ውእቱ ደምየ ዘሐዲስ ሥርዓት ዘይት ከዓው በእንተ ብዙኃን ለኅድገተ ኃጢአት ።

፳፰ እንግዳ ሥርዓት የሚሆን የሐዲስ ርስት የመንግሥት ሰማያት መጽኛ የሚ ሆን በተሐድሶ ጸንቶ የሚኖር ስለ ብዙ ሰዎች የሚፈስ ደሜ ይህ ነው ከሱ ጠጡ ብሎ ሰጣቸው ሐተታ፤ በከፈል ተናገረው አንድ ሰው ተቀብሎ አይፈጽመውምና እስከ ዕለተ ምጽአት ሲሰጥ ይኖራልና ለኅድገተ ኃጢአት ኃጢአት ሊሰረይ ።

፳፱ ወናሁ እብለክሙ ኢይሰቲ እንከ እምይ እዜ እምዝንቱ ሐጺረ ፍሬ ወይን እስከ አንታክቲ ዕለት አመ እሰትዮ ሐዲሰ ምስሌክሙ በመንግሥተ አቡየ ።

፳፱ ባባቴ መንግሥት ማለት ባባቴ ሥልጣን ታድሼ ተነሥቼ ከናንተ ጋራ በጥብርያዶስ እስከም መጣበት ቀን ድረስ ከዚህ የወይን ፍሬ ጭማቂ አል ጠጣም ብየ እነግራችኋለሁ ።

፴ እንቢቦሙ ማር. ፲፬ ፡ ፳፮ ዮሐ. ፲፰ ፡ ፴፪ ዘካር. ፲፫ ፡ ፯ ።

፴ በአሪት የሚደገም አለ ያን ደግመው ። ሰቢሖሙ ። ሥጋውን ደሙን ተቀብለው አንድም እንቢቦሙ አቡነ ዘበሰማያት ደግመው ወሰቢሆሙ ነገረ ጴራቅሊጦስን ተጫውተው ።

፴፩ ወፅኡ ውስተ ደብረ ዘይት ።

፴፩ ወደ ደብረ ዘይት ወጡ ። ሐተታ ሥጋውን ደሙን በመብል በመጠጥ ያደረገውን በሌላ ያላደረ ገው ስለምን ቢሉ የቀረው ከብት በአፍአ ይቀራል መብል መጠጥ ከሰውነት ይዋሐዳልና በውነት እንደ ተዋሐደን ለማጠየቅ ። አንድም መብል መጠጥ ያፋቅራል እንዳፈቀረን ለማጠየቅ ያውስ ቢሆን በሥንዴ በወይን ያደረገው በሌላ ያላደረገው ስለምን ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ትንቢት እምፍሬ

ሥርናይ ወወይን ወቅብዕ በዝኃ ። ቀዳሜ ሕይወቱ ለሰብእ እክል ወማይ ወይን ወሥርናይ ስዘኢይስቲ ወይነ ምንትኑ ሕይወቱ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም መልከ ጼዴቅ በሥንዴ በወይን ይሠዋ ነበር ትንቢቱን ዐውቆ እናግሯል ምሳሌውንም እንጂ ባወቀ አስመስሏል ምሥጢሩ ምንድነው ቢሉ ጌታችን እመቤታችን ቢበሉ የኖሩ ሥንዴ ወይን ነበረ ፍጹም ሥጋውን ፍጹም ደሙን እንደ ሰጠን ለማጠየቅ ። እንድም በመስለ ነገር ስመስ ጠት ሥንዴ ሥብ ሥጋ ይመስሳል ወይንም ትኩስ ደም ይመስላልና ። እንድም ሥንዴ ልባም ሴት የያዘ ችው እንደሆነ ነውር የለበትም ነውር የሌለበት ሕግ ሠራሁላችሁ ሲል ወይንም አንድ ጊዜ የጣሉት እንደሆነ ኃይል እየጨመረ ይሄዳል ኃይል የምት ሆን ሕግ ሠራሁላችሁ ሲል ።
ወእምዝ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኵልክሙ ትክ ህዱኒ በዛቲ ሌሊት ከዚህ በኋላ ጌታ በዚች ሌሊት ሁላችሁ ትክዱኛላችሁ አላቸው ።
እስመ ይብል መጽሐፍ እቀትል ለኖላዊ ወይዘረዉ አባግዕ መርዔቱ ።
መጽሐፍ ጠባቂ ክርስቶስ ይሞታል የመንጋው በጎች ሐዋርያት ይበተናሉ ብሏልና ።

፴፪ ወእምድኅረ ተንሣእኩ እቀድመክሙ ገሊላ
፴፪ ወደ ገሊላ እቀድማችኋለሁ ማለት ከተ ነሣሁም በኋላ መታየትን በገሊላ እጀምርላችኋለሁ ።

፴፫ ወአውሥአ ጴጥሮስ ።
፴፫ ጴጥሮስም መለሰ ።
ወይቤሎ ለእመሂ ኵሎሙ ክህዱከ አንስ ኢይክህ ደከ ግሙራ ።
ሁሉም ቢክዱህ እኔ አልክድህም አለው ።

፴፬ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለከ ከመ በዛቲ ሌሊት ሠልስ ትክህደኒ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ማር ፲፬ ፡ ፳ ።

፴፬ ጌታም በዚች ሌሊት ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ብየ እንድትክደኝ በውነት እነግ ርሃለሁ አለው ።

፴፭ ወይቤሎ ጴጥሮስ እመውትኒ ምስሌከ ወኢይክህደከ ዮሐ.፲፫፡፴፰ ማር ፲፬፡፴፩ ሉቃ ፳፪፡፴፫

፴፭ ጴጥሮስም ካንተ ጋራ እሞታለሁ ሞትከን ሞት አደርጋለሁ እንጅ አልክድህም አለው ፤
ወከማሁ ይቤሉ ኵሎሙ አርዳኢሁ ።
ተመክቶ ያስመካቸዋል ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ እንደሱ ከሉ ጋራ ሞትከን ሞት እናደርጋለን አንክድህም አሉ።

ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ በጌቴሴማን ።

፴፮ ወእምዝ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ምስሌሆሙ ውስተ ዓጸደ ወይን ዘስሙ ጌቴሴማን ።

፴፮ ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱን አስከትሎ ጌቴሴማን ከሚባለው ወይን ቦታ ሄደ ።
ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ንበሩ ዝየ እስከ ሶበ አሐ ውር ከህ ወእጼሊ ።
ደቀ መዛሙርቱን ከዚያ ሂጄ እስከጸልይ ድረስ ከዚህ ቆዩ አላቸው ። አንድም እጸሊ ይላል እጸልይ ዘንድ ።

፴፯ ወነሥአሙ ምስሌሁ ለጴጥሮስ ወለ፪ሆሙ ደቂቀ ዘብዴዎስ ።

፴፯ ሦስቱን ባለሟሎቹን አስከትሎ ሂዶ ስምንቱን በጌቴሴማኒ ትቶ ፤
ወአኀዘ ይትከዝ ወይኅዝን ።
ያዝን ይቆረቆር ጀመር ።

፴፰ ወእምዝ ይቤሎሙ ተከዘት ነፍስየ እስከ ለሞት ።

፴፰ ከዚህ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ ነፍሴ እስከ መለየት ደርሳ አዘነች አላቸው ።
ወንበሩ ዝየ ።
ክዚህ ቆዩ ።
ወትግሁ ምስሌየ ።
ከኔ ጋራ ለመኖር እንደኔ ተግታችሁ አመልክቱ ።

፴፱ ወተአተተ ሕቀ እምሀየ ወሰገደ በገጹ ።
፴፱ ከዚያ ጥቂት እልፍ ብሎ ግንባሩን ምድር አስነክቶ ስገደ ።
በሉቃስ መጠነ ሙጋረ እብን ይላል ድንጊያ ወርውሮ እስከሚደርስበት ።
ወጸለየ ።
አመስከተ ።
ወይቤ አ አቡየ እመሰ ይትከሃል ይኅልፍ እምኔየ ዝንቱ ጽዋዕ ።
ያለኔ ሞት የዓለሙ ድኅነት ያለኔ ሕማር የዓለሙ ክብር አይቻልም እንጂ የሚቻልስ ከሆነ ይህ ጽዋዕ ሞት ይለፍልኝ ወባሕቱ ፈቀደ ዚአከ ይኩን ወኢኮ ፈቀደ ዚአየ ። ነገር ግን ያንተ ፈቃድ ይደረግ እሳለሁ እንጂ የኔ ፈቃድ ይደረግ አልልም ። አንድም በኔ ሞት የዓለም ድኅነት በኔ ኃሣር የዓለ ምም ክብር የሚቻልስ ከሆነ እኔ ከሞትሁላቸው ከኔ ሞት የተነሣ ይህ ጽዋዓ ሞት ይቅርላቸው ። አንድም ከኔ ለምእመናን ይለፍላቸው ፤ እኔን አብነት አድርገው ይሙቱ ።
ወባሕቱ ፈቀደ ዚአከ ይኩን ወኢኮ ፈቃደ ዚአየ ።
ነገር ግን የኔ ፈቃድ ካንተ ፈቃድ ልዩ ሁኖ የኔ ፈቃድ ይሁን አልልም የኔ ፈቃድ ካንተ ፈቃድ ጋራ አንድ ነውና ያንተ ፈቃድ ይሁን እላለሁ እንጂ ፤

፵ ወሖረ ኀበ አርዳኢሁ ።
፵ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ሄደ ።
ወረከቦሙ እንዘ ይነውሙ ።
ተኝተው አገኛቸው ።

ወይቤሎ ለጴጥሮስ ከመዝኑ ስእንክሙ ተጊሃ አሐተ ሰዓተ ምስሌየ ።
ጴጥሮስን ከኔ ጋራ ለመኖር እንደኔ አንድ ሰዓት መትጋት ተሳናችሁ አለው ።

፵፩ ትግሁ ወጸልዩ ከመ ኢትባዑ ውስተ መንሱት ።

፵፩ ወደ ኃጢአት ወደ ክህደት ወደ መከራ ወደ ገሃነም እንዳትገቡ ተግታችሁ ለምኑ ።
እስመ መንፈስ ይፈቅድ ።
ነፍስ ሥራ ልትሠራ ትወዳለችና ትግሁ ።
ወሥጋ ይደክም ።
ሥጋ ግን ደካማ ነውና ኢትባኡ ላለው ።

፵፪ ወካዕበ ሖረ ወጸለየ ።
፵፪ ሁለተኛ ሄዶ አመለከተ ፤
ወይቤ እመ ይትክሃል ይኅልፍ እምኔየ ዝንቱ ጽዋዕ እንበለ እስተዮ ይኩን ፈቃድከ እንዳለፈው በል ።

፵፫ ወገብአ ካዕበ ኀበ አርዳኢሁ ።
፵፫ ፪ተኛ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ሄደ ፤
ወረከቦሙ እንዘ ይነውሙ ።
ተኝተው አገኛቸው ።
እስመ ክብዳ አዕይንቲሆሙ በድቃስ ።
እንቅልፍ ጸንቶባቸዋልና ፤ በልተው ጠጥተዋልና ኃዘን ሰምተዋልና ።
፵፬ ወኀደጎሙ ወሖረ ካዕበ በሣልስት ወጸለየ ኪያሁ ከመ ቃለ እንዘ ይብል ።
፵፬ ሦስተኛ ሂዶ ያነኑ ጸለየ ለቀረበው ካዕበ ለመጀመሪያው ሣልስ አለ ። ሦስት ጊዜ መሆኑ የሦስትነት ቃሉ አለመለወጡ ያንድነት ምሳሌ ።
፵፭ ወእምዝ ገብአ ካዕበ ኀበ አርዳኢሁ ።
፵፭ ከዚህ በኋላ ሁለተኛ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ሄደ ።
ወይቤሎሙ ኑሙ እንከ ወአእርፉ ።
ከእንግዲህስ ወዲህ ዕረፉ አላቸው፤ጊዜው ነውና ንሣአ ሀከይ ሥጋየ መክፈልተከ እንዲል አንድም እኔ ከካስኩላችሁ ዕረፍተ ነፍስ ዕረፉ ። አንድም ይሁዳ እራት ቤት ጭፍራ ይዞ የሚመጣ ነውና እያሳርፋችሁም እንጂ ካሳረፋችሁስ ዕረፉ ለማለት ።
ናሁ በጽሐ ጊዜሁ ወያገብዕዎ ለወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ውስተ እደ ኃጥአን ።
እነሆ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ በኃጥአን እጅ የሚያዝበት ጊዜ ደርሷል አላቸው ።
፵፮ ተንሥኡ ንሑር ናሁ በጽሐ ዘያገብአኒ ።
፵፮ የሚያሲዘኝ ይሁዳ እነሆ መጥቷል ተነሡ እንሂድ አላቸው ።
ዘከመ አግብአ ይሁዳ ለክርስቶስ ወዘከመ ተእኅዘ
፵፯ ወእንዘ ዘንተ ይትናገር ናሁ በጽሐ ይሁዳ ዘያገብእ እም፲ቱ ወ፪ቱ ፩ዱ ማር ፲፬ ፥ ፵፫ ሉቃ ፳፪ ፥ ፵፯ ዮሐ ፲፰ ፥ ፫ ።

፵፯ ይህን ሲናገር ካሥራ ሁለቱ አንዱ ይሁዳ ሊያሲዘው መጣ ወመጽኡ ምስሌሁ ብዙኃንስ ሰብእ በመጣብሕ ወበአብትር እምኀቤሆሙ ለሊቃነ ካህናት ወለሊቃናተ ሕዝብ ።
ሾተል ጎመድ የያዙ ብዙ ሰዎች ሊቃነ ካህናት ዘንድ ከሱ ጋራ መጡ ሐተታ፤ እምስት ገበያ ሰው ይከተሰዋል እግባ መልስ ብሎ ቢጣላንሳ ብለው እሳቸው ከጲላጦስ ዘንድ ይዘው ይመጣሉ እሱ ከነሱ ተቀብሎ ይዞ መጥቷልና ፤

፵፰ ወዘያገብእ ወሀቦሙ ትእምርተ እንዘ ይብል ዘሰዓምኩ ውእቱ ኪያሁ አኃዙ ።

፵፰ የሚያሲዘው ይሁዳ የምስመው እሱ ነው እሱን ያዙ ብሎ ምልክት ሰጣቸው ፤ አንድም የሚሲዝበትን ምልክት ነገራቸው ።

፵፱ ወቀርበ ይእተ ጊዜ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወሰዓሞ ወይቤሎ በሀ ረቢ ።

፵፱ ወደ ጌታ ቀርቦ መምህር ቢሰኛሀን ጥለኛ ሀን እያውለው እያሳድረው ብሎ እጅ ነሳው ፤ ሐተታ ከሱን ሌላ ቢሰኛ ጠበኛ አለው እያውለኝ እያሳድረኝ ቢያሰኘው ነው ።
፶ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ በእንተ ዝንቱኑ መጻእከ እርከየ ።
፶ ወዳጄ ትእምርተ ፍቅሩን ትእምርተ ጸብእ አድርገኸው መጣህን አለው ።
ወእምዝ ቀርቡ ወእንሥኡ እደዊሆሙ ወአሐዝዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
እጃቸውን አንስተው ማለት ጌታን አጽንተው ያዙት ።
፶፩ ወናሁ ተንሥአ እምኀለ ምስሌሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ሰፍሐ እዴሁ ወመልሐ መጥባሕቶ ወዘበጠ ለገብረ ሊቀ ካህናት ።
፶፩ ከጌታ ጋራ ካሉት አንዱ ተነሥቶ ሰይፉን መዞ የሊቀ ካህናቱን ባሪያ መታው ።
ወመተሮ ዕዝኖ ዘየማን ፤
ቀኝ ጆሮውን ቆረጠው ፤ ትፈቅድኑ ንዝብጦሙ ብለውታል በሱቃስ አብሮ መብላት አብሮ ለመሞት እንጂ ነው እንበላቸው እንበላቸው ተብብለዋል ። እሱ ፈጣን ነውና መታው ቀኝ ጆሮውን ቆረጠው ከመታው እንገቱን እይለውም ቢሉ የካህን እጅ አያቀናምና ላንገቱ ያለው ለጆሮው ሆነ ። አንድም እንገቱን ብሎት ቢሆን በሞተ ነበር የጌታም ሞት ርትዕ በተባለ ነበርና ጆሮውንሳ ቢሉ በተአምራት ቀጥሎ ሰታል ፤ ጆሮ የቀጠለ አንገት መቀጠል ይሳነዋልን ብሎ ትንቢቱ ምሳሊው ሊፈጸም ትንቢት ለትትቀረጽ ይእቲ ዕዝን እንተ ኢትሰምእ ለውእቱ ነቢይ ተብሎ ተነግሯል ፤ ምሳሌም ወለእመ አጥረ ይከ ገብረ ዕብራዊ ቅንዮ ስድስተ ዓመተ ወበሳብዕ ዓም አግዕዞ በከንቱ ፤ ዕብራዊ ባሪያ ቢኖርህ በደመወዝ ገዝተህ በሰባተኛው ዓመት ገንዘብ ሳትስጥ

ነጻ አውጣው ትላለች አረት ፤ እሱ ግን የጌታዬ ባሕርዩ ተስማምቶኛል የመቤቴ እንጀራዋ ወጪ ጣፍጦኛል ነጻ መውጣቱ ይቅርብኝ ያለ እንደሆነ ከቤተ እግዚአብሔር ወስደህ ከመድረኩ አስተኝተህ ጆሮውን ተርትረህ አፍንጫውን ስቀህ እስከ ዕለተ ሞቱ ግዛው ትላለች አረት ፤ እንደዚህም ሁሉ በስባተኛው ሺህ ሰዲያብሎስ ከመገዛት ላወጣችሁ መጥቼ ነበር እናንተ ግን ካላችሁ በሥጋችሁ ቄጣር በነፍሳችሁ ዲያብሎስ ይመልጥንባችሁ ለማለት፤ ያውስ ቢሆን ግራይቱ አለመሆኑዋ ቀኝቱ መሆኑዋ ስለምን ቢሉ ከነገደ ይሁዳ የተወለዱ ቀኝ ቀኝ አካላቸውን እየተቀቡ መንግሥትን ከነገደ ሌዊ የተወለዱ ቀኝ ቀኝ አካላቸውን እየተቀቡ ክህነትን ገንዘብ ያደርጉ ነበር ክህነትንም መንግሥትንም እንዳሳለፈባቸው ለማጠየቅ በቀኝ ጆሮው ምትረትን አፀዘበት ።

፶፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አግብእ ለመጥባሕትከ ውስተ ቤታ ዘፍ ፱ ፣ ፮ ራዕ ፲፫ ፣ ፲ ።

፶፪ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ጴጥሮስን ሾተልህን ወደ አፎት ቀጣህን ወደ ትዕግሥት መልስ አለው ።
እስመ ኵሉሙ እለ መጥባሕተ ያነሥኡ በመጥባሕት ይመውቱ ።
በሾተል የገደሉ ሁሉ በሾተል ይሞታሉና ።

፶፫ ይመስለከሙ ዘኢይክል አስተብቍዖቶ ለአቡየ ከመ ይፈኑ ሊተ ዘይበዝኅ እም፲ቱ ወ፪ቱ ሠራዊተ መላእክት ።

፶፫ ካሥራ ሁለቱ ነገደ መላእክት የሚበዙትን ይልክልኝ ዘንድ አባቴን መለመን መማለድ የማይቻለኝ ይመስላችኋልን ፤

፶፬ መብሕቱ እፎ ይትፈጸም ወይበጽሕ ቃለ መጽሐፍ ዘይቤ ። ኢሳ ፶፫ ፣ ፲።

፶፬ ነገር ግን መጽሐፍ የተናገረው እንደምን ይደርሳል ይፈጸማል እኔ ካልሞትኩ ሲል ነው ።
እስመ ከመዝ ሀለዎ ይኩን ።
ይህ ይደረግ ዘንድ አለውና ።

፶፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለሕዝብ ሶቤሃ ከመ ሠራቂኑ ትዴግኑኒ መጻእክሙ በመጥባሕት ወበአብትር ተአኃዙኒ ። ሰቆ ኤር ፬ ፣ ፳ ማር ፲፬ ፣ ፵ ሉቃ ፳፪፡፶፬ ዮሐ ፲፰ ፣ ፳፬ ።

፶፭ ሌባን እግባ መልስ ብሎ ቢጸላንሳ ብለው ሾተል ጎመድ ይዘው በትኩስ ፍለጋ እንዲፈልጉት ሾተል ጎመድ ይዛችሁ ልትይዙኝ መጣችሁን አላቸው ።
ወዘልፈ እነብር ምስሌከሙ በምኵራብ ወእሜህር ዘመትር በምኵራብ ከናንተ ጋራ ሳስተምር እኖር ነበር ወኢአኃዝክሙኒ ።
ያን አልያዛችሁኝም ።

፶፮ ወዝ ኵሉ ዘኮነ ከመ ይብጻሕ ወይትፈጸም ቃለ ነቢያት ።

፶፮ ይህ ሁሉ የተደረገ ነቢያት የተናገሩት ነገር ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ነው ።
ወእምዝ ኃደግዎ ኵሎሙ አርዳኢሁ ወጐዩ ።
ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ ጥለውት ሸሹ ።

ዘከመ ቆመ ኢየሱስ በቅድመ ዓውድ ።

፶፯ ወእለ አኃዝዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወሰድዎ ኀበ ቀያፋ ሊቀ ካህናት ይትጋብኡ ጸሐፍት ።

፶፯ ወሊቃናት ። ጌታን የያዙት ግን ሽማግሎች ወደ ተሰበሰቡበት የካህናት አለቃ ቀያፋ ወዳለበት ይዘውት ሄዱ ፤

፶፰ ወተለዎ ጴጥሮስ እምርኁቅ እስከ ዓፀደ ሊቀ ካህናት ።

፶፰ ጴጥሮስ እስከ ካህናት አለቃ ቦታ ድረስ በሩቅ ተከተለው ።
ወቦአ ውሥጠ ወነበረ ምስለ ወዓልት ይርአይ ማኅለቅቶ ለነገር ።
የነገሩን ፍጻሜ ያይ ዘንድ እንዱን ቅጽር ገብቶ ተቀመጠ፤

፶፱ ወየኃሥሡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወሊቃናት ወኵሉ ዓውድ ስማዕተ ሐሰት በዘይስቅልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፶፱ ጸሐፍትና የካህናት አለቆች ሽማግሎችም ጌታን በሚገሉበት ነገር ይገሉት ዘንድ የሐሰት መሳክርት ይሹ ነበረ ።

፷ ወኢረከቡ ሎቱ ጌጋየ ።

፷ አላገኙበትም ።
ወመጽኡ ብዙኃን ስማዕተ ሐሰት ።
ብዙ የሐሰት ምስክሮች መጡ ወስኡ ቦቱ ነገረ ።
መርታት ተሳናቸው ማለት ነውር አጡበት ።
ወድኅረ መጽኡ ፪ቱ ።
ከዚህ በኋላ ዕውነተኞች ናቸው የሚባሉ ሁለት ሰዎች መጡ ።

፷፩ ወይቤሉ ይቤ ዝንቱ እክል ነሚቶቶ ለቤተ እግዚአብሔር ወበሣልስት ዕለት አኀንጾ ፣ ፪፲፱

፷፩ ይህ ቤተ መቅደስን አፍርሼ በሦስተኛው ቀን እንጸዋለሁ አለ አሉ ።

፷፪ ወተንሥአ ሊቀ ካህናት ወይቤሎ ኢትሰምዕኑ እንዘ መጠነዝ ያስተዋድዩከ እሉ ።

፷፪ ሊቀ ካህናቱ ተነሥቶ ይህን ያህል ሲያጣሉህ ሲያካስሱህ አትሰማምን አለው ።

፷፫ ወኢያውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፤

፷፫ ጌታ አልመለሰለትም ፤ ሐተታ ነገሩ ተርታ ቢሆንበት እንዳልፈራ ለማጠየቅ እንዳይቀርለት ያውቃልና ለጥብዓት ለትዕግሥት አብነት ለመሆን ።
ወይቤሎ ሊቀ ካህናት አመሐልኩከ በእግዚአብሔር

ሕያው ከመ ትንግረኒ እመ እንተሁ ውእቱ ክርስቶስ ወልዱ ለእግዚአብሔር ።
እስከ ክርስቶስ ተብሎ የተነገረልህ የሕያው የእግዚ አብሔር የባሕርይ ልጁ አንተ እንደሆንክ ትነግረኝ ዘንድ በሕያው እግዚአብሔር አማጽኜሀለሁ አለው ።

፷፬ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንተ ትቤ ። ማቴ.፲፮ ፥ ፳፯ ሮሜ ፲፬ ፥ ፲ ፥ ፩ ተሰሎ ፬፥፲፭ ።

፷፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ አንተ ትላለህ አለው ።
ወባሕቱ እብለክሙ እምይእዜሰ ትሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይነብር በየማነ ኃይል ።
ነበረ ካልኡ ብሎ የማን ብኋል እንጂ በክብር ሲል ነው ከእንግዲህስ ወዲህ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስን በእብ ዕሪና ታዩታላችሁ ፥ አንድም በየማነ ኃይል ዓለምን በማሳለፍ ኃይል ፥ ባለው ዕሪና ። ወይመጽእ በደመና ሰማይ ። በባሕርይ ክብሩ መጥቶ ታዩታላችሁ ። ሐተታ የደብረ ታቦር የዕርገት የምጽ አት ደመና የባሕርይ ክብሩ ነው ። አንድም በሥጋ ማርያም መጥቶ ፥ ስማይ ዳግሚት እንዲል ፥ አንድም በክበበ ትስብእት መጥቶ ።

፷፭ ወሠጠጠ አልባሲሁ ሊቃነ ካህናት ።
፷፭ በገዛ እጁ ፈጣሪዩን ላሰድብ ብሎ ሊቀ ካህናቱ ልብሱን ቀደደ ። ሐተታ በኃዘን ምክንያት ልብሱን የቀደደ ፊቱን የነጩ እንደሆን ይሻር ትላ ለች እሪት ፥ ጌታ እንደ ተሾመበት እሱ እንደተሻረ ለማጠየቅ ፥ እንዘ ይብል ምንተ እንከ ትፈቅዱ ሎቱ ሰማዕተ ።
ምን ምስክር ትሹለታላችሁ ፥ ናሁ ጸረፈ ።
ይሳደባል ማለት እነሆ አምላክ ነኝ አለ ።
ወሰማዕክሙ ጽርፈቶ ።
አምላክ ነኝ ሲል ሰምታችኋል ፤

፷፮ ምንተ እንከ ትብሉ ። ኢሳ.፶፥፮ ። ማር፥፲፬፥፷፭
፷፮ ምን ትፈርዳላችሁ ፤
ወአውሥኡ ወይቤሉ ዝንቱ ድልው ለሞት ።
ይህ ሞት ይገባዋል አሉ ።
፷፯ ወእምዝ ተፍኡ ውስተ ገጹ ።
፷፯ ከዚህ በኋላ በፊቱ ተፉበት ፥ ወይትህ ከዩ ወሪቀ ውስተ ገጽየ ።
ወኢሜጥኩ ገጽየ እምኃፍረተ ምራቅ ያለው ትንቢት ሊደርስ ሊፈጸም ። አንድም አዳምን ዲያብሎስ በገጸ ልቡናው ምራቀ ምክሩን እየተፋ ከገሃነም አውርዶት ነበርና ለሱ ካሣ ሊሆን ።
፷፰ ወኰርዕዎ ።
፷፰ ራሱን በዘንግ መቱት ። ወዝብጥ ርእስ ለሕማም ያለው ትንቢት ሊደርስ ሊፈጸም ። አንድም ዲያብሎስ የአዳምን ርእሰ ልቡናውን በዘንግ እየመታ ገሃነም አውርዶት ነበርና ካሣ ሊሆን ።
ወጸፍዕዎ ።

ፊቱን በሻሽ ሸፍነው መቱት እንዘ ይብሉ መኑ ውእቱ ክርስቶስ ዘጸፍዓከ ።
ክርስቶስ በጥፊ የመታህ ማነው ንገረን እያሉ ፥ ሐተታ፤አዳምና ሔዋን የአምላክነት ዕውቀት እን ወቅ ብለው ገሐነም ወርደው ነበርና ለሳቸው ካሣ ሊሆን ።

በእንተ ክህደተ ጴጥሮስ ።

፷፱ ወጴጥሮስ ሀሎ ይነብር አፍአ ውስተ ዓጸድ ሉቃ.፳፪፥፶፭፥፸፤ ዮሐ. ፲፰ ፥ ፲፯ ።

፷፱ ጴጥሮስ ግን አንዱን ቅጽር ገብቶ ተቀ ምጦ ነበር ፤
ወመጽአት ኀቤሁ አሐቲ ወለት ወትቤሎ እንተሂ ምስለ ኢየሱስ ገሊላዊ ሀለውከ ።
አንዲት ብላቴና መጥታ አንተም ከገሊላዊ ከኢየሱስ ጋራ ነበርክ አለችው ።

፸ ወክህደ በቅድመ ኵሉ ሕዝብ እንሰ ኢየ አምሮ ዘትብሊ ።
፸ የምትዪውን አላውቀውም ብሎ በጉባኤ ካደ ።
፸፩ ወወፂአ ኆኅተ ርእየቶ ካልዕት ወለት ።
፸፩ አንዱን በር ወጥቶ ሳለ ሌላዪቱ እየችው ።
ወትቤሎሙ ለእለ ይቀውሙ ዝኒ ሀሎ ምስለ ኢየሱስ ናዝራዊ ።
ተቀምጠው ላሉት ይህም ከናዝሬቱ ኢየሱስ ጋራ ነበር አለቻቸው ።
፸፪ ወክህደ ካዕበ ።
፸፪ ሁለተኛ ካደ ።
ወመሐለ ከመ ኢየአምሮ ለውእቱ ብእሲ ።
ያን ሰው እላውቀውም እንዳላውቀው ብሎ ማለ ፥
፸፫ ወጕንድዮ ሕቀ መጽኡ እለይቀውሙ ።
፸፫ ጥቂት ቆይቶ የተቀመጡት መጡ ።
ወይቤልዎ ለጴጥሮስ አማን አንተሂ እምኔሆሙ ።
እንተም በውነት ከሳቸው ወገን ነህ አሉት ።
ወነገርከ ያዔውቀከ ።
ባነጋገርህ ትታወቃለህ ።
፸፬ ወእምዝ መሐለ ወተረግመ ከመ ኢየአ ምሮ ለውእቱ ብእሲ ።
፸፬ የያዘውን ጥሎ እንዲህ ይጣለኝ የሱን ሞት ለኔ ያድርገው ያን ሰው አላውቀውም ብሎ ማለ ።
፸፭ ወተዘከረ ጴጥሮስ ቃሎ ለእግዚእ ኢየሱስ ዘይቤሎ ሥልሰ ትክህደኒ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ።
፸፭ ጴጥሮስም ጌታ ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ያለውን አሰበ ።
ወወፅአ አፍአ ወበከየ ብካየ መሪረ ።
ከአፍአ ወጥቶ ጽኑ ኃዘን አዘነ ፤ ሐተታ ከሁሉ ይልቅ እኔ እወደው ከሁሉ አስቀድሞ እኔ እክደው ብሎ አዘነ ። የአዳም የዳዊት የቅዱስ ጴጥሮስ ሐዘን አንድ ነው ሳይሰቀቁ ዕንባቸው እንደሰን ውኃ ይወርዳል ።

ምዕራፍ ፳፯ ።

፩ ወጸቢሖ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ወሊቃናተ ሕዝብ ይቅትልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፩ ሲነጋ በነጋ ጊዜ የካህናት አለቆች የሕዝቡም አለቆች ጌታን ሊገድሉት እንግደለው ብለው መከሩ ።

፪ ወአሰርዎ ወሰድዎ ወመጠውዎ ለጲላጦስ መኰንን ማር.፲፭ ፣ ፩ ሉቃ ፳፫ ፣ ፩ ዮሐ. ፲፰ ፣ ፳፰ ።

፪ አሰረው ወሰደው ለጲላጦስ ሰጡት ሐተታ አሰሮን ለመኰንን ዝንጉ አሳልፎ ሰጥቶ ነበርና ልቡ ኣዋ ሊሆን ።

ሬንተ ቀቢጸ ተስፋ ዘይሁዳ ።

፫ ወእምዝ ሶበ ርእየ ይሁዳ ዘአግብኦ ከመ አሰርዎ አግብኦ ውእተ ፴ ብሩረ ለሊቃነ ካህናት ወለሊቃውንተ ሕዝብ ።

፬ እንዘ ይብል አበስኩ ዘአግባእኩ ደመ ንጹሐ ወዘትትወልከ ብእሴ ጻድቀ ።

፫ ከዚህ በኋላ ያሲያዘው ይሁዳ አስርህዎ እን ጃጅውት አርስህዎ ኃጥእ ብለው እንደፈረዱበት ከመ ረሲዐ ወክመ ተኰነነ ኀጥእ ተብሎ እንደተ ፈረደበት ፤

፬ ባየ ጊዜ እሬት ኢትቅትል ብእሴ ጻድቀ ያለችውን አፍርሼ ንጹሕ ደም ያስፈሰስኩ ደግ ሰው ያስገደልኩ አበስኩ ብሎ ያን መባ ብር ለሊቃነ ካህናት ለሕዝብ አለቆች መልሶ ወስዶ ሰጠ ፤ ሐተታ እሬም በተአምራቱ ይድናል እያለ ገንዘቡን እንደ ያዘ አተረለሙ ብሎ ሸጦት ነበርና ።
ወይቤልዎ ሚ ላዕሌነ ወሚ ላዕሌከ ።
ይሉት የወደድነውን ሰጠኸን የወደድከውን ሰጠንህ ከእንግዲህ ወዲህ ካንተ ከኛ ምን አለህ ለኛስ ካንተ ምን አለን ።
ለሊከ አእምር ለርእስከ ።
አንተ ለራስህ ዕወቅ አሉት ።

፭ ወገደፈ ውእተ ብሩረ ውስተ ምኵራብ ወሖረ ወተሐንቀ ወሞተ ግብ. ሐዋ. ፩ ፣ ፲፰ ።

፭ ያን ብር ከምኵራብ ደጅ አፍሶት ሄዶ ታንቆ ሞተ ፤

፮ ወነሥኡ ሊቃነ ካህናት ውእተ ብሩረ ወይቤሉ ኢይደልወነ ንደዮ ውስተ ወርቀ መባዕ እስመ ሤጠ ደም ውእቱ ፤

፮ ሊቃነ ካህናት ያን ብር አንሥተው የደም ዋጋ ነውና ከመባዕ ልንጨምረው አይገባንም አሉ ። ሐተታ፤በህገራቸው የደም ዋጋ ሤጠ ከልብ አስበ ዶነስ ከመባዕ አያገቡም ነበርና ።

፯ ወተማከሮሙ ተሣየጡ ቦቱ ገራኅተ ለብሐዊ ለመቃብረ እንግዳ ፤

፯ ለመጣተኛ ለስደተኛ መቀበሪያ ሊሆን መከረው ቦታ ገዙበት ሐተታ ፤ ከጣኦት ከኃጢአት ፈልሶ ለመጣ መከበሪያ ሊሆን ምእመናን ጥምቀትን ገንዘብ ማድረጋቸውን መናገር ነው ፤

፰ ወተሰምየ ውእቱ ገራኅት ገራኅተ ደም እስከ ዮም ፤ ግብ. ፩ ፣ ፲፱ ።

፰ ያ ቦታ እስካሁን ድረስ የደም ምድር ሲባል ይኖራል ።

፱ ወይእተ አሚረ በጽሐ ቃለ ኤርምያስ ነቢይ ዘይቤ ነሥኡ ፴ ብሩረ ሤጦ ለክቡር ዘአክበርዎ እምደቂቀ እሥራኤል ወወሀብዎ ለገራኅተ ለብሐዊ ዘካ. ፲፩ ፣ ፲፪ ፤

፱ ደቂቀ እሥራኤል በሆሣዕና ያከበሩትን ከደቂቀ እስራኤል ተለይተው የክብርን ዋጋ ፤ አንድም ዘተከሀሉ ይላል ደቂቀ እሥራኤል የተስማሙበትን ለገራኅተ ለብሐዊ የሰጡትን የክብሩን ዋጋ ወሰዱ ብሎ ኤርምያስ የተናገረው ደረሰ ተፈጸመ ።

፲ በከመ አዘዘኒ እግዚአብሔር ፤
፲ ወወሀብዎ ለገራኅተ ለብሐዊ ማለትን እግዚአብሔር እንዳዘዘኝ እናገራለሁ አለ ፤ የማይገባ ማለት ነው ።
ዘከመ ቆመ እግዚእ ኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ፤

፲፩ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ቅድሜሁ ለመስፍን ማር. ፲፭ ፣ ፪ ሉቃ. ፳፫ ፣ ፫ ዮሐ. ፲፰ ፣ ፴፫ ።

፲፩ ጌታ ከጲላጦስ ፊት ቆመ ።
ወሐተቶ ወተስእሎ መስፍን ።
ጲላጦስ ጠየቀው ።
ወይቤሎ አንተኑ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሣቸው አንተ ነህን አለው ።
ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንተ ትቤ ።
አንተ ትላለህ አለው ። አንድም አንተ ያንድ መንደር ንጉሥ ታደርገኛለህ ።

፲፪ ወእንዘ ያስተዋድይዎ ሊቃነ ካህናት ወሊቃውንተ ሕዝብ አልቦ ዘያወሥአሙ ወኢምንተኒ ።
፲፪ የሕዝቡ አለቆችና የካህናት አለቆች ሲያሳጡት ሲያጣሉት ምንም ምን የመለሰላቸው ምላሽ የለም ።

፲፫ ወእምዝ ይቤሎ ጲላጦስ ኢትሰምዖኑ እንዘ መጠነዝ ያስተዋድዩከ ።
፲፫ ይህን ያህል ሲያሳጡህ ሲያካስሱህ አትሰማምን አለው ።

፲፬ ወኢያውሥአ ወኢአሐተኒ ቃለ ፤
፲፬ ጥቂት ስንኳን አልመለሰለትም ሐተታ እንዳለፈው ።
እስከ ያነክር መልአክ ።
ጲላጦስ ይህን ያህል ትዕግሥት ብሎ እስኪያደንቅ ድረስ ።

ዘከመ ኃረይዎ ለበርባን እምነ ኢየሱስ ወከመ ኰነንዎ ።

፲፭ ወቦ ልማድ ለመስፍን ያሕዩ ለሕዝብ ፩ደ እምውስተ ሙቁሓን ዘፈቀዱ ።

፲፭ ከታሰሩት የወደዱትን ይፈታላቸው ዘንድ ለጲላጦስ ልማድ ነበረው ። አንድም በሙ ልማድ ይላል ባመት ባመት ለበዓለ ፋሲካ ክስር ቤት ገብ ተው የወደዱትን ይፈቱ ዘንድ ለሕዝቡ ልማድ ነበራቸው ።
ሐተታ፣በግብጽ ሳሉ ሁለት እስሮች ነበሯቸው እነ ዚያን ፈተው ይዘው ወጥተዋልና ፤ በግብጽ ሳሉማ ምን እስር ነበራቸው ብሎ በግብጽ መኖራቸውን እንደ መታሰር ፤ ከግብጽ መውጣታቸውን እንደ መፈታት አድርገውት በበዓል አንድ አንድ እስር ይፈቱ ነበርና በዚያ ልማድ ።

፲፮ ወቦ አሜሃ ሙቁሕ ዘስሙ በርባን ስሙዕ
፲፮ ያን ጊዜ በርባን የሚባል የታወቀ እስር ነበር ።
ወየአምሮ ኵሉ ።
ወንበዴ መሆኑን ሁሉ ያውቀዋል ።

፲፯ ወእንዘ ጉቡኣን እሙንቱ ይቤሎሙ ጲላ ጦስ ለሕዝብ መኑ ትፈቅዱ አሕዩ ለክሙ ።
፲፯ እሳቸው ባንድነት ተሰብስበው ሳሉ ማን ልፈታላችሁ ትወዳላችሁ ?
በርባንሃኑ ።
በርባንን ነውን ።
ወሚመ ኢየሱስሃኑ ዘይብልዎ ክርስቶስ ።
ወይም ክርስቶስ የተባለ ኢየሱስን ነው አላቸው ።

፲፰ እስመ የአምር ከመ በቅንዓቶሙ አግብእዎ
፲፰ ጠልተው ተመቅኝተው ቀንተው ለሕማም ለሞት አሳልፈው እንደሰጡት ያውቃልና ።

፲፱ ወእንዘ ይነብር ጲላጦስ ዓውደ ለአከት ኀቤሁ ብእሲቱ ።
፲፱ ባደባባይ ተቀምጦ ነገር ሲሰማ ሚስቱ ላከችበት አብሮቅላ ትባላለች ።
እንዘ ትብል ኢቅአ ኢትእብስ ላዕለ ውእቱ ጻድቅ ።
ያን ደግ ሰው እንዳትበድል አስተውል ብላ ።
እስመ ብዙኃ ሐመምኩ በዛቲ ሌሊት በሕልምየ በእንቲአሁ በዚች ሌሊት በሱ ምክንያት በሕልሜ ብዙ ሥቃይ ሳይ አድሬአለሁና ። ሐተታ ምን ስታይ አድራለች ቢሉ እሱን ዘንዶ ሲውጠው እሷን በእ ሳት አለንጋ ሲገርፏት አይታለች ይህን ልካበታለች ፤ አብረው አድረው አልነበረም ቢሉ እነግረዋለሁ ስትል እንበሳ መደብ ወጣ ሲመለስ እነግረዋለሁ ስትል ጨኸት ሰምቶ ወጣ በዚያው እንደወጣ ቀር ቷል ። አንድም ዶርታ መከራ የሚባሉ ከተወለዱ ጀምሮ ተናግረው ሰምተው የማያውቁ ልጆች ነበ ሯቸው ንጹሕ ደም ለሚያፈስ ለዚያ ለባልሽ ወዮለት ብለዋታል ይኸን ልካበታለች ።

፳ ሊቃነ ካህናትሰ ወሊቃውንተ ሕዝብ ጔጕ ዎሙ ለሕዝብ ወአሆ አበልዎሙ ከመ በርባንሃ ያሕዩ ሎሙ ይስአሉ ወኢየሱስሃ ይቅትሉ ማር ፣ ፲፭ ፣ ፲፮ ሉቃ ፳፫ ፲፯ ዮሐ ፲፰ ፡ ፴፱ ግብ ፡ ሐዋ ፡ ፫ ፡ ፲፬ ።

፳ የሕዝቡ አለቆችና ሊቃነ ካህናት ግን በር ባንን አድንልን ኢየሱስን ስቀልልን ብለው ይለምኑ ዘንድ ሕዝቡን አባበሏቸው እሺ በጂ አሰኙዋቸው ።

፳፩ ወአውሥአ መስፍን ወይቤሎሙ መነ ትፈቅዱ እምክልኤሆሙ አሕዩ ለክሙ ።

፳፩ ጲላጦስ መልሶ ከሁለቱ ማናቸውን ላድን ላችሁ ትወዳላችሁ አላቸው ።
ወይቤሉ በርባንሃ ።
በርባንን ነው አሉ ።

፳፪ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ምንተ እንከ እሬስዮ ለኢየሱስ ዘተብህለ ክርስቶስ ።

፳፪ ክርስቶስ የተባለ ኢየሱስን ምን አደር ገዋለሁ ። አንድም እረስዮ ይላል ምን ላድርገው አላቸው ።
፳፫ ወይቤሉ ኵሎሙ ስቅሎ ።
፳፫ ሁሉም ስቀለው አሉ ።
ወይቤሎሙ መስፍን ምንተ እኩየ ገብረ ።
ምን ክፉ ሥራ ሠራ አላቸው ።
ወአፈድፈዱ ጸሪሃ እንዘ ይብሉ ስቅሎ ስቅሎ ።
ስቀለው ብንልህ ስቀለው አሉ ።
፳፬ ወእምዝ ሶበ ርእየ ጲላጦስ ከመ አልቦ ዘይበቍዕ ዘእንበለ ዳዕሙ ዘይበዝኅ ሀከክ ።
፳፬ ጸብዕ ክርክር እየጸና ከመሄድ በቀር የሚ ረባው የሚጠቅመው ነገር እንደሌለ ጲላጦስ ባየ ጊዜ ነሥአ ማየ ወተሐፅበ እደዊሁ በቅድሜሆሙ ለሕዝብ እንዘ ይብል ንጹሕ አነ እምደሙ ለዝ ብእሲ ጻድቅ ። ውኃ አስመጥቶ በዚህ ሰው ደም ከመጣ ፍዳ ንጹሕ ነኝ ብሎ ባደባባይ እጁን ታጠበ በአዕሩገ እስራኤል ልማድ ፤ ታሪክ ከሀገርና ከሀገር መካከል ሰው ሙቶ የተገኘ እንደሆነ ያሰው ለሞተበት አቅራቢያ ለሚ ሆን አገር ሰዎች ውኃ በመንቀል ይዘው ጊደር ነድተው ከበረሃ ይወርዳሉ ቋንጃዋን ይመቷታል ትወድቃለች የዚህን ሰው ደም አላፈሰስንም ያፈሰሰውንም አላየንም ብለው ይታጠባሉ ከገ ዳዩ ወገን ሲደርስ መወየብ ይጀምራል እሱ ሲሆን ፈጽሞ ደም ይሆንበታል ፤ ምእመናን ጥም ቀትን ገንዘብ ማድረጋቸውን መናገር ነው ።
አንትሙ ለሊክሙ አእምሩ ።
እናንት ለራሳችሁ ዕወቁ ።

፳፭ ወአውሥኡ ኵሉ ሕዝብ ወይቤሉ ደሙ ላዕሌነ ወላዕለ ውሉድነ ፤

፳፭ ደሙ በኛም በልጆ ልጆቻችንም ይሁን አሉ ፤ ሐተታ እንዲህ ብለው የተናገሩበት እንደበ ታቸው የሚሸት የሚከረፋ ሁኑዋል ልጆቻቸውም ወንድ የሆነ እንደሆነ በጁ ደም ጨብጦ ባፉ ደም ጎርሶ የሚወለድ ሁኑዋል ሴት የሆነች እን ደሆነ በተፈትሆ የምትወለድ ሁናለች ።

፳፮ ወእምዝ ኣሕየወ ሎሙ በርባንሃ ።
፳፮ ከዚህ በኋላ በርባንን ፈታላቸው ።
ወቀሥፎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወመጠዎሙ ይሰቅልዎ ገረፎ ገርፎ ስቀሉ ብሎ ሰጣቸው ። ሐተታ ካልቀረበ ገር ጆሴ ይበላቸው ብሎ ። እንድም ራርተው ይተ ውታል መስሎት ። እንድም ወመጠዎሙ ዘባንየ ለቅሥፈት ያለው ትንቢት ሊደርስ ሊፈጸም እን ድም ዲያብሎስ የአዳምን ዘባነ ልቡናውን እየገረፈ ገዝነም አውርዶት ነበርና ለዚያ ካሳ ሲሆን እንድም በጌታ የግፍ ድርብ ይደረግበታልና ለልማዱ የሚ ሰቀል አይገረፍም የሚገረፍ አይሰቀልም ነበር ። እሱን ግን ገርፈው የሚሰቅሉት ነውና ።

ዘከመ ተሣለቁ በላዕለ ኢየሱስ ።

፳፯ ወእምዝ መስተራትዓቱ ሐራ ነሥእዎ ለእ ግዚእ ኢየሱስ እምውስተ ዓውድ ወወሰድዎ ኀበ ምኵናን ። መዝ ፳፩ ፣ ፲፯ ማር ፲፭ ፣ ፲፯ ።
፳፯ ከዚህ በኋላ ጭፍራውን የሚመሩ የሚያ ቅናኑ ካደባባይ ወደሚፈረድበት ቦታ ይዘውት ሄዱ ። ሐተታ ቤተ እንግላ ቤተ እጄቀ ባለወገች የሚባሉ ሲታይ ቀራጭ ባለወገች በቤተ መንግሥት እንዳሉ ። ወአስተጋብኡ ኵሎ ሠርዌ ሐራ አለቆች ጭፍራ ቸውን ሰበሰቡ እንድም ኵሎ ሠርዌ ሐራ ጭፍሮች አለቆችን ፤ እንድም ወአስተጋብኡ ኵሎ ሠርዌ ሐራ ብለህ እናበህ ፤ ጭፍሮች ያሏቸው አለቆች ሕዝ ቡን ሰበሰቡ ።
ወሰለብዎ አልባሲሁ ።
ልብሱን ገፈፉት ።
ሐተታ፤የአዳም ልጅነት እንደሄደበት ያጠይቃል ።
፳፰ ወአልበስዎ ከለሜዳ ዘለይ ።
፳፰ ቀይ ግምጃ አለበሱት ፤ ደምህ ይፈሳል ሲሉ ። እንድም ደማችንን ባርባ ዘመን በጥጦስ ታፈስዋለህ ሲሉ ።
፳፱ ወጸፈሩ ሐራ አክሊለ ዘሦክ ወአስተቀ ጸልዎ ዲበ ርእሱ ። ዮሐ ፲፱ ፣ ፪
፳፱ ጭፍሮች የሾህ አክሊል ታተው ደፉለት ሐተታ፣እነገሥንህ ብለውታልና በፍና ተሣልቆ ። እንድም ወወደዩ ጌራ መድኃኒት ዲበ ርእሱ በአክ ሊል ዘአስተቀጸለቶ እሙ ያለው ትንቢት ሊደርስ ሊፈጸም ድርሳነ መድኃኔ ዓለም ሽህ ጥቃቅን ስባ ታላላቅ እሾህ ያለው የብረት ዘውድ ነው ይላል እንደምን ነው ቢሉ ነገር እንደዚህ ነው ያለ ቢሆን ኢትስብሩ ዓፅሞ ያለው በፈረሰ ነበር ።

ወአስተእኃዝዎ ህለተ ውስተ የማኑ ።
በቀኝ እጁ ዘንግ አስያዙት እነገሥንህ ብለውታልና በፍና ተሣልቆ ፤ እንድም ብርዒ ይላል አብነት ፤ ብርዕ አስያዙት ሥራ ፈት ነህ ሲሉ ጽሕፈትንማ ርእስ ጥበባት እንጅ ይለዋል ብሎ ኃጢአታችንን በፍዳ ታጽፍብናለህ ሲያስኛቸው ነው ።
ወአስተብረኩ ቅድሜሁ ፤
ሰገዱለት ፤
ወተሣለቁ ላዕሌሁ ፤
ዘበቱበት ፤
ወይቤልዎ በሀ ንጉሠ አይሁድ ፤
የአይሁድ ንጉሣቸው ቢሰኛህን ጠበኛህን እያውለው እያሳድረው አሉት ከነሱ ሌላ ቢሰኛ ጠበኛ አለውን እያውለን እያሳድረን ሲያስኛቸው ነው ።

፴ ወይወርቁ ላዕሌሁ ።
፴ በፊቱ ተፉበት ።
ሐተታ እንዳለፈው ።
ወነሥኡ ህለተ ወኰርዕዎ ርእሶ ።
ያስያዙትን ዘንግ ተቀብለው ራሱን መቱት ፤ ሐተታ እንዳለፈው

፴፩ ወተሣሊቆሙ ላዕሌሁ ሰለብዎ ውእተ ከለ ሜዳ ዘለይ ፤

፴፩ ከዘበቱበት በኋላ ያለበሱትን ቀይ ግምጃ ገፈፉት ።
ወአልበስዎ አልባሲሁ ።
የጥንት ልብሱን አለበሱት የአዳም ልጅነት እንደ ተመለሰለት ያጠይቃል ።
ወወሰድዎ ይሰቅልዎ ።
ሊሰቅሉት ይዘውት ሄዱ ።

፴፪ ወእንዘ ይወጽኡ ረከቡ ብእሴ ቀሬናዌ ዘስሙ ስምዖን አትወቶ እምሐቅል ። ማር ፲፭ ፣ ፳፩ ሉቃ ፳፫ ፣ ፳፮ ።
፴፪ ሊሰቅሉት ይዘውት ሲሄዱ ስምዖን የሚ ባል የቀሬናዮ ሰው ከተሠወረበት ሲመለስ አገኙ ፤
ወአበጥዎ ይጹር መስቀሎ ፤
መስቀሉን ይሸከም ዘንድ ነተቱት ፤ ሐተታ ነገር ፈርቶ ተሰውሮ ውሏል ነገር ተፈጽሟል ብሎ ሲወጣ አገኙት አንተም የሱ ወገን ነህ መስቀሉን ተሸከም ብለው አሸከመውታል ፤ ምሥጢሩ ግን ጌታ ከበ ረከተ መስቀሉ እንዳሳተፈው ያጠይቃል ፤

፴፫ ወበጺሖሙ ብሔረ ዘስሙ ጎልጎታ ዘበ ትርጓሜሁ ቀራንዮ ። ማር ፲፭ ፣ ፳፪ ሉቃ ፳፫ ፣ ፴፫ ዮሐ ፲፱ ፣ ፲፯ ።
፴፫ ባንዱ ልሳን ቀራንዮ ወደሚሉት ጎልጎታ በደረሱ ጊዜ ።
፴፬ ወወሀብዎ ይስተይ ወይነ ወሐሞተ ድሙረ ፤
፴፬ ሐሞት የተቀላቀለበት ወይን ይጠጣ ዘንድ ሰጡት ፤

ወጥዒሞ አበየ ሰትየ ።
ቀምሶ አልጠጣም አለ ።

ዘከመ ተሰቅለ ኢየሱስ

፴፭ ወእምዝ ሰቀልዎ ማር ፲፭ ፥ ፳፬ ሉቃ ፳፫ ፥ ፴፫ ዮሐ ፲፱ ፥ ፲፰ ። መዝ ፳፩ ፥ ፲፰ ።

፴፭ ከዚህ በኋላ ሰቀሉት ።
ወተካፈሉ አልባሲሁ እንዘ ይትዓፀው ።
ልብሱን በዕፃ ተካፈሉ ፤
በከመ ጽሑፍ ወተካፈሉ አልባስየ ለርእሶሙ ወተዓፀው ዲበ አራዝየ ተብሎ በነቢይ እንደ ተጻፈ ፤

፴፮ ወነበሩ የዓቅብዎ ህየ ፤
፴፮ ሲጠብቁት ዋሉ ፤
፴፯ ወአንበሩ መልዕልተ ርእሱ ጽሒፎሙ መጽሐፈ ጌጋዩ ዘይብል ኢየሱስ ናዝራዊ ንጉሦሙ ለአይሁድ ፤

፴፯ የናዝሬቱ ኢየሱስ የአይሁድ ንጉሣቸው ነው የሚል በደሉን የሚናገር ደብዳቤ ከራሱ በላይ ከመስቀሉ ትርፍ ጠርቀው ተውት ፤

፴፰ ወእምዝ ሰቀሉ ምስሌሁ ፪ተ ፈያተ ፤
፴፰ ከዚህ በኋላ ሁለት ወንበዶች ከሱ ጋራ ሰቀሉ ፤
አሐደ በየማኑ ፤
አንዱን በቀኙ ፤
ወአሐደ በፀጋሙ ፤
አንዱን በግራው አነገሥንህ ብለውታልና በፍና ተሣልቆ ፤ ሐተታ ቀኛዝማችና ግራዝማች ቢትወደድ ግራ ቢትወደድ ሾምንልህ ሲሉ አንድም ለማሳሳት በቀኝ በግራ የመጣው ያ ምንድነው ወንበዴ ይሉታል ያሳ የመካከለኛው ይላል ያስ ከዚህን ልዩ ነው ለማለት አንድም ተኈለቆ ምስለ ጊጉያን ያለው ትንቢት ሊደርስ ሊፈጸም ፤ ይህንም ሊቁ ከመ ይደምሬነ ምስለ ነፍሰ ጻድቃን ብሎ ተርጕሞታል ምሥጢሩን ግን እኛን ኃጥአንን በግራ ታቆመናለህ ሲያስኛቸው ነው ፤

፴፱ ወእለሂ የኃልፉ ይፀርፉ ላዕሌሁ እንዘ የሐውሱ ርእሶሙ ፤
፴፱ የሚያልፉ የሚያገድሙት ራሳቸውን እየ ነቀነቁ ይሰድቡት ነበር ።
፵ ወይብሉ ኦ ዘይነስቶ ለቤተ መቅደስ ወየሐንጾ በሣልስት ዕለት አድኅን ርእሰከ ዮሐ ፪ ፥ ፲፱ ።
፵ ቤተ መቅደስን አፍርሰህ በሦስተኛው ቀን እሰራዋለሁ የምትል ራስህን አድን እያሉ ።
እመሰ አማን ወልደ እግዚአብሔር አንተ ረድ እመ ስቀልከ ።
የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንክ ከመስቀልህ ውረድ ።
፵፩ ወከማሁ ሊቃነ ካህናት ይሣለቁ ምስለ ጸሐፍት ወሊቃናት ።

፵፩ እኒያ እንደሰደቡት ሊቃነ ካህናትም ከጸሐፍትና ካሰቆች ጋራ ሰደቡት ።

፵፪ እንዘ ይብል ባዕደ ያድኅን ወርእሶ ኢይክል አድኅኖ ፤

፵፪ ሌላውን ያድናል ራሱን ማዳን አይቻለውም እያሉ ። ማቴ ፪ ፥ ፲፰ ።
እመሰ ንጉሠ እሥራኤል ውእቱ ለይረድኬ ይእዜ እምነ መስቀሉ ንርአይ ወንእመን ቦቱ ።
የእሥራኤል ንጉሥ ከሆነ ከመስቀሉ ይውረድና አይተን እንመንበት ። ሐተታ ወርዶም ቢሆን ፈርቶ ነው ባሉ ነበር እንጂ ባላመኑትም ነበር ። ሶበሰ ወረደ እግዚእነ እምነ መስቀሉ እመርህ ከመ ውእቱ ፈርሀ እሞት እንዲል ።

፵፫ እመሂ ተአመነ በእግዚአብሔር ናሁ ይእዜ ያድኅኖ ፤ መዝ ፳፩ ፥ ፰ ።

፵፫ በእግዚአብሔር ከታመነ ማለት የእግዚአብሔር ልጅ ከሆነ እነሆ ዛሬ ያድነው ።
አመ ይፈቅዶ ።
ስንኳን ይወልደው ይወደው እደሆነ ።
እስመ ይብል ወልደ እግዚአብሔር አነ ።
የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ ይላልና ።

፵፬ ወከማሁ ፈያትኒ እለ ተሰቅሉ ምስሌሁ ይዘነጕግዎ ።

፵፬ እነዚያ እንደሰደቡት ከሱ ጋራ የተሰቀሉ ወምበዶችም ሰደቡት ፈያታይ ዘየማንም ቢሉ ፀሐይን አይቶ እስኪመለስ ድረስ ጥቂት ጥቂት ያደራርግ ነበር ።

በእንተ ጻዕሩ ወሞቱ ለኢየሱስ

፵፭ ወእምስሱ ሰዓት ጸልመ ኵሉ ዓለም እስከ ተሱዓት ሰዓት ፤

፵፭ ከቀትር እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ ጨለማ ሆነ ።

፵፮ ወጊዜ ተሱዓት ሰዓት ጸርሐ እግዚእ ኢየሱስ በቃል ዓቢይ ። መዝ ፳፩ ፥ ፩
፵፮ በዘጠኝ ሰዓት ጊዜም ጌታ አሰምቶ ተናገረ ፤
እንዘ ይብል ኤሎሄ ኤሎሄ ኤልማስ ለማ ሰበቅታኒ ዝውእቱ ብሂል አምላኪየ አምላኪየ ለምንት ኀደገኒ ፤
ኤሎሄ ኤሎሄ ያለውን አምላኪየ አለው ኤልማስ ያለውን ለምንትኑ አለው ሰበቅታኒ ያለውን ኀደገኒ ብሎ ተረጕመው አምላኪየ አምላኪየ ለምንት ተዉከኝ አለ ኃደገ ብየ ሲል በኀዱጋኑ ተገብቶ ይጸልያል ።
፵፯ ወሰሚዖሙ እለ ይቀውሙ ይቤሉ ኤልያ ስሃ ይጼውዕ ዝሰ ።
፵፯ ከዚያ ቆመው ያሉት ኤሎሄ ኤሎሄ ሲል ሰምተው ይህስ ኤልያስን ይጠራል አሉ ።

፵፰ ወውእተ ጊዜ ሮጸ ፩ እምኔሆሙ ወነሥአ ሰፍነገ ወመልአ ብሒአ ወአሰረ ውስተ ህለት ወአሰ አዘዞ ውስተ አፉሁ ወአስተዮ ።

፵፰ ያን ጊዜ ከሳቸው አንዱ ፈጥኖ ሰፍነግ ወሰደ መጣጣውን መልቶ በዘንግ አስሮ አጠጣው ሐተታ፤ሰፍነግ የጁህ ባዘቶ እንደ ዓይነ በጐ ያለ ውኃ የሚያነግ ቤት የሚጠርጉበት ነው ።

፵፱ ወቦ እለ ይቤሉ ኅድጉ ንርአይ ለእመ ይመጽእ ኤልያስ ያድኅኖ ።

፵፱ ኤልያስ መጥቶ ያድነው እንደሆነ ተውት እንይ ያሉ አሉ ።

፶ ወጸርሐ እግዚእ ኢየሱስ በዓቢይ ቃል ።
፶ ጌታ አሰምቶ ተናገረ ።
ወመጠወ ነፍሶ ወወፅአት መንፈሱ ሶቤሃ ፤
ቅድስት ነፍሱ ከሥጋው ተለየች ።
ወመጽአ ፩ ወነሥአ ኲናተ ወረገዞ ገቦሁ ወውኅዘ ደም ወማይ ።
ቆመው ካሉት አንድ ሰው ጦሩን አንሥቶ ጎኑን ወጋው ወኃና ደም ሳይቀላቀል ፈሰሰ ።

፶፩ ወተሠጠ መንጦላዕተ ቤተ መቅደስ እም ላዕሉ እስከ ታሕቱ ፪ ጎጼጾን ፫፣ ፲፱ ።
፶፩ የቤተ መቅደስ መጋረጃ ከላይ እስከ ታች ተቀደደ ።
ወኮነ ፪ኤ ክፍለ ።
ክሁለት ተከፈለ ።
ወመጽአ መልአክ ኀሩይ እማእከለ ኵሎሙ መላእ ክት እንዘ ይእኅዝ በእዴሁ ሰይፎ ክሡተ ክመ ያጥ ፍዖሙ ለዓላውያን ፍጡነ ወሰበ ከልዓዮ ምሕረቱ ለክርስቶስ ዘበጦ ዝኩ መልአክ በሰይፉ ለመንጦላ ዕተ ምኵራብ ወሠጠጦ ወረሰዮ ፪ተ እምላዕሉ እስከ ታሕቱ እንዲል ኖራውን ስነጠቀው ፤ አንድም አን ዱን ዘሀ ክሁለት አደረገው ።
አድለቅለቀት ምድር ።
ምድር ተናወጠ መርገመ ሥጋ ጠፋ ።
ወነቅዓ ኰኵሕ ።
እዕባን ተፈተቱ መርገመ ነፍስ ጠፋ ።
፶፪ ወተከሥቱ መቃብራት ።
፶፪ መቃብራት ተከፈቱ ሙስና መቃብር ጠፋ ።
ወተንሥኡ ብዙኃን አብድንቲሆሙ ለጻድቃን ።
የብዙ ጻድቃን በድን ማለት አምስት መቶ ሙታን ከመስቀል እግር ተነሡ ።
፶፫ ወቦኡ ውስተ ሀገር ቅድስት እምድኅረ ተንሥአ ።
፶፫ ከተነሣም በኋላ ወደቅድስት ሀገር ወደ ኢየሩሳሌም ገቡ ።
ወአስተርአይዎሙ ለብዙኃን ።
ለብዙ ሰዎች ታዩዋቸው እለ ለዘመዶቻቸው ሦስቱን ቀን ወዴት ኑረው ቢሉ በደብረ ዘይት ።

፶፬ ወመኰንንሰ ፻ሲ ወእለ ምስሌሁ የዓቅብዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ርእዮሙ ውእተ ድልቅልቀ ፈርሁ ጥቀ ።
፶፬ የመቶ አዝማች ከሱም ጋራ ጌታን ሲጠ ብቁት የዋሉት መናወጡን ማለት የተደረገውን ተአምራት ባዩ ጊዜ ፈጽመው ፈሩ ።
ወይቤሉ አማን ወልደ እግዚአብሔር ውእቱ ።
ፀውነት የእግዚአብሔር ልጅ ነው ።
፶፭ ወሀለዋ ህየ ብዙኃት አንስት እለ ይሬእያ እምርኁቅ ኵሎ ዘኮነ
፶፭ ከዚያም የተደረገውን ሁሉ ርቀው የሚያዩ ብዙ ሴቶች ነበሩ ወውእቶን እለ ተለዋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ እምገሊላ ።
እሳቸውም ኢየሱስን ከገሊላ የተከተሉት ፤
እለ ይትለአካሁ ።
የሚያገለግሉት ናቸው ።
፶፮ ወእማንቱ ማርያም መግደላዊት ፤
፶፮ ብዙ ሴቶችም የተባሉ ማርያም መግደላዊ ናት መግደሎን ይባላል አገሯ ።
ወማርያም እመ ያዕቆብ ወእሙ ለዮሳ ፤
የዮሳና የያዕቆብ እናት ናት ።
ወእሞሙ ለደቂቀ ዘብዴዎስ ።
የዘብዴዎስ ልጆች እናት ማርያም ባውፍልያ ናት ።

ዘከመ ተቀብረ ኢየሱስ ።

፶፯ ወመስዮ መጽአ ብእሲ ባዕል እምአርማ ትያስ ዘስሙ ዮሴፍ ።
፶፯ ሲመሽ በመሸ ጊዜ ዮሴፍ የሚባል ባለጸጋ ሰው መጣ ።
ወውእቱ ይፀመዶ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ከጌታ ዘንድ ይማር ነበር ።
፶፰ ወሖረ ኀበ ጲላጦስ ወሰአለ ሥጋሁ ለእግ ዚእ ኢየሱስ
፶፰ ከጲላጦስ ሂዶ ፣ የጌታን ሥጋ ላውርድ ብሎ ለመነ ፤
ወአዘዘ ጲላጦስ የሀብዎ ።
ጲላጦስ ስጡት ብሎ አዘዘ ።
፶፱ ወነሢኦ ሥጋሁ ዮሴፍ ገነዞ በሰንዱናት ንጹሕ ።
፶፱ ዮሴፍ ሥጋውን አውርዶ በድርብ በፍታ ገነዘው ።
፷ ወቀበሮ ውስተ መቃብር ሐዲስ ዘሎቱ አው ቀረ ውስተ ኰኵሕ ።
፷ ለራሱ ብሎ ባሳነጸው ባዲስ መቃብር ቀበ ረው ። ሐተታ እንግዳ ሥራ እሠራላችኋለሁ ሲል ። አንድም እንደ ኤልሳዕ ገባሬ ተአምራት ነቢይ በተቀበረበት እንጂ ቢቀበር አስነሣው እንዳይሉ ። ወአንኰርኰረ እብነ ዓቢየ ዲበ ኆኅተ መቃብር ወኃ ለፈ ።
ታላቅ ደንጊያ አገላብጦ መቃብሩን ገጥሞት ሄደ ።

፷፩ ወሀለዋ ህየ ማርያም መግደላዊት ወካል ዕታኒ ማርያ ይነብራ ኀበ መቃብር ።

፷፩ ማርያም መግደላዊት ማርያም ባውፍልያ ከመቃብሩ ፊት ለፊት ተቀምጠው ነበር ።

፷፪ ወበሳኒታ እንተ ይእቲ እምድኅረ ዓርብ ተጋብኡ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን ኀበ ጲላጦስ ።
፷፪ ያችም ከዓርብ ቀጥላ ናት በነጋው ቅዳሜ ፈሪሳውያንና ሊቃነ ካህናት ወደጲላጦስ ተሰብስበው
፷፫ ወይቤልዎ ተዘከርነ እግዚኦ ዘይቤ ዝኩ መስሐቲ እመ ሕያው ውእቱ እመ ሣልስት ዕለት እትነሣእ ።

፷፫ ያመስሐቲ በሕይወተ ሥጋ ሳለ በሦስተኛው ቀን እነሣለሁ ያለውን እናውቃለንና ።
፷፬ አዝዝ እንከ ይዕቀቡ መቃብሪሁ እስከ ሠሉስ መዋዕል ከመ ኢይምጽኡ አርዳኢሁ ወኢይሰርቅዎ ሌሊተ ወኢይበሉ ለሕዝብ ተንሥአ እምነ ሙታን ።
፷፬ ደቀ መዛሙርቱ መጥተው ሌሊት ሰርቀው ከሙታን ተለይቶ ተነሣ ብለው ለሕዝቡ እንዳያስተምሩ መቃብሩን እስከ ሦስት ቀን ይጠብቁ ዘንድ እዘዝ አሉት ።
ወትከውን ደኃሪተ ጌጋዩ እንተ ተአኪ እምቀዳሚት ።
የኋላ ስህተቱ ከቀደመው የጸና ይሆናል ።
፷፭ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ንሥኡ ሠገራተ ሑሩ ወእጽንዑ መቃብሪሁ በከመ ተእምሩ ።
፷፭ ጲላጦስም ጭፍራ ወስዳችሁ እንደምታውቁ አጽንታችሁ አስጠብቁ አላቸው ።
፷፮ ወሖሩ ወአጽንኡ ወቀተሩ መቃብሮ ።
፷፮ ሂደው አጽንተው መቃብሩን ቈለፉት ።
ወኃተምዋ ለይእቲ እብን ምስለ ሠገራት ።
ጭፍራውን ይዘው ቈለፉ ። ሐተታ በህልቀቱ ወበህልቀተ መገብቱ እንዲል ተጠራጥረዋል እሱ እሳቸውን ጠርጥሯቸዋልና በማተሚያው ያትማል እሳቸው እሱን ጠርጥረውታልና በማተሚያቸው ያትማሉ ።

በእንተ ትንሣኤሁ ለኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፳፰ ።

፩ ወሠርከ ሰንበት ለጸቢሐ እሑድ መጽአት ማርያም መግደላዊት ወካልዕታኒ ማርያም ይርአያ መቃብረ ። ማር ፲፮ ፡ ፩ ዮሐ ፳ ፡ ፲፩ ።
፩ ቅዳሜ ማታ ለእሑድ አጥቢያ ማርያም መግደላዊት ሌላይቱም ማርያም መቃብሩን ያዩ ዘንድ መጡ ማርያም ባውፍልያ ናት ።
፪ ወናሁ ኮነ ድልቅልቅ ዓቢይ ።
፪ ታላቅ ንውጽውጽታ ተደረገ ።
እስመ መልአከ እግዚአብሔር ወረደ እምሰማይ ወቀርበ ወአንኰርኰራ ለይእቲ እብን እምአፈ መቃብር ወነበረ ዲቤሃ ።
መልአኩ ከሰማይ ወርዶ ደንጊውን ከመቃብር ላይ አንስቶ ተቀምጦበት ነበርና ።

፫ ወራእዩ ከመ ዘመብረቅ ።
፫ መልኩ እንደ ፀሐይ ብሩህ ነው ኢትርአይ ግርማ ርእየቱ ለኤልያብ እንዲል ።
ወልብሱ ፀዓዳ ከመ በረድ ።
ልብሱ እንደ በረዶ ነጭ ነው ወርኃ ትፍሥሕት ወርኃ ተድላ ነው ሲል ።

፬ ወእምግርማሁ ተሀውኩ እለ የዓቅቡ መቃብረ ወኮኑ ከመ አብድንት ።

፬ እሱን ከመፍራታቸው የተነሣ መቃብሩን የሚጠብቁት ደንግጠው እንደ በድን ሆኑ ። ሐተታ ፤ ነፍስ አልተለያቸውምና ከመ ዓብድንት አለ ።

፭ ወአውሥአ ውእቱ መልአክ ወይቤሎን ለአንስት እለ ይቀውማ ኢትፍርሃ አንትንሰ ።
፭ መልአኩ ሴቶችን እናንተ አትፍሩ አላቸው
እስመ አአምር ከመ ኢየሱስሃ ዘተሰቅለ ተኃሥሣ ።
የተሰቀለውን ኢየሱስን እንድትሹ ዐውቃለሁና ።
፮ ኢሀሎ ዝየሰ ።
፮ ከዚህ ግን የለም ።
ዳዕሙ ተንሥአ በከመ ይቤ ።
እነሣለሁ እንዳለ ተነሥቷል እንጂ ።
ወባሕቱ ነዓ ርእያ መካኖ ኀበ ተቀብረ ።
ነገር ግን የተቀበረበትን ቦታ መጥታችሁ እዩ ።
፯ ወፍጡነ ሑራ ወንግራሆሙ ለአርዳኢሁ ከመ ተንሥአ እምነ ምውታን ።
፯ ፈጥናችሁ ሂዳችሁ ከሙታን ተለይቶ እንደ ተነሣ ለደቀ መዛሙርቱ ንገሯቸው ።
ወናሁ ይቀድመክሙ ገሊላ ።
በገሊላ ይቀድማችኋል ማለት መታየትን በገሊላ ይጀምርላችኋል ፤
ወበህየ ትሬእይዎ ።
በገሊላ ታዩታላችሁ ።
ናሁ አይዳዕኩክን ።
እነሆ ነገርኳችሁ ።
፰ ወኃለፋ ፍጡነ እልኩ አንስት እምኀበ መቃብር በፍርሃት ወበረዓድ ወበፍሥሐ ዓቢይ ።
፰ በታላቅ ደስታና በፍርሃት ከመቃብሩ ፈጥነው ሄዱ ። ሐተታ መልአክ አይተዋልና በፍርሃት ትንሣኤውን ሰምተዋልና ደስ ብሏቸው ሄዱ ።
ወሮጻ ይንግራሆሙ ለአርዳኢሁ ።
ለደቀ መዛሙርቱ ሊነግሯቸው ፈጥነው ሄዱ ።
፱ ወእንዘ የሐውራ ይንግራሆሙ ተራከቦን እግዚእ ኢየሱስ በፍኖት ።
፱ ሊነግሯቸው ሲሄዱ ጌታ ከመንገድ ታያቸው ወይቤሎን በሀከን ፤
እንዴት ሰነበታችሁ አስታረቅኋችሁ አላቸው ።

ወቀሪቦን ወአኃዛ እገሪሁ ወሰገዳ ሎቱ ።
ቀርበው እግሩን ይዘው እጅ ነሥተው ሰገዱለት ።
፲ ወእምዝ ይቤሎን እግዚእ ኢየሱስ ኢትፍርሃ
፲ ከዚህ በኋላ ጌታ አትፍሩ አላቸው ።
ሑራ ንግራሆሙ ለአኃውየ ከመ ይሑሩ ገሊላ ፤
ገሊላ ይሄዱ ዘንድ ለወንድሞቼ ሄዳችሁ ንገሯቸው፤
በወህየ ይሬእዩኒ ፤
በገሊላ ያዩኛል ፤

ዘከመ ጌጥዎሙ ።

፲፩ ወኃሊፎን እማንቱ አተው ሠገራት ሀገረ ወነገሩ ለሊቃነ ካህናት ኵሎ ዘከመ ኮነ ።

፲፩ ሴቶች ከሄዱ በኋላ ጭፍሮች ከከተማ ገብተው የተደረገውን ሁሉ እንደተደረገ ለሊቃነ ካህናት ተናገሩ ።

፲፪ ወተጋብኡ ወተማከሩ ምስለ ሊቃውንት ወወሀብዎሙ ብዙኃ ወርቀ ለሠገራት ።

፲፪ ተሰብስበው ካለቆች ጋራ መክረው ለጭፍሮች ብዙ ወርቅ ሰጧቸው ።

፲፫ ወይቤልዎሙ በሉ አርዳኢሁ ሌሊተ መጽኡ ወሰረቅዎ እንዘ ንነውም ንሕነ ።
፲፫ እኛ ተኝተን ሳለን ሌሊት መጥተው ደቀ መዛሙርቱ ሰርቀው ወሰዱት በሉ አሏቸው ።
፲፬ ወእምከመ ተሰምዓ ዝነገር በኀበ መልአከ አሕዛብ ንሕነ ነአምኖ ።
፲፬ ይህ ነገር በጲላጦስ ዘንድ የተሰማ እንደሆነ እኛ እናስረዳዋለን ።
ወለክሙሰ ናድኅነክሙ ።
እናንተንም ከቅጣት እናድናችኋለን ።
ወናጸድቅ ነገረክሙ ነገራችሁንም እናስረዳለን ።
ወዘእንበለ ኃዘን ንሬስየክሙ ።
ደስ እናሰኛችኋለን አሏቸው ።
፲፭ ወነሢአሙ ሠገራት ውእተ ወርቀ ገብሩ በከመ መሐርዎሙ ።
፲፭ ጭፍሮች ገንዘቡን ተቀብለው እንደነገሯቸው አደረጉ ማለት ሰርቀው ወሰዱት አሉ ።
ወወፅአ ዝንቱ ነገር በኃበ አይሁድ እስከ ዮም ።
እስካሁን ድረስ በአይሁድ ዘንድ ሰርቀው ወሰዱት፤ ተብሎ ሲነገር ይኖራል ። ሐተታ አለቆቻቸው አራትናቸው እየራሳቸው ጠይቀዋቸዋል አንዱን ቢጠይቁት ዐሥራ አንዱ ደቀ መዛሙርቱ ሰርቀው ወሰዱት አለ ። አንዱ መቶ ሃያው ቤተ ሰቡ ሰርቀው ወሰዱት አለ ፣ አንዱ ፤ ዮሴፍና ኒቆዲሞስ ሰርቀው ወሰዱት አለ ። አንዱን ፣ እኔ ተኝቼ ነበር ሁሉንም አላየሁም አለ ፤ ከመዝኑ ኮነ ነገርክሙ ዝርዙረ ወዝርወ ብሎ በሰይፍ አስፈጇቿቸዋል ።
፲፮ ወአርዳኢሁሰ ፲ቱ ወ፩ዱ ሖሩ ውስተ ገሊላ ኀበ ደብር ዘአዘዞሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

፲፮ ዐሥራ አንዱ ደቀ መዛሙርቱ ግን ሄዱ ወዳላቸው ቦታ ወደገሊላ ሄዱ ።

፲፯ ወሶበ ርእይዎ ሰገዱ ሎቱ ።
፲፯ ባዩትም ጊዜ ሰገዱለት ።
ወመንፈቆሙሰ ናፈቁ ።
እኩሌቶቹ ተጠራጠሩ አለ ቶማስን ሲያይ ፤ ወንፍቃ ለሌሊት እንዲል ።

፲፰ ወቀርበ እግዚእ ኢየሱስ ወተናገሮሙ እንዘ ይብል ተውህበኒ ሥልጣን ሰማይ ወምድር ።

፲፰ ጌታ ቀርቦ ሰማይን ምድርን የማሳልፍበት ሥልጣን ተሰጠኝ ብሎ ነገራቸው ። ሐተታ ነፍስና ሥጋው ተለያይተው ነበርና የኒያን ተዋሕዶ ሲያይ ተውህበ ሊተ አለ አንጂ የተሰጠው በማኅፀን ሲዋሐድ ነው ።
በከመ ፈነወኒ አቡየ አነኒ እፌንወክሙ ።
እኔን አባቴ ላስተምር እንደላከኝ እናንተንም እልካችኋለሁ ።

፲፱ ሑሩ ወመሐሩ ኵሎ አሕዛበ ። ማር፣፲፯፣፵ ።
፲፱ ሄዳችሁ ሰውን ሁሉ አስተምሩ ። ወእንዘ ታጠምቅዎሙ በሉ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ።
ስታጠምቋቸውም በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ብላችሁ አጥምቋቸው ።

፳ ወመሐርዎሙ ኵሎ ይዕቀቡ ኵሎ ዘአዘዝኩክሙ ።
፳ መሐርዎሙ ዘአዘዝኩክሙ ይዕቀቡ ዘአዘዝኩክሙ ብለህ ግጠም ያዘዝኋችሁን ሁሉ አስተምሯቸው ።
ወናሁ አነ እሄሉ ምስሌክሙ በኵሉ መዋዕል እስከ ኅልፈተ ዓለም ።
እኔም እነሆ እስከ ዓለም ፍጻሜ ድረስ ባላችሁበት ዘመን አድሬባችሁ እኖራለሁ በሐዋርያት መላውን መናገር ነው ።
መልአ ጽሕፈት ብሥራቱ ለማቴዎስ ሐዋርያ ፩ዱ እም፲ወ፪ቱ ሐዋርያት ።
ካሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ ማቴዎስ የጻፈው ወንጌል ደረሰ ተፈጸመ ።
ወኮነ ጸሐፎ በፍልስጥዔም በአስተሐምሞ መንፈስ ቅዱስ እምድኅረ ዕርገቱ ለእግዚእነ ውስተ ሰማይ ዘበአጸሮግዮ በስማኒት ዓመት ።
ጌታ በሥጋ ወደሰማይ ካረገ በኋላ በስምንተኛው ዓመት መንፈስ ቅዱስ እያተጋው በፍልስጥዔም የጻፈው ።
ወበቀዳሚት ዓመተ መንግሥቱ ለቀላውዴዎስ ቄሣር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ በመጀመሪያው ዓመት ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ፣ አስተምሮ ላስጨረሰን ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይግባው አሜን ።

| ኍልቈ ምዕራፍ ዓቢይ ዘወንጌለ ማቴዎስ ። | የማቴዎስ ወንጌል ዓቢይ ምዕራፍ ቍጥር ። |
|---|---|
| ምዕራፍ ፩ መጽሐፈ ልደቱ ። | የልደቱ መጽሐፍ ። |
| ም ፪ ወተወሊዶ ። | በተወለደ ጊዜ ። |
| ም ፫ ወበውእቱ መዋዕል ። | በዚያ ወራት ። |
| ም ፬ ወእምዝ ወሰዶ መንፈስ ። | ከዚህ በኋላ ወሰደው ። |
| ም ፭ ወርእዮ እሕዛበ ። | ብዙ ሰው አይቶ ። |
| ም ፮ ወባሕቱ ዐቁ ። | ነገር ግን ዕወቁ ። |
| ም ፯ ኢትኰንኑ ። | አትፍረዱ ። |
| ም ፰ ወእንዘ ይወርድ እምደብር ። | ከተራራ ሲወርድ ። |
| ም ፱ ወዐሪጎ ውስተ ሐመር ። | ከመርከብ በወጣ ጊዜ ። |
| ም ፲ ወጸውዖሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ። | ዐሥራ ሁለቱን ጠራ ። |
| ም ፲፩ ወኮነ ድኅረ ፈጸመ ። | አስተምሮ ከጨረሰ በኋላ ። |
| ም ፲፪ ወበውእቱ መዋዕል ። | በዚያ ወራት ። |
| ም ፲፫ ወበይእቲ ዕለት ወጺአ ። | በዚያች ቀን ከቤት ወጥቶ ። |
| ም ፲፬ ወበውእቱ መዋዕል ሰምዓ ሄሮድስ ። | በዚያ ወራት ሄሮድስ ሰማ ። |
| ም ፲፭ ወእምዝ ቀርቡ ኀበ ኢየሱስ ። | ወደ ጌታ ቀረቡ ። |
| ም ፲፮ ወመጽኡ ፈሪሳውያን ወሰዱቃውያን ። | ፈሪሳውያንና ሰዱቃውያን መጡ ። |
| ም ፲፯ ወእምድኅረ ስሱ መዋዕል ። | ከስድስት ቀን በኋላ ። |
| ም ፲፰ ወበይእቲ ሰዓት ። | በዚያች ሰዓት ፤ |
| ም ፲፱ ወኮነ እምዘፈጸመ ኢየሱስ ። | አስተምሮ ከጨረሰ በኋላ ፤ |
| ም ፳ እስመ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ። | መንግሥተ ሰማያት ባለቤትን ትመስላለች ። |
| ም ፳፩ ወቀሪቦ ኢየሩሳሌም ። | ወደ ኢየሩሳሌም በቀረበ ጊዜ ። |
| ም ፳፪ ወአውሥአ ኢየሱስ ዳግመ ። | ጌታ ዳግመኛ መለሰ ፤ |
| ም ፳፫ ወእምዝ ነገሮሙ ኢየሱስ ለሕዝብ ። | ጌታ ለሕዝቡ ነገራቸው ፤ |
| ም ፳፬ ወወጺኦ እምቤተ መቅደስ ። | ከቤተ መቅደስ በወጣ ጊዜ ፤ |
| ም ፳፭ አሜሃ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ። | ያን ጊዜ መንግሥተ ሰማያት ሙሽራን ትመስላለች። |
| ም ፳፮ ወኮነ እምዘፈጸመ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ። | አስተምሮ ከጨረሰ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ ነገራቸው |
| ም ፳፯ ወጸቢሖ ተማከሩ ። | ሲነጋ ሊገድሉት መከሩ ። |
| ም ፳፰ ወሰርከ ሰንበት ። | ቅዳሚ ማታ ። |

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌለ ማቴዎስ ። | | የማቴዎስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|
| በእንተ መጽሐፈ ትውልድ ዘኢየሱስ ክርስቶስ ። | ምዕራፍ ፩ ቍጥር ፩ | የኢየሱስ ክርስቶስን የትውልዱን ታሪክና ቍጥር ስለ መንገር ። |
| በእንተ ልደተ ክርስቶስ ። | ቍ ፲፰ | ስለ ጌታ መወለድ ። |
| ዘከመ መጽኡ ሰብአ ሰገል ውስተ ቤተ ልሔም ። | ም ፪ ቍ ፩ | ሰብአ ሰገል ወደ ቤተ ልሔም እንደ መጡ ስለመ ንገር ። |
| ዘከመ ጐየ ውስተ ግብጽ ። | ቍ ፲፫ | ወደ ግብጽ እንደ ሄደ ። |
| በእንተ ቅትለት ዘሕፃናት ። | ቍ ፲፮ | ስለ ሕፃናት መሞት ። |
| በእንተ ሚጠት እምነ ግብጽ ። | ቍ ፲፱ | ከግብጽ ስለ መመለስ ። |
| በእንተ ስብከት ዘዮሐንስ መጥምቅ ። | ም ፫ ቍ ፩ | ስለ ዮሐንስ መጥምቅ ማስተማር ። |
| በእንተ ጥምቀት ዘኢየሱስ | ቍ ፲፫ | ስለ ጌታ መጠመቅ ። |
| በእንተ ተመከሮት ዘኢየሱስ | ም ፬ ቍ ፩ | ስለ ጌታ መፈተን ። |
| ዘከመ ነበረ ኢየሱስ በቅፍርናሆም ። | ቍ ፲፪ | ጌታ በቅፍርናሆም እንደ ተቀመጠ ። |
| በእንተ አርባዕቱ ቀዳማውያን ሐዋርያት ። | ቍ ፲፰ | ስለ አራቱ ሐዋርያት መመረጥ ። |
| በእንተ ቀዳማዊ ስብከት ወመንክራቱ ለኢየሱስ። | ቍ ፳፫ | ጌታ መጀመሪያ ስለ አስተማረውና ስለ አደረገው ተአምራቱ ። |
| ዘከመ ሰበከ መልዕልተ ደብር በእንተ ብፁዓን | ም ፭ ቍ ፩ | ስለ ብፁዓን በተራራ ላይ እንዳስተማረ ። |
| በእንተ ሐዲስ ኪዳን ተአርዮታ ምስለ ብሊት ። | ቍ ፲፯ | ብሉይና ሐዲስን ስለ ማስተካከል ። |
| በእንተ ንጽሕት ሕሊና ወውሂበ ምጽዋት ወበእንተ ጾም ወጸሎት ። | ም ፮ ቍ ፩ | ምጽዋትን በመስጠት በጾም በጸሎት ልብን ስለ ማንጻት ። |
| በእንተ ዘይደልዎሙ ለክርስቲያን ወበእንተ ንዋየ ዓለም ። | ቍ ፲፱ | ለክርስቲያን ስለሚገባቸው ነገርና ስለ ዓለም ገንዘብ |
| በእንተ ትእዛዛት ። | ም ፯ ቍ ፩ | ስለ ትእዛዛት ። |
| በእንተ አድኅኖተ ለምጻዊ ። | ም ፰ ቍ ፩ | ለምጽ የታመመውን ስለ ማዳን ። |
| በእንተ ገብረ መስፍን ። | ቍ ፭ | ስለ ሹም ባሪያ ። |
| በእንተ ሐማተ ጴጥሮስ ። | ቍ ፲፬ | ስለ ጴጥሮስ አማት ። |
| በእንተ ዘከመ ይደሉ ተሊዎተ ኢየሱስ | ቍ ፲፰ | ጌታን መከተል እንዲገባ ። |
| በእንተ ዘከመ አኅድአ ለባሕር | ቍ ፳፫ | ባሕርን ጸጥ እንዳደረገ ። |
| በእንተ አጋንንት ዘብሔረ ጌርጌሴኖን | ም ፰ ቍ ፳፰ | በጌርጌሴኖን ስለ ነበሩ አጋንንት ። |
| በእንተ መጻጉዕ | ም ፱ ቍ ፩ | መፃጕዕን እንደ አዳነ ። |
| በእንተ ዘከመ ተጸውዐ ማቴዎስ ። | ቍ ፱ | ማቴዎስ እንደ ተመረጠ ። |
| በእንተ ዘከመ ይደልዎሙ ለክርስቲያን ጾሚመ ፤ | ቍ ፲ | ለክርስቲያን መጾም እንዲገባ ። |
| በእንተ ወለተ ኢያኤሮስ ወበእንተ ደም ዘይውኅዝ | ቍ ፲፰ | የኢያኢሮስን ልጅና ደሟ የሚፈስን ስለ አዳነ ። |
| በእንተ ፪ቱ ዕውራን ። | ቍ ፳፯ | ሁለት ዕውሮች እንደ ተከተሉት ። |
| በእንተ ጽሙም ዘቦቱ ጋኔን ። | ቍ ፴፪ | ደንቆሮ ጋኔን ስለ አደረበት ። |
| በእንተ ዘከመ አንሶሰወ ኢየሱስ ውስተ ገሊላ ። | ቍ ፴፭ | ጌታ በገሊላ ዞሮ ስለ አስተማረ ። |
| በእንተ ዘከመ ተፈነው ሐዋርያት ። | ም ፲ ቍ ፪ | ሐዋርያት እንደ ተላኩ ፤ |

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌለ ማቴዎስ ። | | | የማቴዎስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|---|
| በእንተ ዘከመ መሐሮሙ ኢየሱስ ለሐዋርያት ። | | ቍ ፭ | ጌታ ሐዋርያትን እንዳስተማረ ። |
| በእንተ ኢየሱስ ወአርዳኢሁ ለዮሐንስ መጥምቅ ። | ም ፲፩ | ቍ ፪ | ስለ ጌታና ስለ ዮሐንስ ተማሪዎች ። |
| በእንተ ዘከመ ወደሶ ኢየሱስ ለዮሐንስ መጥምቅ ። | | ቍ ፯ | ጌታ ዮሐንስን እንደ አመሰገነው ። |
| በእንተ ዘከመ ኄሰን ለአኅጕር ኢነሳሕያት ። | | ቍ ፳ | ያሳመኑትን እንደ ነቀፋቸው ። |
| በእንተ ድኅነት ። | | ቍ ፳፭ | ስለ ማዳን ። |
| በእንተ ሰንበት ወሰዊት | ም ፲፪ | ቍ ፩ | ስለ ቅዳሜና ስለ እሸት ። |
| በእንተ ዘየብሰት እዴሁ ። | | ቍ ፲ | እጁ ስለ ደረቀች ። |
| በእንተ ርኅራኄሁ ለኢየሱስ ። | | ቍ ፲፭ | ስለ ጌታ ለሰው ማዘን ። |
| በእንተ ዕውር ወጽሙም ዘቦቱ ጋኔን ። | | ቍ ፳፪ | ስለ ዕውርና ደንቆሮ ጋኔን ያደረበት ። |
| በእንተ ጽልሑት ዘፈሪሳውያን ፤ | | ቍ ፴፩ | ስለ ፈሪሳውያን ተንኮል ። |
| በእንተ ትእምርተ ዮናስ ። | | ቍ ፴፰ | ስለ ዮናስ ምልክት ። |
| በእንተ መናፍስት ርኩሳን ። | | ቍ ፵፫ | ስለ ክፉዎች አጋንንት ፤ |
| በእንተ ሰብአ ቤቱ ለእግዚእ ኢየሱስ ። | | ቍ ፵፮ | ስለ ጌታ ቤተ ሰብ ፤ |
| በእንተ ምሳሌ ዘራኢ ። | ም ፲፫ | ቍ ፩ | ስለ ገበሬ ዘር ምሳሌ ፤ |
| በአንተ ምሳሌ ዘሥርናይ ሠናይ ወዘክርዳድ ። | | ቍ ፳፬ | ስለ በጎ ሥንዴና ስለ ክርዳድ ምሳሌ ፤ |
| በእንተ ምሳሌ ዘሕጠተ ሰናፔ ። | | ቍ ፴፩ | ስለ ሰናፍጭ ቅንጣት ምሳሌ ። |
| በእንተ ምሳሌ ዘብሑእ ። | | ቍ ፴፫ | ስለ እርሾ ምሳሌ ። |
| በእንተ ፍካሬ ዘምሳሌ ክርዳድ ። | | ቍ ፴፮ | የእንክርዳድ ምሳሌን ስለ መተርጐም ፤ |
| በእንተ መድፍን ወባሕርይ ወገሪፍ ። | ምዕራፍ ፲፫ | ቍጥር ፵፬ | ስለ ተቀበረ ዕንቍና መረብ ። |
| በእንተ ዘከመ ሖረ ኢየሱስ ውስተ ናዝሬት ፤ | | ቍ ፶፫ | ጌታ ወደናዝሬት እንደ ሄደ ፤ |
| በእንተ ዘከመ ሐለየ ሄሮድስ ሳዕለ ኢየሱስ ። | ም ፲፬ | ቍ ፩ | ሄሮድስ በጌታ ላይ እንዳሰበ ። |
| በእንተ ምትረተ ዮሐንስ መጥምቅ ። | | ቍ ፫ | ስለ ዮሐንስ መቆረጥ ። |
| በእንተ ቀዳሚት አብዝኆተ ኅብስት ። | | ቍ ፲፫ | መጀመሪያ እንጀራ እንዳበረከተ ። |
| በእንተ ዘከመ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ መልዕልተ ማይ | | ቍ ፳፪ | ጌታ በውኃ ላይ እንደ ሄደ ። |
| በእንተ ዘከመ ዐደወ ውስተ ጌንሴሬጥ ። | | ቍ ፴፬ | ወደ ጌንሴሬጥ እንዳሻገረ ። |
| በእንተ ፈሪሳውያን ወሥርዓቶሙ ። | ም ፲፭ | ቍ ፩ | ስለ ፈሪሳውያን ሥራት ፤ |
| በእንተ ከነናዊት እም ። | | ቍ ፳፩ | ስለ ከነናዊት ሴት ። |
| በእንተ ዘከመ ተፈወሱ ካልዓን ሕሙማን ። | | ቍ ፳፱ | ሌሎች በሽተኞች እንደዳኑ ። |
| በእንተ ካልዕት አብዝኆተ ኅብስት ። | | ቍ ፴፪ | ሁለተኛ እንጀራ ስለ አበረከተ ። |

| መክሥተ ክርክስት ዘወንጌለ ማቴዎስ ። | | የማቴዎስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|
| በእንተ ምሳሌ ንጉሥ ዘገብረ ከብካበ ለወልዱ ፡ | ም ፳፪ ቍ ፩ | ስልጅ ሠርግ ስለ አደረገ ንጉሥ ምሳሌ ። |
| በእንተ ዘከመ ይደሉ ውሂበ ጸባሕት ለቄሣር ። | ቍ ፲፭ | ለቄሣር ግብር መስጠት እንዲገባ ። |
| በእንተ ሰዱቃውያን ወትንሣኤ ሙታን ። | ቍ ፳፫ | ስለ ሰዱቃውያንና ስለ ትንሣኤ ሙታን ። |
| በእንተ ዓቢይ ትእዛዘ እግዚአብሔር ። | ቍ ፴፬ | ለስ እግዚአብሔር ትእዛዝ ። |
| በእንተ መሢሕ ወልደ ዳዊት ምዕራፍ ፳፪፡ | ቍ፤ ፵፩ | ስለ መሢሕ ክርስቶስ የዳዊት ልጅ ። |
| በእንተ መደልዋን ፈሪሳውያን | ም ፳፫ ቍ ፩ | ስለ ግብዞች ፈሪሳውያን ። |
| በእንተ እከየ ፈሪሳውያን ። | ቍ ፲፫ | ስለ ፈሪሳውያን ክፋት ። |
| በእንተ ዘከመ ኄሳ ለኢየሩሳሌም | ቍ ፴፯ | ኢየሩሳሌምን እንደ ነቀፋት ። |
| በእንተ ዘከመ አቅደመ ነጊረ ሙስናሃ ለቤተ መቅደስ ወለኢየሩሳሌም | ም ፳፬ ቍ ፩ | የኢየሩሳሌምንና የቤተ መቅደስን ጥፋት እንደ ተናገረ |
| በእንተ ካልአዊት ምጽአት ዘወልደ ዕጓለ እመሕያው | ቍ ፳፱ | ስለ ሁለተኛዪቱ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ መምጣት ። |
| በእንተ ዘከመ ይደልዎ ተጊህ ለክርስቲያን ። | ቍ ፵፪ | ለክርስቲያን መትጋት እንዲገባው ። |
| በእንተ ፲ቱ ደናግል ጠባባት ወዓብዳት ። | ም ፳፭ ቍ ፩ | ስለ ልባሞችና ስለ ሰነፎች ዐሥር ደናግል ። |
| በእንተ ምሳሌ መክልይ ። | ቍ ፲፬ | ስለ ወርቅ ምሳሌ ። |
| በእንተ ኅልቀተ ዓለም | ቍ ፴፩ | ስለ ዓለም ማለፍ ። |
| ዘከመ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት በሳዕለ ኢየሱስ | ም ፳፮ ቍ ፫ | የካህናት አለቆች በጌታ ላይ እንደ መከሩ ። |
| በእንተ ዘከመ ረፈቀ ኢየሱስ ለድራር በቢታንያ ወተካይዶቱ ለይሁዳ | ቍ ፮ | ጌታ በቢታንያ ለራት እንደ ተቀመጠ ይሁዳም ከሊቃነ ካህናት ጋራ እንደ ተማማለ ። |
| በእንተ ደኃሪት ድራር ወእስተዳልዎ ። | ቍ ፲፯ | ስለ ሁለተኛዪቱ ራት መዘጋጀት ። |
| በእንተ ዘከመ ከሠተ ኢየሱስ ለዘያገብኦ ። | ቍ ፳ | የሚያሲዘውን ጌታ እንደ ገለጠ ። |
| በእንተ ዘከመ ሠርዓ ኢየሱስ አኰቴተ ቍርባን ። | ቍ ፳፮ | ጌታ ቍርባንን እንደሠራ ። |
| በእንተ አቅደመ ኢየሱስ ነጊረ ዕልወተ አርዳኢሁ ፡ | ቍ ፴ | ጌታ የተማሪዎቹን ክህደት አስቀድሞ እንደ ተናገረ። |
| በእንተ ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ በጌቴሴማን ። | ቍ ፴፮ | ጌታ በጌቴሴማን እንደጸለየ ። |
| በእንተ ዘከመ አግብኦ ይሁዳ ለክርስቶስ ወዘከመ ተእኅዘ | ቍ ፵፯ | ይሁዳ ክርስቶስን እንደ አሲያዘው ክርስቶስም እንደ ተያዘ ። |
| በእንተ ዘከመ ቆመ ኢየሱስ በቅድመ ዓውድ ። | ቍ ፶፯ | ጌታ ባደባባይ እንደ ቆመ ። |
| በእንት ክህደተ ጴጥሮስ ። | ቍ ፷፱ | ጴጥሮስ ጌታን እንደካደው ። |
| በእንተ ቀቢጸ ተስፋ ዘይሁዳ | ም ፳፯ ቍ ፫ | ይሁዳ ተስፋ እንደቆረጠ ። |
| በእንተ ዘከመ ቆመ ኢየሱስ በቅድመ ጲላጦስ ። | ቍ ፲፩ | ጌታ በጲላጦስ ፊት እንደቆመ ። |

## የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል፤
## ቅዱስ ማርቆስ እንደ ጻፈው።

ብሥራተ ማርቆስ ረድኡ ፩ዱ እምድ ወ፪ቱ አር ድእት ጸሎቱ ወበረከቱ የሃሉ ምስለ ኵሎሙ ሕዝበ ክርስቲያን ፤ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ማርቆስ ማለት ንህብ ማለት ነው ፤ ንህብ ከሁሉ እንዲቀስም አስቀድሞ ከክርስቶስ ኋላ ከሐዋርያት ተምሯልና ፤ አንበሳ ማለት ነው ። አንበሳ ለሳም ጌታው እንደሆነ እንዲሰብረው አምልኮተ ጣዖትን ከግብጽ አጥፍቷልና ፤ አንድም ከሆነ ልኡክ ማለት ነው ። ብሥራተ ማረ ማርቆስ ይላል ቀተደ ረራቢ ቀለም ነው ሁሉም ከሆነ ማለት ነው እመል እክዋ ሲኖዲቆስ ባለ ጊዜ መልእክትም ሲኖዲቆስም ክታብ ማለት እንደሆነ ፥ ይህም ቃል የመለስቱ ምዕት ነው እንደ ማቴዎስ ተርጓ ። ይህን ዓለም ዕጣ በጣ ብለው ተካፍለው ለማስተማር በሚወጡበት ጊዜ ለቅዱስ ጴጥሮስ ሮም በዕጣ ደርሰዋለች አም ስተኛ ግብጽን እንስቷል ። ይህስ አይደለም ብሎ ግብጽ በዕጣ ደረሰችው ። አምስተኛ ሮምን አንስቷል የንጉሡ ነገሥት መዲና ናትና ርሱም ሊቀ ሐዋርያት ነውና ፤

ለእርድኡት ግን ዕጣ የላቸውም አንዱም ሁለቱም እየሆኑ አንዱን ሐዋርያ አንዱም ሁለቱም አንዱን ሐዋርያ ተከትለው ሄደዋል ። ማርቆስም ጴጥሮስን ተከትሎ ሄዷል ግብጽን ለማ ርቆስ ሰጥቶት እሱም ሮም ወርዷል።ማርቆስ ከዚህ ገብቶ ጌታ ከፅንስ ጀምሮ ያደረገውን ታምራት ያስ ተማረውን ትምህርት የሠራውን ትሩፋት ቢነግ ራቸው ከአምልኮተ ጣዖት ወደ አምልኮተ እግዚአ ብሔር ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ ተመለሱ አመኑ ተጠመቁ ።

ትምህርት ካልደረሰበት ለማዳረስ ወጥቶ በሚሄድ በት ጊዜ አባታችን በቃል ያስ ይረሳል በመጽ ሐፍ ያስ ይወረሳልና ጻፍልን ብለው በዚያ ምክን ያት ይጽፋል ።

አንድም እሱ እንዳባትነቱ ይጽፋል ። መዋዕለ ጽሕፈት ፤

ሐተታ፤እንደ ማቴዎስ ፥ ጸሐፍቱም ሁለቱ ከሐዋርያት ሁለቱ ከአርድዕት ናቸው ሐዋርያት ጨርሰው እንዲጽፉት ያላደረገ ሁለቱን ከአርድ ዕት ያጻፈ ስለምን ቢሉ ሐተታ ፥ እንደ ማቴዎስ አርድእት ጨርሰው እንዲጽፏት ያላደረገ ሁለቱን ከሐዋርያት ያጻፈ ስለምን ቢሉ ሐተታ፥እንደ ማቴ ዎስ ጸሐፍቱንስ ከፍ ብሎ አምስት ስድስት ሣቅ ብሎ ሁለት ሦስት ያላደረገ ስለምን ቢሉ ። ሐተታ እንደ ማቴዎስ ፤ ሀገርም ልሳንም ሐተታ እንዶ ማቴዎስ ፤ ወንጌልሂ ብለህ አትት ይህን አርእስት ሠለስቱ ምዕት ሰጥተዋል ብለህ ጨርሰህ ተርጓ ። ልመናው ክብሩ ይደርብንና ከሰባ ሁለቱ አርድዕት አንዱ ማርቆስ የጻፈው ወንጌል ይህ ነው ።

### በእንተ ስብከተ ዮሐንስ ።

### ምዕራፍ ፩ ።

፩ ቀዳሚሁ ለወንጌለ እግዚእን ኢየሱስ ክር ስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ሕያው በከመ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ነቢያት ናሁ አነ እፌኑ መልአኪየ

፪ ቅድመ ገጽከ ዘይጸይሕ ፍኖተከ በቅድሜከ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ፤

፫ ወይብል ጺሐሑ ፍኖተ እግዚአብሔር ወአርዩ መጽያሕቶ ። ኢሳ ፵፥፫። ማቴ ፫፥፫ ሉቃ ፫፥፬። ዮሐ ፩፥፳፫ ።

፩ ሕያው የሚሆን የእግዚአብሔር አብ የባ ሕርይ ልጁ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያስተማ ረው ፤ ፪ የወንጌል ጥንቱ ጥምቀተ ዮሐንስ ስብ ከተ ዮሐንስ ነው በከመ ጽሑፍ ውስተ መጻሕፍተ ነቢያት ። ሚክ ፥ ፫ ፥ ፩ ።

፪ በመጻሕፍተ ነቢያት እንደ ተነገረ ዘንድ ። አንድም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያስተማረው የወንጌል ጥንቱ በመጻሕፍተ ነቢያት እንደ ተነ ገረ ዘንድ ነው ። አንድም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያስተማረው የወንጌል ጥንቱ እምላክ ሰው እንደ ሆነ ዘንድ ነው ።

በከመ ጽሑፍ ።

በመጻሕፍተ ነቢያት እንደተነገረ ፥ እፌኑ ያለውን ይሻል ። አንድም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያስ ተማረው የወንጌል ጥንቱ ሰው አምላክ እንደሆነ ዘንድ ነው ። መልአኪየ ያለውን ይሻል ። በከመ ጽሑፍ በመጻሕፍተ ነቢያት እንደተነገረ ዘንድ ። አንድም ቀዳሚሁ ለወንጌለ ኢየሱስ ክርስቶስ የወ ንጌል ጥንቱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ነው ። በከመ ጽሑፍ በመጻሕፍተ ነቢያት እንደተነገረ ዘንድ ። ሐተታ መጻሕፍተ ነቢያት ያስ እንደ ሆን አያሳስትም መጽሐፈ ነቢይ ያስ እንደሆነ እፌኑ መልአኪየ ያለ ሚልክያስ ቃለ ዓዋዲ ያለ ኢሳይያስ ነው ። ምነው ነቢይ አለ ቢሉ ያንድ ገን ዘብ ሽህ ያሳዝብ እንዲሉ ነቢይ የሁሉ ስም ነውና መጽሐፈ ኢሳይያስ ይላል አብነት ኢሳይያስ እን

ዳባት እንደመምር ሚልክያስ እንደ ልጅ እንደ ደቀ መዝሙር ናቸውና ።

፬ ወሀሎ ዮሐንስ ያጠምቅ በገዳም

፬ ዮሐንስ በምድረ በዳ ያስተምር ነበር ።
ወይሰብክ ጥምቀተ ለንስሐ ወይትኃደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ ኃጢአታቸው ሊሠረይላቸው የንስሐ ጥምቀትን ያስተምር ነበር ።

፭ ወየሐውሩ ኀቤሁ ኵሎሙ ሰብአ ይሁዳ ወኢየሩሳሌም ፡ ማቴ ፫ ፡ ፭ ።

፭ የኢየሩሳሌምና የይሁዳ ሰዎች ሁሉ ወደሱ ይሄዱ ነበር ፤ ወያጠምቆሙ ለኵሎሙ በፈለገ ዮርዳኖስ እንዘ ይትአመኑ ኃጢአቶሙ ፤ ኃጢአታቸውን እየተናዘዙ ሁሉንም በዮርዳኖስ ወንዝ ያጠምቃቸው ነበር ።

፮ ወልብሱ ለዮሐንስኒ ዘጸጕረ ገመል ማቴ ፫ ፡ ፬ ። ዘሌ ፲፩ ፡ ፳፪ ። ሉቃ ፫ ፡ ፲፮ ። ዮሐ ፩ ፡ ፳፯ ። ግብ ፯ ፡ ፭ ።

፮ የዮሐንስ ልብሱ የግመል ጸጕር ነበር ፤ ወቅናቱ ዘአዲም ውስተ ሐቌሁ በወገቡም የሚታጠቀው የነት መታጠቂያ ነበር ፤ ወሲሳዩ አንበጣ ወመዓረ ጸደና ምግቡም የምድረ በዳ ማርና አንበጣ ነበር ።

፯ ወሰበከ ወይቤ ይመጽእ እምድኅሬየ ዘይጸንዕ እምኔየ ።

፯ ከኔ የበረታ ከኔ በኋላ ይመጣል ፤ ወኢይደልወኒ እድንን ወእፍታሕ ቶታነ አሣዕኒሁ እምእገሪሁ፤ የጫማውን ጠፍር ተጐንብሼ እፈታ ዘንድ የማይገባኝ ፤ ሐተታ እጼር ማቴዎስ እድንን ማርቆስ እፍታሕ ሉቃስ መገናኛው ዮሐንስ ፤ እንዲህ ግን ስለ ሆነ እድንን ይቀድማል እፍታሕ ይከተላል እጼር በመጨረሻ ነው ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ።

፰ ወአንሰ አጠምቀክሙ በማይ ፤

፰ እኔ በውኃ አጠምቃችኋለሁ ፤ ወውእቱሰ ያጠምቀክሙ በመንፈስ ቅዱስ ፤ እሱ ግን በመንፈስ ቅዱስ ያጠምቃችኋል ።

በእንተ ጥምቀት ወተመክሮት ዘኢየሱስ ።

፱ ወይእተ አሚረ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ እምናዝሬት ዘሀገረ ገሊላ ።

፱ በዚያን ጊዜ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከገሊላ ክፍል ከናዝሬት መጣ ።
ወአጥመቆ ዮሐንስ በፈለገ ዮርዳኖስ ።
በዮርዳኖስ ወንዝ ዮሐንስ አጠመቀው ።

፲ ወወፂአ እማይ ርእየ ተሰጥቀ ሰማይ ። ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፳፪ ። ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፴፪ ።

፲ ከውኃውም በወጣ ጊዜ ሰማይ ሲቀደድ አየ ። ሐተታ ። ማቴዎስ ተርኀወ ይላል ከዚህ ማርቆስ ተሰጥቀ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ። ከዚህ ግን ማርቆስ ተሰጥቀ ማለቱ ስለ ክብረ መንፈስ ቅደስ ነው ።
ወወረደ መንፈስ ቅዱስ ከመ ርግብ ወነበረ ዲቤሁ።
መንፈስ ቅዱስም እንደ ርግብ ወርዶ ተቀመጠበት ።

፲፩ ወመጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል አንተ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ወኪያከ ሠመርኩ ።

፲፩ ደስታዬን የማይብህ የምወድህ ልጄ አንተ ነህ የሚል ድምጽ ከወደ ሰማይ ተሰማ ። ሐተታ ማቴዎስ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ አለው ይላል ፤ ማርቆስ አንተ ውእቱ ወልድየ አለው አለ እንደ ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎታል ። ማርቆስ ወልድየ አንተ ያለው ትንቢት እንደ ተፈጸመለት ለማጠየቅ አንተ ውእቱ ወልድየ አለው አለ እንጂ ። ፩ም ፡ ነገር እንደ ማርቆስ ከውኃው ሳለ አንተ ውእቱ ወልድየ ብሎታል ። አሁን ወልድ የባሕርይ ልጅነቱን የማያውቅ ሁኖ አይደለም በወልድ ለዮሐንስ ለመናገር ነው እንጂ ። እኮ ዘእስእለከ ከመ ትንሥእሙ እምዓለም ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ ትዕቀቦሙ እምእኩይ ባለ ጊዜ አብ የማያውቅ ሁኖ እንዳይደለ በአብ ለሐዋርያት ለመናገር እንደሆነ ። ከውኃው ከወጣ በኋላ እንደ ማቴዎስ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎታል በዮሐንስ ለሕዝቡ ለመናገር ።

፲፪ ወአውፅኦ መንፈስ ሶቤሃ ገዳመ ። ማቴዎስ ፬ ፡ ፩ ፡ ሉቃ ፬ ፡ ፩ ።

፲፪ በዚያም ጊዜ መንፈስ ወደምድረ በዳ አወጣው ፤

፲፫ ወነበረ ሐቅለ ፵ መዓልተ ወ፵ ሌሊተ ፤

፲፫ በምድረ በዳም አርባ ሌሊትና አርባ መዓልት ተቀመጠ ።
ወያሜክሮ ሰይጣን ።
ሰይጣን ይፈታተነው ነበር ።
ወነበረ ምስለ አራዊት ።
ከአራዊት ጋራ ይኖር ነበር ። ርኅቀተ መካኑን ያጠይቃል ።
ወይትለአክዎ መላእክት ።
መላእክትም ያገለግሉት ነበር ።
ዘከመ እኅዝ ኢየሱስ ይስብክ ወይኅረይ ቀደምተ ሐዋርያት ፤

፲፬ ወእምድኅረ እኃዝዎ ወሞቅሕዎ ለዮሐንስ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ ገሊላ ወሰበከ ወንጌለ መንግሥተ እግዚአብሔር ማቴ ፡ ፬ ፡ ፲፪ ፡ ሉቃ ፡ ፬ ፲፬ ዮሐ፡ ፬ ፡ ፵፫ ።

፲፬ ዮሐንስን ይዘው ካሠሩት በኋላ ጌታ ወደ ገሊላ መጥቶ የእግዚአብሔር መንግሥት ወንጌልን አስተማረ ።

፲፭ እንዘ ይብል በጽሐ ጊዜሁ ።
፲፭ ጊዜው ደረሰ ።
ወቀርበት መንግሥተ ሰማያት መንግሥተ ሰማ
ያትም ቀረበች ንስሑ ወእመኑ ።
በወንጌል ንስሐ ግቡ በወንጌልም እመኑ እያለ ።

፲፮ ወእንዘ የኃልፍ መንገለ ባሕረ ገሊላ
ረከቦሙ ለስምዖን ወለእንድርያስ እኁሁ እንዘ ይወ
ድቁ መርበብቶሙ ውስተ ባሕር ፣ ማቴ ፣ ፬ ፣ ፲፰፣
ሉቃ፣፭፣፪ ።

፲፮ በገሊላም ባሕር አጠገብ ሲሄድ ስምዖንን
ወንድሙን እንድርያስንም መረባቸውን ከባሕር
ሲጥሉ አገኛቸው ።
እስመ መሠግራን እሙንቱ፡ዓሣ አጥማጆች ነበሩና ።

፲፯ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ንዑ ትል
ዉኒ ።

፲፯ ጌታም ኑ ተከተሉኝ አላቸው ወእሬስየክሙ
መሠግራነ ሰብእ ሰውን እንድታጠምዱ አደርጋችኋለሁ
፲፰ ወኃደጉ መሣግሪሆሙ ወተለውዎ ሶቤሃ
፲፰ ያን ጊዜም መረባቸውን ትተው ተከተሉት
፲፱ ወኃሊፎ ሕቀ እምህየ ረከቦሙ ለያዕቆብ
ወለዮሐንስ እኁሁ ደቂቀ ዘብዴዎስ ።

፲፱ ከዚያም ጥቂት እልፍ ብሎ የዘብዴዎስ
ልጆች ያዕቆብን ወንድሙን ዮሐንስንም አገኛቸው
ወለሊሆኒ ምስሌሆሙ ።
እሱም ከሳቸው ጋራ ነበር ።
እንዘ ይሠርዑ ወያስተሣንዩ መሣግሪሆሙ ።
መረባቸውን ሲያበጁ ማለት ያደፈውን ሲያጥቡ
የተቆረጠውን ሲቀጥሉ ።

፳ ወጸውዖሙ በጊዜሃ ። ወኃደጉ ዘብዴዎስሃ
አባሆሙ ምስለ አሳቡ ውስተ ሐመር ወተለውዎ
፳ ጠራቸው፡አባታቸውን ዘብዴዎስን ከሚያተኞቹ
ጋራ በታንኳ ትተውት ሄደው ተከተሉት ፣ ምስለ
አሳቡ ብሎ በማርቆስ ያቀናዋል ያልነው ይህ ነው ።
ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ በቅፍርናሆም ለዘቦቱ ጋኔን ።
፳፩ ወሖሩ ቅፍርናሆም ። ማቴ ፣ ፬ ፣ ፲፫ ፣
ሉቃ ፣ ፬ ፣ ፴፩ ።
፳፩ ቅፍርናሆም ሄዱ ።
ወቦአ በሰንበት ምኵራበ ወእንዘ ይምህሮሙ ፣
ቀዳሚ በምኵራብ ገብቶ ያስተምር ጀመረ ።
፳፪ ወአንከሩ ምሕሮቶ ማቴ ፣ ፯፣ ፳፰ ።
፳፪ ትምህርቱንም አደነቁ ።
እስመ ከመ መኰንን ይሜህሮሙ ወአኮ ከመ ጸሐፍቶ
ሙ እንደ ጸሐፍት ያይደለ ፣ ሥልጣን እንዳለው ያስ
ተምራቸው ነበርና ።
፳፫ ወሀሎ ፩ ብእሲ ዘጋኔን ውስተ ምኵራብ ።
ሉቃ፣፬ ፣ ፴፫ ።
፳፫ ከምኵራብ ጋኔን ያደረበት ሰው ነበር ።

፳፬ ወአውየወ ወይቤ ምንት ብየ ምስሌከ
ኢየሱስ ናዝራዊ ።

፳፬ የናዝሬቱ ኢየሱስ ካንተ ጋራ ምን ጠብ
አለኝ ።
መጻእከኑ ታጥፍአነ ።
ልታጠፋን መጣህን ፣
ነአምረከ ከመ አንተ ቅዱሱ ለእግዚአብሔር ፤
የእግዚአብሔር ቅዱስ ሆይ ማንም እንደሆንህ
እናውቅሀለን ብሎ ጮኸ

፳፭ ወገሠጾ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳፭ ጌታም ገሠጸው
ወይቤሎ ተፈጸም አፉከ ዝም በል ።
ወፃእ እምኔሁ
ከሱም ውጣ አለው ።

፳፮ ወአስተራገጾ ውእቱ ጋኔን አኩይ ፤
፳፮ ቢስ ጋኔን እንዘፈዘፈው ሐተታ ይሰማ
ዋልና ጽንዓ ተአምራቱን ለማጠየቅ ፣ እንድም
ውደቅ ሌባ ባሉት ጊዜ ከሳንቃው ከመድረኩ እየተ
ማታ እንዲወጣ ፣
ወአውየወ በዓቢይ ቃል ፣
በታላቅ ቃልም ጮኸ ።
ወወፅአ እምኔሁ
ከሱ ወጣ ።

ሐተታ ምኵራቡ ያለ ከተራራ ላይ ነው ያሉ እንደ
ሆነ ሲያስተምር ውሎ ጉባኤ ሲፈታ ከምኵራብ
ገብቶ ፈውሶት ሂዷል ምኵራቡ ከተራራው በታች
ነው ያሉ እንደሆነ ሲያስተምር ውሎ ከተራራው
ወርዶ ከምኵራቡ ገብቶ ፈውሶት ይሄዳል ።

፳፯ ወደንገፁ ኵሎሙ እለ ርእዩ ዘንተ ።
፳፯ ይህን ያዩ ሁሉ አደነቁ ።
ወይቤሉ በበይናቲሆሙ ምንትኑ ዝንቱ ትምህርት
ሐዲስ ይህ እንግዳ ትምህርት ምድነው እስመ በትእዛዝ
ይኤዝዞሙ ለአጋንንት ርኵሳን ከመ ይጻኡ ።
ርኩሳን አጋንንት ይወጡ ዘንድ ያዛቸዋልና ። እን
ድም ትእምህርት ብለህ ይህ እንግዳ ምልክት ምን
ድርነው በትእዛዝ ውጡ ብሎ አጋንንትን የሚያዛቸው
ወይትኤዘዙ ሎቱ ።
አጋንንትም የሚወጡለት ይህ እንግዳ ምልክት
ምንድነው አሉ ።

፳፰ ወተሰምዓ ነገሩ ውስተ ኵሉ በሐውርተ
ገሊላ ።
፳፰ ተአምራቱ በገሊላ አውራጃ ሁሉ ተሰማ ፤

በእንተ ሐማተ ጴጥሮስ ወካልዓን
ሕሙማን እለ ተፈወሱ

፳፱ ወወፂአ እምኵራብ ቦአ ቤተ ስምዖን ።
ማቴ ፣ ፰ ፣ ፲፬ ። ሉቃ ፣ ፬ ፣ ፴፱ ።

፳፱ ከምኵራብም ወጥቶ ከስምዖን ቤት ገባ ወምስሌሁ እንድርያስ ወያዕቆብ ወዮሐንስ ።
ያዕቆብና እንድርያስ ዮሐንስም ከሱ ጋራ ነበሩ ።

፴ ወርእያ ሐማቱ ለስምዖን እንዘ ትፈጽን ወትሰክብ ።

፴ የስምዖን አማት ምንሽ ታማ ነበረች ። ወነገርዎ በእንቲአሃ ።
የሷን ነገር ነገሩት ።

፴፩ ወቀርበ ኀቤሃ ወአኀዘ እዴሃ ወአንሥአ
፴፩ ቀርቦ እጇዋን ይዞ አሥነሣት ወኃደጋ ፈፀንታ ሶቤሃ ።
ያን ጊዜ ሆድ ዝማዋ ፈጥኖ ተቀት ።
ወተንሥአት ወተልእከቶሙ ። ተነሥታ አገለገለቻቸው ፥ ማቴዎስ ነገርዎ አላለም ከዚህ ማርቆስ ነገርዎ አለ እንደምን ነው ፥ አይጣላም ቢሉ አይጣላም ከመንገድ ሳለ ነግረዉታል ከቤት ከገባ በኋላ አልነገሩትም ። ያን ከመንገድ የነገሩትን ይዞ አድኑዋታል ፥ ከቤት ከገባ በኋላ አለመንገራቸውን ሲያይ ማቴዎስ ነገርዎ አላለም ፤ ከመንገድ መንገራቸውን ሲያይ ማርቆስ ነገርዎ አለ ። አንድም ነገር እንደ ማርቆስ ፥ ከመንገድ ሳለ ነግረውታል ። ከቤት ገብቶ ነገሩን እሳቸው ያንሱ ብሎ ዝም ብሏል ሁለተኛ ነግረውት ፈዉሷታል ነገሩን ያንሱት ብሎ ዝም ስላለ ማቴዎስ ነገርዎ አላለም ፤ ሁለተኛ መንገራቸውን ሲያይ ማርቆስ ነገርዎ አለ ።

፴፪ ወመስዮ ጊዜ የዓርብ ፀሐይ አምጽኡ ኀቤሁ ኵሎ ድውያነ ወእለሂ እኁዛነ አጋንንት ።
፴፪ ሲመሽ ፀሐይ በሚገባበት ጊዜ ድውያንን ሁሉ ጋኔን ያደረባቸውንም ወደርሱ አመጧቸው ።

፴፫ ወተጋብኡ ኵሎሙ ሰብአ ሀገር ኀበ አንቀጽ
፴፫ ሰዎች ሁሉ ከበር ተሰብስበው
፴፬ ወፈወሶሙ ለብዙኃን ድውያን ወሕሙማን ፥ ሉቃ ፥ ፬ ፥ ፵፩ ።

፴፬ ብዙ ድውያንን አዳናቸው ወአውፅአሙ ለብዙኃን አጋንንት ።
ብዙ አጋንንትንም አወጣቸው ወኢያብሖሙ ይንብቡ ይናገሩ ዘንድ አላሰናበታቸውም ዝም በሉ አላቸው፤ እስመ አእመርዎ ከመ ውእቱ ክርስቶስ ።
ክርስቶስ እንደ ሆነ ስላወቁት ።
፴፭ ወበጽባሕ ተንሥአ ወአሌለየ ጥቀ ወወፂአ ሖረ ሐቅለ ወጸለየ በህየ ።
፴፭ ማለዳ ገሥግሦ ወጥቶ በረሃ ሂዶ በዚያ ጸለየ ።
፴፮ ወዴገንዎ ስምዖን ወእለ ምስሌሁ ፥
፴፮ ስምዖን ከሱም ጋራ የነበሩት ተከተሉት።
፴፯ ወሶበ ረከብዎ ይብልዎ ኵሉ ሕዝብ የኃሥሡከ ።

፴፯ ባገኙት ጊዜ ሁሉ ይሹሃል አሉት ።
፴፰ ወይቤሎሙ መልኡ ንሑር ካልኣተኒ አኀጉረ
፴፰ ወደሌላውም አገር ተነሡ እንሂድ አላቸው ከመ በህየኒ እስብክ ።
ፀዚያም አስተምር ዘንድ ።
እስመ እንበይነ ዝ ግብር መጻእኩ ።
ስለዚህ ነገር ሰው ሁኛለሁና ።

፴፱ ወሖረ ወሰበከ በምኵራባቲሆሙ ውስተ ኵሉ ገሊላ ።

፴፱ ሂዶ በገሊላ ሁሉ በምኵራብ አስተማረ ። ወያወፅእ አጋንንተ ።
ጋኔን ያወጣ ነበር ።

፵ ወመጽአ ኀቤሁ ዘለምጽ ማቴ፥ ፰ ፥ ፪ ። ሉቃ፥ ፫፥፲፪ ።

፵ ለምጽ የያዘው ሰው መጣ ፥
ሰገደ ሎቱ አስተብረከ ወአስተብቍዖ ።
ሰገደ ማለደው ።
ወይቤሎ እግዚኦ እመሰ ፈቀድከ ትክል አንጽሖትየ
አቤቱ ከወደድህስ እኔን ማዳን ይቻልሃል አለው ።

፵፩ ወምሀሮ እግዚአ ኢየሱስ ፥
፵፩ ጌታም ራራለት ፥
ወሰፍሐ እዴሁ ወገሠሦ ፥
እጁን ዘርግቶ ዳሰሰው ፥
ወይቤሎ ፈቀድኩ ንጻሕ ፥
አወዳለሁ ዳን አለው ።

፵፪ ወዘንተ ብሂሎ ሐይወ ለምጹ ሶቤሃ ።
፵፪ ይህን በተናገረ ጊዜ ለምጹ ፈጥኖ ዳነ ፤
፵፫ ወገሠጾ ወፈነዎ ወይቤሎ ዑቅ ኢትንግር ወኢለመኑሂ ፤
፵፫ ለማንም ለማን እንዳትነግር አስተውል ብሎ ገሥጾ ሰደደው ።
፵፬ ወሑር ወአፍትን ርእሰከ ለካህን ሌዋ፥፲፬፥፪።
፵፬ ነገር ግን ሂደህ ራስህን ለካህን አስመርምር።
ወአብእ መባፀከ በእንተ ዘነጻሕከ ፤
ስለ ነጻሕም መባሕን ስጥ ።
በከመ አዘዘ ሙሴ ።
ከመ ይኩን ስምዓ ላእሌሆሙ
ሙሴ እንዳዘዘ መፈራረጃ ይሆንባቸው ዘንድ ፥ ማቴዎስ ዘለምጽን ያስቀድማል ሐማተ ጴጥሮስን ወደኋላ ያደርጋል ማርቆስ ሐማተ ጴጥሮስን አስቀድሞ ዘለምጽን አስከተለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ለወንጌልና ለድጓ ቀራ የለውም ።
፵፭ ወወፂአ አኀዘ ይሰብክ ወይንግር ብዙኃ እስከ ያንከሩ ኵሉ ሀገር ።
፵፭ ብወጣም ጊዜ ሰው ሁሉ እስኪያደንቅ ብዙ ተናገረ ያወራም ጀመረ ።
ወሰበነ በዊአ ሀገር ክሡተ ። ተገልጦ ወደ ሀገር መግ

ባቱ ተጣነው ሕቱቃኀበሰው ጥቂ ነዋሪ ነበርና እም
ስት ገበያ ሰው ይከተለው ነበርና ።
አላ አፍአ ገዳመ ይነብር ።
ብቻውንስ በገዳም ይገኝ ነበር እንጂ ።
ወይመጽኡ ኀቤሁ ስብእ እምኵሉ ።
ከየቦታውም ሰዎች ሁሉ ወደሱ ይመጡ ነበር ።
አንድም ወስዕነ እያልክ መልስ ፣ከሥጋዌ አሰቀ
ድሞ መወሰን ተሳነው ከመወሰን በአፍአ ነበር
እንጂ አንድም ከሥጋዌ አሰቀድሞ ታይቶ ተአም
ራት ማድረግ ተሳነው ታይቶ ታአምራት ከማድረግ
በእፍአ ነበር እንጂ አንድም ከሥጋዌ እሰቀድሞ
በሰው ልቡና ማደር ተሳነው በሰው ልቡና ከማደር
በእፍአ ነበር እንጂ ። አንድም በመዓልት በደብረ
ዘይት መዋል ተሳነው በመዓልት በምኵራብ ሲያ
ስተምር ይውል ነበር እንጂ አንድም በሌሊት
በምኵራብ ማደር ተሳነው ሌሊት በደብረ ዘይት
ሲጸልይ ያድር ነበር እንጂ ።

በከመ ሐይወ መጻጕዕ ።

ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወቦአ ካዕበ ሀገረ ቅፍርናሆም ማቴ፣ ፱፡ ፩ ።

፩ ሁለተኛ ወደቅፍርናሆም ገባ ።
ወእምድኅረ ጕንዱይ መዋዕል ሶበ ሰምዑ ሰብአ
ዜናሁ ከመ ሀሎ ውስተ ቤት ።
ከቤት እንዳለ ከጥቂት ቀን በኋላ ሰዎች ነገሩን
በሰሙ ጊዜ ።

፪ ተጋብኡ ኀቤሁ ብዙኃን ሕዝብ እስከ ኢያ
ገምሮሙ መካን ።

፪ ቦታ እስኪጠባቸው ብዙ ሰዎች ወደሱ ተሰ
በሰቡ ።
ወኢኀበ ጥንት ።
በደጅም ቢሆን ።
ወኮነ ይነግሮሙ ቃሎ ለእለ መጽኡ ኀቤሁ ።
ወደሱ ለመጡ ነገርን ይነግራቸው ነበር ማለት
ወንጌልን ያስተምራቸው ነበር ። አንድም ቃሉ
ይላል አካላዊ ቃል ያስተምራቸው ነበር ።

፫ ወአምጽኡ ኀቤሁ ድውየ መጻጕዓ እንዘ
ይጸውርዎ በዓራት እርብዕቱ እደው ። ሉቃ፣ ፭፣ ፲፰።

፫ እራት ሰዎች ባልጋ ተሸክመው ደዌ የጸ
ናበት ሰው አመጡለት ።

፬ ወሶበ ስዕኑ አብኦቶ ኀቤሁ እስመ ጽፉቅ
ሰብእ ኀበ ሀሎ እግዚእ ኢየሱስ ።

፬ ጌታ ካለበት ቦታ ብዙ ሰው ነበርና ወደ
ጌታ ማቅረብ በተሳናቸው ጊዜ ወጽፉቅ በዋዌ
ቤታ እንዲል ።
ዓርጉ ናሀስ ወነሠቱ ጠፈረ ቤት ወአውረድዎ
ምስለ አራቱ ዘዲቤሁ ይሰክብ ውስቴ መፃጕዕ ።
ከሰገነቱ ወጥተው ማገሩን አፍርሰው አስፋፍተው
ድውዩን ከናልጋው አገቡት ። አንድም ቤተ ምሕ
ኃይ ቤተ ምክራም አላቸው ። በበጋ የሚያኖሙት
በክረምት የሚደፉት እለ ያን አንሰተው አወረዱት

፭ ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ሃይማኖቶሙ ይቤሎ
ለውእቱ መፃጕዕ ወልድየ ተኃድገ ለከ ኃጢአትከ።

፭ ጌታ ሃይማኖታቸውን አይቶ ያን ድውይ
ኃጢአትህ ተሰርዮልሐል አለው ።

፮ ወሀለዉ ህየ ጸሐፍት ይነብሩ ኢዮ፣ ፲፬ ፣ ፫
ኢሳ ፣ ፵፫ ፣ ፴፭ ።

፮ ጸሐፍት ከዚያ ተቀምጠው ነበር ።
፮ ወሀለዪ በልቦሙ ወይቤሉ ምንትኑ ዝ ዘከ
መዝ ጽርፈተ ይነብብ ።

፯ በልባቸው አሰበው ይህ እንዲህ ያለ ስድብ
ለምን ይናገራል ፣ መኑ ይክል ኃዲገ ኃጢአት ዘእን
በለ ፩ እግዚእብሔር ።
ያላንድ እግዚአብሔርስ ኃጢአት ማስተስረይ የሚ
ቻለው ማነው አሉ ።

፰ ወአእመሮሙ እግዚአ ኢየሱስ በመንፈሱ
ከመ ከመዝ ይሔልዩ ወይቤሎሙ ለምንት ከመዝ
ትሔልዩ እኩየ በልብክሙ ፣

፰ ጌታም እንዲህ እንዲያስቡ በመንፈሱ ዐውቆ
ለምን እንዲህ ክፉን ታስባላችሁ ።

፱ ምንት ይቀልል እምብሂሎቱ ለዝ መፃጕዕ
ተኃድገ ለከ ኃጢአትከ ወእምብሂለ ተንሥእ ወን
ሣእ አራተከ ወሑር በእገሪከ ።

፱ ይህን ድውይ ኃጢአትህ ተሰረየልህ ከማ
ለትና ተነሥተህ አልጋህን ተሸክመህ ሂድ ከማ
ለት ማናቸው ይቀላል አላቸው ።

፲ ከመ ታእምሩ ከመ ብውህ ሎቱ ለወልደ
ዕጓለ እመሕያው ይኅድግ ኃጢአተ በዲበ ምድር።

፲ በምድር ላይ ኃጢአት ያስተሰርይ ዘንድ
ለሰው ልጅ ሥልጣን እንዳለው ልታውቁ ።

፲፩ ወካዕበ ይቤሎ ለውእቱ ድውይ ለከ፤እብለከ
ተንሥእ ወንሣእ አራተከ ውእቱ ቤተከ ።

፲፩ ዳግመኛ ያን ድውይ ተነሥተህ አልጋህን
ተሸክመህ ወደቤትህ ሂድ እልሃለሁ አለው ።

፲፪ ወተንሥአ ሶቤሃ ወነሥአ አራቶ ወወፅአ
በቅድመ ኵሎሙ ሰብእ ።

፲፪ ያን ጊዜውንም ተነሥቶ አልጋውን ተሸ
ክሞ በሰው ሁሉ ፊት ወጣ ።
ወአንከሩ ኵሎሙ ሕዝብ ወአዕኰትዎ ለእግዚአ
ብሔር ፤ ሰዎች ሁሉ አድንቀው እግዚአብሔርን
አመሰገኑት ።
ወይቤሉ ኢርኢነ ግሙራ ዘከመዝ ።
ከቶ እንዲህ ያለ አላየንም አሉ ።

ዘከመ ተጸውዖ ሌዊ ።

፲፫ ወአምዝ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ካዕበ መን
ገለ ጽንፈ ባሕር ።

፲፫ ከዚህ በኋላ ጌታ ወደ ባሕር ዳር ወጣ ።
ወሖሩ ኀቤሁ ኵሉ ሕዝብ ።
ሕዝቡ ሁሉ ወደሱ ሄዱ ።
ወመሀሮሙ ።
አስተማራቸው ።

፲፬ ወኃሊፎ እምህየ ርእዮ ለሌዊ መጸብሐዊ
ወልደ እልፍዮስ እንዘ ይነብር ኀበ ምጽባሕ ።
ማቴ፡፱ ፡ ፱ ፡ ሉቃ ፡ ፭ ፡ ፳፯ ።

፲፬ ከዚያም አልፎ ሲሄድ የእልፍዮስን ልጅ
ሌዊን ከሚያስገብርበት ቦታ ተቀምጦ አየው ።
ሐተታ፤ ማቴዎስን ወልደ ዲቁ ይለዋል ከዚህ ወልደ
እልፍዮስ አለው እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ
አይጣላም ። ላንድ ሰው ሁለት ስም አለውና ።
አንድም አንዱ ያባቱ አንዱ የእያቱ ።
ወይቤሎ ነዓ ትልወኒ ።
ተከተለኝ አለው ፡ ወተንሢአ ተለዎ ተነሥቶ ተከ
ተለው ።

፲፭ ወእንዘ ይመስሕ ውስተ ቤቱ እግዚእ ኢየ
ሱስ ።

፲፭ ከዚህ በኋላ ጌታ በቤቱ ተቀምጦ ሲበላ ፡
ሀለው ምስሌሁ ብዙኃን ኃጥአን ወመጸብሐን ዘረ
ፈቁ ምስለ እግዚእ ወአርዳኢሁኒ ።
ብዙ ቀራጮችና ኃጥአን ከጌታና ከደቀ መዛሙርቱ
ጋራ ተቀምጠው የበሉ ነበሩ ።
ወብዙኃን እሙንቱ እለ ይተልውዎ ፡
የተከተሉትም ብዙ ነበሩ ።
ወኮኑ ይተልውዎ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ።
ጸሐፍት ፈሪሳውያንም ተከትለውት ነበር ፡

፲፮ ወርእዮሙ ከመ ይበልዕ ምስለ ኃጥአን
ወመጸብሐን ።

፲፮ ከኃጥአንና ከመጸብሐን ጋራ ሲበላ ባዩት
ጊዜ ፡ ይቤልዎሙ ለአርዳኢሁ ለምንት ይበልዕ
ወይሰቲ ሊቅክሙ ምስለ ኃጥአን ወመጸብሐን ፡
ደቀ መዛሙርቱን መምህራችሁ ከመጸብሐን ጋራ
ለምን ይበላል አሏቸው ፡ ማቴዎስ አርድእተ ዮሐ
ንስ ጠየቁት ይላል ፡ ከዚህ ማርቆስ ጸሐፍት ፈሪሳ
ውያን ጠየቁት አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ
አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ፡ ፈሪሳውያን
አርድእተ ዮሐንስን ጠይቁልን ብለዋቸው ጠይቀ
ውታል ፡ ማርቆስ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ጠየቁት
ማለቱ ኋላ ተከትለው ሄደው ጠይቀውታል እግ
ላጅ የሰደደ ሰው እብሮ ተከትሎ ሄዶ እንዲናገር አን
ድም ነገር እንደ ማርቆስ ነው ፈሪሳውያን ሄደው ጠይ
ቀውታል ባይመልስላቸው ለኛስ አልመለሰልንም እና
ንተ ሂዱችሁ ጠይቁት ብለዋቸው አርድእተ ዮሐ
ንስ ሂደው ጠይቀውታል እንጂ ማቴዎስ ይሀን
ተካፍለው ጽፈዋል ።

፲፯ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ይቤሎሙ ሕሙ
ማን ይፈቅድዎ ለዓቃቤ ሥራይ ወአኮ ጥዑያን
፩፡ጢሞ፡ ፩፡፲፭ ።

፲፯ ጌታም ይህን ሰምቶ ባለመድኃኒትን ድው
ያን ይሹታል እንጂ ጤነኞች አይሹትም ። ወኃ
ጥአነ አጸውዕ መጻእኩ ወአኮ ጻድቃነ ።
ጻድቃንን ያይደለ ኃጥአንን ልጠራ መጥቻለሁ
ኦ ላቸው ።

በእንተ ጾም ዘክርስቲያን ።

፲፰ አርዳኢሁሰ ለዮሐንስ ወእለሂ ፈሪሳውያን
ኮኑ ይጾውሙ ።

፲፰ የዮሐንስ ደቀ መዛሙርትና የፈሪሳውያን
ወገኖች ይጦሙ ነበርና ።
ወመጽኡ ወይቤልዎ በእፎ አርዳኢሁ ለዮሐንስ ወአ
ርዳኢሆሙ ለፈሪሳውያን ይጾውሙ ።
የፈሪሳውያንና የዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ስለምን
ይጦማሉ ።
ወአርዳኢከ ኢይጾውሙ ።
ደቀ መዛሙርትህ ግን አይጦሙም አሉት ።

፲፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ
ይክሉኑ ደቂቀ ለመርዓዊ ጸዊመ አምጣነ ሀሎ መር
ዓዊ ምስሌሆሙ ።

፲፱ ጌታም የሰርግ ልጆች ከሙሽራ ጋራ ሳሉ
መጾም ይቻላቸዋልን አላቸው ።

፳ ወባሕቱ ይመጽእ መዋዕል አመ ይነሥእዎ
ለመርዓዊ እምኔሆሙ ። ማቴ፡፱፡፲፭ ። ሉቃ ፭፡ ፴፭።

፳ ነገር ግን ሙሽራው ከሳቸው የሚለይበት
ዘመን ይመጣል ።
ወአሜሃ ይጾውሙ ፤
ያን ጊዜ ይጦማሉ ።

፳፩ ወአልቦ ዘይጠቅብ ግምደ ድርግሃ ውስተ
ስጠተ ልብስ ብሉይ ።

፳፩ ባረጀ ልብስ ቀዳዳ አዲስ እራፊ የሚሰፋ
የለም ።
ወእመ አኮሰ ያነቅዖ ጥቅቡ ሐዲስ ለብሉይ ።
ያለዚያ ግን ማለት ቢሰፋት ግን አዲሱ እራፊ
አሮጌውን ይቀድዋል ።
ወየዓብዮ ለሰጠቱ ።
ቀዳዳውን ያሰፋዋል ።

፳፪ ወአልቦ ዘይወዲ ወይነ ሐዲሰ ውስተ ዝቅ
ብሉይ ።

፳፪ ጉሽ ጠጅ ባረጀ ረዋት የሚያኖር የለም።
እስመ ያነቅዖ ወይን ሐዲስ ለዝቅ ብሉይ ።
ጉሽ ጠጅ ያረጀውን ረዋት ይቀደዋልና ።
ወወይንሂ ይትከዓው ። ጠጁም ይፈሳልና ።

ወዝቄሂ ይትኃጐል ።
ረዋቱም ይጠፋልና ።
ወባሕቱ ስወይንሰ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ሐዲስ
ይወድይዎ ፤ አዲሱን ጠጅ ግን ባዲስ ረዋት
ይኾሙታል ፡ ማቴ ፡ ፲፮ ፥ ፱ ፡ ወይትዓቀቡ በበ
ይናቲሆሙ ።እሉ በሳቸው ይጠባበቃሉ ።

በእንተ ሰዊተ ሥርናይ ወሰንበት ።

፳፫ ወእምዝ ወፈረ እግዚእ ኢየሱስ በሰንበት
ማእከለ ገራውህ ፤

፳፫ ከዚህ በኋላ ጌታ ቅዳሜ በርሻ መካከል ሄደ።
ወአርዳኢሁኒ ምስሌሁ ።
ደቀ መዛሙርቱም ከሱ ጋራ ነበሩ ፤
ወእኀዙ ይምሐው ሰዊተ ወይበልዑ ፤
እሸት እያሹ ይበሉ ጀመር ፤
ወይደሐሑ ሎቱ ፍኖተ ፤
የተቃወሰውንም ያቃኑለት ጀመረ ፤

፳፬ ወይቤልዎ ፈሪሳውያን ርኢ ዘይገብሩ አር
ዳኢከ ዘኢይከውን ገቢረ በሰንበት ።

፳፬ ፈሪሳውያን ደቀ መዛሙርትህ ቅዳሜ ሊሠ
ሩት የማይገባ ሥራ ሲሠሩ አስተውል አሉት ።

፳፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ግሙራ
ኢያንበብክሙኑ ዘገብረ ዳዊት አመ ርኅበ፡፩ነገ ፳፡፯።

፳፭ ዳዊት በተራበ ጊዜ ያደረገውን ከቶ አል
ተመለከታችሁም ።
ወውእቱኒ ።
እሱም ።
ወእለ ምስሌሁ ፤
ከሱም ጋራ ያሉ ፤

፳፮ ዘከመ ቦአ ቤተ እግዚአብሔር እንዘ አብ
ያታር ሊቀ ካህናት ወበልዐ ኅብስተ መሥዋዕት
ዘኢይደልዎ ሰበሊዕ ዘእንበለ ለካህናት ለባሕቲቶሙ
ወወሀቦሙ ለእለ ምስሌሁ ወበልዑ ፡ ዘሌ፥፳፬፡፱።

፳፮ አብያታር ሊቀ ካህናት ሁኖ ሳለ ከቤተ እግ
ዚአብሔር ገብቶ ለካህናት ብቻ ይገባቸዋል እንጂ
ሊበላው የማይገባውን መሥዋዕቱን በልቶ ከሱም
ጋራ ላሉ ሰጧቸው እንደበሉ ዳዊት ያደረገውን
ከቶ አልተመለከታችሁምን ፤ ሐተታ ሊቀ ካህናቱ
አቤሜሌክ አይደለም ቢሉ ምሉና ዱግ ሁነው ተሹ
መው ነበር ።

፳፯ ወይቤሎሙ ሰንበትሰ በእንተ ሰብእ ተፈ
ጥረት ወአኮ ሰብእ በእንተ ሰንበት ።

፳፯ ሰንበት ለሰው ተፈጥራለች እንጂ ሰው
ስለሰንበት አልተፈጠረም አላቸው ።

፳፰ ወወልደ ዕጓለ እመሕያው ውእቱ እግ
ዚእ ለሰንበት ፤

፳፰ የሰንበት ጌታዋ የሰው ልጅ ነው ።

ምዕራፍ ፫ ።

በእንተ ዘየብሰት እዴሁ ፤

፩ ወቦአ ካዕበ ምኵራበ በሰንበት ማቴ፡፲፪፥፱ ።
ሉቃ ፮ ፥ ፯ ።

፩ ሁለተኛ ወደ ምኵራብ ቅዳሜ ገባ ።
ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ ዘየብሰት እዴሁ ።
ከዚያም እጁ የሰለለ ሰው ነበር ፤

፪ ወይትዓቀብዎ ለእመ ይፌውሶ በሰንበት
ከመ ያስተዋድይዎ ።

፪ ሊያሳጡት ቅዳሜ ይፈውሰው እንደሆነ
ብለው ይጠብቁት ነበር ።

፫ ወይቤሎ ለውእቱ ብእሲ ዘጽውስት እዴሁ
ተንሥእ ወቁም ማእከለ ።

፫ ያን እጁ የሰለለች ሰው ተነሥተህ ከመካ
ከል ቁም አለው ፤

፬ ወይቤሎሙ ይከውንኑ በሰንበት ገቢረ ሠናይ
አው ገቢረ እኩይ ።

፬ ቅዳሜ በጐ ሥራ መሥራት ይሻላልን ወይም
ክፉ ሥራ መሥራት ፤
አሕይዎ ነፍስኑ ወሚመ ቀቲል የሚገባ ነፍስ
መግደል ነውን ወይስ ማዳን አላቸው ።
ወአርመሙ ።
ዝም አሉ ፤ ማቴዎስ ይከውንሁ ብለው አሳቸው
ጠየቁት ይላል ማርቆስ እሱ ጠየቃቸው አለ እንደ
ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ይከውንሁ
ብለው ቢጠይቁት ምሳሌ በግዕን ነግሮ ተንሥእ
ወቁም ማእከለ ብሎ ይከውንሁ አላቸው አርመሙ
ዝም አሉ ስፋሕ እዴከ ይለዋል አንድም እንደ ማቴ
ዎስ ይከውንሁ ቢሉት ተንሥእ ወቁም ማእከለ
ብሎ ምሳሌ በግዕን ነገራቸው ዝም አሉ ስፋሕ
እዴከ ይለዋል ፤ አንድም እንደ ማቴዎስ ይከውንሁ
ቢሉት መልሶ ይከውንሁ ገቢረ ሠናይ በሰንበት
አሕይዎ ነፍስኑ ወሚመ ቀቲል አላቸው ። ወአር
መሙ ዝም አሉ ምሳሌ በግዕን ነግሮ ተንሥእወቁም
ማእከለ ብሎ ስፋሕ እዴከ ይለዋል ።

፭ ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይትመአዕ
ወይቴከዝ በእንተ ዑረተ ልቦሙ ።

፭ ስለ ልቡናቸው ድንቁርና እያዘነ ጌታ በቁጣ
አያቸው ።

ወእምዝ ይቤሎ ለውእቱ ብእሲ ስፋሕ እዴከ ወሰ
ፍሐ እዴሁ ። ያን ሰው እጅህን ዘርጋ አለው እጁን
ዘረጋ ።
ወሐይወት ወኮነት ከመ ካልዕታ ድና እንደ ሁለተ
ኛይቱ ሆነች ፤

፮ ወወፂኦሙ ፈሪሳውያን ሶቤሃ ተማከሩ ምስለ
ሰብአ ሄሮድስ ከመ ይትቅልዎ ።

፮ ፈሪሳውያን ወጥተው ከሄሮድስ ሰዎች ጋራ ሊገሉት ተማከሩ ።

በእንተ ካልዓን ተአምራት ዘኢየሱስ ፤

፯ ወተግኅሠ እግዚእ ኢየሱስ ምስለ አርዳኢሁ መንገለ ባሕር ።

፯ ጌታ ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ወደ ባሕር ሄደ
፰ ወተለውዎ ብዙኃን ጥቀ እምገሊላ ወእምይሁዳ ወእምኢየሩሳሌም ።
፰ ከይሁዳና ከገሊላ ከኢየሩሳሌም እጅግ ብዙ ሰዎች ተከተሉት ። ወእምኤዶምያስ ወእማዕዶተ ዮርዳኖስ ።
ከዮርዳኖስ ማዶና ከኤዶምያስም ።
ወእምጢሮስ ወእምሲዶና ።
ከሲዶናና ከጢሮስም ።
ወብዙኃን ጥቀ መጽኡ ኀቤሁ ሰሚዖሙ ኵሎ ዘገብረ ያደረገውን ሁሉ የሰሙ እጅግ ብዙ ሰዎች ናቸው ።
፱ ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ያጽንሑ ሎቱ ሐመረ ከመ ኢይትጋፍዕዎ ሰብእ ።
፱ ሰዎቹ እንዳይገፉት ደቀ መዛሙርቱን መርከብ አቆዩኝ አላቸው ።
፲ እስመ ለብዙኃን አሕየዎሙ
፲ ብዙ ሰዎችን አድኖዋቸዋልና ።
ወኮኑ ይትጋፍዕዎ እስከ ይወድቁ ዲቤሁ ።
ከላዩ ላይ እስቲወድቁ ድረስ ይጋፉት ነበር ።
ወእስተብቍዕዎ ከመ ይግሥሥዎ ኵሎሙ ሕሙማን ሕሙማን ሁሉ ሊዳስሱት ይማልዱ ነበር ።
፲፩ ወእለሂ አኀዛነ አጋንንት ርኩሳን እምከመ ርእይዎ ይሰግዱ ሎቱ ።
፲፩ ርኩሳን አጋንንት ያደሩባቸው ሁሉ ያዩት እንደሆነ ይሰግዱለት ነበር ።
ወእንዘ ይጸርሑ ወይብሉ አማን አንተ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ።
ጮኸው የእግዚአብሔር ልጅ በውነት አንተ ነህ አሉ ፤
፲፪ ወኮነ ብዙኃ ይጌሥጾሙ ከመ ኢያግህድዎ
፲፪ እንዳይገልጡት ፤
ወከመ ኢይከሥቱ ግብሮ ፤
ሥራውንም እንዳይገልጡ ብዙ ገሠጻቸው ።

በእንተ ዘከመ ኀረዮሙ ለሐዋርያት ።

፲፫ ወዓርገ ደብረ ወጸውዓ እለ ፈቀደ ። ማቴ ፲ ፥ ፩ ፤ ሉቃ ፮ ፥ ፲፫ ፥ ፱ ፥ ፩ ።
፲፫ ከተራራ ወጥቶ የወደዳቸውን ጠራ ማለት ሹመት ሽረት አደረገ ወመጽኡ ኀቤሁ ።
ወደሱ ሄዱ ።
ወኀረየ ፲ተ ወ፪ተ ወሰመዮሙ ሐዋርያተ ፤
ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት መረጠ ።
ወረሰዮሙ ከመ የሀልዉ ምስሌሁ ።
ከሱም ጋራ እንዲኖሩ አደረጋቸው ። ሐተታ ደጃ
ዝማች በተሾመ ጊዜ ፈጥኖ እንዲይሄድ ወግ ታሪክ ሲያጠና እንዲሰነብት ።

፲፬ ወፈነዎሙ ይስብኩ ።
፲፬ ያስተምሩ ዘንድ ላካቸው ።
፲፭ ወአብሐሙ ያውፅኡ አጋንንተ ወይፈውሱ ዱያነ ።

፲፭ አጋንንትን ያወጡ ዘንድ ድውያንንም ይፈውሱ ዘንድ ሥልጣን ሰጣቸው ።

፲፮ ወሰመዮሙ በበአስማቲሆሙ ፤
፲፮ በየስማቸው ጠራቸው ።
ወሰመዮ ለስምዖን ጴጥሮስ
ስምዖንን ጴጥሮስ አለው

፲፯ ወለያዕቆብ ወልደ ዘብዴዎስ ወለዮሐንስ እኁሁ ሰመዮሙ በእኔርጌስ ።
፲፯ ያዕቆብንም የዘብዴዎስን ልጅ ዮሐንስንም የያዕቆብን ወንድም በአኔርጌስ አላቸው ደቂቀ ነጐድጓድ ብሂል የነጐድጓድ ልጆች ማለት ነው ፤
ሐተታ ፥ በርጌስ ማለት በዕብራይስጥ ልሳን ልጅ ማለት ነው ። ጌስ ደቂቀ ነጐድጓድ ማለት ነው አኔ ትርፍ ቀለም ነው ። እልመስጦአግያ እንደማለት አልም ትምህርት ስጦ ትርፍ አግያ ኅቡእት እንደሆነ ደቂቀ ነጐድጓድ አለ ፥ ደቂቀ ምሥጢር ደቂቀ መለኮት ሲል ነው ። ደቂቀ ነጐድጓድ ማለቱ በምሳሌ ነው ርጡብ ጢስ ከርጡብ ምድር ይቡስ ጢስ ከይቡስ ምድር ወጥቶ አንድ ደመና ይሆናል ከውቅያኖስ ውኃ ጠልፎ ሲወጣ ነጐድጓድ ያሰማል ፥ እኒህም ከቤተ ክህነት ከቤተ መንግሥት ተወልደው ቢያ ስተምሩ ተሰምተዋልና ደቂቀ ነጐድጓድ አላቸው ።
፲፰ ወእንድርያስ ፥
፲፰ እንድርያስ
ወፊልጶስ ።
ፊልጶስ ፥
ወበርተሎሜዎስ ፥
በርተሎሜዎስ ፤
ወማቴዎስ
ማቴዎስ ፤
ወቶማስ
ቶማስም
ወያዕቆብ ወልደ እልፍዮስ
የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ
ወታዴዎስ
ታዴዎስ
ወስምዖን ቀነናዊ
ቀነናዊ ስምዖን ።
፲፱ ወይሁዳ አስቆሮታዊ ዘውእቱ ዘአግብኦ
፲፱ የአስቆሮት ሰው የሚሆን ያሲያዘው ይሁዳ
፳ ወበዊአ ቤተ መጽኡ ካዕበ ብዙኃን እሕዛብ እስከ ኢያበውህዎ ይብላዕ እክለ ።

፳ ከቤት በገባ ጊዜ እንጀራ ይበላ ዘንድ እስኪሳነው ድረስ ብዙ አሕዛብ ሁለተኛ መጡ ። ዘከመ እስተዋደይዎ ለኢየሱስ ከመ ያወፅኦ አጋ ንንተ በብዔል ዜቡል ።

፳፩ ወሰሚዖሙ አዝማዲሁ መጽኡ የአኃዝዎ
፳፩ ዘመዶቹም ሰምተው ሊይዙት መጡ ። እስመ ስሕወ ልቡ ይቤልዎ ።
ልቡሻ እለው ብለዋልና ፤

፳፪ ወጸሐፍትኒ እለ ወረዱ እምኢየሩሳሌም ይቤሉ ብዔል ዜቡል አኀዞ ። ማቴ ፣ ፱፣ ፴፬ ።

፳፪ ከኢየሩሳሌም የወረዱ ጸሐፍት ብዔል ዜቡል አድሮበታል ።

ወበመልአኮሙ ለአጋንንት ያወፅኦሙ ለአጋን ንት ። በሰይጣን አሊቃ ሰይጣናትን ያወ ጣል አሉ ።

፳፫ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ እፎ ይክል ሰይጣን ለሰይጣን አው ፅኦቶ ፤

፳፫ ጌታ ጠርቶ ሰይጣን ሰይጣንን ማው ጣት እንደምን ይቻለዋል ብሎ ምሳሌ መስሎ ነገ ራቸው ።

፳፬ ወመንግሥትኒ ዘበበይናቲሃ ትትናፈቅ ኢት ቀውም ይእቲ መንግሥት ።

፳፬ እርስ በርሱዋ የምትከፋፈል መንግሥት አት ጸናም ።

፳፭ ወእመኒ ቤት ተናፈቀት በበይናቲሃ ኢት ቀውም ይእቲ ቤት ፤

፳፭ ቤትም እርስ በርሷ ብትከፋፈል ያች ቤት አትጸናም ።

፳፮ ወሰይጣንሂ ለእመ ተንሥአ በበይናቲሁ ወተናፈቀ ኢይቀውም ።

፳፮ ሰይጣንም እርስ በርሱ ቢጣላ ቢለያይም አይጠናም ።
እላ ማኅለቅተ ይረክብ ።
ተፍጻሜተ ሲል ነው ። ፍጻሜ አለበት እንጅ ።

፳፯ ወአልቦ ዘይክል በዊእ ቤተ ኃያል ወበ ርብሮተ ንዋዩ ለእመ ኢቀደመ አሲሮቶ ለኃያል ።

፳፯ ብርቱውን አስቀድሞ ካላሰረ ወደብርቱ ቤት መግባት ገንዘቡንም መዝረፍ የሚቻለው የለም ወትምህ ይበረብር ቤቶ ።
ከያዘው በኋላ ግን ቤቱን ይበዘብዛል ፤

፳፰ አማን እብለከሙ ኵሉ ኃጢአት ወፅ ርፈት ይትኀደግ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ፤ ማቴ ፲፪ ፣ ፴፩ ። ሉቃ. ፲፪ ፣ ፲ ። ዮሐ. ፫፣፲፯ ።

፳፰ ኃጢአት ሁሉ ለሰው ልጅ እንዲሰረይ እውነት እነግራችኋለሁ ።

፳፱ ወዘሰ ጸረፈ ዲበ መንፈስ ቅዱስ ኢይት ኃደግ ሎቱ ለዓለም ፤

፳፱ መንፈስ ቅዱስን የሰደበ ግን ለዘለዓለም ስርየት የለውም ወይትኴነን በደይን ለዝልፉ ።
በገሃነም የዘወትር ፍርድ ይፈረድበታል እንጂ ።

፴ እስመ ይቤልዎ ጋኔን ርኩስ አኃዞ ።
፴ ርኩስ ጋኔን አድሮበታል ብለውታልና ።

በእንተ አዝማዲሁ ለኢየሱስ

፴፩ ወመጽኡ እሙ ወአኃዊሁ ወቆሙ አፍአ።
፴፩ ወንድሞቹና እናቱ መጥተው በውጭ ቆሙ እስመ ስህወ ልቡ ይቤሉ ይቤልዎሙ መጽኡእሙ ወአኃዊሁ ብለህ ግጠም ወለአኩ ኀቤሁ ይጸውዕዎ ሊጠሩት ማለት ጥሩልን ብለው ላኩ ፤
ወይነብሩ ብዙኃን ስብእ ምስሌሁ ።
ብዙ ሰዎች ከሱ ጋራ ተቀምጠው ነበር ።

፴፪ ወይቤልዎ ናሁ እምከኒ ወአኃዊከኒ አፍአ ይቀውሙ ወየኃሥሡከ

፴፪ እነሆ እናትህና ወንድሞችህ በውጭ ቆመው ይሹሀል አሉት ።

፴፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ መኑ ይእቲ እምየ
፴፫ እናቴ ማናት ፤
ወእለ መኑ እሙንቱ አኃውየ ፤
ወንድሞቼስ እነማናቸው ብሎ መለሰላቸው ሐተታ፤ ማቴዎስ የነገረው አንድ ነው ይላል ማርቆስ ብዙ እለ እንደምነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ የነገረው አንድ ይሁዳ ነው ፤ ማርቆስ ብዙ ማለቱ መናገር የሁሉ ፈቃድ ከሆነ ብሎ ነው ።

፴፬ ወነጸሮሙ ለእለ ይነብሩ ዓውደ ወይቤ ሎሙ ነዮሙ እምየኒ ወአኃውየኒ ።

፴፬ በዙሪያው ተቀምጠው ወደነበሩት አይቶ እነሆ እናቴም ወንድሞቼም እላቸው ።

፴፭ እስመ ኵሉ ዘይገብር ፈቃዶ ለእግዚአ ብሔር ውእቱ እኁየኒ ወእኅትየኒ ወእምየኒ ፤

፴፭ ወንድሜም እኅቴም እናቴም የእግዚአ ብሔርን ፈቃድ የሚያደርግ ሁሉ ነው ።

በእንተ ምሳሌ ዘራዒ

ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወአኀዘ ካዕበ ይምሐሮሙ ለአሕዛብ አንተ መንገለ ባሕር ። ማቴ ፲፫ ፣ ፩ ሉቃ ፰ ፣ ፬ ።

፩ ዳግመኛ በባሕር አጠገብ ያስተምራቸው ጀመር ።
ወተጋብኡ ኀቤሁ ብዙኃን ሰብእ እስከ ሶበ የዓርግ ውስተ ሐመር ወይነብር ።
ከመርከብ ወጥቶ እስኪቀመጥ ብዙ ሰዎች ወደሱ ተሰበሰቡ ። ወኵሉ ሰብእ ውስተ ሐይቅ ይቀውሙ ሕዝቡ ሁሉ ከወደቡ ተቀምጠው ነበር ።

፪ ወመሐሮሙ ወመሰለ ሎሙ ብዙኃ ፤
፪ ብዙ መስሎ አስተማራቸው ።

፫ ወይቤሎሙ እንዘ ይሜሕሮሙ ስምዑ ፤
፫ ሲያስተምራቸውም ስሙ አላቸው ።
ወፈረ ይዝራእ ዘይዘርእ ፤
የሚዘራ ሊዘራ ወጣ ።

፬ ወእንዘ ይዘርዕ ቦ ዘወድቀ ውስተ ፍኖት ።
፬ ሲዘራ ከመንገድ የወደቀ ዘር አለ ፤
ወመጽኡ አዕዋፍ ወበልዕዎ ፤
አዕዋፍም መጥተው የበሉት ፤

፭ ወቦ ዘወድቀ ዲበ ኰኵሕ ኀበ አልቦ መሬት ብዙኅ ።
፭ ብዙ መሬት ከሌለበት ጭንጫ የወደቀ ።
ወፍጡነ በቈለ ፤
ፈጥኖም የበቀለ ዘር አለ ፤
እስመ አልቦ ዕመቅ ለመሬቱ
ለመሬቱ ጥልቅነት የለውምና ፤
፮ ወሠረቀ ፀሐይ አውዐዮ ፤
፮ ፀሐይ በወጣም ጊዜ ደረቀ ።
እስመ ኢኮነ ዕሙቀ መሬቱ መሬቱ ጥልቅ አይደለምና
ወአልቦ ሥርው ፤
ሥር የለውምና ።
የብሰ ፤ ደረቀ
፯ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ወሐነቆ ሦክ ኢፈረየ
፯ ከሾህ ውስጥ ወድቆ እሾህ አንቆት ያላፈራም ዘር አለ ።
፰ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይት
፰ ከመልካም ምድር የወደቀ፤
ወበቈለ ። የበቀለ
ወልሕቀ ። ያደገ
ወፈረየ ። ያፈራ
ወወሀበ ፍሬ ።
ፍሬውን ያቋረጠ ዘር አለ ።
ቦ ዘ፴ ። ሠላሳ ያፈራ አለ ፤
ወቦ ዘ፷ ። ስሳም ያፈራ አለ ።
ወቦ ዘ፻ ።
መቶም ያፈራ አለ ።

፱ ወይቤሎሙ ዘቦ እዝን ሰሚዐ ለይስማዕ።
፱ ጆሮ ያለው ይስማ አላቸው ።
፲ ወሶበ ተባሕተወ ተስእልዎ እለ ኮኑ ምስሌሁ ምስለ ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ምሳሌሁ ለዝንቱ ነገር ፤
፲ ብቻውንም በሆነ ጊዜ ከሱም ጋራ የነበሩት ከሥራሁለቱ ጋራ ምሳሌውን ጠየቁት ።
፲፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለክሙ ተውሀበ ታእምሩ ምሥጢራ ። ለመንግሥተ እግዚአብሔር ።
፲፩ የእግዚአብሔርን መንግሥት ምሥጢር ማወቅ ለናንተ ተሰጥቷችኋልና ።
ወለእለ እፍአሰ በምሳሌ ይከውኖሙ ኵሉ ።
በውጭ ሳሉ ግን ነገር ሁሉ በምሳሌ ይሆንባቸዋል ።

፲፪ ወርእየ ይርአዩ ወኢይርአዩ ። ኢሳ ፮፥፱ ማቴ ፲፫፥፲፬ ዮሐ ፲፪፥፵ ግብ ፳፰፥፳፮ ሮሜ ፲፩፥፰።
፲፪ ማየትን አይተው እንዳይመለከቱ ።
ወሰሚዐ ይሰምዑ ወኢይሌብው ።
መስማትም ሰምተው እንዳያስተውሉ ።
ከመ ኢይነስሑ ።
እንዳይመለሱ ።
ወኢይሣሃሎሙ ይቅር እንዳይላቸው ። ወኢይትኀደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ ።
ኃጢአታቸውም እንዳይሰረይላቸው ።

፲፫ ወይቤሎሙ ኢተአምሩኑ ዛተ ምሳሌ ።
፲፫ ይህን ምሳሌ ዐታውቁምን ።
እፎ እንከ ተአምሩ ኵሎ አምሳለ ።
ምሳሌውን ሁሉ እንደምን ታውቃላችሁ ማለት ይህን ሳታውቁ ሌላውን እንደምን ታውቃላችሁ ይህን ሳታውቁ ሌላውን ታውቁን አላቸው ።

፲፬ ዘይዘርዕሰ ቃለ እግዚአብሔር ውእቱ ፤
፲፬ ዘሪው ቃለ እግዚአብሔር ነው ።

፲፭ ወእሉ እሙንቱ እለ ውስተ ፍኖት ኀበ ተዘርዐ ቃል እምከመ ሰምዑ ቃለ ይመጽእ ሰይጣን ሶቤሃ ወይነሥእ እምልቦሙ ቃለ ተዘርዓ ።
፲፭ በመንገድም የተመሰሉ ቃል የሚዘራበት የተባሉ ከሰሙ በኋላ ሰይጣን ፈጥኖ መጥቶ የተዘራውን ቃል ከልባቸው የሚወስድባቸው ናቸው ።
፲፮ ወእሉ ካዕበ እሙንቱ ዘውስተ ኰኵሕ ተዘርዑ እለ ይሰምዑ ቃለ ወይትዌከፍዎ ሶቤሃ በፍሥሐ ።
፲፮ ዳግመኛም በጭንጫ የተዘሩትን ቃል ሰምተው ለጊዜው ደስ ብሏቸው የሚቀበሉት ናቸው ።
፲፯ ወአልቦ ሥርው ።
፲፯ ሥር ግን የላቸውም ።
ወጊዜሃ ዳዕሙ እሙንቱ
ለጊዜው ናቸው እንጂ ፤
ወእምከመሰ ኮነ ምንዳቤ ወስደት በእንተዝ ቃል የዓልው ሶቤሃ ።
ስለዚህ ነገር ስደትና መከራ የሆነ እንደሆነ ግን ፈጥነው ይክዳሉ ።
፲፰ ወእሉ እሙንቱ እለ ውስተ ሦክ ተዘርዑ እለ ይሰምዕዎ ለቃል ።
፲፰ ወሕሊና ዝንቱ ዓለም ወፍትወተ ብዕል ወባዕዳንኒ ኵሉ ፍትወት ይበውእዎ ወየሐንቅዎ ለቃል ። ፩ ፡ ጢሞ ፮፥፲፯ ።
፲፱ በሾህ የተዘሩ ቃልን ሰምተው ብልጽግና መውደድና ።
፲፱ የዚህ ዓለም አሳብ ሌላውም መመኘት ሁሉ መጥቶ ነገሩን የሚያንቀው ነው ።
ወኢይፈሪ ።
አያፈራም ።

፳ ወእሉ እሙንቱ እለ ውስተ ምድር ሠና ይት ተዘርዑ እለ ይሰምዑ ቃለ ወይትዌከፍዎ፥

፳ በመልካም ምድር የዘሩት ግን ቃልን ሰም ተው የሚቀበሉት ወይፈርዩ ።　　የሚያፈሩ

| | |
|---|---|
| ፩ዱ ፴ ። | አንዱ ሠላሳ ፥ |
| ወ፩ዱ ፷ ፥ | አንዱ ስሳ ። |
| ወ፩ዱ ፻ ፥ | አንዱ መቶ ፥ |

፳፩ ወይቤሎሙ ቦኑ ዘየሐቱ ማኅቶተ ወያ ነብራ ታሕተ ከፈር ። ማቴ ፭፥፲፭፥ ሉቃ ፰፥፲፮ ፥

፳፩ እንቅብ ቅርጫት ሊደፋባት ፋና የሚያ በራ የለም ። እንደዚህም ሁሉ ላይተረጉም የሚ መስል የለም ፥
አላ ያነብርዋ ዲበ ተቅዋማ ፥
ከመቅረዝ ላይ ሊያኖሩት ነው እንጂ ሊተረጉም ነው እንጂ ፥

፳፪ ወአልቦ ኅቡእ ዘኢይትከበት ። ማቴ ፲፥ ፪ ሉቃ ፮፥፴፫ ።

፳፪ የማይገለጥ የተሰወረ የለምና ፥
ወአልቦ ከዱን ዘኢይትከሠት ።
የማይገለጥ የተሸፈነ የለምና ፥

፳፫ ወዘቦ እዝነ ሰሚዓ ለይስማዕ
፳፫ ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ ።
፳፬ ወይቤሎሙ ለብዉ ዘትሰምዑ ማቴ ፯፥፪ ሉቃ ፮፥ ፴፰ ፥
፳፬ የምትሰሙ እናንተ አስተውሉ ፥
በውእቱ መሥፈርት ዘሰፈርክሙ ይሰፍሩ ለክሙ
በሰፈራችሁበት መሥፈሪያ ይሰፍሩላችኋል ።
ወይዌስኩክሙ
ይጨምሩላችኋልም እንደ አእምሯችሁ ሕጸጽ መጠን እንዲመስሉባችሁ ዕወቁ አላቸው ።
፳፭ እስመ ለዘቦ ይሁብዎ
፳፭ ላለው ይሰጡታል
ወይዌስክዎ ። ማቴ ፲፫፥፲፪ ሉቃ ፰፥፲፰ ፲፱፥፳፮፤
ይጨምሩለታልና ።
ወለዘሰ አልቦ እለሂ ቦ የሐይድዎ ።
የሌለውን ግን ያለውን ቅሉ ይወስዱበታል ።
በእንተ ዘርዕ መማዕረር ።
፳፮ አኮኑ ከመዝ ርትዕት ይእቲ መንግሥተ ሰማያት ከመ ብእሲ ዘይዘርዕ ሠናየ ዘርዓ ውስተ
፳፯ ገራንቱ ወነዊሞ ይትነሣእ መዓልተ ወሌ ሊተ ወይዋሕዮ
፳፯ ነዊሞ ሌሊተ ይትነሣእ መዓልተ ብሰሀ ግጠም ፥ መንግሥተ ሰማይ ሕገ ወንጌል ፥ ሕገ ወን ጌል ተስፋ ፥ ተስፋ ኢየሱስ
፳፯ ክርስቶስ በርሻው መልካም ዘር ዘርቶ ሌሊት ተኝቶ ቀን ተነሥቶ እርሻውን የሚጐበኝ ገበሬን ትመስላለች እኮን ፥ ትመስል የሰምን ፥ ሐተታ ፥ ጌታ ኑሮ ኑሮ ለበውከሙኑ ማለቱን መናገር ነው ።
ወዘርዑ የዓቢ ወይልሕቅ ፥
ዘሩም በቅሎ ያድጋል ።

፳፰ ወውእቱሰ የአምር ከመ ባሕቲታ ምድር ትሁብ ፍሬሃ ፥

፳፰ እሱም ምድር የዘሩባት እንደሆነ ፍሬ እን ድታቀርጥ ዐውቆ ይዘራባታል ፥ እኔም የተማራችሁ እንደሆነ ከፍጹምነት እንድትደርሱ ዐውቄ አስተ ምራችኋለሁ ። አንድም ውእቱሰ የአምር ከመ ኢትሁብ ምድር ፍሬ ፥ ምድር ካልዘሩባት ፍሬ እንዳታቀርጥ ዐውቆ ይዘራል ። እኔም ካልተማራ ችሁ ከፍጹምነት እንዳትደርሱ ዐውቄ አስተምራ ችኋለሁ ፥ አንድም ውእቱሰ ኢየአምር ከመ ትሁብ ወከመ ኢትሁብ ፍሬ ይላል ፥ እሱ ታቀርጥም እንደ ሆን አታቀርጥም እንደሆን ሳያውቅ ይዘራል ። እኔ ግን የተማራችሁ ያወቃችሁ እንደሆነ ፍጹማን እንድትሆኑ ከፍጹምነት እንድትደርሱ አውቄ አስ ተምራችኋለሁ ።
ቀዳማዊ ሣዕረ ፥
መጀመሪያ ሣዕርን ማለት ቡቃያ ወእምዝ ሰብለ ፥ ቀጥሎ ዝርዝር ወእምሰብል ይመልእ ፍጹመ ሥርናየ በዛላው ሥንዴን ይመላል ማለት ጎምር ይሆናል ።
፳፱ ወሶበ ፈጸመ ፈርየ ይፈኑ ማዕፀደ ።
፳፱ ፈጽሞ ባፈራ ጊዜ ማለት መከር በደረሰ ጊዜ አጫጅ ይልካል ። አንድም ቡቃያ ጥንተ ስብ ከት ዝርዝር ቂሣርያ ጎምር ደብረ ታቦር ይፌኑ ማዕ ፀደ ዕለተ ዓርብ ፥ አንድም ቡቃያ ቂሣርያ፥ ዝርዝር ደብረ ታቦር፤ ጎምር ዕለተ ዓርብ ይፌኑ ማዕፀደ ትን ሣኤ ዕርገት ዕለተ ምጽአት ። አንድም ንጽሐ ሥጋ ንጽሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና፥ ይፈኑ ማዕፀደ ሞት ሠና ይት ነው ።
እስመ በጽሐ ማዕረር ፤
መከር ደርሷልና ።

በእንተ ኅጠተ ሰናፔ ።

፴ ወይቤ በምንት አስተማስላ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ።
፴ የእግዚአብሔርን መንግሥት በምን እመስላታለሁ ።
ወምንተ ትመስል ።
ማንንስ ትመስላለች ።
፴፩ ትመስል ኅጠተ ሰናፔ እንተ ተዘርዓት ውስተ ምድር ማቴ ፲፫፥፴፩ ፥ ሉቃ ፲፫፥፲፰ ።
፴፩ በምድር የተዘራች የሰናፍጭ ቅንጣትን ትመስላለች ።
፴፪ ወእምከመ ተዘርዓት ትበቍል ፥
፴፪ በተዘራችም ጊዜ ትበቅላለች ።
ወተዓቢ እምኵሉን አህማላት ፤

ከሰምስም ሁሉም ትበልጣለች ወትገብር አዕጹቀ ዓበይተ ታላላቅ ቅርንጫፎችም ታወጣለች ። እስከ ይክሉ አዕዋፈ ሰማይ አጽልሎ ታሕተ አዕጹቂሃ ፤
የሰማይ ወፎች ከጽላዋ በታች ማረፍ እስኪቻላቸው

፴፫ ወበዘከመዝ አምሳል ተናገሮሙ ቃሎ በአ ምጣነ ይክሉ ሰሚዓ ፤

፴፫ መስማት በሚቻላቸው መጠን እንዲህ ባለ ምሳሌ ቃሉን ነገራቸው ።

፴፬ ወዘእንበለ ምሳሌሰ ኢተናገሮሙ ።
፴፬ ያለ ምሳሌ ግን አልነገራቸውም ወበባ ሕቲቶሙ ለአርዳኢሁ ይፌክር ኵሎ ።
ለደቀ መዛሙርቱ ግን ለብቻቸው ሁሉን ይተረጉም ላቸው ነበር ።

፴፭ ወይቤሎሙ ለአ ርዳኢሁ ንዕዱ ማዕዶተ ።
፴፭ በዚያም ቀን በመሸም ጊዜ ደቀ መዛሙ ርቱን ወደማዶ እንሂድ አላቸው ።
፴፮ ወኃደጎሙ ለሕዝብ ወነሥእዎ በሐመር ምስሌሆሙ ። ማቴ ፰፥፳፫ ሉቃ ፰፥፳፪፥ ፴፮ ።
፴፮ ሕዝቡን አሰናብቶ በመርከብ ይዘውት ሄዱ ወቦ ካልዓትኒ አሕማር ምስሌሆሙ ።
ሌሎችም መርከቦች ከሳቸው ጋራ ነበሩ ።
፴፯ ወመጽአ ዐውሎ ዓቢይ ነፋስ ።
፴፯ ታላቅ ዓውሎ ነፋስ መጣ ወይሰውጥ ማየ አሞገድ ውስተ ሐመር እስከ ይመልእ ማየ ውስተ ሐመር ።
ውኃው መርከቡን እስኪሞላው ድረስ ውኃውን እያፈሰ ከመርከቡ ይጨምረው ነበር ።
፴፰ ወውእቱሰ መንገለ ከዋላ ሐመር ከተር ኢሶኖመ እሱ ግን በከበሮ ቤት በኩል
፴፰ ከንዱን ተንተርሶ ተኝቶ ነበር ።
ወአንቅሕዎ ። ቀሰቀሱት ።
ወይቤልዎ ሊቅ ኢየኃዝነከኑ እንዘ ንመውት ፤
መምህር ሆይ ስንሞት አናሳዝንህም አሉት ።
፴፱ ወተንሥአ ወገሠፆሙ ለነፋሳት
፴፱ ተነሥቶ ነፋሳትን ገሠጻቸው ።
ወይቤሳ ለባሕር ተፈጸሚ ወአርምሚ ።
ባሕርን ጸጥ በይ ዝም በይ አላት ወኀደገ ነፋስ ።
ነፋስ መንፈሱን ተወ ።
ወኮነ ዓቢይ ዛኅን ፤
ታላቅ ጸጋታም ተደረገ ፤
፵ ወይቤሎሙ ምንትኑ ያፈርኃከሙ አ ድኩማን ።
፵ እናንተ ደካሞች ምን ያስፈራችኋል ፤
ከመዝኑ አልብከሙ ሃይማኖት ፤
እንዲህ ሃይማኖት የላችሁምን አላቸው ።
፵፩ ወፈርሁ ዓቢየ ፍርሃተ
፵፩ ፈጽመው ፈሩ ፤

ወተበሀሉ በበይናቲሆሙ መኑ እንጋ ውእቱ ዝንቱ ዘይትኤዘዙ ሎቱ ባሕርኒ ወነፋሳትኒ ።
ባሕርም ነፋሳትም የሚታዘዙ ለት ይህ ማነው እንጃ አሉ ።

## ምዕራፍ ፭ ።

፩ ወበጺሖሙ ማዕዶተ ባሕር ኀበ ብሔረ ጌርጌሴኖን ። ማቴ ፰፥፳፰።ሉቃ ፰፥፳፮ ።

፩ በባሕር ማዶ ወዳለ ወደ ጌርጌሴኖን ደረሱ።
፪ ወወሪዶ እምሐመር ተቀበሎ ሶቤሃ ብእሲ ዘአኩይ ጋኔን ላዕሌሁ ወጺአ እመቃብር ፤

፪ ከመርከቡ በወረደ ጊዜ ርኩስ ጋኔን የያዘው ሰው ከመቃብር ወጥቶ ተገናኘው ።

፫ ወይነብር ውስተ መቃብር
፫ ከመቃብር ይኖር ነበር ።
ወስዕንዎ አውፅኦቶ በመዋቅሕትኒ እንዘ ዘልፈ ይሞቅሕዎ ዘወትር ሲያስሩት በሰንሰለት ስንኳ ማጽ ናት ተሳናቸው ።
ወአልቦ ዘይክል አድክሞቶ ።
የሚችለው አልነበረም ።

፬ እስመ መዋቅሕተኒ ይሰብር
፬ እግር ብረቱንም ይሰብረው ነበርና ።
ወሰናስለኒ ይቀጠቅጥ ።
ሰንሰለቱንም ያወልቅ ነበረና ።
ወያዓቅብዎ ደቅ
ሕፃናት ይጠብቁት ነበርና ሐተታ፥ ግብረ አበር ናቸውና ብር ብር እያሉ አንድም ኃያል ሲል ነው ለይትነሥኡ ደቅነ ወይትዋነዩ በቅድሜነ እንዲል

፭ ወዘልፈ የዓወዩ መዓልተ ወሌሊተ በው ስተ መቃብር ወበውስተ አድባር ፤

፭ ሁልጊዜም በመዓልትና በሌሊት በመቃብ ርና በተራራ ይጮሀ ነበረ ።
ወይጌምድ ሥጋሁ በእብን
ሥጋውንም በድንጊያ ይፈጨው ነበር
፮ ወሶበ ርእዮ ለእግዚእ ኢየሱስ እምርኁቅ ሮፀ ወሰገደ ሎቱ ፤
፮ ጌታን በሩቅ ባየው ጊዜ መጥቶ ሰገደለት።
፯ ወጸርሐ በዓቢይ ቃል ወይቤ ምንት ብየ ምስሌከ ኢየሱስ ወልደ እግዚአብሔር ልዑል ፤
፯ የልዑል የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ሆይ ካንተ ጋራ ምን ጠብ አለኝ ።
አምሐለከ በእግዚአብሔር ሕያው ከመ ኢትሣቅየኒ እንዳታሰቃየኝ በሕያው በእግዚአብሔር አምልሐለሁ ብሎ በታላቅ ቃል አሰምቶ ተናገረ ።
፰ እስመ ይቤሎ ለውእቱ ጋኔን እኩይ ፃእ እምላዕሌሁ ።
፰ ያን ርኩስ ጋኔን ውጣ ይለው ነበርና ።

፱ ወተሰአሎ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ መኑ ስምከ ፧

፱ ኢየሱስም ስምህ ማነው ብሎ ጠየቀው ። ወይቤሎ ውእቱ ጋኔን ሌጌዎን ስምየ እስመ ብዙኃን ንሕነ ፤ ያም ጋኔን ብዙ ነንና ስሜ ሌጌዎን ነው አለ ። ሐተታ ቁጥ ማለት ነው ዘበእንተ መዓቶሙ ተሰምዩ ሌጌዎን እንዲል ።

፲ ወአስተብቍዖ ብዙኃ ከመ ኢይሰድዶ እፍአ እም ብሔር ።

፲ ካገር ወደውጭ እንዳይሰዳቸው መላልሶ ለመነው ።

፲፩ ወቦ ህየ መራዕየ አኅርው ብዙኃ ይትረዓይ መንገለ ደብር ፤

፲፩ ከዚያ ብዙ የሪያ መንጋ በተራራ አጠገብ ተሰማርቶ ነበር ።

፲፪ ወአስተብቍዕዎ ብዙኃ እሉ አጋንንት ወይቤልዎ እመሰ ታወጽአነ ፈንወነ ውስተ አኅርው ከመ ንባዕ ላዕሌሆሙ ።

፲፪ በእሪያዎች እንገባባቸው ዘንድ አሰናብተን ብለው ለመኑት ።

፲፫ ወአብሖሙ እግዚእ ኢየሱስ

፲፫ ጌታም ፈቀደላቸው ።

ወወፂኦሙ እሙንቱ አጋንንት ቦኡ ላዕለ አኅርው እኒያም አጋንንት ከሰዎቹ ወጥተው በእሪያዎች ገቡ ወዓብዱ እሙንቱ መራዕይ ወፀድፉ ውስተ ባሕር የሪያወም መንጋ ሁሉ ሮጠው ከባሕር ወደቁ ።

ወኮኑ መጠነ ፳፻

ሁለት ሺህ ያህሉ ነበር

ወሞቱ ውስተ ባሕር

በባሕርም ውስጥ ሞቱ ።

፲፬ ወጐዩ ኖሎት ወዜነው ለአኅጉር ወለአዕፃዳት

፲፬ እሪያ ጠባቆች ግን ሸሽተው በአደባባይና በሀገሩ አወሩ ፤

ወወጽኡ ይርአዩ ዘኮነ ፤

የሆነውንም ለማየት ወጡ

፲፭ ወርእዩ ወመጽኡ ኀበ እግዚእ ወረከብዎ ለዘጋኔን እኀዞ እንዘ ይነብር ድኁነ ወልቡሲ ገቢሮ ወልቡሰ ልብሶ ዝኩ ዘአኀዞ ሌጌዎን ።

፲፭ ወደጌታም በመጡ ጊዜ ያ ጋኔን ያደረበትን ሰው አእምሮው ተመልሶ ልብሱን ለብሶ ከጌታ ጋራ ተቀምጦ አገኙት ሐተታ ማቴዎስ ሁለት ሰዎች ናቸው ይላል፤ማርቆስ አንድ ሰው አለ አንደም ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ሁለት ናቸው ማርቆስ አንድ ማለቱ ለመንገር ከበቃ ብሎ አንድም አንዱ የፀናበት አንዱ ያልፀና በት ነው ማቴዎስ የጸናበትንም ያልጸናበትንም ቆጥሮ ሁለት አለ ማርቆስ ያልጠናበትን ትቶ አንድ አለ ፣

ወፈርሁ ፤

ፈሩ ።

፲፮ ወዜነውዎሙ እለ ርእዩ ዘከመ ኮነ ዘጋኔን ወዘበእንተ አኅርው ፤

፲፮ ጋኔን ያደረበት ሰው የሆነውን በእሪያዎችም የተደረገውን ያዩ ሰዎች ነገሩዋቸው ፤

፲፯ ወአኀዙ ያስተብቍዕዎ ከመይግዕ እምዶ ወሎሙ ።

፲፯ ካገራቸው ይሄድ ዘንድ ይለምኑት ጀመሩ፤

፲፰ ወዓሪጎ ሐመረ ወአስተብቍዖ ውእቱ ዘጋኔን ይሖር ምስሌሁ ፤

፲፰ ከመርከብ በወጣ ጊዜም ያ ጋኔን ያደረበት ሰው ከሱ ጋራ ይሄድ ዘንድ ማለደው ። ሐተታ ምናልባት ሽቶ ይመለስብኛል ብሎ ፈርቶ ፤

፲፱ ወከልኦ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ሑር ውእቱ ቤተከ ኀበ አሊአከ ።

፲፱ ጌታ ከለከለው ምናልባት ሽቶ ላለው አጣህ ምናልባት አይደለም ወደቤትህ ወደወገኖችህ ሂድ አለው። ወንግር ኵሎ ዘገብረ ለከ እግዚአብሔር

እግዚአብሔር ያደረገልህን አትስምር አለው ።ሐተታ ይመለስብኛል ብሎ ፈርቶ ላለው አይዞህ አይመለ ስብህም ከቤትህ ሂደህ እግዚአብሔር ያደረገልህን ተአምራት አስተምር አለው ወዘከመ ተሣሃለከ ይቅርም እንዳለህ ተናገር ፣

፳ ወሖረ ወእኃዘ ይሰብክ በዐሥሩ አኅጉር ኵሎ ዘገብረ ሎቱ ኢየሱስ ።

፳ ጌታ ያደረገለትን ሁሉ ባሥሩ አገር ያስተ ምር ጀመረ ።

ወአንከሩ ኵሎሙ

ሁሉም አደነቁ ።

ዘከመ ፈወሶን ለእንተ ደም ይውኅዛ ወለወለተ ኢያ ኢሮስ ።

፳፩ ወካዕበ ዓደወ እግዚእ ኢየሱስ በሐመር ማዕዶተ ።

፳፩ ዳግመኛም ጌታ በመርከብ ወደማዶ ተሻገረ ወተጋብኡ ብዙኃን ሰብእ ኀቤሁ ኀበ ሐይቀ ባሕር በባሕር አጠገብ ሳለ ብዙ ሰዎች ወደሱ ተሰበሰቡ

፳፪ ወመጽአ ኀቤሁ ፩ዱ ብእሲ መጋቤ ምኵራብ ዘስሙ ኢያኢሮስ

፳፪ የምኵራብ ሹም ኢያኢሮስ የሚባል አንድ ሰው ወደሱ መጣ ወሶበ ርእዮ ሰገደ ሎቱ ታሕተ እገሪሁ ፤ ባየውም ጊዜ ከእግሩ በታች ሰገደለት

፳፫ ወብዙኃ አስተብቍዖ

፳፫ እጅግም ለመነው ።

ወይቤ ወለትየ አልጸቀት ትሙት

ልጄ ልትሞት ቀርባለች

ወባሕቱ ነዓ ደይ እዴከ ላዕሌሃ ወተሐዩ

ነገር ግን መጥተህ እጅህን ጫንባት ትድናለች ።

፳፬ ወሖረ እግዚእ ኢየሱስ ምስሌሁ ወተለ
ውዎ ብዙኃን ሰብእ ፤

፳፬ ብዙ ሰው ተከተሉት ከሱ ጋራ ሔደ ፤
ወተጋፍዕዎ
ያጨንቁት ነበር ።

፳፭ ወመጽአት ብእሲት እንተ ደም ይውኅዛ
እምነ ፲ቱ ወ፪ቱ ክረምት

፳፭ ካሥራሁለት ዓመት ጀምሮ ደም የሚ
ፈሳት ሴት መጣች ።

፳፮ ወብዙኃ አሕመምዋ ብዙኃን ዓቀብተ
ሰራይ እንዘ ይፌውስዋ ።

፳፮ እናድናታለን እያሉ ብዙ ባለመድኃኒቶች
ብዙ አደከሟት ።
ወአስተዋጽአት ኵሎ ንዋያ ወአኅለቀት ።
ገንዘቧን ሁሉ አውጥታ ጨረሰች
ወአልቦ ዘበቍዓ ዘእንበለ ዳዕሙ ዘአልህማ
እየጸናባት ከመሄድ በቀር የረባት የጠቀማት የለም
ሰብእ ጥቀ እኩይ ውእቱ ወአርዌ ምድር ይልሕም
እከየ እንዲል ። ዘእንበለ ዘብእሲ ዘእንበለ ዘተወሰከ
ሕማም ይላል እየባሰባት እየታከለባት ከመሄድ
በቀር የጠቀማት የለም ።

፳፯ ወሰሚዓ በእንተ እግዚእ ኢየሱስ መጽ
አት ወቦአት ማዕከለ ሰብእ ወገሠሠት ጽንፈ ልብሱ
እንተ ድኅሬሁ ።

፳፯ የጌታን ነገር በሰማች ጊዜ መጥታ ከሰው
መካከል ገብታ በኋላ የልብሱን ዘርፍ ዳሰሰች

፳፰ እንዘ ትብል እምከመ ገሠሥኩ ጽንፈ
ልብሱ አሐዩ እምደዌየ ።

፳፰ የልብሱን ዘርፍ የያዝኩ እንደሆነ እድ
ናለሁ ብላ ፥

፳፱ ወሶቤሃ ነጽፈ ነቅዓ ደማ ፤

፳፱ ያን ጊዜውንም የደሟ ምንጭ ደረቀ።
ወአንከረት ርእሳ ወሐይወት እምደዌሃ
ከደዌዋ እንደዳነች እሷ አደነቀች ። አንድም ወአ
እመረት ርእሳ ፥ ጥዒና ተሰማት ።

፴ ወአእመረ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ወፅአ
ኃይል እምኔሁ ወተመይጠ ኀበ ሰብእ ይቤሎሙ
መኑ ገሠሠኒ ጽንፈ ልብስየ

፴ ጌታም ኃይል ከሱ እንደወጣ ዐውቆ ወደ
ሰዎቹ ተመልሶ የልብሴን ዘርፍ የያዘኝ ማነው አላቸው

፴፩ ወይቤልዎ አርዳኢሁ ኢትሬኢኑ ሰብእ
እንዘ ይትጋፍዑከ እንተ ትብል መኑ ገሠሠኒ ጽንፈ
ልብስየ ።

፴፩ ደቀ መዛሙርቱ ሰው ሲያጨንቅህ አታ
ይምን የልብሴን ዘርፍ ማን ዳሠሠኝ ትላለህ አሉት

፴፪ ወተመይጠ ከመ ይርአይ ዘገብረ ዘንተ

፴፪ ይህን ያደረገን ሊያይ ተመለሰ

፴፫ ወፈርሃት ይእቲ ብእሲት

፴፫ ያች ሴት ፈራች
ወርእደት ጥቀ
እጅግ ተጨነቀች
እስመ አእመረት ዘኮነ ላዕሌሃ
የተደረገባትን ስላወቀች
ወመጽአት ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወሰገደት ሎቱ
ታሕተ እገሪሁ
ወደ ጌታ መጥታ ሰገደችለት ወነገረቶ ኵሎ ጽድቀ
እውነቱንም ሁሉ ነገረችው

፴፬ ወይቤላ ወለትየ ሃይማኖትኪ አሕየወተኪ
እትዊ በሰላም ።

፴፬ ልጄ ሃይማኖትሽ አድኖሻልና በደህና
ሂጅ አላት ።
ወሕየዊ እምደዌኪ
ከደዌሽም ተፈወሽ አላት

፴፭ ወእንዘ ይትናገር ምስሌሃ መጽኡ ምስሌሃ
ኀበ መጋቤ ምኵራብ ወይቤልዎ ወለትከሰ ሞተት
ወኢታፃምዎ እንከ ለሊቅ ።

፴፭ ከሷ ጋራ ሲናገር ሰዎች ወደሹሙ መጥተው
ልጅህስ ሞታለች ከእንግዲህስ ወዲህ መምርን እታ
ድክመው አሉት ። ሐተታ ማቴዎስ ወለትየ ሞተት
አለው ይላል ። ማርቆስ አልጸቀት ትሙት አለው
አለ ፥ እንደምነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር
እንደ ማቴዎስ ነው ወለትየ ሞተት ብሎታል ሞተች
አልክ ቢለው ደንግጦ አልጸቀት ትሙት ብሎታል
እንደ ማርቆስ ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ። አንድም
ነገር እንደ ማርቆስ ነው እልፀቀት ትሙት ብሎ
ታል ዝግጥግጥ ቢልበት ፈጥኖ ይሄድልኛል ብሎ
ወለትየ ሞተት ይለዋል ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ።
አንድም አልጸቀት ትሙት ብሎታል ብላቴኖች
መጥተው ወለትከሰ ሞተት ኢታፃምዎ እንከ ለሊቅ
አሉት የብላቴኖቹን ቃል ይዞ ሞተት ብሎታል
የፊተኛውን ማርቆስ የኋለኛውን ማቴዎስ ጻፉ ነገር
እንደ ማቴዎስ ነው ።

፴፮ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይትናገርዎ
ይቤሎ ለመጋቤ ምኵራብ ኢትፍራህ ተአመን ዳዕሙ
ተሐዩ ወለትከ ።

፴፮ ጌታ ግን ሲነግሩት ሰምቶ የምኩራቡን
ሹም እመን እንጂ አትፍራ ልጅህም ትድናለች አለው

፴፯ ወከልዓ ከመ እልቦ ዘይትልዎ ዘእንበለ
ጴጥሮስ ወያዕቆብ ወዮሐንስ እኁሁ ለያዕቆብ ።

፴፯ ከያዕቆብ ከጴጥሮስ ከያዕቆብ ወንድም
ከዮሐንስም በቀር የሚከተለው እንዳይኖር ከለከለ

፴፰ ወቦአ ቤቶ ለመጋቤ ምኵራብ

፴፰ ከምኩራብ ሹም ቤት ገባ ።

ወረከቦሙ እንዘ ይትሐወኩ ወይበክዩ ወየአወይዉ ብዙኃ ሲያለቅሱና ሲታወኩ በብዙም ሲጮሁ አገ ኛቸው ።

፴፱ ወቦአ ወይቤሎሙ ለምንት ትትሐወኩ፤
፴፱ ገብቶ ለምን ትታወካላችሁ አላቸው ።
ወትበክዩ
ለምን ታለቅሳላችሁ
ሕፃንሰ ኢሞተት
[illegible] አልሞተችም አላቸው
አላ ትነውም ።
ተኝታለች እንጂ አላቸው ።

፵ ወሰሐቅዎ ሳቁበት
፵ ወእሚሮ ሰደደ ኵሎ ወነሥኦሙ ለአቡሃ ወለእማ ለሕፃን ወእለ ምስሌሁ ወቦአ ኀበ ሀለ ወት ሕፃን ።
[illegible] ሁሉን አስወጥቶ የብላቴናይቱን እናትና አባት ከእርሱም ጋራ የነበሩትን ይዞ ብላቴናይቱ ካለ ችበት ገባ ።

፵፩ ወአኀዛ እዴሃ ለሕፃን ፤
፵፩ የብላቴናይቱን እጁዋን ያዛት
ወይቤላ ጣቢታ ቁሚ
ጣቢታ ቁሚ አላት ፤
ተንሥኢ ወለትየ ብሂል በትርጓሜሁ ። ትር ጓሜው ልጄ ተነሺ ማለት ነው ።

፵፪ ወተንሥአት ሶቤሃ ይእቲ ወለት ወአን ሶሰወት ።

፵፪ ያችም ብላቴና ፈጥና ተነሥታ ሄደች ።
ወ፲ቱ ወ፪ቱ ክረምታ
አሥራ ሁለት ዓመት ሁኑዋት ነበር ።
ወደንገጹ ሶቤሃ ዓቢየ ድንጋጼ
ያን ጊዜም ታላቅ ድንጋጼ ደነገጡ ።

፵፫ ወገሠጾሙ ለአቡሃ ወለእማ ብዙኃ ከመ አልቦ ዘየአምር ዘንተ

፵፫ ይህን ማንም ማን የሚያውቀው እንዳይ ኖር እናት አባቷን ብዙ ገሠጻቸው ።
ወእዘዘ የሀብዋ ዘትበልዕ
የምትበላውም ስጧት አለ ።

በከመ ሰበከ ኢየሱስ በናዝሬት

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወወፂአ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ ቦአ ሀገሮ። ማቴ ፲፫፥፶፬ ሉቃ ፬፥፲፮ ።

፩ ከዚያም ወጥቶ ወደ ሀገሩ ገባ
ወተለውዎ አርዳኢሁ
ደቀ መዛሙርቱ ተከተሉት ።

፪ ወበሰንበት መሐሮሙ በምኵራብ
፪ ቅዳሜ በምኵራብ አስተማራቸው ።
ወብዙኃን ያጸምዕዎ ወያነክሩ እንዘ ይብሉ እም አይቴ ሎቱ ዝንቱ ኵሉ ትምህርት ።
ብዙ ሰዎች ሰምተው ይህ ሁሉ ከወዴት ተገኘለት ብለው አደነቁ ።
ወምንትኑ ዛቲ ጥበብ እንተ ተውህበት ሎቱ
ይህችስ የተሰጠችው ጥበብ ምንድናት ። ወዝኒ ኃይል ዘይትገበር በእደዊሁ ።
ይህስ በጁ የሚደረግ ኃይል ምንድን ነው ።

፫ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልዱ ለፀራቢ ዮሐ ፮፥ ፵፪ ።

፫ የፀራቢ ልጅ አይደለምን
ወወልደ ማርያም
የማርያምስ ልጅ አይደለምን ።
ወአኀዊሁኒ ያዕቆብ ወዮሳ ወይሁዳ ወስምዖን ፤ ወንድሞቹስ ዮሳና ያዕቆብ ይሁዳም ስምዖንም አይ ደሉምን ። ወአኮኑ አኃቲሁኒ ሀለዋ ዝየ ኀቤነ እኅቶቹስ ከኛ ዘንድ ያሉ አይደለምን ብለው ።
ወተአቅፉ ።
በሱ ምክንያት ተጠራጠሩ ።

፬ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አኮኑ ምንት ነቢይ ዘእንበለ በሀገሩ ወበቤቱ ወበኀበ አዝማዲሁ ማቴ ፲፫፥ ፶፯ ። ሉቃ ፬፥ ፳፬ ። ዮሐ ፬፥ ፵፬ ።

፬ ጌታም ነቢይ በሀገሩና በወገኑ በቤቱም በቀር አይናቅም አላቸው ።

፭ ወኢገብረ ኃይለ በህየ ዘእንበለ ኅዳጣን ድውያን ዘአንበረ እዴሁ ዲቤሆሙ ወአሕየዎሙ

፭ እጁን ጭኖ ካዳናቸው ከጥቂት በሽተኞች በቀር በዚያ ኃይል ተአምራት አላደረገም።

፮ ወአንከረ ኢአሚኖቶሙ ።
፮ አለማመናቸውን አደነቀ
ወአንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ኵሉ አህጉረ አድያም እንዘ ይሜህር ።
እያስተማረ በአውራጃው ሀገር ሁሉ ተመላለሰ ።

ዘከመ ፈነዎሙ ለሐዋርያት ይስብኩ ።

፯ ወጸውዖሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሐዋርያት ። ማቴ ፲ ፥ ፩ ። ማር ፫ ፥ ፲፬ ። ሉቃ ፱ ፥ ፩ ።

፯ አስራ ሁለቱን ሐዋርያት መረጣቸው ።
ወፈነዎሙ ፪፪ቱ ሁለት ሁለቱን ላካቸው ሐተታ አንዱ ቢደክም አንዱ ያጸናዋልና ለእመ ወድቀ ፩ዱ ያነሥኦ ካልዑ ፈትል ሥሉስ ኢይትበተክ እንኒ ዘይትራዳዕ እኁዋሁ ከመ ሀገር እንተ ባቲ ጥቅም እንዲል ። ወአብሆሙ ላዕለ አጋንንት አኩያን በከፉ አጋንንት ላይ ሥልጣን ሰጣቸው ።

፰ ወአዘዞሙ ከመ አልቦ ዘይስነቁ ለፍኖት
፰ ለመንገድም ስንቅ እንዳይዙ አዘዛቸው ።
ወኢይንሥኡ ዘእንበለ በትር ባሕቲታ ።
ከበትር ብቻ በቀር እንዳይዙ ሐተታ፡ ማቴዎስ ኢበትረ ይላል ፡ ከዚህ ማርቆስ ዘእንበለ በትር አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም አምልኮቱን እስኪያውቁ ድረስ አትያዙ ይላል አምልኮቱን ካወቁ በኋላ ግን ቢይዙም ባይዙም አይጎዳምና ዘእንበለ በትር አለ አንድም ማቴዎስ ጌጸኛውን አትያዙ ሲል ኢበትረ አለ ። ማርቆስ ተራውን ሲል ነው ። አንድም በትር ሳይቀር አትያዙ ሲል ነው ። ወኢኅብስተ ።
እንጀራ ስንኳ ።
ወኢጽፍነተ ።
ከረጢትም ። ኢወርቀ
ወኢብሩረ ።
ወርቅ ብር አትያዙ ።
ወኢጸሪቀ ውስተ ቅናቶሙ ።
በመታጠቂያቸውም ናስ ፤

፱ ዘእንበለ አሣዕን ዘውስተ እገሪሆሙ ።
ግብ ፲፪ ፡ ፰ ።

፱ በእግራቸው ካለ ጫማ በቀር ፤
ሐተታ ፡ ማቴዎስ ኢአሣዕነ ይላል ከዚህ ማርቆስ ዘእንበለ አሣዕን አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም አምልኮቱን እስኪያውቁ ድረስ አታድርጉ ይላል አምልኮቱን ካወቁ በኋላ ግን ቢያደርጉትም ባያደርጉትም አይጎዳምና ዘእንበለ አሣዕን አለ አንድም ማቴዎስ ጌጸኛውን ሲል ነው ፤ አንድም ጫማ ሳይቀር አታድርጉ ሲል ነው አግብኡ ሊተ ንዋይየ ዘእንበለ ብእሲትየ እንዲል ። ወኢይልበሱ ፪ኤ ከዳናተ ሁለት ልብስም እንዳይለብሱ ፤

፲ ወይቤሎሙ ቤተ ኀበ ቦእክሙ ሀየ ንበሩ እስከ አመ ትወጽኡ እምሀየ ።

፲ ከዚያ እስከትወጡ ድረስ በገባችሁበት ቤት ኑሩ ።

፲፩ ወብሔረ ኀበ ኢተወከፉክሙ ወኢሰምዑክሙ ወኢአክሙ እምሀየ ንግፉ ፀበለ እገሪክሙ
ማቴ ፲፡፲፬፡ ሉቃ ፱፡፭ ፡ ግብ ፲፫፡፶፩ ።

፲፩ የማይሰሟችሁና የማይቀበሏችሁ ሰዎች ካሉበት ሀገር ወጥታችሁ የግራችሁን ትቢያ አራግፉ ከመ ይኩን ስምዓ ላዕሌሆሙ ምስክር ይሆንባቸው ዘንድ ።
አማን እብለክሙ ከመ ይረክባ ሳሕተ ሰዶም ወገሞራ አመ ዕለተ ደይን እምይእቲ ሀገር ።
ከዚያች አገር ይልቅ ሰዶም ገሞራ በፍርድ ቀን ዕረፍትን እንዲያገኙ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፲፪ ወወፂኦሙ ሰበኩ ከለሄ ከመ ከሉ ይኔሥሑ
፲፪ በወጡም ጊዜ ሁሉ ንስሐ ይገቡ ዘንድ አስተማሩ ።

፲፫ ወብዙኃነ አጋንንተ ያወጽኡ ፤
፲፫ ብዙ አጋንንትም ያወጡ ነበር
ወይቀብዕዎሙ ቅብዓ ለብዙኃን ድውያን ። ያዕ ፭፡፲፬ ።
ብዙ በሽተኞችንም ዘይት ይቀቧቸው ነበር ።
ወየሐይዉ
ይድኑም ነበር ፡ ሐተታ መጽሐፈ ቀንዲል የሚባል አለ ያን በዘይት እየደገሙ ይቀቧቸው ነበርና ። አንድም ጸሎቱን ቀብዕ አለው ሌላውን የሚቀባው ሰው እጁን ሳይነካው እንዳይቀር ጸሎትም የሚጸልይ ሰው ራሱን ሳይጠቅም ሌላውን አይጠቅምምና

ዘከመ ስምዓ ኮነ ዮሐንስ መጥምቅ ።

፲፬ ወሰሚዖ ሄሮድስ ንጉሥ እስመ ከሡተ ኮነ ስሙ ወይቤ ዮሐንስ መጥምቅ ተንሥአ እምነ ምውታን ማር ፲፬፡፪ ሉቃ ፱፡፰ ።

፲፬ ሄሮድስ ንጉሥ ስሙ እንደተገለጠ ሰምቶ ዮሐንስ መጥምቅ ከሙታን ተለይቶ ተነሥቷል ። ወበእንተዝ ይትገበር ሎቱ ኃይል ስለዚህ ኃይል ይደረግለታል ይረዳዋል አለ ።

፲፭ ወቦ እለ ይቤሉ ኤልያስ ውእቱ
፲፭ ኤልያስ ነው ያሉም አሉ ። ወቦ እለ ይቤሉ ነቢይ ውእቱ ነቢይ ነው ያሉም አሉ ።
ወአመ አኮ ከመ ፩ዱ እምነቢያት ። ወይም
ከነቢያት አንዱ ነው አሉ ።

፲፮ ወሰሚዖ ሄሮድስ ይቤ ዮሐንስ ውእቱ ዘአነ መተርኩ ርእሶ ።

፲፮ ሄሮድስ ግን በሰማ ጊዜ እኔ እራሱን የቈረጥኩት ዮሐንስ ነው አለ ።
ውእቱ ተንሥአ እሙታን
እሱ ከሙታን ተነሥቷል።
፲፯ እስመ ውእቱ ሄሮድስ ፈነወ አግብርቲሁ ወአኃዞ ለዮሐንስ ወሞቅሖ ። ሉቃ ፫፡፲፱ ።
፲፯ እሱ ሄሮድስ ብላቴኖቹን ልኮ ዮሐንስንም ይዞ በግዞት አኑሮት ነበርና ።
በእንተ ሄሮድያዳ ብእሲተ ፊልጶስ እኁሁ ።
በወንድሙ በፊልጶስ ሚስት በሄሮድያዳ ምክንያት
፲፰ እስመ ኪያሃ አውሰበ እስመ ይቤሎ ዮሐንስ ኢይደልወከ ታውስብ ብእሲተ እኁከ ። ዘሌ ፲፡፰፡፲፮።
፲፰ እሷን ስላገባ ዮሐንስ የወንድምህን ሚስት ልታገባ አይገባህም ይለው ነበርና ።
፲፱ ወተቀየመቶ ሄሮድያዳ ።
፲፱ ሄሮድያዳም ቂም ይዛበት ነበርና ።
ወፈቀደት ትቅትሎ ።

ሊቃስገድሰውም ትወድ ነበር ፤
ወሰዕነት ።
አልተቻላትም ማለት ነውር አጣችበት ።

፳ እስመ ኮነ ይፈርሆ ሄሮድስ ለዮሐንስ ።
፳ ሄሮድስ ዮሐንስን ይፈራው ነበርና ።

እስመ የእምር ከመ ብእሲ ጻድቅ ወቅዱስ
ውእቱ
ደግ ሰው ቅዱስም እንደሆነ ስላወቀ ።
ወይትዓቀቦ
ይጠባበቀው ነበር
ወብዙኃ ሰምዓ በኀቤሁ
በሱ ዘንድ ብዙ ነገር ሰምቶ
ወይፈቅድ ይርአይ ተአምረ ዘይገብር
የሚያደርገውን ተአምራት ሊያይ ይወድ ነበር
ወያስተሐውዝ
[illegible] ነበር
ወይፈቅድ ይስምኦ
ሊሰማው ይወድ ነበር ።

፳፩ ወኮነት ዕለተ እመ ይገብር ሄሮድስ በዓለ
በዕለተ ተወልደ ።

፳፩ ሄሮድስ የተወለደበትን በዓል አድርጎ በነ
በረ ጊዜ
አምቢሖ መኳንንቲሁ
መኳንንቱ ቀኛዝማች ግራዝማቹ ።
ወመላእክቲሁ
አለቆቹን
ወመሳፍንቲሁ
ደጃዝማቾቹን
ወመዓብያኒሁ
ሹማምንቱን
ወአበይተ ሀገረ ገሊላ ።
የገሊላን ታላላቆችን ማለት ወይዛዝሩን ምሳ አበላ ።

፳፪ ወቦአት ወለተ ሄሮድያዳ ወዘፈነት
፳፪ ወለተ ሄሮድያዳ ገብታ ዘፈነች
ወአሥመረቶ ለሄሮድስ
ሄሮድስን ደስ አሰኘችው
ወለእለ ይረፍቁ ምስሌሁ
[illegible] ጋራ የተቀመጡትን ደስ አሰኘች ።
[illegible] ንጉሥ ለይእቲ ወለት ለአልኀ ዘትፈቅዲ
[illegible] ንጉሥም ያችን ብላቴና የምትወጅውን
[illegible] እሰጥሻለሁ አላት ።

፳፫ ወመሐለ ላቲ ከመ የሀባ ዘሰአለቶ እስከ
[illegible] ።

፳፫ [illegible] መንግሥቱ እኩሌታ ስንኳን የከመ
[illegible] ዘንድ ማለላት ።
[illegible] ።
[illegible] ወትቤላ ለእማ ምንተ እስእሎ

፳፬ ወጥታም እናቷን ምን ልለምነው አለቻት
ወትቤላ ርእሶ ለዮሐንስ መጥምቅ
የዮሐንስ መጥምቅን ራስ አለቻት ።

፳፭ ወቦአት ሶቤሃ ኀበ ንጉሥ እንዘ ትጔጒዕ
ወሰአለቶ ።

፳፭ ያን ጊዜውንም ፈጥና ወደ ንጉሡ ገብታ
ለመነችው ።
ወትቤሎ እፈቅድ ይእዜ ተሀበኒ ርእሶ ለዮሐንስ
መጥምቅ ። የዮሐንስ መጥምቅንም ራስ በገበታ
አሁን ትሰጠኝ ዘንድ እለምንሃለሁ አለችው ።

፳፮ ወተከዘ ንጉሥ በእንተ መሐላሁ
፳፮ ንጉሥ ስለ ማላው አዘነ ።
ወበእንተዝ እለ ይረፍቁ ምስሌሁ ።
ከሱ ጋራ ስለ ተቀመጡት
ወኢፈቀደ ይዕበያ
ሊነሳት ግን አልወደደም ።

፳፯ ወፈነወ ንጉሥ ሶቤሃ መስተራትእተ ሐራ
፳፯ የዚያን ጊዜም ንጉሡ ጭፍራውን የሚ
ያቅናኑትን ላከ
ወአዘዘ ያምጽኡ ርእሶ ፤
ራሱን ያመጡ ዘንድ አዘዘ ፡

፳፰ ወሖሩ ወመተሩ ርእሶ ለዮሐንስ መጥ
ምቅ በቤተ ሞቅሕ ።

፳፰ ሂደው በግዞት ቤት ራሱን ቆረጡ
ወአምጽኡ ርእሶ በፃሕል ወሀብዋ ለይእቲ ወለት
ራሱንም በገበታ አምጥተው ለዚያች ብላቴና ሰጧት
ወይእቲኒ ወለት ወሀበት ለእማ ያችም ብላቴና
ለናቷ ሰጠች ።
፳፱ ወሰሚዖሙ አርዳኢሁ ሖሩ ወነሥኡ በድኖ
ወቀበርዎ
፳፱ ደቀ መዛሙርቱ በሰሙ ጊዜ ሄደው በድ
ኑን አንስተው ቀበሩት
ዘከመ ተመይጡ ሐዋርያት ።
፴ ወተጋብኡ ሐዋርያት ኀበ እግዚእ ኢየሱስ
ወነገርዎ ኵሎ ዘገብሩ ።
፴ ሐዋርያት ወደ ጌታ ተሰብስበው ያደረጉትን
ሁሉ ነገሩት ወዘከመ መሐሩ ።
እንዳስተማሩም ነገሩት
፴፩ ወይቤሎሙ ንዑ ንሑር ገዳመ ባሕቲትነ
ወታዕርፉ ሕቀ ። ማቴ. ፲፬ ፤ ፲፫ ። ሉቃ. ፱ ፤ ፲ ።
ዮሐ. ፮ ፤ ፩ ።
፴፩ ጥቂትም ታርፉ ዘንድ ኑ ለብቻችን ወደ
ምድረ በዳ እንሂድ አላቸው ።
፴፪ እስመ ብዙኃን እለ የሐውሩ ወይገብኡ
፴፪ የሚወጡ የሚገቡ ብዙ ነበሩና
ወኢያበውሕዎሙ ይብልዑ እክለ ፡
እህል ይበሉ ዘንድ አያሰናብቷቸውም ነበርና ።

እስመ ኢያስተርክቡ
ጊዜም አላገኙምና

፴፫ ወሖሩ ሐቅለ በሐመር ባሕቲቶሙ
፴፫ ብቻቸውንም በመርከብ ወደምድረ በዳ ሄዱ ።
ወርእይዎሙ እንዘ የሐውሩ ወአእመርዎሙ ብዙኃን
ብዙ ሰዎችም ሲሄዱ አይተዋቸው ዐወቋቸው
ወሖሩ እንተ እግር ኀቤሁ እምኵሉ አኅጉር
ከየሀገሩ ወጥተው በእግር ወደሱ ሄዱ ።
ወተቃደምዎሙ ወመጽኡ ኀቤሁ ፡
ቀድመዋቸውም ወደሱ መጡ ።

ዘከመ አብዝኃ በቀዳሚ ኅምስ ኅብስተ

፴፬ ወወጺኦ እግዚእ ኢየሱስ ርእየ ብዙኃ ሰብአ ማቴ ፱ ፡ ፴፮ ፡ ፲፬ ፡ ፴ ።

፴፬ ጌታም በወጣ ጊዜ ብዙ ሰው አየ ።
ወመሐሮሙ
አስተማራቸውም
እስመ ከመ አባግዕ ዘአልቦ ኖላዊ እሙንቱ
ጠባቂ እንደሌላቸው ኢባግዕ ናቸውና
ወአኃዘ ይምሐሮሙ ብዙኃ
ብዙ ያስተምራቸው ጀመር ።

፴፭ ወእምድኅረ ብዙኅ ሰዓት መጽኡ አርዳኢሁ ወይቤልዎ ሐቅል ውእቱ ዝ ብሔር

፴፭ ከጥቂት ሰዓት በኋላም ደቀ መዛሙርቱ መጥተው ይህ ቦታ ምድረ በዳ ነው ።
ወሰዓቱኒ ወድዓ መስየ ።
ጊዜው ፈጽሞ መሽቷል ።

፴፮ ሠዓር ሰብአ ይሖሩ ውስተ አዕፃዳት ወይ ሣየጡ ሎሙ ሲሳየ ። ሉቃ ፱ ፡ ፲፪ ።

፴፮ ወደ መንደር ሄደው ምግባቸውን ይገዙ ዘንድ ሕዝቡን አሰናብታቸው አሉ ሐተታ ወምዕተ ክዊና እንደ ማቴዎስ ወእምድኅረ ብዙኅ ሰዓት እንደ ማርቆስ ወተቈልቈለ ፀሐይ እንደ ሉቃስ መገናኛ ዮሐንስ በተገናኝ ሲመሽ ማለት ነው ፍትሖሙ ማቴዎስ ሠዓር ሰብአ ማርቆስ ፈንዎሙ ሉቃስ መገ ናኛ ዮሐንስ በተገናኝ አሰናብት አሉት ።
፴፯ እስመ አልቦሙ ዘይበልዑ
፴፯ የሚበሉት የላቸውምና
ወአውሥአ ወይቤሎሙ ሀብዎሙ አንትሙ ዘይ በልዑ ።
እናንተም የሚበሉትን ስጡቸው አላቸው
ወይቤልዎ አርዳኢሁ ንሑርኑ
ወንሣየጥ በ፪፻ ዲናር ኅብስተ
በሁለት ድሪም እንጀራ እንገዛ ዘንድ እንሂድን አሉት
፴፰ ወይቤሎሙ ሑሩ ወርእዩ ሚመጠን ኃባ ውዝ ብከሙ ።

፴፰ ምን ያህል እንጀራ እንዳለ ሄዳችሁ እዩ አላቸው ።
ወርእዮሙ ይቤልዎ ኃምስ ኅብስት ወ፪ቲ ዓሣት
አይተው አምስት እንጀራ ሁለት ዓሣም አለ አሉት።

፴፱ ወአዘዞሙ ለኵሎሙ ያርፍቅዎሙ በበ ምርፋቃቲሆሙ ዲበ ሐመልማለ ሣዕር፡ዮሐ ፮፡፲ ፡

፴፱ በለመለመ ሣር ላይ በየመቀመጫቸው ሁሉንም ያስቀምጧቸው ዘንድ አዘዛቸው ።

፵ ወረፈቁ በበምርፋቃቲሆሙ
፵ ተከፍለው ተከፍለው ተቀመጡ በበ፻ት መቶ መቶው
ወበበ፶ ።
አምሳ አምሳው አንድም መቶ መቶውን ባምሳ ሰደቃ አምሳ አምሳውን በመቶ ሰደቃ ።

፵፩ ወነሥአን ለ፭ ኅብስት ወለክልኤቲ ዓሣት ወነጸረ ሰማየ ።
፵፩ አምስቱን እንጀራ ሁለቱንም ዓሣ ይዞ ወደሰማይ አየ ።
ወባረከ ። ባረከም ።
ወፈተተ ኅብስተ ወወሀቦሙ ለአርዳኢሁ ያቅርቡ ሎሙ ። ኅብስቱን ቈርሶ ያቀርቡላቸው ዘንድ ለደቀ መዛሙርቱ ሰጣቸው ።
ወከፈሎሙ ለኵሎሙ እም፪ቲ ዓሣትኒ ።
ሁለቱንም ዓሣ ለሁሉ ከፈለ
፵፪ ወበልዑ ኵሎሙ ወጸግቡ ።
፵፪ ሁሉም በልተው ጸገቡ ።
፵፫ ወአግኃሡ ዘተርፈ ፍተታተ ፲፪ መሶ መሳይምተ ።
፵፫ የተረፈውንም ቁራሽ ዐሥራ ሁለት መሶብ አነሱ ።
ወእምዓሣሁኒ ።
ዓሣውም ።
፵፬ ወአለዉ በልዕዎ ፭ ውእቱ ኅብስት ዕደው ፶፻ት
፵፬ ያን እንጀራ የበሉት ሰዎች ግን ወንዶቹ አምስት ሽህ ናቸው ።
ዘከመ ሖረ ዲበ ማይ
፵፭ ወአዝበርሙ ሶቤሃ ለአርዳኢሁ ይዕርጉ ሐመረ ወይቅድምዎ ማዕዶተ ቤተ ሳይዳ ፡
፵፭ ወደመርከብ ገብተው ወደቤተ ሳይዳ ወደ ማዶ ይቀድሙት ዘንድ በዚያን ጊዜ ደቀ መዛሙር ቱን ግድ አላቸው ።
እስከ ሶበ ይሥዕሮሙ ለሕዝብ ።
ሕዝቡን እስኪያሰናብት ድረስ ወእምድኅረ ፈነ ዎሙ ሖረ ወኃለፈ እምህየ ።
አሰናብቷቸው ከዚያ ወጣ ።
ወዓርገ ደብረ ከመ ይጸሊ ። ሊጸልይም ወደተራራ ወጣ ።

፵፯ ወመስዮ ብሔር ሀለወት ሐመር ማእከለ ባሕር ።

፵፯ በመሸም ጊዜ መርከቢቱ ከባሕር መካከል ነበረች ።
ወውእቱሰ ባሕቲቱ ሀሎ ውስተ ምድር ።
እሱ ግን ብቻውን በምድር ነበር ።

፵፰ ወርእዮሙ እንዘ የሐውሩ ወጥቀ ይትመነደቡ ።

፵፰ እጅግም እየተጨነቁ ሲሄዱ አያቸው ።
ወየሐምሞሙ ነፋስ ።
ነፋስም ያስጨንቃቸው ነበር
እስመ እምገጾሙ ውእቱ
ከወደፊታቸው ነውና ።

፵፰ ወበራብዕት ሰዓተ ሌሊት መጽአ ኀቤሆሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ የሐውር ዲበ ባሕር ማቴ ፲፬፥፳፭ ።

፵፰ ባራተኛው ሰዓተ ሌሊት ጌታ በባሕር ላይ እየሄደ መጣ ።
ወፈቀደ ይትዓደዎሙ
ሊያልፋቸውም ወደደ ፤

፵፱ ወሶበ ርእይዎ የሐውር ዲበ ባሕር መሰለሙ ምትሐት ።

፵፱ በባሕር ላይ ሲሄድ ባዩት ጊዜ ምትሐት መሰላቸው ።

፶ ወኵሎሙ ርእይዎ ወደንገፁ
፶ ሁሉም አይተው ደነገጡ
ወአውየው ።
ጮሁም ።
ወነበቦሙ ሶቤሃ ። ያን ጊዜ ተናገራቸው።
ወይቤሎሙ ተአመኑ ከመ አነ ውእቱ ።
እኔ እንደሆንኩ እመኑ አላቸው
ወኢትፍርሁ ፤
አትፍሩ ።

፶፩ ወዓርገ ኀቤሆሙ ውስተ ሐመር ።
፶፩ ወደመርከብ ወደሳቸው ወጣ ።
ወሀደገ ነፋስ
ነፋስም ጸጥ አለ
ወፈድፋደ ተደሙ ፤
ፈጽመው ተደነቁ ።
ወአንከርዎ
አደነቁት ፤

፶፪ ወአመሂ ኅብስት ኢለበዉዎ
፶፪ በእንጀራው ጊዜ አላስተዋሉም ነበር
እስመ ጽኑዕ ልቦሙ
ልቡናቸው ተሸፍኖዋልና ።

ዘከመ ገብረ መንክራተ በጌንሴሬጥ በገሚሠ ጽንፈ ልብሱ ።

፶፫ ወሶበ አደዉ ወበጽሑ ምድረ ጌንሴሬጥ ማቴ ፴፬፥፴፬ ።

፶፫ ተሻግረውም ከጌንሴሬጥ ምድር በደረሱ ጊዜ አርሰዩ ሆየ ፤
ከዚያ መርከባቸውን አስጠጉ ።

፶፬ ወወፂኦሙ እምሐመር አእመርዎ ሶቤሃ ሰብአ ይእቲ ሀገር

፶፬ ከመርከቡም በወጡ ጊዜ ያን ጊዜ የዚያ አገር ሰዎች አወቁት ።
፶፭ ወሮጹ ውስተ ኵሉ በሐውርት ወአምጽኡ ድውያነ በአራታት
፶፭ ወደየሀገሩ ሮጡ ድውያንንም ባልጋ አመጡ
ወይወስዱ ኀበ ሰምዑ ከመ ሀሎ ውእቱ ሀየ
እሱ ያለበትን ወደሰሙበት ይወስዱቸዋል ።
፶፮ ወውስተ አንጕር ወአዕፃዳት ኀበ ቦአ ውስተ ምሥያጣት ያነብርዎሙ ለድውያን ።
፶፮ ከገባበት ቦታና አገር ድውያንን ካደባባዩ ያኖሯቸው ነበር ወአስተብቍዕዎ ከመ ይግሥሡ ጽንፈ ልብሱ ።
የልብሱንም ጫፍ ይይዙ ዘንድ ማለዱት ፤
ወኵሎሙ እለ ገሠሥዎ የሐይዉ ።
የያዙትም ሁሉ ይድኑ ነበር ።

በእንተ ፈሪሳውያን ወሥርዓቶሙ

## ምዕራፍ ፯ ።

፩ ወተጋብኡ ኀቤሁ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መጺኦሙ እምኢየሩሳሌም ።

፩ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ከኢየሩሳሌም መጥተው ወደሱ ተሰበሰቡ ።

፪ ወርእይዎሙ ለአርዳኢሁ እንዘ ይበልዑ እክለ ዘእንበለ ይትሐፀቡ እደዊሆሙ ። ማቴ ፲፭፥፪ ።

፪ ደቀ መዛሙርቱን እጃቸውን ሳይታጠቡ ሲበሉ አዩዋቸው ።

፫ እስመ ፈሪሳውያንሰ ወኵሎሙ አይሁድ ለእመ በሕቁ ኢተሐፅቡ እደዊሆሙ ኢይበልዑ እክለ
፫ ፈሪሳውያን ግን አይሁድ ሁሉ እጃቸውን በጅጉ ሳይታጠቡ አይበሉም ነበርና ። መላልሰውደም እስኪሰርበው እስኪመለጥ ድረስ ካልታጠቡ አይበሉም እስመ የዓቅቡ ሥርዓቶሙ ለረበናት ።
የረበናትን ሥርዓት ይጠብቁ ነበርና ።
፬ ወዘሂ ተሣየጡ እምሥያጥ ኢይበልዑ ለእመ ኢያጥመቅዎ ።

፬ ከገበያም የተገዛውንም በውኃ ካላጠቡ አይ በሉ ይነበር ።
ወባዕደኒ ብዙኀ ኅርመተ ዘይትዓቀቡ ።
ሌላም የሚጠብቁት ብዙ ሥርዓት አለ ።
ወያጠምቁ ጽዋዓተኒ
ጽዋውንም ያጥቡት ነበር ።
ወቈሳቍሳተ ።
ብርቱን ድስቱን ።
ወጽሕርታተ ፤
ማድጋውን ፤
ወአራታተ ፤ አልጋውን ።

፭ ወይቤልዎ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ለምንት ኢየሐውሩ አርዳኢክ በክመ ሰርዐ ረበናት ።

፭ ጸሐፍት ፈሪሳውያንም ደቀ መዛሙርትህ እንደሽማግሎች ሥርዓት ለምን አይሄዱ አሉት ወዘእ ንበለ ይትሐፀቡ እደዊሆሙ ይበልዑ እከለ ። እጃቸውንስ ሳይታጠቡ ለምን እህል ይበላሉ ።

፮ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ አመደልዎን ሠናየ ተነበየ ኢሳይያስ ላዕሌክሙ እንዘ ይብል ዝ ሕዝብ በከናፍሪሆሙ ያከብሩኒ ወበልቦሙሰ ነዋኀ ይርኁቁ እምኔየ ። ኢሳ ፳፱ ፥ ፲፫ ።

፮ እናንት ግብዞች ኢሳይያስ ፡ እኒህ ሕዝብ በከንፈራቸው ያከብሩኛል በልባቸው ግን ፈጽመው ከኔ ይርቃሉ ብሎ ኢሳይያስ እውነት ተናገሮባችኋል ።
ወከንቶ ያመልኩኒ ።
በከንቱ ያመልኩኛል ።

፯ እንዘ ይሜህሩ ሥርዓታተ ትእዛዛተ ሰብእ ።
፯ በሰዎች ሥርዓት ትምህርት እያስተማሩ ።
፰ ወየኃድጉ ትእዛዛተ እግዚአብሔር ወየዓቅቡ ትእዛዘ እጓለ እመሕያው ።

፰ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ትተው የሰውን ሥርዓት ይጠብቁ ነበረና ። ጥምቀታተ ጽዋዓት ወቍሳቍሳተ
ጽዋውን ብርቱን ድስቱንም ማጠብ ።
ወጽርሐታተ ።
ማድጋውን ወባዕደኒ ብዙኀ ዘይመስሎ ለዝንቱ ።
ሌላውንም ይህን የመሰለውን ሁሉ ።
፱ ወይቤሎሙ ርቱዕኑ ትዕልው ትእዛዘ እግዚአብሔር ከመ ትዕቀቡ ትእዛዘ ርእስክሙ ፥
፱ የራሳችሁን ትእዛዝ ትጠብቁ ዘንድ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ልታፈርሱ ይገባልን አላቸው ።
፲ ወሙሴ ይቤለክሙ አክብር አባከ ወእመከ ዘፀ ፳ ፥ ፲፬ ። ዘዳ ፭ ፥ ፲፮ ። ኤፌ ፮ ፥ ፪ ። ዘፀ ፳፩ ፥ ፲፯ ። ዘሌ ፳ ፥ ፱ ። ምሳ ፳ ፥ ፳ ።
፲ ሙሴ እናትና አባትክን አክብር ብሏችኋል ወዘአኅሰመ ቃለ ላዕለ አቡሁ ወእሙ ሞተ ለይሙት አባትና እናቱንም የሰደበ ፈጽሞ ይሙት ።

፲፩ ወአንትሙሰ ትብልዎ ዘይቤሎ ለአቡሁ
፲፩ እናንተ ግን ላባቱ የሚመልሰውን ትሩፋ ታላችሁ ፤
አው ለእሙ ፤
ወይም ለናቱ የሚመልሰውን ቍርባን ዘረባሀከ እም ኔየ ብሂል ከኔ ያገኘሽውን ቍርባን ነው ማለት ነው ፤

፲፪ ኢታበውህዎ ይግበር ምንተኒ ለአቡሁ ወለ እሙ ።

፲፪ ላባትና ለናቱ ምን ምን ያደርግ ዘንድ አታ ሰናብቱትም ፤

፲፫ ወትሥዕሩ ቃለ እግዚአብሔር በእንተ ትእ ዛዝ ዘሠራዕክሙ ።

፲፫ ለሠራችሁት ሥራት የእግዚአብሔርን ትእ ዛዝ ታፈርሳላችሁ ።
ወዓዲ ብዙኀ በአምሳለ ዝንቱ ዘትገብሩ ።
ዳግመኛም ሌላም የምትሠሩት ይህን የመሠለ ብዙ አለ
፲፬ ወጸውዖሙ ካዕበ ለሕዝብ ወይቤሎሙ ስምዑ ኵልክሙ ወለብው ። ማቴ ፲፭ ፥ ፲ ።
፲፬ ሁለተኛ ሕዝቡን ጠርቶ ስሙ እወቁ አላቸው
፲፭ አልቦ ዘይበውእ እምአፍአ ውስተ አፉሁ ለሰብእ ዘይክል አርኵሶቶ ።
፲፭ ከውጭ ወደ ሰው አፍ የሚገባው ሊያ ረክሰው አይችልም ዘእንበለ ዳዕሙ ዘይወፅእ እም ልቡ ለሰብእ ውእቱ ያረኵሶ ለሰብእ ።
ከሰው ልብ የሚወጣ እሱ ያረክሰዋል እንጂ ፤
፲፮ ዘቦ እዝነ ሰሚዕ ለይስማዕ ፤
፲፮ ጆሮ ያለው ይስማ ።
ወበዊአ ቤተ እምኅበ ሕዝብ ተስእልዎ አርዳ ኢሁ ዘንተ አምሳለ ።
ከሕዝቡም ዘንድ ወደ ቤት በገባ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ይህን ምሳሌ ጠየቁት ፤
፲፯ ወይቤሎሙ እንትሙኒ ከመዝኑ ኢትሌብዉ
፲፯ እናንተም እንዲህ ገና አታውቁምን
፲፰ ኢተአምሩኑ ከመ ኵሉ ዘእምአፍአ ይበ ውእ ውስተ ሰብእ ኢይክል አርኵሶቶ ።
፲፰ ከውጭ ወደ ሰው የሚገባው ሁሉ ሰውን እንዳይጐዳው አታውቁምን ።
፲፱ እስመ ኢይበውእ ውስተ ልቡ ዘእንበለ ውስተ ከርሡ ከመ ።
፲፱ ወደ ሆዱ ብቻ ነው እንጂ ወደ ልቡ አይ ገባምና ።
ወጽመ ይትከዓው እንዘ ያነጽሕ ኵሎ መባልዕተ መብሉን ሁሉ ሲያጠራ ቆይቶም ይወጣል ።
፳ ወይቤሎሙ ዘይወጽእ እምአፉሁ ለሰብእ ውእቱ ያረኵሶ ለሰብእ ።
፳ ከሰው የሚወጣው እሱም ሰውን ይጐዳዋል ዘፍ ፮ ፥ ፭ ።

፳፩ እስመ እምውሥጠ ልበ ለሰብእ ይወፅእ ኵሉ ሕሊና እኩይ

፳፩ ከሰው ከልቡ ውሥጥ ክፉ አሳብ ሁሉ ይወጣልና ።
ዘውእቱ ዝሙት ፤
ይህም ዝሙት ነው
ወቀቲል መግደል ።
ወሰርቅ
መስረቅ

፳፪ ወሐዊረ ብእሲተ ብእሲ
፳፪ ወደ ጐልማሳ ሚስት መሄድ
ወትዕግልት ቅሚያ
ወእከይ ክፋት ።
ወጕሕሉት ክዳት
ወጽልሑት ሽንገላ ።
ወምርዓት ድርዓት
ወጽርፈት ስድብ ።
ወትዕቢት ትዕቢት
ወሕመሚ ዓይን ምቀኝነት
ወዕበድ ስንፍና ።

፳፫ ዝንቱ ኵሉ እኩይ ይወፅእ
፳፫ እምውሥጥ ይህ ሁሉ ክፉ
ነገር ከውስጥ ይወጣል
ወያረኵሶ ለሰብእ ።
ሰውን ይጐዳዋል ፤

በእንተ ከነናዊት ።

፳፬ ወተንሢአ እግዚእ ኢየሱስ እምህየ ሖረ ብሔረ ጢሮስ ወሲዶና ፤ ማቴ ፲፭ ፡ ፳፩ ።

፳፬ ጌታም ከዚያ ተነሥቶ ወደጢሮስና ወደ ሲዶና ሄደ ።
ወቦአ ቤተ ወኢፈቀደ ያእምሮ መኑሂ ።
ከቤትም ገባ ማንም ማን ሲያውቀው አልወደደም።
ወስእነ ተከብቶ ።
መሠወርም አልተቻለውም
፳፭ ወእምዝ ሰምዓት በእንቲአሁ አሐቲ ብእሲት እንተ ጋኔን እኩይ አኀዛ ለወለታ ፤
፳፭ ከዚህም በኋላ ልጅዋን ርኩስ ጋኔን የያዘባት አንዲት ሴት የሱን ነገር ሰማች ።
መቦአት ወሰገደት ሎቱ ታሕተ እገሪሁ ።
ገብታም ከእግሩ በታች ሰገደችለት ።
፳፮ ወአረማዊት ይእቲ ብእሲት ፤
፳፮ ያችም ሴት አረማዊት ናት ።
ወሲሮፊኒቂሳዊት ።
ሲሮፊኒቂሳዊትም ናት ሐተታ አረማዊት ከነናዊት ከንዓናዊት ጽርአዊት ሶርያዊት ሲሮፊንቂሳዊት ይላታል ስምንት ጋዋ ያላት ናት የሰውትውልድ ከብዙ ወገን ነውና ።

ወሰአለቶ ያውፅእ ጋኔነ እምወለታ ።
ከልጅዋ ጋኔን ያወጣላት ዘንድ ለመናችው

፳፯ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ኅድጊ ቅድመ ምዕረ ይጽገቡ ውሉድ ፤

፳፯ ጌታም ቀድሞ ልጆች ይጽገቡ አላት ።
እስመ አኮ ሠናይ ነሢአ ኅብስተ ውሉድ ወወሪብ ለከለባት ።
የልጆችን እንጀራ ነሥቶ ለውሾች መስጠት አይገባምና ፤

፳፰ ወተሰጥወቶ ።
መለሰችለት ።
ወትቤሎ እወ እግዚኦ ከለባትኒ ይበልዑ በታሕተ ማዕድ ፍርፋሬተ ዘያወድቁ ደቂቅ ።

፳፰ እምነ ነው ውሾም ልጆች ከማዕድ የጣሉትን ፍርፋሪ ይበላሉ አለችው ።

፳፱ ወይቤላ በዝንቱ ቃልኪ ሑሪ ወጽአ ውእቱ ጋኔን እምወለትኪ

፳፱ ስለዚህም ነገርሽ ሂጂ ጋኔኑም ከልጅሽ ወጥቷል አላት ።
፴ ወሖረት ወአተወት ቤታ
፴ ወደቤቷም ተመለሰች ።
ወረከበታ ለወለታ ልብስታ ወትነብር ዲበ ዓራታ
ልጅዋን ልብሷንም ለብሳ ባልጋውም ተቀምጣ አገኘቻት ወኃደጋ ጋኔና ።
ጋኔኑዋም ተዋት ።

ዘከመ ፈወሶ ለፅሙም ወጽሙም ።

፴፩ ወኃሊፎ ካዕበ እምጢሮስ ወሖረ እንተ ሲዶና ወባሕረ ገሊላ እንተ ፲ቱ አኅጉር ።

፴፩ ዳግመኛ ከጢሮስ አልፎ ባሥሩ ሀገር መካከል ወደ ገሊላ ባሕርና ወደ ሲዶና ሄደ ።

፴፪ ወአምጽኡ ኀቤሁ በሐመ ወጽሙመ ።
ማቴ ፱ ፡ ፴፪ ሉቃ ፲ ፡ ፲፬ ።

፴፪ ደንቆሮም ድዳም ይዘው ወደሱ መጡ ።
ወአስተበቍዕዎ ከመ ይደይ እዴሁ ላዕሌሁ ።
እጁንም ይጭንበት ዘንድ ማለዱት ።

፴፫ ወአግኅዎ እምሰብእ ባሕቲቱ
፴፫ ብቻውንም ከሰው ለየው
ወወደየ አፃብዒሁ ውስተ እዘኒሁ
ጣቱንም ከጆሮው ጨመረች
ወተፍአ ፤
ምራቁንም ተፋበት ፤
ወገሠሠ ልሳኖ ፤
ምላሱንም ዳሰሰው ።
፴፬ ወነጸረ ሰማየ ፤
፴፬ ወደሰማይ አየ ፤
ወአስተምሐረ ።
አዘነም ፤

ወይቤ ኤፍታሕ ኤፍታሕ
ኤፍታሕ ኤፍታሕ አለ
ተረጓሙ ብሂል
ተከፈት ማለት ነው ።
፴፭ ወሶቤሃ ተከሥተ ዕዘኒሁ ።
፴፭ ያንጊዜም ጆሮው ተከፈተ ።
ወተፈትሐ ማዕሠረ ልሳኑ
የምላሱም ዕሥራት ተፈታ
ወተናገረ ርቱዓ
አቃንቶም ተናገረ
፴፮ ወገሠፆሙ ኢይንግሩ ወኢለ
፴፮ መኑሂ ለማንም
ለማን እንዳይናገሩ ገሠፃቸው ።
ወእምጣነ ይከልዖሙ ውእቱ ፈድፋደ ይነግሩ ሎቱ
እሳቸው ግን በከለከላቸው መጠን ይናገሩ ነበር ።
፴፯ ወፈድፋደ ያነክርዎ ወእንዘ ይብሉ ሠናይ ኵሉ ዘገብረ ዝንቱ ብእሲ ።

፴፯ ይህ ሰው የሠራው ምን ያምር እያሉ ፈጽመው ያደንቃሉ ለጽሙማን ያሰምዖሙ
ደንቆሮዎችን ያሰማቸዋል
ወለበሐማን ያነብቦሙ
ዲዳዎችን ያናግራቸዋል ።

በከመ አብዝኀ ኅብስተ ዳግመ ።

ምዕራፍ ፰ ።

፩ ወይእቲ አሚረ ካዕበ ብዙኀ ሰብእ እንዘ ሀሎ አልቦሙ ዘይበልዑ ማቴ ፲፭፡ ፴፪ ።

፩ በዚያም ወራት ብዙ ሰው ሳለ የሚበሉት አልነበራቸውም ።

፪ ወጸውዖሙ ለአርዳኢሁ ወይቤሎሙ ያምሕሩኒ እሉ ሰብእ
፪ ደቀ መዛሙርቱን ጠርቶ እኒህ ሰዎች ያሳዝኑኛል ለኔ ከእኔ ጋራ ናሁ ሠልሰ ዕለት እንዘ ይጸንሑኒ ።
፫ ሲጠብቁኝ ሦስተኛ ቀናቸው ነውና ።
ወአልቦሙ ዘይበልዑ
የሚበሉትም የላቸውም
፫ ወእመኒ ሠዓርክዎሙ ርኁባኒሆሙ ይእቲው አብያቲሆሙ ይደክሙ በፍኖት ።

፫ ወደ ቤታቸውም ይገቡ ዘንድ ተርበውም ባሰናበታቸው በመንገድ ይደክማሉ ።
ወእለሂ መጽኡ እምርኁቅ
ከሩቅም የመጡ አሉ ።
፬ ወይቤልዎ አርዳኢሁ መኑ ዘይከል በዝየ በገዳም አጽግቦቶሙ ኅብስተ ለዝንቱ ኵሉ ሕዝብ
፬ ደቀ መዛሙርቱ በዚህ በገዳም ይህን ሁሉ ሕዝብ ማጽገብ የሚቻለው ማነው አሉ ፤

፭ ወይቤሎሙ ሚመጠን ኅብስትክሙ ።
፭ ምን ያህል እንጀራ አላችሁ አላቸው
ወይቤልዎ ሰብዐ
ሰባት ነው አሉት ።

፮ ወአዘዞሙ ለሰብእ ይርፍቁ ዲበ ምድር
፮ ሰዎቹን ከምድር ይቀመጡ ዘንድ አዘዛቸው
ወነሥአ ለሰብዑ ኅብስት
ሰባቱንም እንጀራ ያዘ ።
ወአእኰተ አመሰገነ
ወፈተተ። ቈረሰ
ወወሀቦሙ ለአርዳኢሁ ያቅርቡ ሎሙ ለሕዝብ
ያቀርቡላቸው ዘንድ ለደቀ መዛሙርቱ ሰጣቸው ።
ወአቅረቡ ለሰብእ
ለሰዎችም አቀረቡ

፯ ወቦሙ ዓሣ ኅዳጥ
፯ ጥቂት ዓሣም ነበራቸው ።
ወባረከ ኪያሁኒ
ያንም ባረከው ።
ወይቤሎሙ አቅርቡ ሎሙ ዘኒ
ይህን አቅርቡላቸው አላቸው ።

፰ ወበልዑ ወጸግቡ ።
፰ በልተውም ጸገቡ
ወዘአግኃሡ ዘተርፈ ፍተታተ መልዓ ፯ተ አስፈ ፈዳተ ።
ያነሡት የቍራሽ ትራፊ ሰባት እንቅብ መላ ።

፱ ወእለሰ በልዑ የአክሉ ፬፻ ።
፱ የበሉትም አራት ሺህ ያህላሉ ወእምዝ ፈነ ዎሙ ሶቤሃ ይሑሩ ።
ከዚህም በኋላ ይሄዱ ዘንድ አሰናበታቸው ።

፲ ወእምዝ ዓርገ ሐመረ ምስለ አርዳኢሁ ወበጽሐ ውስተ ደወለ ድልማኑታ ።

፲ ከዚህም በኋላ ከመርከብ ገብቶ ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ወደ ድልማኑታ ሄደ ።
ዘከመ ኀሠሡ ትእምርተ እምሰማይ ።
፲፩ ወወጽኡ ፈሪሳውያን ። ማቴ ፲፡ ፮፡ ፩ ሉቃ ፲፩፡ ፲፮ ።
፲፩ ፈሪሳውያንም ወጡ ።
አኀዙ ይትኃሠሥዎ
ይከራከሩትም ጀመር
ወሰአልዎ ትእምርተ እምሰማይ እንዘ ያሜክርዎ
ሲፈትኑት ከሰማይ ምልክት ለመኑት ።
፲፪ ወተከዘ በመንፈሱ
፲፪ በልቡም ተቈረቈረ
ወይቤ ምንትኑ ተኃሥሥ ትእምርተ ዛቲ ትውልድ
ይች ትውልድ ለምን ምልክት ትሻለች ።
፲፫ እግን እብለክሙ ከመ ኢይትወሀባ ለዛቲ ትውልድ ትእምርት ።

፲፪ ለዚህች ትውልድ ምልክት አይሰጣትም
ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።
ወኃደጎሙ ወዓርገ ካዕበ ሐመረ ወሖረ ማዕዶተ።
ትቷቸው ሁለተኛ በመርከብ ተጭኖ ወደ ማዶ ሄደ።

፲፬ ወረስዑ ነሢአ ኅብስት ማቴ ፲፮ ፡ ፭ ፡
፲፬ እንጀራ መውሰድን ረሱ
ወአልቦሙ ዘእንበለ አሐቲ ኅብስት ምስሌሆሙ
ውስተ ሐመር
እርሳቸውም ካንዲት እንጀራ በቀር በመርከብ አል
ነበራቸውም ሐተታ ማቴዎስ ዘእንበለ አሐቲ አሳ
ለም ማርቆስ ዘእንበለ አሐቲ አለ እንደምን ነው
አይጣላም ቢሉ አይጣላም ካነስ ዘንድ የለም ማለት
ልማድ ነውና ማቴዎስ ዘእንበለ አሐቲ አላለም
ወበውስተ ውሁድኒ ንብል አልቦ አንዲል አንድም
ማርቆስ አንዲት ሳትቀር ሲል ነው ። አግብኡ ሊተ
ንዋይየ ዘእንበለ ብእሲትየ እንዲል ።

፲፭ አዘዞሙ ወይቤሎሙ ዑቁ ወተዓቀቡ እምነ
ብሑዓ ፈሪሳውያን ወእምነ ብሑእሙ ለሄሮድሳ
ውያን ።

፲፭ ከሄሮድሳውያንና ከፈሪሳውያን እርሾ እስ
ተውላችሁ ተጠበቁ ብሎ አዘዛቸው ።

፲፮ ወሐለዩ በበይናቲሆሙ
፲፮ እስበሳቸው እስዑ ወይቤሉ
እስመሁ ኅብስተ ኢነሣእነ ።
እንጀራ ስለአልያዝን ነውን አሉ

፲፯ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ
ምንተ ትሔልዩ በልብክሙ ።

፲፯ ጌታም አውቆባቸው በልባችሁ ምን ታስ
ባላችሁ አላቸው ።
እስመሁ ኅብስት አልብክሙ
እንጀራ የላችሁምና ነው ።
ዓዲኑ ተአምሩ ወኢትሌብዉ ገና አላወቃችሁም
ልብ አላረጋችሁም ።
ልብክሙኑ ጽሉል
ልባችሁ ደንቆሮ ነውን
፲፰ ወአዕይንት ብክሙ ወኢትሬእዩ ማር ፯
፴፭ ዮሐ ፱፤ ፲፩
፲፰ ዓይን አላችሁ አታዩም
ወዕዘነ ብክሙ ወኢትሰምዑ ጆሮም አላችሁ አት
ሰሙም ወኢትዜከሩኑ ።
አታስቡምን
፲፱ ዘአመ ኃምሱ ኅብስት ፈተትኩ ለ፶፻ ብእሲ
፲፱ ላምስት ሺህ ሰው አምስት እንጀራ
በቈረስኩ ጊዜ ።
ሚመጠነ አግኃሥክሙ አክፋረ ዘመልዓ ፍተታተ
የቆረሰ የተረፈውን ቁራሽ ምን ያህል ቅርጫት የመላ
አነሳችሁ አላቸው ።

ወይቤልዎ ፲ተ ወ፪ተ
አሥራ ሁለት ነው አሉት

፳ ወይቤሎሙ አመኒ ሰብዐ ኅብስተ ለ፬፻
ብእሲ ሚመጠነ አግኃሥክሙ አስፈሬዳተ ዘመልዓ
ፍተታተ ዘተርፈ ።

፳ ላራት ሺህ ሰው ሰባት እንጀራ በቈረስኩ
ጊዜ የተረፈውን ቁራሽ ስንት እንቅብ የመላ አነሳችሁ
ወይቤልዎ ሰብዐ
ሰባት ነው አሉት ።

፳፩ ወይቤሎሙ እፎ እንከ ዘኢትሌብዉ
፳፩ እንኪያ አለማስተዋላችሁ እንደምን ነው
አላቸው ።

በእንተ ዕውር ዘቤተ ሳይዳ ።

፳፪ ወበጺሖሙ ቤተ ሳይዳ አምጽኡ ኅቤሁ
ዕውረ ።

፳፪ ወደ ቤተ ሳይዳም በደረሱ ጊዜ ዕውርን
ወደሱ አመጡ
ወአስተብቍዕዎ ይግሥሦ
ይዳስሰው ዘንድ ማለዱት
፳፫ ወአኀዞ በእዴሁ ለውእቱ ዕውር ወአው
ጽኦ አፍአ እምሀገር
፳፫ ያን ዕውር በጁ ይዞ ከሀገርም አፍአ
አወጣው ።
ወተፍዓ ውስተ አዕይንቲሁ
ባይኑም ተፋበት
ወገሠሦ ዳሰሰውም
ወይቤሎ ምንተ ትሬኢ
ምን ታያለህ አለው
፳፬ ወነጸረ ወይቤ እሬኢ ሰብአ ከመ ዕፀው
ያንሶስዉ
፳፬ አይቶ ሰዎች እንደዛፍ ሲመላለሱ አያለሁ
አለ ። ሐተታ ዕውር ሆኖ ተወልዷል ያለ እንደሆነ
በምን ዐውቆ ቢሉ ፀበትሩ ከተወለደ በኋላ ታውሯል
ያሉ እንደሆነ የተመቸ ።
፳፭ ወገሠሦ አዕይንቲሁ ካዕበ
፳፭ ሁለተኛ አይኑን ዳሰሰው
ወርእየ ጥዑነ
ፍጹም ብርሃን አየ
ወነጸረ ኵሎ ብሩሃ
ሁሉን ገልጦ አየ ።
፳፮ ወፈነዎ ቤቶ
፳፮ ወደ ቤቱም ሰደደው
ወይቤሎ ኢትባእ ውስተ አዕፃዳት
ወደ መንደርም አትግባ ።
ወአልቦ ዘትነግር በውስተ ሀገርኪ
በመንደርም ለማንም አትናገር አለው።ሐተታ ዕውር
የባሕታውያን ምሳሌ ጥቂት ጊዜ የተሰጣቸው እንደ

ሆነ ሰውን ሁሉ በግዕዝ እንስሳ ያዩታል ሁሌተኛ ቢዳስሰው ፈጽሞ እንዳየ ፍጹም ጸጋ የተሰጣቸው እንደሆነ ኃጥእ ጻድቅ አግኚ መናፍቅ ሳይለዩ ሁሉን ይወዳሉና ።

በእንተ ተእምኖተ ጴጥሮስ ።

፳፯ ወሖረ እግዚእ ኢየሱስ ወአርዳኢሁ፡ውስተ አኅጉረ ቂሣርያ ዘፊልጶስ ማቴ ፲፮፥፲፫ ሉቃ ፱፥፲፰

፳፯ ጌታ ወደ ፊልጶስ አገር ወደ ቂሣርያ መንደሮች ሄደ ።
ወተስእሎሙ ለአርዳኢሁ በፍኖት መኑ ይብለኒ ሰብእ ከመ አነ ውእቱ ።
እኔ እንደሆንኩ ሰው ማን ይለኛል ብሎ ደቀ መዛሙርቱን በመንገድ ጠየቃቸው ።
፳፰ ወይቤልዎ ዮሐንስሃ መጥምቀ ፤
፳፰ ዮሐንስ መጥምቅን ይሉሃል ።
አው ኤልያስሃ ።
ወይም ኤልያስን
አው ፩ዱ እምነቢያት
ወይም ከነቢያት አንዱን ይሉሃል አሉት ፤
፳፱ ወይቤሎሙ አንትሙኬ መኑ ትብሉኒ
፳፱ እናንተስ ማነው ትሉኛላችሁ አላቸው
ወተሠጥዎ ጴጥሮስ ወይቤሎ አንተ ውእቱ ክርስቶስ
ጴጥሮስም አንተ ክርስቶስ ነህ ብሎ መለሰ ።
፴ ወገሠጾሙ ከመ ኢይንግሩ ወኢለመኑሂ በእንቲአሁ ።

፴ ለማንም ለማን እንዳይናገሩ ገሠጻቸው ።

በእንተ ትንቢት ዘሕማማት

፴፩ ወአኀዘ ይምሐሮሙ ከመ ሐለዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው ብዙኃ ያሕምምዎ ወያመክርዎ ረበናት ወሊቃነ ካህናት ።
፴፩ ጌታም ሽማግሎች የካህናት አለቆች ይፈትኑት ዘንድና ብዙ መከራ ያመጡትበት ዘንድ እንዳለው ያስተምራቸው ጀመር ፤
ወይቀትልዎ ።
እንዲገድሉት ።
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛውም ቀን እንዲነሳ ፤
፴፪ ወገሃደ ነገሮሙ ዘንተ ነገረ ።
፴፪ ይህንም ነገር ገልጦ ነገራቸው ።
ወአኀዘ ይገሥፆ ።
ይቆጣውም ጀመር ።
፴፫ ወተመይጠ ወነጸረ ኀበ አርዳኢሁ ።
፴፫ ተመልሶም ወደ ደቀ መዛሙርቱ አየ ።
ወገሠፆ ለጴጥሮስ ።
ጴጥሮስንም ተቆጣው ።
ወይቤሎ ሑር እምድኅሬየ ሰይጣን ።
አንተ ሰይጣን ከኋላዬም ሂድ አለው ።
እስመ ኢትሄሊ ዘእግዚአብሔር ዘእንበለ ዘእጓለ እመሕያው ።
የሰውን እንጂ የእግዚአብሔርን አታስብምና ።

በእንተ ኀዲገ ርእስ ዘክርስቲያን ።

፴፬ ወጸውዖሙ ለሕዝብ ምስለ አርዳኢሁ ።
ማቴ ፲ ፥ ፴፰ ፤ ፲፮ ፥ ፳፬ ሉቃ ፱ ፥ ፳፫ ፤ ፲፬ ፥ ፳፯
፴፬ ሕዝቡን ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ጠራቸው ።
ወይቤሎሙ ዘይፈቅድ ይጸመደኒ ይጽልዕ ለነፍሱ ወያጥብዕ ወይንሣእ መስቀሎ ሞቶ ወይትልወኒ ።
ሊያገለግለኝም የሚወድ ጨክኖ የሞትን መስቀል ተሸክሞ ይከተለኝ አላቸው ።
፴፭ ዘይፈቅድ ያድኅና ለነፍሱ ለይግድፋ ሉቃ ፲፯ ፥ ፴፫ ዮሐ ፲፪ ፥ ፳፭ ።
፴፭ ነፍሱን ሊያድናት የወደደ ይጣላት ።
ወዘገደፋ ለነፍሱ በእንቲአየ ወበእንተ ወንጌል ይረክባ ስለኔ ስለ ወንጌልም ነፍሱን የጣለ ያገኛታል ማለት ያድናታል ።
፴፮ ወምንት ይበቍዖ ለሰብእ ለእመ ኮሎ ዓለመ ረብሐ ወነፍሶ ኃጕለ ።
፴፮ ነፍሱን ካጣ ዓለሙን ሁሉ ቢያተርፍ ለሰው ምን ይረባዋል ።
፴፯ ወምንት እምወሀበ ሰብእ ቤዛሃ ለነፍሱ ።
፴፯ ወይስ ለነፍሱ ቤዛ ሰው ምን በሰጠ ።
፴፰ ወዘኒ ኃፈረኒ ወኃፈረ ቃልየ በዛቲ ትውልድ ዘማ ወኃጥእት ። ማቴ ፲ ፥ ፴፫ ። ሉቃ ፱ ፥ ፳፮ ፥ ፲፪ ፥ ፱ ።
፴፰ ዘማ ኃጢአተኛም በምትሆን በዚህች ትውልድ ያፈረኝን በነገሬም ያፈረውን ፤
ወልደ እጓለ እመሕያውኒ የኃፍሮ አመ ይመጽእ ።
በስብሐተ አቡሁ ምስለ መላእክቲሁ ቅዱሳን ወልደ እጓለ እመሕያው ክርስቶስም ባባቱ ምስጋና ከቅዱሳን መላእክት ጋራ በመጣ ጊዜ ያፍረዋል ።

ምዕራፍ ፱ ።

፩ ወይቤሎሙ ሀለው እምእለ ይቀውሙ ዝየ እለ ኢይጥዕምዎ ለሞት እስከ ይሬእይዋ ለመንግሥተ እግዚአብሔር እንዘ ትመጽእ በኃይል ማቴ ፲፯ ፥ ፳፰ ። ሉቃ ፱ ፥ ፳፯ ።

፩ የእግዚአብሔር መንግሥት በኃይል መጥታ እስኪያዩዋት ድረስ ከዚህ ቁመው ካሉት ሞትን የማይቀምሷት አሉ ብዬ እነግራችኋለሁ ።

ዘከመ ተወለጠ ራዕዩ በደብረ ታቦር ።

፪ ወእም ሰዱስ ዕለት ነሥኦሙ ኢየሱስ ለጴጥሮስ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ ።

፪ ኢየሱስ በስድስተኛው ቀን ጴጥሮስን ያዕቆብንና ዮሐንስንም ወሰዳቸው ።

ወዓሪጎሙ ደብረ ነዋኀ በባሕቲቶሙ ።
ለብቻቸውም ወደ ረጅም ተራራ አወጣቸው ።
ወተወለጠ ራእዩ በቅድሜሆሙ ።
መልኩም በፊታቸው ተለወጠ ።

፫ ወአልባሲሁኒ በረቀ ወፃዕደወ ጥቀ ።
፫ ልብሱ አበራ እጅግም ነጭ ሆነ ።
ወኢይክል መሐፒል ከማሁ አፃዕድዎቶ በዲበ ምድር
በምድር ላይ ሸማ አጣቢ እንደሱ ነጭ ማድረግ የማ
ይቻለው አንድም መሐፒል ሳሙና ነው ።

፬ ወአስተርአይዎሙ ሙሴ ወኤልያስ እንዘ
ይትናገሩ ምስለ እግዚእ ኢየሱስ ።

፬ ኤልያስና ሙሴ ከጌታ ጋራ ሲነጋገሩ ታዩ
ዋቸው ።

፭ ወአውሥአ ጴጥሮስ ።
፭ ጴጥሮስ መለስ ።
ወይቤሎ ለእግዚእ ኢየሱስ ረቢ ይኄይሰነ ንንበር ዝየ
መምህር ከዚህ ብንቀመጥ ለኛ መልካም ነው ።
ወንግበር ሠለስተ ማኅደረ ።
ምስትም ዳስ እንሥራ አለው ።
፩ደ ለከ ። አንዱን ላንተ ። ወ፩ደ ለሙሴ ። ወ፩ደ
ለኤልያስ ።
አንዱንም ለሙሴ ። አንዱንም ለኤልያስ ።
ወኢየአምር ዘይብል ።
የሚናገረውን አያውቅም ነበር ።
እስመ ድንጉፃን እሙንቱ ።
ደንግጠውም ነበርና ።
፯ ወመጽአ ደመና ብሩህ ወጸለሎሙ ።
፯ ብሩህ ደመና መጥቶም ሠወራቸው ።
ወመጽአ ቃል እምደመና ዘይብል ዝንቱ ውእቱ
ወልድየ ዘአፈቅር ።
ከደመናም የምወደው ልጄ ይህ ነው ።
ወሎቱ ስምዕዎ ።
የሱንም ስሙት የሚል ቃል ተሰማ ።
፰ ወእምዝ ነጸሮሙ ግብተ አልቦ ዘርእዩ
ዘእንበለ እግዚእ ኢየሱስ ባሕቲቱ ምስሌሆሙ ።
፰ ድንገትም በተመለከቱ ጊዜ ጌታን ብቻ
ከሳቸው ጋራ ነው እንጂ ያዩት የለም ።
፱ ወእንዘ ይወርዱ እምደብር አዘዞሙ እግዚእ
ኢየሱስ ኢይንግሩ ወኢለመኑሂ ዘርእዩ ዘእንበለ
አመ ተንሥአ ወልደ እጓለ እመሕያው እምነ ምው
ታን ማቴ ፲፯ ፥ ፱ ።
፱ ከተራራም ሲወርዱ ጌታ የሰው ልጅ ከሙ
ታን በተነሣ ጊዜ ነው እንጂ ሳይነሣ ያዩትን ለማንም
ለማን እንዳይናገሩ አዘዛቸው ።
፲ ወዓቀቡ ቃሎ ። ሚል ፱ ፥ ፭ ።
፲ ነገሩንም አስተዋሉ ።
ወኃሠሠዎ ምንት ውእቱ ተንሥኦ እምነ ምውታን ።
ከሙታን መነሣት ምንም እንደሆነ ተመራመሩ ።

፲፩ ወተስአልዎ አርዳኢሁ ወይቤልዎ ይቤሉ
ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ኤልያስ ይቀድም መጺአ ።
ኢሳ ፶፫ ፥ ፫ ፤ ፱ ፥ ፭ ።

፲፩ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ኤልያስ አስቀድሞ
ይመጣል ይላሉ ብለው ጠየቁት ።

፲፪ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ኤልያስ ይመጽእ
ቅድመ ወያስተራትዕ ኵሎ ።

፲፪ ኤልያስ አስቀድሞ መጥቶ ሁሉን ያቅናናል
ብሎ መለሰላቸው ።
ወአፎ ጽሑፍ በእንተ ወልደ እጓለ እመሕያው ከመ
ብዙኃ የሐምምዎ ወይሜንንዎ ።
በሰው ልጅ መከራ እንዲያመጡበት እንዲንቁትም
እንደምንስ ተጻፈ ።

፲፫ ወባሕቱ እብለክሙ ኤልያስ ወድአ መጽአ
ማቴ ፲፯ ፥ ፲፫ ።
፲፫ ነገር ግን ኤልያስ ፈጽሞ እንደመጣ ።
ወገብሩ ላዕሌሁ ኵሎ ዘፈቀዱ በከመ ጽሑፍ በእን
ቲአሁ ።
ስለሱ እንደ ተጻፈ የወደዱትንም ሁሉ እንዳደ
ረጉበት እነግራችኋለሁ ።
፲፬ ወመጽአ ኀበ አርዳኢሁ ።
፲፬ ወደ ደቀ መዛሙርቱም መጣ ወረከበ ብዙ
ኃነ ሰብአ ኀቤሆሙ ።
ከሳቸውም ዘንድ ብዙ ሰው አገኘ ።
ወጸሐፍትኒ እንዘ ይትኀሠሥዎሙ ጸሐፍቶችም ሲጠ
ይቋቸው ።
በእንተ ዘከመ ሐይወ ዘአስተራገየ ጋኔኑ ።
፲፭ ወሶበ ርእይዎሙ ኵሎሙ ሰብእ ደንገጹ
ወሮጹ ሶቤሃ ወእምኅዎ ።
፲፭ ሰዎችም ባዩት ጊዜ ደንግጠው ያንጊዜው
ንም ሮጠው ተገናኙት ።
፲፮ ወተስእሎሙ ለጸሐፍት ።
፲፮ ጸሐፍትን ጠየቃቸው ።
ምንተኑ ትትኃሠሥዎሙ ።
ለምን ትመራመሯቸዋላችሁ ።
፲፯ ወአውሥአ ፩ዱ እምውስተ አሕዛብ ።
ሉቃ ፱ ፥ ፴፰ ።
፲፯ ከአሕዛብ አንዱ መለሰ ።
ወይቤሎ ሊቅ አምጻእክዎ ለወልድየ ኀቤከ ።
መምህር ሆይ ልጄን ወደ አንተ አምጥቼዋለሁ ።
እስመ ጋኔን በሐም አንዞ ።
ድዳ ጋኔን አድሮበታልና ።
፲፰ ወሀበ ረከቦ ይነጽሖ ።
፲፰ ባገኘውም ሥፍራ ሁሉ ይጥለዋል ።

| | |
|---|---|
| ወያስተራግፆ ። | ያራግጠዋልም ። |
| ወያሴውኖ ። | ያስለግገዋልም ። |
| ወያስይኖ ። | ያሸነዋል ። |
| ያስንኖ ። | ስምንምን ያደርገዋል ። |

ወየሐቅዮ ስነኒሁ ። ጥርሱንም ያፋጫል ።
ያየብሶ ። ያደርቀውማል ።
ወእቤሎሙ ለአርዳኢከ ያውፅእዎ ።
ደቀ መዛሙርትህንም ያወጡት ዘንድ አልኋቸው ።
ወስዕንዎ ፈውሶቶ ። መፈወሱም ተሳናቸው

፲፱ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ኦ ትውልድ አንተ አልባቲ ሃይማኖት እስከ ማዕዜኑ እሄሉ ምስሌከሙ ።

፲፱ እናንተ ሃይማኖት የሌላችሁት ትውልድ እስከመቼ ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ።
እስከ ማዕዜኑ አትዔገሠከሙ እስከ መቼስ እታገሣችኋለሁ ።
አምጽእዎ ዝየ ኀቤየ ።
ወዲህ ወደኔ አምጡት አላቸው ።

፳ ወወሰድዎ ኀቤሁ ።
፳ ወደሱ ወሰዱት ።
ወሶበ ርእዮ ውእቱ ጋኔን ነጽሖ ሶቤሃ ውስተ ምድር
ያም ጋኔን ባየው ጊዜ ያንጊዜውን በምድር ጣለው ።
ወአስተራገጾ ። አራገጠው ።
ወአስወኖ ። አስለገው ፤

፳፩ ወተስአሎ እግዚእ ኢየሱስ ለአቡሁ ።
፳፩ ጌታ አባቱን ጠየቀው ፤
ወይቤሎ እማዕዜ ዘእኀዞ ።
ከምን ጊዜ ጀምሮ ነው የያዘው አለው ።
ወይቤሎ እምንዕሱ ።
ከትንሽነቱ ጀምሮ ነው አለው ።
፳፪ ወዘልፈ ያወድቆ ኀበ እሳት ወውስተ ማይ ።
፳፪ ዘወትር ከእሳትና ከውኃ ከገደል ይጥለዋል።
ከመ ይቅትሎ ። ሊገድለው ፤
ወባሕቱ በዘትክል ርድአኒ ።
ነገር ግን በሚቻልህ እርዳኝ ፤
ወመሐረኒ ። እዘንልኝ ፤
፳፫ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ እስመ ትቤ በዘትክል ርድአኒ እመ ትክል እሚነ ኵሉ ይትከሃል ለዘየአምን ።

፳፫ ጌታም አንተ እላመንከምና በተቻለህ እርዳኝ ትላለህ እንጂ ለሚያምንስ ሁሉ ይቻለዋል ፤ አንድም አንተ ባታምን በተቻለህ እርዳኝ ትላለህ እንጂ ለሚያምን ግን ሁሉ ይቻለዋል ።
፳፬ ወጸርሐ አቡሁ ለውእቱ ወልድ ወይቤ አአምን ።
፳፬ የብላቴናውም አባት እምናለሁ ብሎ እሰምቶ ተናገረ ።
ርድአ ለድካመ ሃይማኖትየ ።
ማመኔን እንዘው ማለት ሃይማኖቴን ፍጹም አድርግልኝ አለ ።
፳፭ ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ይትራወጽ ሰብእ ።

፳፭ ጌታም ሰዎች ሲራወጡ ባየ ጊዜ ።
ገሠፆ ለውእቱ ጋኔን ።
ያን ርኩስ መንፈስ ገሠፀው ።
ወይቤሎ ጋኔን እኩይ ወበሓም አነ እኤዝዘከ ትፃዕ እምኔሁ ።
አንተ ድዳ ደንቆሮውም ጋኔን ከሱ ትወጣ ዘንድ ፤
እኔ አዝዛለሁ አለው ።
ወኢትባእ እንከ ዳግመ ላዕሌሁ ።
ከእንግዲህም ወዲህ አትመለስበት ።
፳፮ ወእግዓረ ብዙኃ ፤
፳፮ ብዙ አስጨነቀው ።
ወአስተራገፆ ወወፅአ
አራግጦት ወጣ ።
ወኮነ ከመ በድን
እንደ በድን ሆነ ።
እስከ ይብሉ ብዙኃን ሞተ
ብዙ ሰዎች ሞተ እስኪሉ ድረስ ።
፳፯ ወእኀዞ እግዚእ ኢየሱስ በእዴሁ ወእንሥኦ
፳፯ ጌታ በጁ ይዞ እነሣው ።
ወተንሥአ ፤ ተነሣ ።
፳፰ ወበዊኦሙ ቤተ ይቤልዎ አርዳኢሁ በባሕቲቶሙ በእፎ ስዕነ ንሕነ አውፅኦቶ ።
፳፰ ከቤት በገቡም ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ እኛ ማውጣት እንደምን ተሣነን አሉት ።
፳፱ ወይቤሎሙ ዝንቱ ዘመድ ኢይክል አውፅኦቶ ዘእንበለ በጾም ወበጸሎት ።
፳፱ ይህ ዘመድ ያለ ጾም ያለ ጸሎት ያወጣ ዘንድ አይችልም አላቸው ።
፴ ወወፂኦ ሀየ ሖረ አንተ ገሊላ ።
፴ ከዚያም ወጥቶ ወደ ገሊላ ሄደ ።
ወኢፈቀደ ያእምርዎ ።
ሊያውቁት ግን አልወደደም ።

ዘከመ አቅደመ ነጊረ መዊቶቱ ፤

፴፩ ወመሐሮሙ ለአርዳኢሁ ማቴ ፲፯፥ ፳፩ ። ሉቃ ፱ ፥ ፳፪-፴፩ ።
፴፩ ደቀ መዛሙርቱን አስተማራቸው ፤
ወይቤሎሙ ሀለዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው ይግባዕ ውስተ እደ ሰብእ ኃጥአን ።
ክርስቶስ በሰው እጅ ይሰጥ ዘንድ አለው ፤
ወይቀትልዎ ፤ ይገድሉታል ።
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛውም ቀን ይነሣል ።
፴፪ ወኢያእመሩ ዘይቤሎሙ ።
፴፪ የነገራቸውን ግን አላወቁትም ።
ወይፈርህዎ ተስእሎቶ ሊጠይቁትም ፈሩ ።

በእንተ ትሕትና ወትዕግሥት ዘክርስቲያን ፤

፴፫ ወበጺሖ ቅፍርናሆም ወበዊአ ቤተ ይቤሎሙ ምንተኑ ሐለይክሙ በፍኖት በበይናቲክሙ ።

፴፫ ቅፍርናሆም ደርሶ በቤትም በገባ ጊዜ ከመንገድ ምን አስባችሁ ነበር ብሎ ጠየቃቸው ።

፴፬ ወአርመሙ ማቴ ፲፰ ፥ ፩ ሉቃ ፱ ፥ ፵፮
፴፬ ዝም አሉ ።
እስመ ተበሀሉ በበይናቲሆሙ በፍኖት መኑ እንጋ የዓቢ እምኔሆሙ ።
ከሳቸው ማናቸው እንዲበልጥ በመንገድ እርስ በርሳቸው ተነጋግረው ነበርና ።

፴፭ ወነበረ ወጸውአሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ።
፴፭ ተቀምጦም አሥራ ሁለቱን ጠራቸው ።
ወይቤሎሙ ዘይፈቅድ ይኩን ሊቀ ለያትሕት ርእሶ ለኵሉ ።
በላይ ሊሆን የሚወድ ራሱን ለሁሉ ያዋርድ ።
ወይኩውን ላዕኩ ለኵሉ ።
ለሁሉም አገልጋይ ይሁን አላቸው ።

፴፮ ወነሥአ ሕፃነ ወዓቀሞ ማዕከሎሙ ።
፴፮ ሕፃኑን ወስዶ በመካከላቸው አቆመው ።
ወአንበሮ ውስተ ሕፅኑ ።
ባጠገቡ አኖረው ።
ወይቤሎሙ ዘተወክፈ ዘከመዝ ሕፃነ በስምየ ኪያየ ተወክፈ ።
እንደዚህ ሕፃን ያለውን በስሜ የተቀበለ እኔን ተቀበለኝ ።

፴፯ ወዘኒ ተወክፈ ኪያየ አኮ ኪያየ ባሕቲቶ ዘተወክፈ ዘእንበለ ዘፈነወኒ ።
፴፯ እኔንም የተቀበለ የላከኝን ነው እንጂ እኔን ብቻ የተቀበለ አይደለም ሐተታ በመንገድ ሳለ መኑ የዓቢ ተባብለዋል ከዚህ በኋላ ከቤት ገብቶ ቆይቶ በመንገድ ምን ተባብላችሁ ነበር አላቸው አወቀብን ብለው አርመሙ ዝም አሉ ምሳሌ ሕፃን ነገራቸው አንድም ከመንገድ መኑ የዓቢ ተባብለዋል ከቤት ገብቶ ከመንገድ ምን ተባብላችሁ ነበር አላቸው ማን ይበልጣል ተባብለን ነበር አሉት ምሳሌ ሕፃንን ነገራቸው አርመሙ አንድም ከመንገድ መኑ የዓቢ ተባብለዋል ከቤት ገብቶ ምሳሌ ሕፃንን ነገራቸው። አላወቀብንም እንዳይሉ በዚያውስ ላይ በመንገድ ምን ተባብላችሁ ነበር አላቸው ።
አርመሙ ፤ ዝም አሉ ።
፴፰ ወአውሥኦ ዮሐንስ ወይቤሎ ሊቅ በዘር ኢነ እንዘ ያወጽእ አጋንንተ በስምከ ወከላዕናሁ ። ሉቃ ፱ ፥ ፵፱
፴፰ መምህር ሆይ በስምህ አጋንንትን ሲያወጣ አይተን የከለከልነው አለ ብሎ ዮሐንስ ተናገረ ።
እስመ ኢተለወከ ምስሌነ ።
ከኛ ጋራ አልተከተለህምና ማለት እንደኛ አላመነብህምና ፤
፴፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢትከልእዎ ፩ቆሮ ፲፪ ፥ ፫ ።

፴፱ ጌታም አትከልክሉት አላቸው ።
እስመ አልቦ ዘይገብር ኃይለ በስምየ ወይክል ፍጡነ አንሥኦ ቃለ ሳዕሌየ ።
በስሜ ኃይል እየሠራ ፈጥኖ በኔ ላይ ክፉ ሊናገር አይችልምና ማለት እኔን ዕሩቅ ብእሲ እያለ በኔ ስም ተአምራት ማድረግ የሚቻለው የለምና ።

፵ እስመ እምከመ ኢኮነ ዕድውክሙ ቢጽክሙ ውእቱ ።

፵ ባለጋራችሁም ካልሆነ ወንድማችሁ ነው። ማለት እኔንም ዕሩቅ ብእሲ ካላለ ወንድማችሁ ነው ።
፵፩ ወዘአስተየክሙ ጽዋዓ ማይ ቈሪር በስምየ እስመ እለ ክርስቶስ አንትሙ አማን እብለክሙ ኢየኃጕል ዕሤቶ ። ማቴ ፲ ፥ ፵፪ ።
፵፩ የክርስቶስ ወገን ናችሁና ብሎ በስሜ ጽዋ ውኃ ያጠጣችሁ ዋጋውን አያጣም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

## ዘከመ ይደሉ አጥፍኦተ ዕቅፍት

፵፪ ወዘአስሐቶ ለ፩ እምእሉ ንዑሳን እለ የአምኑ ብየ ይኄይሶ ከመ ይዕሥሩ በክሣዱ ማኅረፀ አድግ ወያሥጥምዎ ውስተ ልጎተ ባሕር ። ማቴ ፲፰ ፥ ፮ ሉቃ ፲፯ ፥ ፪ ።
፵፪ በኔ ካመኑ አንዱን ያሳተ አህያ የሚፈጭ በትን የወፍጮ ድንጊያ ባንገቱ አስረው ከባሕር ጥልቅ ሊያሰጥሙት ይሻለዋል ።
፵፫ ወእመኒ እዴከ ታስሕተከ ምትራ ። ማቴ ፭ ፥ ፴ ፤ ፲፰ ፥ ፰ ፤
፵፫ እጅህም ብታስትሕ ቁረጣት ።
እስመ ይኄይሰከ ምቱረ እድ ትባእ ውስተ ሕይወት እምትባእ ምስለ ፪ኤሆን እደዊከ ውስተ እሳተ ገሃነም
፵፬ ኀበ እጼሁ ኢይነውም ወእሳቱ ዘኢይጠፍእ
፵፬ ትሉ ወደማይተኛበት እሳቱም ወደማይጠፋበት ወደ ገሃነም ሁለት እጅ ኑሮህ ከምትገባ እጅህ ተቆርጦ ወደ ሕይወት ብትገባ ይሻልሃልና ።
፵፭ ወእመኒ እግርከ ታስሕተከ ምትራ ።
፵፭ እግርህም ብታስትህ ቁረጣት ።
እስመ ይኄይሰከ ሐንካስከ ትባእ ውስተ ሕይወት እምትባእ ምስለ ፪ሆን እገሪከ ውስተ እሳተ ገሃነም ።
፵፮ ኀበ ዕጼሁ ኢይነውም ወእሳቱ ኢይጠፍእ ። ኢሳ ፷፮ ፥ ፳፬
፵፮ ትሉ ወደማይተኛበት እሳቱም ወደማይጠፋበት ወደ ገሃነመ እሳት ሁለት እግር ኑሮህ ከምትገባ አንካሳ ሁነህ ወደ ሕይወት ብትገባ ይሻልሃልና።
፵፯ ወእመኒ ዓይንከ ታስሕተከ ምልሖ ።
፵፯ ዓይንህም ብታስትህ አውጥተህ ጣላት ።
እስመ ይኄይሰከ ነቋረከ ትባዕ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር እምትባእ ምስለ ፪ሆን አዕይንቲከ ውስተ ገሃነም ዘእሳት ።
፵፰ ኀበ ዕጼሁ ኢይነውም ወእሳቱ ኢይጠፍዕ።

፵፯ ትሉ ወደማይቶኛበት እሳቱም ወደማይ ጠፋበት ወደገሃነመ እሳት ሁለት ዓይን ኑሮህ ከምትገባ አንድ ዓይንህ ጠፍቶ ወደ መንግሥተ እግዚአብሔር ብትገባ ይሻልሃልና ።

፵፰ እስመ ኵሉ በእሳት ይትሜላህ ።
ዘሌዋውያን ፪ ፣ ፲፫ ።

፵፱ ሁሉ በእሳት ይጣፍጣል አኮን ወኵሉ ዘይጠባሕ ይትሜላህ በጼው ።
የሚሠዋውን ሁሉ በጨው ያጣፍጡታል ።

፶ ሠናይ ውእቱ ጼው ።

፶ ጨው መልካም ነው ።
ወእመሰ ጼው ለስሐ በምንት እንከ ይቄስምዎ ።
ማቴ ፭ ፣ ፲፫ ። ሉቃ ፲፬ ፣ ፴፬ ።
ጨው ግን አልጫ ከሆነ በምን ያጣፍጡታል ።
ጼወ ርከቡ በበይናቲከሙ ።
እናንተ በናንተ ጼው አግኙ ።
ወተሰነአው ። ተስማሙ ።
አንድም እስመ ኵሉ በእሳት ይትሜላህ ብለህ መልስ ሥራውን ሁሉ በሃይማኖት ይሠሩታል ።
ወኵሉ ዘይጠባሕ ፤ ሥራውን ሁሉ በፍቅር ይሠሩታል ።
ሠናይ ውእቱ ጼው ፤ ፍቅር መልካም ነው ።
ወእመሰ ጼው ለስሐ ።
ፍቅር ከሌለ የሚሠራውን ሥራ ሁሉ በምን ይሠሩታል
ጼወ ርከቡ ፤ ፍቅርን ያዙ ።
ወተሰነአው ብሎ ገልጠው ተስማሙ ።

ዘከመ ተግሕሠ ኢየሱስ እም ኢየሩሳሌም ።

ምዕራፍ ፲ ።

፩ ወተንሥአ እምህየ ሖረ ብሔረ ይሁዳ እንተ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ። ማቴ ፲፱ ፣ ፩ ።

፩ ከዚያ ተነሥቶ በዮርዳኖስ ማዶ ይሁዳ ከሚ ባል አገር ሄደ ።
ወሖሩ ምስሌሁ ሕዝብ ።
ሕዝቡም ከሱ ጋራ ሄዱ ።
ወመሐሮሙ በከመ ያስምድ ።
እንደለመደ አስተማራቸው ።

ዘከመ ኢይደሉ ኅዲገ ብእሲት
ወእውስቦ ካልዕት ።

፪ ወመጽኡ ካዕበ ፈሪሳውያን ወተሰእልዎ ።
፪ ዳግመኛ ፈሪሳውያን መጥተው ጠየቁት ።
እንዘ ይብሉ ቦኑ ይከውንኑ ለብእሲ ኅዲገ ብእሲቱ ።
ለሰውም ሚስቱን መፍታት ይገባዋልን ብለው ፤
እንዘ ያሜክርዎ ፤ ሲፈትኑት ።

፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ምንትኑ አዘዘከሙ ሙሴ ።

፫ ሙሴ ምን አዘዟችሁ ነበር ብሎ መለሰላቸው ።
፬ ወይቤልዎ አዘዘነ ሙሴ ንጽሕፍ ላቲ መጽሐፈ ኅዳጋቲሃ ወንድኅራ ። ዘዳ ፳ ፣ ፴፩ ።

፬ ሙሴ የፍችዋን መጽሐፍ ጽፎ ሰጥቶ ይፍታት ብሎ አዞናል አሉት ።

፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ በከመ እከየ ልብከሙ ወሀበከሙ ሙሴ ዘንተ ትእዛዘ ትድኅሩ እንስቲያክሙ ።

፭ ጌታም ሙሴ እንደልቡናችሁ ክፋት ሚስቶቻችሁን ትፈቱ ዘንድ አዘዛችሁ ብሎ መለሰላቸው ።

፮ ወእምፍጥረትሰ ተባዕተ ወአንስተ ገብረ እግዚአብሔር ።

፮ ከፍጥረት መጀመሪያ ግን እግዚአብሔር ተባዕትና አንስት አደረገ ።

፯ ወበእንተ ዝንቱ የኃድግ ብእሲ አባሁ ወእሞ ወይትልዋ ለብእሲቱ ። ዘፍ ፪ ፣ ፳፬ ማቴ ፲፱ ፣ ፭ ፩ቆሮ ፯ ፣ ፲ ኤፌ ፭ ፣ ፴፩ ።

፯ ስለዚህ ሰው አባትና እናቱን ትቶ ሚስቱን ይከተላል ማለት ከሚስቱ ጋራ አንድ ይሆናል ።
ወይከውኑ ፪ሆሙ ፩ደ ሥጋ ፩ ቆሮ ፯ ፣ ፲፯ ።

፰ ሁለቱም አንድ ሥጋ ይሆናሉ ።
ናሁኬ ኢኮኑ ፪ተ ፤ እነሆ ሁለትም አይደሉም ።

፰ አላ አሐዱ ሥጋ እሙንቱ ፤
አንድ ሥጋ ናቸው እንጂ ።

፱ ዘእግዚአብሔር እንከ አስተፃመረ ሰብእ ኢይፍልጥ ።

፱ እግዚአብሔር ያገናኘውን ሰው አይለይ ።
ሐተታ፣ማቴዎስ ፈሪሳውያን ጠየቁት ይላል ማርቆስ እሉ ጠየቃቸው አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ይከውናሁ ለብእሲ ይድኅር ብእሲቶ በኵሉ ዘአበሰት ሎቱ ቢሉት ኢያንበብክሙኑ ዘውስተ ኦሪት ዘከማ ፈጠሮሙ ተባዕተ ወአንስተ ገብሮሙ ብእሴ ወብእሲተ ረሰዮሙ ።
ወበእንተዝ የኃድግ ብእሲ አባሁ ወእሞ ወይተልዋ ለብእሲቱ ይላቸዋል ፤ ለምንትኑ እንከ አዘዘነ ሙሴ ይሉታል ፤ ምንተ እንከ አዘዘከሙ ይላቸዋል ፤ ሙሴሰ እዘዘነ ንጽሐፍ ላቲ መጽሐፈ ኅዳጋቲሃ ወንድኅራ ይሉታል፤እሱም ሙሴሰ አዘዘከሙ በከመ እከየ ልብከሙ ትድኅሩ አንስቲያክሙ ወእምፍጥረትሰ አኮ ከመዝ ዘእግዚአብሔር አስተፃመረ ሰብእ ኢይፍልጥ ይላቸዋል ፤ አንድም ይከውናሁ ለብእሲ ቢሉት ዘእግዚአብሔር አስተፃመረ ሰብእ ኢይፍልጥ ይላቸዋል ፤ ለምንት አዘዘነ ሙሴ ይሉታል ፤ ምንትኑ አዘዘከሙ ይላቸዋል ፤ ሙሴሰ አዘዘነ ንጽሐፍ ላቲ መጽሐፈ ኅዳጋቲሃ ወንድኅራ ይሉታል ፤ እሱም ሙሴሰ አዘዘክሙ በከመ እከየ ልብከሙ ትድኅሩ እንስቲያክሙ ወእምፍጥረትሰ አኮ ከመዝ ብሎ ኢያ

ንበብከሙኑ ዘውስተ ኦሪት ዘከመ ተዲሙ ፈጠሮሙ ተባዕተ ወአንስተ ገብሮሙ ብእሲ ወብእሲተ ረሰዮሙ ወበእንተዝ የኃድግ ብእሲ አባሁ ወእሞ ፤ ወይተልዋ ለብእሲቱ ወይከውኑ ክልኤሆሙ ፩ደ ሥጋ ወናሁ ኢኮኑ ፪ኤተ አላ ፩ዱ ሥጋ ፤ ሙንቱ ደላቸዋል ፤ አንድም ይከውኖሁ ቢሉት ምንትን አዘዘ ከሙ ሙሴ ይላቸዋል ። ሙሴስ አዘዘን ይሉታል ፤ ሙሴስ አዘዘከሙ በከመ እከየ ልብከሙ እምፍጥትስ ብሎ ዘእግዚአብሔር አስተፃመረ ሰብእ ኢይፍልጥ ይላቸዋል ።

፲ ወበቤት ካዕበ ተስእልዎ አርዳኢሁ በእንተ ዝንቱ ።

፲ ስለዚህ ነገር ደቀ መዛሙርቱ ዑለተኛ በቤት ጠየቁት ።

፲፩ ወይቤሎሙ ዘደኃረ ብእሲቶ ወሖረ ካልዕተ ዘመወ ላዕሌሃ ።

፲፩ ሚስቱን የፈታ ሌላይቱንም ያገባ ሰሰነባት።

፲፪ ወእንተሂ ደኃራ ምታ ወሖረት ካልዓ ዘመወት ።

፲፪ ባሏ የፈታትም ሌላ ወንድ ብታገባ ሰሰነች እላቸው ።

ዘከመ ባረኮሙ ኢየሱስ ለሕፃናት ።

፲፫ ወአምጽኡ ኀቤሁ ሕፃናተ ይግሥሦሙ ።

፲፫ ሕፃናትን ይዳስሳቸው ወደሱ አመጡቸው ።

ወገሠጽዎሙ አርዳኢሁ ለእለ አምጽእዎሙ ።

ደቀ መዛሙርቱ ግን ያመጧቸውን ተቆጧቸው ።

፲፬ ወርእየ እግዚእ ኢየሱስ ተምዓ ።

ጌታም አይቶ ተቆጣ ።

፲፬ ወይቤሎሙ ኅደጉ ሕፃናተ ይምጽኡ ኀቤየ ወኢትክልእዎሙ ሕፃናትን ወደኔ ይመጡ ዘንድ አትከልክሏቸው ።

እሰመ ለከመዝ እሉ ደእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር መንግሥተ እግዚአብሔር እንደዚህ ላሉ ናትና ።

፲፭ አማን እብለከሙ ዘኢተቀበላ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ከመ ሕፃን ኢይበውእ ።

፲፭ መንግሥተ እግዚአብሔርን እንደ ሕፃን ያልተቀበላት አይገባትም ብየ በውነት እነግራች ኋለሁ ።

፲፮ ወአንበሮሙ ውስተ ሕፅኑ ወባረኮሙ ።

፲፮ ባጠገቡ አኑሮ ባረካቸው ።

ወወደየ እዴሁ ዲቤሆሙ ።

እጁንም ጫነባቸው ።

በእንተ ወሬዛ ባዕል ።

፲፯ ወእንዘ የሐውር በፍኖት መጽአ ፩ዱ ብእሲ ወሰገደ ሎቱ ።

ማቴ ፲፱ ፥ ፲፫ ሉቃ ፲፰ ፥ ፲፭

፲፯ በመንገድ ሲሄድ አንድ ሰው መጥቶ ሰገደለት ።

ወይቤሎ ሊቅ ኄር ምንተ እግበር ከመ እረስ ሕይወተ ዘለዓለም ቸር መምህር ሆይ የዘላለምን ሕይወትን እወርስ ዘንድ ምን ላድርግ አለው ።

፲፰ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ምንተ ትብለኒ ኄር ።

፲፰ ጌታም ምን ቸር ትለኛለህ ፤

አልቦ ኄር ዘእንበለ ፩ዱ እግዚአብሔር ፤

ያላንድ እግዚአብሔር ቸር የለም አለው ።

፲፱ ተአምር ትእዛዛተ ። ዘፀ ፳ ፥ ፲፫

፲፱ ትእዛዞን ታውቃለህ ፤

ኢትዑር ብእሲተ ብእሲ ።

ወደጉልማሳ ሚስት አትሂድ ፤

ኢትቅትል ነፍሰ ፤　　ነፍስ አትግደል ።

ኢትሥርቅ ፤　　አትሥረቅ

ኢትኩን ስምዓ በሐሰት ፤

በሐሰት አትመስክር ።

ኢትሂድ ፤　　አትቀማ ።

አክብር አባከ ወእመከ ፤

አባት እናትህን አክብር ።

፳ ወአውሥአ ወይቤሎ ሊቅ ዘንተ ኵሎ ዓቀብኩ እምንዕስየ ።

፳ መምህር ሆይ ይህን ሁሉ ከሕፃንነቴ ጀምሮ ጠብቄዋለሁ ብሎ መለሰ ።

፳፩ ወነጸሮ እግዚእ ኢየሱስ ።

፳፩ ጌታም ወደሱ ተመለከተ ።

ወአፍቀሮ ፤　　ወደደውም ።

ወይቤሎ አሐተ ፈቀድከ ፍጹመ ትኩን አሐቲ ተርፈተከ ።

ፍጹም ልትሆን ከወደደ ህስ አንዲት ቀርታሃለች ።

፳፪ ሖር ሢጥ ኵሎ ዘብከ ወሀብ ለነዳያን ።

፳፪ ሂደህ ያለህን ሸጠህ ለድሆች ስጥ ።

ወትረክብ መዝገበ በሰማያት ፤

በሰማይ ገንዘብ ታገኛለህ ።

ወጹር መስቀለ ሞትከ ወነዓ ትልወኒ ።

የምትሞትበትንም መስቀል ተሸክመህ መጥተህ ተከተለኝ ።

ወተከዘ በእንተ ዝንቱ ነገር ወሖረ ትኩዞ ።

ስለዚህ ነገር አዝኖ ተከዞም ሄደ ፤

እስመ ብዙኅ ጥሪቱ ፤

ገንዘቡ ብዙ ነበርና ።

ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ።

ጌታም ወደ ደቀ መዛሙርቱ አየ ።

፳፫ ወይቤሎሙ እፎ ዕፁብ ለዘቦ ንዋይ በዊአ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፫ ገንዘብ ላለው ሰው ወደ መንግሥተ እግዚአብሔር መግባት እንደምን ጭንቅ ይሆን አላቸው ።

፳፬ ወአንከሩ አርዳኢሁ በዘንቱ ነገር ።
፳፬ ደቀ መዛሙርቱም ይህን ነገር አደነቁ ። ወካዕበ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ደቂቅየ እፎ ዕጹብ ለዘቦ ንዋይ በዊዕ ውስተ መንግሥተ ሰማያት ።
ዳግመኛም ጌታ ለደቀ መዛሙርቱ ልጆቼ ለባለጸጎች ወደ መንግሥተ ሰማያት መግባት እንደምን ጭንቅ ይሆንባቸዋል አላቸው ።

፳፭ ይቀልል ይኅልፍ ገመል እንተ ቀፈረ ሐፅ እምባዕል ይባዕ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
፳፭ ባለ ጸጋ ከብቱን ጨርሶ መጥውቶ ወደ መንግሥተ እግዚአብሔር ከሚገባ ገመል ከነጭነቱ በደጋኑና በጅማቱ መካከል ቢያልፍ ይቀላል ። ይህስ ያልፋል ብሎ ደጋኑ ብስ አለው በዚያ ቢያልፍ ይቀላል ሲል ነው ። ሐተታ ማቴዎስ ስቍረተ መርፍዕ ይላል ከዚህ ማርቆስ ቀፈረ ሐፅ አለ እንደምን ነው አይለያይም ቢሉ አይለያይም የለሁት ቀን ትምህርት የልሳን መለያየት ነው ።

፳፮ ወፈድፋደ አንከሩ ወተባሀሉ በበይናቲሆሙ መኑ እንከ ይክል ድኂነ ።
፳፮ እጅግም አድንቀው እንግዲህ መዳን የሚቻለው ማነው ተባባሉ ።
፳፯ ወነጸሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ብኀበ ሰብእ ኢይትከሃል ዝ ።
፳፯ ጌታ አይቷቸው ይህ በሰው ዘንድ አይቻልም ።
ወበኀበ እግዚአብሔርሰ ኵሉ ይትከሃል ።
በእግዚአብሔር ዘንድ ግን ሁሉ ይቻላል አላቸው ።

በእንተ ዕሤቶሙ ለእለ
ይተልውዎ ለኢየሱስ ።

፳፰ ወአኀዘ ጴጥሮስ ይቤሎ ናሁ ኬ ንሕነ ኀደግነ ኵሎ ወተለውናከ ። ማቴ ፲፱ ፡ ፳፯ ። ሉቃ ፲፰ ፡ ፳፰ ።
፳፰ ጴጥሮስም እነሆ እኛ ሁሉን ትተን ተከትለንሃል ይለው ጀመር ።
፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ አልቦ ዘየኀድግ አብያተ ወአኃወ አበ ወእመ ወብእሲተ ወውሉደ ወገራውህ በእንቲአየ ወበእንተ ወንጌልየ ።
ዘኢይትዓሠይ ምዕተ ምክዕቢተ በዝንቱ ዓለም አብያተ ወአኃወ ወአንተ አበ ወእመ ወገራውሃ በስደት ።
፳፱ ጌታም እኅቶቹንና ወንድሞቹን አባቱንና እናቱንም ልጆቹንና ሚስቱን እርሻውንም ስለኔ ስለ ወንጌልም በስደት የተወ ፣ ቤቶችን እኅቶችንና ወንድሞችንም አባትና እናትንም እርሻንም በዚህ ዓለም መቶ ዕፅፍ የማያገኝ የለም ብሎ መለሰላቸው ።

፴ ወበዓለምስ ዘይመጽእ ሕይወተ ዘለዓለም ።
፴ በሚመጣውም ዓለም የዘላለም ሕይወትን ያገኛል ።
፴፩ ወብዙኃን ቀደምት ይከውኑ ድኃርተ ። ማቴ ፲፱ ፡ ፴ ።
፴፩ ነገር ግን ብዙ የፊተኞች የኋለኞችን ይሆናሉ ።
ወደኃርትኒ ይከውኑ ቀድመ ።
የኋለኞችም ወደፊት ይሆናሉ ።
በእንተ ካልዕ ትንቢት ዘሕማማት ።

፴፪ ወበፍኖት እንዘ የዓርግ ኢየሩሳሌም ። ሉቃ ፲ ፡ ፳ ፡ ፴ ፡ ፩ ።
፴፪ ወደ ኢየሩሳሌም ሲሄድ በመንገድ ፤
ይቀድሞሙ እግዚእ ኢየሱስ ፤
ጌታም በፊታቸው ነበር ፤
ደንገጹ ፤ ደነገጡ ።
ወእለሂ ይተልውዎ ፈርሁ ፤
የተከተሉትም ፈሩ ።
ወነሥኦሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ፤
አሥራ ሁለቱንም ይዟቸው ሄደ ።
ወአኀዘ ይንግሮሙ ዘሀለዎ ይርከቦ ፤
ይደርስበት ዘንድ ያለውንም ይነግራቸው ጀመር ።
፴፫ ወይቤሎሙ ናሁ ነዓርግ ኢየሩሳሌም ።
፴፫ እነሆ ወደ ኢየሩሳሌም እንወጣለን ።
ወይእኅዝዎ ለወልደ እጓለ እመሕያው ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ።
ሊቃነ ካህናትና ጸሐፍት ክርስቶስን ይይዙታል ።
፴፬ ወይኴንንዎ በሞት ፤
፴፬ የሞት ፍርድም ይፈርዱበታል ።
ወይሜጥውዎ ለአሕዛብ ፤
ለአሕዛብ አሳልፈው ይሰጡታል ።
ወይሣለቁ ላዕሌሁ ።
ይዘብቱበታል ።
ወይዌርቅዎ ፤ ይተፉበታል ።
ወይቀሥፍዎ ፤ ይገርፉታል ።
ወይቀትልዎ ፤ ይገሉታል ።
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛውም ቀን ይነሣል ።

በእንተ ገሥዖ ትዝሕርት ዘደቂቀ ዘብዴዎስ ።

፴፭ ወአንዘ የሐውሩ ምስሌሁ ያዕቆብ ወዮሐንስ ፪ሆሙ ደቂቀ ዘብዴዎስ ይቤልዎ ሊቅ ንፈቅድ ትግበር ለነ ዘስአልናከ ።
፴፭ ሁለቱም የዘብዴዎስ ልጆች ያዕቆብና ዮሐንስ ከሱ ጋራ ሲሄዱ የለመንህን ልታደርግልን እንወዳለን አሉት ። ሐተታ ማቴዎስ እናታቸው ሄዳ ተናገረች ይላል ማርቆስ እሳቸው ተናገሩ አለ ፤ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው እሷ ሄዳ ተናግራለች ማርቆስ እሳቸው ተናገሩ ማለቱ አብረው ሄደው መናገራቸውን ሲያይ

ዛሬ አማላጅ የሰደደ ሰው አብሮ ሄዶ እንዲናገር እንድም ነገር እንደ ማርቆስ ነው ፊት አሳቸው ተና ግረዋል እምታለሁ እስቀላለሁ ብላቸው ሹመት ይለምኑኛል ብሎ ሳይመልስላቸው ቀረ ። ለኛስ አልመለሰልንም በዚያ በዘመድሽ ዕወቂበት አንች ሄደሽ ተናገሪልን ብለዋት እሷ ሄዳ ተናግራለች ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ።

፴፮ ወይቤሎሙ ምንተ ትፈቅዱ እግበር ለክሙ

፴፮ ምን ላደርግላችሁ ትወዳላችሁ አላቸው ።

፴፯ ወይቤልዎ ሀበነ ንንበር ፩ድነ በየማንከ ወ፩ድነ በጸጋምከ በውስተ ስብሐቲከ ።

፴፯ በጌትነትህ አንዳችን በቀኝህ አንዳችን በግ ራህ እንቀመጥ ዘንድ ስጠን አሉት ።

፴፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢተአምሩ ዘትስእሉ ።

፴፰ ጌታም የምትለምኑትን ዐታውቁም አላቸው ትክሉኑ ሰትየ ጽዋዕ ዘአነ እሰቲ እኔ የምጠጣውን ጽዋ ትጠጡ ዘንድ ትችላላችሁን ።
ወተጠምቆትየኒ ዘአነ እጠመቅ ትጠመቁኑ ።
እኔ የምጠመቀውንስ ጥምቀት ትጠመቁ ዘንድ ትች ላላችሁን አላቸው ።

፴፱ ወይቤልዎ እወ ንክል ።

፴፱ እንችላለን አሉት ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ጽዋዕየሰ ዘአነ እሰቲ ትሰትዩ ።
የምጠጣውንስ ጽዋ ትጠጣላችሁ ፤
ወተጠምቆትየኒ ዘአነ እጠመቅ ትጠመቁ ፤
የምጠመቀውንም ጥምቀት ትጠመቃላችሁ ፤

፵ ወነቢረሰ በየማንየ ወበፀጋምየ አኮ እነ ዘእ ሁበክሙ ።

፵ በቀኜና በግራ መቀመጥን ግን እኔ እምሰ ጣችሁ አይደለሁም ።
አላ ለካልዓን እስተዳለወ ሎሙ እቡየ ዘበሰማያት ።
የሰማይ አባቴ ለሌሎች አዘጋጅቶላቸዋል እንጂ ።

፵፩ ወሰሚዖሙ ፲ቱ ተምዑ ዲበ ፪ቱ አኃው ያዕቆብ ወዮሐንስ ።

፵፩ ዐሥሩ ሰምተው በሁለቱ ወንድማማች በያዕቆብና በዮሐንስ ተቆጡ ።

፵፪ ወጸውዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኢተአምሩኑ ከመ መላእክቲሆሙ ለአሕዛብ ይኴን ንዎሙ ሉቃ ፳፪ ፡ ፳፭ ።

፵፪ ጌታም ጠርቶ አሕዛብን አለቆቹ እንዲ ፈርዱባቸው ታላላቆችም እንዲፈርዱባቸው አታው ቁም አላቸው ።

፵፫ ወለክሙሰ አኮ ከማሁ ፤

፵፫ ለናንተስ እንዲህ አይሆንም አላ ዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ ይኩንክሙ ገብረ ።
ከናንተ በላይ ሊሆን የሚወድ ተንኛ ይሁናችሁ ።

፵፬ ወዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ዓቢየ ይኩንክሙ ላዕከ ።

፵፬ ከናንተ ታላቅ ሊሆን የወደደ አገልጋይ ይሁናችሁ እንጂ ።

፵፭ እስመ ወልደ ዕጓለ እመሕያውኒ ኢመጽአ ከመ ይትለአክዎ ዘእንበለ ዳኢሙ ከመ ይትለአክ ።

፵፭ የሰው ልጅ ክርስቶስ ስንኳ ሊያገለግል ነው እንጂ ሊያገለግሉት አልመጣምና ።
ወከመ ይቤዝዎሙ ለብዙኃን በነፍሱ ።
በነፍሱም ለውጥ ብዙዎችን ሊያድናቸው ነው እንጂ ።

በእንተ ዕውር ወልደ በርጤሜዎስ ።

፵፮ ወቦአ ኢያሪኮ ። ማቴ ፳ ፡ ፳፱ ሉቃ ፲፰ ፡ ፴፭

፵፮ ወደ ኢያሪኮ ገባ ።
ወሶበ ወፅአ እምኢያሪኮ ወአርዳኢሁኒ ምስሌሁ ወሰብእኒ ብዙኅ ።
ደቀ መዛሙርቱም ብዙ ሰዎችም ከሱ ጋራ ሁነው ከኢያሪኮም በወጣ ጊዜ ።
ሀሎ ጤሜዎስ በርጤሜዎስ ዕውር ይነብር ውስተ ፍኖት ወይስእል ።
ዕውሩ ጤሜዎስ የበርጤሜዎስ ልጅ ከመንገድ ተቀ ምጦ ይለምን ነበር ። ሐተታ በር በዕብራይስጥ ልሳን ልጅ ማለት ነው ፤ ዕውር የዕውር ልጅ ማለት ነው ።

፵፯ ወሰሚዖ ከመ ኢየሱስ ናዝራዊ የኀልፍ ከልሐ ወይቤ ተማሃለኒ ኢየሱስ ወልደ ዳዊት ።

፵፯ የናዝሬቱ ኢየሱስ እንደሆነ ሰምቶ የዳዊት ልጅ ኢየሱስ ሆይ ማረኝ ብሎ አሰምቶ ተናገረ ።

፵፰ ወገሠጽዎ ብዙኃን ከመ ያርምም ።

፵፰ ብዙ ሰዎች ዝም ይል ዘንድ ተቆጡት ።
ወአፈድፈደ ከሊሐ ።
እሱ ግን ጩኸትን አበዛ ።
ወይቤ ወልደ ዳዊት ተሣሃለኒ ።
የዳዊት ልጅ ማረኝ አለ ።

፵፱ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ወአዘዘ ይጸውዕዎ ።

፵፱ ጌታም ቁሞ ጥሩት አለ ።
ወጸውዕዎ ለእውሩ ዕውር ።
ያንም ዕውር ጠሩት ።
ወይቤልዎ ተአመን ወተንሥእ ይጼውዓከ ሊቅ ።
መምር ይጠራሀልና እምነህ ተነሣ አሉት ።

፶ ወተንሥአ ወገደፈ ልብሶ ።

፶ ልብሱን ጥሎ ተነሣ ።
ወለብሰ ልብሶ ወመጽአ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።
ልብሱንም ለብሶ ወደ ጌታ መጣ ። ሐተታ መምር ይጠራሃልእሉት እፈፍ ብሎ ሲነሣ ልብሱ ወደቀበት አንሥቶ ለብሶ ይሄዳል ፤ አንድም የዘወትር ተርታ ልብስና ከሰው የሚደርስበት ደሀና ልብስ አለው የዘወትሩን ትቶ ደሀናውን ልብስ ለብሶ ሄደ ።

፶፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ምንተ ትፈቅድ እግበር ለከ ።

፶፩ ጌታም መለሰ ምን ላደርግልህ ትወዳለህ አለው ።
ወይቤሎ ውእቱ ዕውር ረቡኒ ከመ እርአይ ።
መምር ሆይ አይ ዘንድ ነው አለው ።

፶፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር ሃይማኖትከ አሕየወተከ ።

፶፪ ጌታም ሂድ ሃይማኖትህ አድናሃል አለው ።
ወርእየ ሶቤሃ ። ያን ጊዜውንም አየ ።
ወተለዎ በፍኖት ፤ በመንገድም ተከተለው ።

## ዘከመ ቦአ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም

## ምዕራፍ ፲፩

፩ ወአልጺቆሙ ኢየሩሳሌም ኀበ ቤተ ፋጌ ወቢታንያ እንተ ገቦ ደብረ ዘይት ፈነወ ፪ተ እምአርዳኢሁ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፩ ሉቃ ፲፱ ፡ ፳፱ ።

፩ ኢየሩሳሌም በደረሱ ጊዜ ወደ ደብረ ዘይት አጠገብ ወደ ቢታንያና ወደ ቤተ ፋጌ ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ላከ ።

፪ ወይቤሎሙ ሑሩ ውስተ ሀገር እንተ ቅድሜክሙ ።

፪ በፊታችሁ ወዳለ አገር ሂዱ አላቸው ።
ወበዊአክሙ ሶቤሃ ትረክቡ ዕዋለ አድግ ዕሡረ ዘኢተጽዕና ሰብእ ።
በገባችሁም ጊዜ ሰው ያልተቀመጠበት ያህያ ግልገል ታስሮ ታገኛላችሁ ።
ፍትሕዎ ወአምጽእዎ ሊተ ።
ፈታችሁ አምጡልኝ ።

፫ ወለእመቦ ዘይቤለክሙ ምንተ ትገብሩ በሉ እግዚኡ ይፈቅዶ ።

፫ ምን ታደርጋላችሁ ያላችሁም ሰው ቢኖር ጌታ ይሻዋል በሉ ። ሐተታ ማቴዎስ ዕድግትንም ዕዋልንም ይጽፋል ማርቆስ ዕዋልን ብቻ ጻፈ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ሁለት ናቸው ማርቆስ አንድ ማለቱ ለመናገር ከበቃ ብሎ ነው ፤ አንድም ማቴዎስ መምህረ አሕዛብ ወሕዝብ ነውና የሁለቱንም ምሳሌ ተናገረ ማርቆስ ግን መምህረ አሕዛብ ነው እንጂ መምህረ ሕዝብ አይደለምና የአሕዛብን ምሳሌ ዕዋልን ብቻ ለይቶ ተናገረ ።
ወሶቤሃ ይፌንወከሙ ዝየ ።
ያን ጊዜውንም ወደዚህ ይልካችኋል ።

፬ ወሖሩ ወረከቡ ዕዋለ ዕሡረ ኀበ አንቀጽ ውስተ ፍኖት ።

፬ ሄደውም ግልገሉን ከመንገድ አጠገብ ባደባባይ ታሥሮ አገኙት ።
ወፈትሕዎ ፤ ፈቱትም ።

፭ ወይቤልዎሙ እለ ይቀውሙ ሀየ ምንተ ትገብሩ ዘትፈትሑ ።

፭ ቆመው ያሉትም ውርንጫውን የምትፈቱት ምን ታደርጋላችሁ አሏቸው ።

፮ ወይቤልዎሙ በከመ አዘዞሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

፮ ጌታ እንዳዘዛቸውም ነገሯቸው ወኀደግዎሙ ተዋቸውም ።

፯ ወወሰድዎ ለዕዋል ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ። ዮሐ ፲፪ ፡ ፲፬ ።

፯ ግልገሉንም ወደጌታ አመጡት ።
ወረሐዉ አልባሲሆሙ ላዕሌሁ ወአጽአንዎ ።
ልብሳቸውንም ጎዝጉዘው አስቀመጡት ።

፰ ወብዙኃን እለ ነጸፉ ቆጽለ መቲሮሙ እምዕፀው ።

፰ ቅጠል ከዛፍ እየቆረጡ የጎዘጎዙም ብዙ ናቸው ።
ወቦ እለ ነጸፉ አልባሲሆሙ ውስተ ፍኖት ።
ልብሳቸውንም ከመንገድ የጐዘጐዙ አሉ ።

፱ እለኒ ይመርሑ ወእለኒ ይተልው ይኬልሁ ወይብሉ ሆሣዕና ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር ።

፱ በፊትም በኋላም ይሄዱ የነበሩት በእግዚአብሔር ስም የሚመጣው የተባረከ ሆሣዕና ነው ብለው አሰምተው ተናገሩ ።

፲ ወቡርክት እንተ ትመጽእ መንግሥት በስመ እግዚአብሔር እንተ አቡነ ዳዊት ። መዝ ፻፲፯ ፡ ፳፮ ማቴ ፳፩ ፡ ፱ ሉቃ ፲፱ ፡ ፴፰ ።

፲ በእግዚአብሔር ስም የምትመጣ ያባታችን የዳዊት መንግሥትም የተባረከች ናት ። ሐተታ ዳዊት በትንቢት ያከናወናት ቡርክት እንተ ትመጽእ መንግሥት ያላት ማለት ነው ሆሣዕና በአርያም ።
በሰማይ መድኃኒት መባል ይገባዋል አሉ ።

፲፩ ወቦአ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ኀበ ቤተ መቅደስ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፲ ።

፲፩ ጌታም ወደ ኢየሩሳሌም ወደ ቤተ መቅደስ ገባ ።
ወርእይዎ ኵሉ ሕዝብ ።
ሕዝቡም ሁሉ አዩት ።
ወሶበ መስየ ሖረ ቢታንያ ምስለ ፲ቱ ወ፪ቱ ።
በመሸም ጊዜ ወደቢታንያ ከሥራሁለቱ ጋራ ወጣ ።

## በእንተ በለስ ዘተረግመት ።

፲፪ ወበሳኒታ ሶበ ወጽአ እምቢታንያ ርኅበ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፲፱

፲፪ በነጋውም ከቢታንያ በወጣ ጊዜ ተራበ።

፲፫ ወርእየ ዕፀ በለስ እምርኁቅ ዘባቲ ቈጽል ።

፲፫ በሩቅም ቅጠል ያላት በለስ አየ ።

ወሐረ ይርአይ እመቦ ዘይረክብ በውስቴታ ።
በዚ ፍሬ ያገኝ እንደሆነ ሊያይ ሄደ ።
ወበጺሖ ኀቤሃ አልቦ ዘረከበ ዘእንበለ ቈጽል ባሕቲቱ
ወደርሷም በደረሰ ጊዜ ከቅጠል ብቻ በቀር ያገኘው
የለም ።
እስመ ኢኮነ ጊዜሁ ሰበለስ ።
የበለስ ወራት አልነበረምና ።

፲፬ ወአውሥአ ወይቤላ አልቦ ፍሬ ዘይበልዕ
እምኔኪ ለዓለም ።

፲፬ ለዘለዓለም ካንቺ ፍሬ የሚበላ አይኑር አላት
ወሰምዑ አርዳኢሁ ።
ደቀ መዛሙርቱም ሰሙ ።

በእንተ አለ ያረኵሱ ቤተ መቅደስ

፲፭ ወበጽሐ ኢየሩሳሌም ወቦአ ቤተ መቅደስ ።
፲፭ ኢየሩሳሌም ደረሰ ወደ ቤተ መቅደስም ገባ
ወአኀዘ ይሰድድ እለ ይሣየጡ በምኵራብ ።
በምኵራብ ዋጋ የሚያያርጉትን ያስወጣ ጀመረ ።
ወገፍትዓ ማዕዳቲሆሙ ለመወልጣን ።
የለዋጮችንም ማዕዳቸውን ገለበጠ ።
ወመናብርቲሆሙ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ።
ርግብ የሚሸጡትንም ወምበር ፤

፲፮ ወከልአ ከመ ኢያብኡ ንዋየ ውስተ ምኵ
ራብ ።

፲፮ ወደ ምኵራብ ገንዘብ እንዳያግቡ ከለከለ ።
፲፯ ወመሐሮሙ ወይቤሎሙ አኮኑ ጽሑፍ ዘይ
ብል ቤትየሰ ቤተ ጸሎት ይኩን ለኵሉ አሕዛብ ።
ኢሳ ፶፮ ፣ ፯ ኤር ፯ ፣ ፲፩ ።
፲፯ ቤቴ ለአሕዛብ ሁሉ የጸሎት ቤት ይሁን
የሚል ጽሑፍ ያለ አይደለምን ብሎ አስተማራቸው ።
ወአንትሙሰ ረሰይክምዎ በዓተ ፈያት ወሠረቅት ።
እናንተ ግን የሌቦችና የወንበዶች ዋሻ አደረጋችሁት፤
የገበያውን መፈታት ማቴዎስ እሑድ ይላል ማርቆስ
ሰኞ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ፤
ደገኛውን ገበያ እሑድ ፈቶታል ጥቃቅኑን ገበያ ሰኞ
ፈቶታል ።
፲፰ ወሰምዑ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወኃ
ሠሡ እንተ ኀበ ይቀትልዎ ።
፲፰ ሊቃነ ካህናትና ጸሐፍት ሰምተው የሚ
ገድሉበትን ምክንያት ይፈልጉ ጀመር ።
መፈርህዎ ፤　　　ፈሩት ።
እስመ ኵሉ ሕዝብ ያነክሩ ምሕሮቶ ።
ሕዝቡ ሁሉ ትምርቱን ያደንቁ ነበርና ።
፲፱ ወሶበ መሰየ ወጽአ አፍአ እምሀገር ።
፲፱ በመሸም ጊዜ ከከተማው ወደ ውጪ ወጣ ።
በእንተ ትወክልት ኀበ እምላክ
፳ ወበጽብሐ በነግህ ረከብዋ ለይእቲ በለስ
ይብሰተ እምሥርዋ ።

፳ በነጋው ሲመለሱ ያችን በለስ ከሥርዋ
ደርቃ አገኙዋት ፤ ሐተታ ይብስተ በለሰን ማቴዎስ
ሰኞ ይላል ማርቆስ ማክሰኞ አለ እንደምን ነው አይ
ጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ሰኞ
ማታ ረገሟት መድረቅ ጀምራለች ማክሰኞ ተነ
ቃቅላ ወድቃለች መድረቅ የጀመረችበትን ሲያይ
ማቴዎስ ሰኞ አለ ተነቃቅላ የወደቀችበትን ሲያይ
ማርቆስ ማክሰኞ አለ ፤ አንድም የደረቀችም የወደ
ቀችም ሰኞ ነው መሸቶባቸው ሳያይዋት ሄደዋል
ማክሰኞ ቢመለሱ ተነቃቅላ ወድቃ አይተዋታል
ማቴዎስ የደረቀችበትን ሲያይ ሰኞ አለ ማርቆስ
ያዩበትን ሲያይ ማክሰኞ አለ ።

፳፩ ወተዘከረ ጴጥሮስ ቃሎ ለእግዚእ ኢየሱስ
ወይቤሎ ሊቅ ነያ እንታክቲ በለስ እንተ ረገምካ
የብሰት ።

፳፩ ጴጥሮስ አስቦ መምህር ሆይ እነሆ ያች
የረገምካት በለስ ደረቀች አለው ።

፳፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ
ለእመ ኮነ ውስቴትክሙ ሃይማኖተ እግዚአብሔር
ማቴ ፳፩ ፣ ፳፩ ።

፳፪ ጌታ ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው
እግዚአብሔርን ማመን በናንተ ቢኖር ።

፳፫ አማን እብለክሙ ለእመ ትብልዎ ለዝንቱ
ደብር ተንሥእ ወተወረው ውስተ ባሕር ወኢና
ፈቅሙ በልብክሙ ወተአመንክሙ ይከውን ዘነበ
ብክሙ ወትረክቡ ።

፳፫ እውነት እላችኋለሁ ይህን ተራራ ተነሥተህ
ወደ ባሕር ተወርወር ብትሉት በልቡናችሁም ባት
ጠራጠሩ ብታምኑ እንደተናገራችሁት ሆኖ ታገኛ
ላችሁ ።

፳፬ ወበእንተዝ ዕብለክሙ ኵሎ ዘጸለይክሙ
ወሰአልክሙ እንዘ ትትአመኑ ከመ ትረክቡ ወይ
ከውነክሙ ። ማቴ ፯ ፣ ፯ ፤ ፳፩ ፣ ፳፪ ።
፳፬ ስለዚህ እምላካችሁ የጸለያችሁትን የለመ
ናችሁትንም ሁሉ እንድታገኙ እንዲያደርግላችሁ
እነግራችኋለሁ ።
፳፭ ወሶበሂ ትጼልዩ ኅድጉ ለቢጽክሙ ዘተ
ሐየስክምዎሙ ።
፳፭ በምትጸልዩበትም ጊዜ ወንድሞቻችሁን
የነቀፋችሁባቸውን ይቅር በሉ ።
ከመ ይኅድግ ለክሙ አቡክሙ ዘበሰማያት አበሳክሙ፤
ሰማያዊ አባታችሁ በደላችሁን ይቅር ይላችሁ ዘንድ
፳፮ ወእመሰ አንትሙ ኢኀደግሙ አቡክሙኒ
ሰማያዊ ኢየኀድግ ለክሙ ።
፳፮ እናንተ ግን ይቅር ካላላችሁ ሰማያዊ አባ
ታችሁም ይቅር አይላችሁም ።

በእንተ ተስእሎት ዘዮሐንስ መጥምቅ

፳፯ ወሖረ ካዕበ ኢየሩሳሌም ። ሉቃ ፳ ፥ ፩

፳፯ ሁለተኛ ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ ።
እንዘ ያንሶሱ በምኵራብ መጽኡ ኀቤሁ ሊቃነ
ካህናት ።
በምኵራብ ሲመላለስ ጻፎችና ሊቃነ ካህናት ወደሱ
መጡ ።
ወረበናት ።
ሽማግሎችም ።

፳፰ ወይቤልዎ በመባሕተ መኑ ትገብር ዘንተ ፤
፳፰ ይህን በማን ሥልጣን ታደርጋለህ ።
ወመኑ አብሐከ ትግበር ዘንተ ።
ይህን ታድርግ ዘንድ ማን አሰናበተህ አሉት ።

፳፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እነሂ እሴእ
ለክሙ አሐተ ነገረ ።

፳፱ ጌታም እኔም አንድ ነገር እጠይቃችኋለሁ ።
ወንግሩኒ ፤ እናንተም ንገሩኝ ።
እነሂ እየድዓክሙ ፤ እኔም እነግራችኋለሁ ።
በመባሕተ መኑ እገብር ከመዝ ።
ይህን የማደርገው በማንም ሥልጣን እንደሆነ ።

፴ ጥምቀቱ ለዮሐንስ እም አይቴኑ ።
፴ የዮሐንስ ጥምቀት ከወዴት ናት ።
እምሰማይኑ አው እምሰብእ ።
ከሰማይን ነው ወይስ ከሰውን ነው አላቸው ።
አይድኡኒ ፤ መልሱልኝ ።

፴፩ ወተባሐሉ በበይናቲሆሙ ለእመ ንብሎ
እምሰማይ ይብለነ ለምንት ኢአመንክምዎ ።

፴፩ እርስበሳቸውም እሰቡ ከሰማይ ብንለው
ምነው አላመናችሁበት ይለናል ።

፴፪ ወሰእመኒ ንብሎ እምሰብእ ንፈርሆሙ
ለሕዝብ ።

፴፪ ከሰው ብንለውም ሕዝቡን እንፈራቸዋለን
እስመ ኵሎሙ ከመ ነቢይ ይሬእይዎ ለዮሐንስ ።
ሁሉም ዮሐንስን እንደ ነቢይ ያዩት ነበርና ።

፴፫ ወተሰጥውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወይቤልዎ
ኢነአምር ።

፴፫ አናውቅም ብለው ለጌታ መለሱለት ።
ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፤
ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ እነኒ ኢይነግረከሙ በመባሕተ መኑ
እገብር ከመዝ ።
እኔም በማንም ሥልጣን ይህን እንዳደርግ አልነግ
ራችሁም አላቸው ።

በእንተ እኩያን ዐቀብተ ወይን

ምዕራፍ ፲፪

፩ ወእኀዘ ይመስል ሎሙ ። ኢሳ፭፥ ፩ ኤር፥
፪ ፥ ፳፩ ማቴ ፳፩ ፥ ፴፫ ሉቃ ፳ ፥ ፱ ።

፩ ይመስልላቸው ጀመረ ።
ይቤሎሙ ብእሲ ተከለ ዓጸደ ወይን ።
ሰው ወይን ተከለ ።
ወጸቆና ፤ ቅጥር ቀጠረለት ።
ወአክረየ ምክያደ ፤
መጥመቂያም አስማሰለት ።
ወሐነጸ ማኅፈደ ውስቴቱ ።
በሱም ግንብ ሠራ ።
ወሤመ ሎቱ ዓቀብተ ወነገደ ።
ጠባቂም ሹሞ ሄደ ።

፪ ወፈነወ ገብሮ ኀበ ዓቀብተ ወይን በጊዜሁ
ያምጽእ ሎቱ እምፍሬ ወይኑ ።

፪ ከወይኑም ፍሬ ያመጣለት ዘንድ ባሪያውን
በጊዜው ወደ ጠባቆች ላከ ።

፫ ወእኀዝዎ ፤
፫ ያዙት ።
ወቀሠፍዎ ፤ ገረፉት ።
ወፈነውዎ ዕራቆ ፤
ባዶውንም ሰደዱት ።

፬ ወካዕበ ፈነወ ኀቤሆሙ ካልዓኒ ገብሮ ።
፬ ደግሞ ሌላውንም ባሪያውንም ወደሰቸው ላከ።
ወኪያሁኒ ወገርዎ ፤ እሱንም ደበደቡት ።
ወኰርዕዎ ፤ መቱትም ።
ወፈነውዎ አኅሲሮሙ ፤
አዋርደውም ሰደዱት ።

፭ ወፈነወ ሣልሳዩኒ ገብሮ ፤
፭ ሦስተኛውንም ባሪያውን ላከ ፤ ሐተታ ዮሐ
ንስ መጥምቅ ነው ።
ወኪያሁኒ ቀተልዎ ፤
እሱንም ገደሉት ።
ወፈነወ ባዕዳነኒ ብዙኃነ ።
ሌሎችንም ብዙዎችን ላከ ።
ቦ ዘቀሠፉ ፤ የገረፉት አለ ።
ወቦ ዘቀተሉ ፤ የገደሉትም አለ ።

፮ ወቦቱ ፩ዱ ወልድ ዘያፈቅር ።
፮ የሚወደው አንድ ልጅም ነበረው ።
ወፈነዎ ኀቤሆሙ ድኅረ ኵሉ እንዘ ይብል የኃፍርዎ
ለወልድየሰ ።
ከሁሉ በኋላ ልጀንስ ያፍሩታል ብሎ ልጁን ላከ ።

፯ ወይቤሉ ዓቀብት ዝንቱ ውእቱ ወራሲሁ
፯ ጠባቆቹም እነሆ ወራሹ ይህ ነው ።
ንዑ ንቅትሎ ። ኑ እንግደለው ።
ወንርከብ ርስቶ ፤

ርስቱንም እንውረሰው አሉ ።

፰ ወአኃዝዎ ወአውፅእዎ አፍአ እምአፀደ ወይን ወቀተልዎ ።

፰ ይዘውም ከወይኑ ቦታ ውጭ አውጥተው ገደሉት ።

፱ ምንተ እንከ ይሬስዮሙ በዓለ ወይን ።
፱ የወይኑ ባለቤት ምን ያደርጋቸዋል ።
አኮኑ ይመጽእ ወይቀትሎሙ ለእልክቱ ዓቀብት ።
መጥቶ ጠባቆችን ይገድላቸው የለምን ።
ወይሁብ ወይኖ ለካልዓን ።
ወይኑንም ለሌላ ጠባቆች ያስጠብቃል ።

፲ ወዘኒ ኢያንበብክሙኑ ውስተ መጽሐፍ እብን እንተ ዘመነንዋ ነደቅት ይእቲ ኮነት ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ፡ መዝ ፻፲፯ ፡ ፳፪ ኢሳ ፳፰ ፡ ፲፮ ማቴ ፳፩ ፡ ፵፪ ግብ ፬ ፡ ፲፩ ሮሜ ፱ ፡ ፴፫ ፩ጴጥ ፪ ፡ ፯ ፡
፲ እናንተ የናቃችሁት ድንጊያ የማዕዘን ራስ ሆነች ያለውን መጽሐፍ አላሰባችሁምን ።
፲፩ እምኀበ እግዚአብሔር ኮነት ዛቲ ።
፲፩ ይህችም ከእግዚአብሔር ሆነች ።
ወነካር ይእቲ ለአዕይንቲነ ።
ለዓይናችንም ድንቅ ናት ።
፲፪ ወፈቀዱ የአኀዝዎ ።
፲፪ ሊይዙትም ወደዱ ።
ወፈርህዎሙ ለሕዝብ ።
ሕዝቡንም ፈሩ ።
ወአእመሩ ከመ በእንቲአሆሙ ይቤ ዘንተ እምሳለ ።
ይህንም ምሳሌ ስለርሳቸው እንደተናገረው ዐወቁ ።
ወኀደግዎ ወሖሩ ።
ትተውትም ሄዱ ።

### ዘከመ አመክርዎ ለኢየሱስ በእንተ ውሂበ ዲናር

፲፫ ወፈነዉ ኀቤሁ ፈሪሳውያን ምስለ ሰብአ ሄሮድስ ከመ ያስሕትዎ በቃሉ ። ማቴ ፳፪ ፡ ፲፭ ሉቃ፡ ፳፡ ፳ ።
፲፫ በነገሩ ሊያስቱት ፈሪሳውያን ከሄሮድስ ሰዎች ጋራ ወደሱ ላኩ ።
፲፬ ወመጽኡ ኀቤሁ ወይቤልዎ ሊቅ ነአምር ከመ ጻድቅ አንተ ።
፲፬ ወደሱም መጥተው መምር ሆይ እውነተኛ እንደሆንክ እናውቃለን ።
ወኢየኃዝነከ መኑሂ ።
ማንንም ማንን እንዳታፍር ።
ወኢታደሉ ለገጸ ሰብእ ።
ለሰው ፊትም እንዳታደላ ።
በጽድቅ ትሜህር ፍኖተ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርን መንገድ በውነት እንድታስተምር እናውቃለን ።

፲፭ ይከውንሁ ነሁብ ጸባሕተ ዲናር ለንጉሢ ።
፲፭ ለቄሣር ግብር መስጠት ይገባልን ።
እው እልቦ ።
ወይም አይገባም አሉት ።

፲፮ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ጕሕሉቶሙ ለምንት ታሜክሩኒ ።

፲፮ ጌታም ሽንገላቸውን ዐውቆባቸው ለምን ትፈትኑኛላችሁ ።
አምጽኡ ዲናረ ወእርእዩኒ ።
ዲናሩንም አምጥታችሁ አሳዩኝ አላቸው ።
፲፯ ወአምጽኡ ሎቱ ። ሮሜ ፲፫ ፡ ፯ ።
፲፯ አመጡለት ።
ወይቤሎሙ ዘመኑ መልክዑ ወመጽሐፉ ።
ጽፈቱስ መልኩስ የማነው አላቸው ።
ወይቤልዎ ዘንጉሢ ።
የቄሣር ነው አሉት ።
ሀቡ ዘንጉሢ ለንጉሢ ።
የቄሣርን ለቄሣር ስጡ ።
ወዘእግዚአብሔር ግበሩ ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር ።
ወአንከርዎ ፤ አደነቁት ።

በእንተ ሰዱቃውያን ወትንሣኤ ሙታን ።

፲፰ ወመጽኡ ኀቤሁ ሰዱቃውያን እለ ይብሉ አልቦ ትንሣኤ ሙታን ። ማቴ ፳፪፡ ፳፫ ሉቃ፡ ፳፡ ፳፯።
፲፰ የሙታን ትንሣኤ የለም የሚሉ ሰዱቃውያን ወደሱ መጡ ።
ወተስእልዎ ፤ ጠየቁት ።
፲፱ ወይቤልዎ ሊቅ ሙሴ ጸሐፈ ለነ ወለእመቦ ዘሞተ እኁሁ ወኀደገ ብእሲቶ ወአልቦቱ ውሉድ እኁሁ ያውስባ ለብእሲቱ ። ዘፀ ፳፭ ፡ ፭ ።
፲፱ ወንድሙ ልጅ ሳይወልድ ሚስቱን ትቶ የሞተ እንደሆነ ወንድሙ ሚስቱን ያግባት ።
ወያቅም ዘርዓ ለእኁሁ ።
ለወንድሙ ልጅ ይተካ ብሎ ሙሴ ጽፎልናል ።
፳ ሀለው ኀቤነ ፯ቱ አኃው ።
፳ ሰባት ወንድማማቾች ነበሩ ።
ወአውሰበ ዘይልሕቅ ብእሲተ ።
ታላቁ ሚስት አገባ ።
ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።
ልጅ ሳይወልድ ሞተ ።
፳፩ ወአውሰባ ካልዑ ።
፳፩ ሁለተኛውም አገባት ።
ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።
ልጅ ሳይወልድ ሞተ ።
ወሣልሱኒ ከማሁ ።
ሦስተኛውም እንዲሁ ።

፳፪ ወ፯ሆሙ እውሰብዋ ፤
፳፪ ሰባቱም አገቧት ።
ወኢኀደጉ ውሉደ ።
ልጅ ግን አልነበራቸውም ።
ወድኅረ ኵሎሙ ሞተት ይእቲ ብእሲት ።
ከሁሉም በኋላ ያች ሞተች ።

፳፫ ወእመሰ የሐይው ምውታን ለመኑ እምኔሆሙ ትከውኖ ብእሲተ ።

፳፫ ሙታን በተነሡ ጊዜ ለማናቸው ሚስት ትሆናለች ።
እስመ ፯ሆሙ እውሰብዋ ፤
ሰባቱም አግብተዋታልና ።

፳፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ አኮኑ በእንተ ዝንቱ ስሕትክሙ በኢያእምሮ መጻሕፍት ።
መጻሕፍትን ባለማወቅ ።
በኢኃይለ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር ኃይልንም ባለማወቅ በደላችሁ ።

፳፭ እመሰ የሐይው ምውታን ኢያወስቡ ወኢይትዋሰቡ ።

፳፭ ሙታን በተነሡ ጊዜ አያገቡም አይጋቡም።
አላ ከመ መላእክተ እግዚአብሔር ይከውኑ እሙንቱ በሰማያት ።
በሰማይ እንዳሉ መላእክት ይሆናሉ እንጂ ።

፳፮ ወከመሰ የሐይው ምውታን ኢያንበብክሙኑ በውስተ መጽሐፈ ሙሴ ዘይቤሎ እግዚአብሔር በኀበ ዕፀ ጳጦስ ዘፀ ፫ ፥ ፮ ማቴ ፳፪ ፥ ፴፪ ።

፳፮ ምውታንማ እንዲነሡ በቍጥቋጦው ዘንድ እግዚአብሔር እንደነገረው የሙሴን መጽሐፍ አላነበባችሁምን ።
እንዘ ይብል አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክከ ።
አምላክህ እግዚአብሔር እኔ ነኝ
አምላከ አብርሃም ፤
የአብርሃም አምላክ ።
ወአምላከ ይስሐቅ ፤
የይስሐቅ አምላክ ።
ወአምላከ ያዕቆብ ፤
የያዕቆብ አምላክ ።

፳፯ ኢኮነኬ አምላከ ምውታን ።
፳፯ የሙታን አምላክ አይደለም ።
አላ አምላከ ሕያዋን ውእቱ ፤
የሕያዋን አምላክ ነው እንጂ ።
ወእንትሙሰ ብዙኃ ትጌግዩ ፤
እናንተስ ብዙ ትስታላችሁ ።

በእንተ ቀዳማዊ ትእዛዝ

፳፰ ወመጽአ ፩ዱ ጸሐፊ ሰሚዖ ከመ ተኃሥሥዎ ወሶበ ርእየ ከመ ሠናየ ተሠጥዎሙ ። ማቴ ፳፪ ፥ ፴፭ ።
እንደ ተከራከሩት በሰማ ጊዜ መልካም እንደመለሰላቸው ባየ ጊዜ አንድ ጸሐፊ ወደሱ መጣ ።
ወተሰእሎ ወይቤሎ ዓይ ትእዛዝ ቀዳሚት እምኵሉ ከሁሉም የምትቀድም ትእዛዝ ማንኛይቱ ናት ብሎ ጠየቀው ።

፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
ዘዳ ፮ ፥ ፬ ።

፳፱ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ዛቲ ይእቲ ቀዳሚት እምኵሉ ትእዛዝ ።
ከትእዛዝ ሁሉ የምትቀድም ይህች ናት ።
ስማዕ እሥራኤል እግዚአብሔር አምላክከ ፩ዱ ውእቱ እግዚአብሔር ።
እሥራኤል ሆይ አምላክህ እግዚአብሔር አንድ እግዚአብሔር እንደሆነ ስማ ።

፴ ወአፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ።
፴ አምላክህ እግዚአብሔርንም በልብህ ሁሉ ውደደው ።
ወበኵሉ ነፍስከ ፥ ወበኵሉ ሕሊናከ ።
በነፍስህም ሁሉ ፥ በሕሊናህም ሁሉ ።
ወበኵሉ ኃይልከ ።
በኃይልህም ሁሉ ።
ዛቲ ይእቲ ትእዛዝ ቀዳሚት እምኵሉ ።
ከሁሉም የምትቀድም ትእዛዝ ይህች ናት ።

፴፩ ወካልዕታሂ እንተ ትመስላ አፍቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ። ዘሌ ፲፱ ፥ ፲፰ ማቴ ፳፪ ፥ ፴፱ ሮሜ ፲፫ ፥ ፱ ገላ ፭ ፥ ፲፬ ያዕ ፪ ፥ ፰ ።
፴፩ ሁለተኛይቱም የምትመስላት ባልንጀራህን እንደ ራስህ ውደድ ናት ።
ወዘየዓቢ እምእላንቱ ትእዛዛት አልቦ ።
ከነዚህ ትእዛዞች የሚበልጥ የለም ።

፴፪ ወይቤሎ ውእቱ ጸሐፊ ሠናየ ትቤ ሊቅ ።
፴፪ ያም ጸሐፊ መምህር ሆይ መልካም ተናገርኽ አለው ።
አማን ፩ዱ ውእቱ እግዚአብሔር ።
እግዚአብሔር በእውነት አንድ ነው ።
ወአልቦ ባዕድ ዘእንበሌሁ ።
ከሱም በቀር ሌላ የለም ።

፴፫ ወከመ ታፍቅሮ በኵሉ ልብከ ።
፴፫ በልብህ ሁሉ ትወደው ዘንድ ።
ወበኵሉ ነፍስከ ።
በነፍስህም ሁሉ ።
ወበኵሉ ሕሊናከ ፤ በሕሊናህም ሁሉ ።
ወበኵሉ ኃይልከ ፤ በኃይልህም ሁሉ ።

ወከመ ታፍቅር ቢጽከ ከመ ነፍስከ ።
ባልንጀራህን እንደ ራስህ ብትወድ ።
ወዝንቱ ይኄይስ እምኵሉ መባዕ ወመሥዋዕት ።
ከመሥዋዕትና ከመባዕም ሁሉ ይህ ይሻላል ።

፴፬ ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ጠቢብ ውእቱ ይቤሎ ኢኮንከ ርሑቀ እመንግሥተ እግዚ አብሔር ።

፴፬ ጌታም ብልህ እንደሆነ አይቶ ከእግዚአ ብሔር መንግሥት የራቅህ አይደለህም አለው ።
ወአልቦ እንከ ዘተሀበለ ይስአሎ ።
ከዚህም ወዲያ ሊጠይቀው የደፈረ የለም ።

በእንተ ማስያስ ወልደ ዳዊት

፴፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይሜ ህሮሙ በምኵራብ እፎ ይብሉ ጸሐፍት ወልደ ዳዊት ውእቱ ክርስቶስ ።
፴፭ ጌታም በምኵራብ ሲያስተምራቸው ጻፎች ክርስቶስ የዳዊት ልጅ ነው እንደምን ይላል ብሎ ጠየቃቸው ።
፴፮ ወለሊሁሰ ዳዊት ይቤ በመንፈስ ቅዱስ ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ እስከ አገብአሙ ለጸላእትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ። መዝ ፻፱ ፥ ፩ ማቴ ፳፪ ፥ ፵፬ ሉቃ ፳ ፥ ፵፪
፴፮ እሱ ግን ዳዊት በመንፈስ ቅዱስ ጌታ ጌታዬን ጠላቶችህን ከእግርህ መርገጫ በታች እስከ አግባቸው በቀኜ ተቀመጥ አለው ብሏል ።
፴፯ ወለሊሁ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ እፎ እንከ ይከውኖ ወልደ ።
፴፯ እሱ ዳዊት ጌታዬ ያለው እንደምን ልጁ ይሆናል ።
ወኵሎ ሕዝብ ውእቱ ያጸምዕዎ ። ማቴ ፳፫ ፥ ፩ ሉቃ ፲፩ ፥ ፵፫ ።
ሕዝቡም ሁሉ ደስ ብሏቸው ይሰሙት ነበር ።

በእንተ መደልዋን ጸሐፍት

፴፰ ወይቤሎሙ እንዘ ይሜህሮሙ ዑቁ ወተ ገኃሡ እምጸሐፍት እለ ይፈቅዱ ያንሶስው ተላቢሶሙ
፴፰ ሲያስተምራቸው ተላብሰው መመላለስን ከሚወዱ ከፈሪሳውያን ተጠበቁ ተለዩም አላቸው
ወይትአምኅዎሙ ዐምሥያጥት ።
በገበያም ምርቃትን የሚወዱ ።
፴፱ ወነቢረ ፍጽም በውስተ አዕዋዳት ።
፴፱ ባደባባይም ፊት ለፊት መቀመጥን የሚ ወዱ ።
ወርእሰ ምርፋቃት በውስተ ምስሐት ።
በምሳ ጊዜ በራስጌ መቀመጥን ።
፵ እለ ይውህጥዎሙ ለአብያተ መበለታት ።
፵ የድሆችን ቤት የሚበሉባቸው ።
ወይትሜካየኑ በነዋኅ ጸሎቶሙ ።
በረጅም ጸሎታቸውም የሚተነኰሉ ።
እሉ ይረክቡ ዘየዓቢ ኵነኔ ።
እነሀ የሚበልጥ ፍርድ ይቀበላሉ ።

በእንተ ዘከመ ወደሳ ለመበለት ነዳይት በውሂቦተ ጸሪቅ ።

፵፩ ወነቢሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ኖኅተ ምኵ ራብ እንጻረ ሙዳየ ምጽዋት ይርአይ ሰብአ ዘያበውኡ ጸሪቀ ወይወድዩ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ። ሉቃ ፳፩ ፥ ፩ ።

፵፩ መባ የሚሰጡትን በሳጥንም የሚያኖሩትን ያይ ዘንድ ጌታ በዕቃ ቤቱ አፋዛኝ ባለ በምኵራብ ደጅ ተቀምጦ ሳለ ፤
ወብዙኃን አብዕልት እለ አብኡ ብዙኃ ።
ብዙ ባለጠጎችም ብዙ አገቡ ።
፵፪ ወመጽአት አሐቲ ብእሲት ነዳይት መበለት
፵፪ አንዲት ድኃ ሴት መጣች ።
ወአብአት ፪ተ ጸሪቀ ።
ሁለት ጸራይቅም አገባች ፤
ዘይብልዎ ቆንደራጢስ ፤
ቆንደራጢስ የሚሉት ፤
ሐተታ ሁለት ጸራይቅ ያለውን አንድ አድርጎ ቆን ደራጢስ አለ ሁለቱን ተረን አንድ ቀመት ሁለቱን ቀመት አንድ ድሪም እንደማለት ፤
አንድም የሙርኙ እንጀራ አንድም ዝብስ ብርት ነው በሞረድ ሲሞርዱት ጊዜ ይረግፋል ያን ሰብስበው ለእንጀራ ይሸጡታልና ፤

፵፫ ወጸውአሙ ለአርዳኢሁ ።
፵፫ ደቀ መዛሙርቱንም ጠራቸው ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ ከመ ዛቲ ነዳይት መበለት አብዝ ኃት አብአ እምኵሎሙ እለ አብኡ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ።
በመባው ሣጥን ከጣሉ ሁሉ ይህች ሴት አብዝታ እንደሰጠች በውነት እነግራችኋለሁ ።
፵፬ እስመ ኵሎሙ እለ አብኡ እምተረፎሙ አብኡ ።
፵፬ ያቀረቡት ሁሉ ትራፊያቸውን አግብተ ዋልና ።
ወይእቲሰ እምተፅናሳ ኵሎ ዘባቲ አብአት ኵሎ መንበርታ ፤
ይህች ግን በድኅነት ሳለች ያላትን ሁሉ አገባች ።
ሐተታ እኒያ ከቤታቸው ሄደው እንደ ገና ተድላ የሚ ያደርጉ የሚበሉ የሚጠጡናቸውና ፤ እሷ ግን የሚያ የምትውል ናትና ፤ ይህች ሴት የኅጥአን ነፍስ እኒያ የጻድቃን ምሳሌ ፤ ጻድቃን ምን አለብን ብለው ተዘ ልለው ይኖራሉ ፤ የኃጥአን ነፍስ ግን አላበጀሁም ብላ በታዝን ስታለቅስ ትኖራለች ። ጻድቃን ነን ከሚሉ ከኒያ ይልቅ ኃጥእት ነን ነፍስ አብዝታ ሥራ ሠርታለች ብዬ እነግራችኋለሁ ።

በአንተ ንስተት ቤተ መቅደስ
ወኢየሩሳሌም ።

## ምዕራፍ ፲፫

፩ ወወፂአ እምኲራብ ይቤሎ ፩ዱ እምአርዳ
ኢሁ ሊቅ ርኢ ምንተ ይመስል ንድቁ ወዕበኒሁ
ማቴ፡ ፳፬ ፡ ፩ ።

፩ ከምኲራብ በወጣም ጊዜ ከደቀ መዛሙርቱ
አንዱ መምህር ሆይ ድንጊያውንና ሕንጻውን ምን
ይመስላል እየው አለው ።

፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ። ሉቃ፡፲፫ ፡ ማ፬
ሉቃ ፡ ፳፩ ፡ ፮ ።
፪ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ትሬኢኑ ዘንተ ኲሎ ንድቀ ዓቢየ ።
ይህን ታላቅ ሥራ ታያስህን ።
ኢይትኃደግ ዝየ እብን ዲበ እብን ዘኢይትነሰት ።
የማይፈርስ ሆኖ ድንጊያ በደንጊጊያ ላይ አይቀርም ።
፫ ወእንዘ ይነብር ውስተ ደብረ ዘይት አንጻረ
ምኲራብ ተስአልዎ በባሕቲቶሙ ጴጥሮስ ወያዕቆብ
ወእንድርያስ ።
፫ በደብረ ዘይት በምኲራብ አንጻር ተቀመጦ
ሳለ ያዕቆብና ጴጥሮስ እንድርያስም ለብቻቸው
ጠየቁት ።
፬ ወይቤልዎ ንግረነ ማዕዜ ይከውን ዝንቱ ።
፬ ይህስ የሚደረገው መቼ ነው ንገረን ።
ወምንት ትእምርቱ አመ ይከውን ዝንቱ ኲሉ ።
ይህስ ሁሉ በተደረገ ጊዜ ምልክቱ ምንድር ነው
አሉት ።
፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ። ኤፌ ፭ ፡ ፮
፪ ተሰ፡ ፪ ፡ ፫ ።
፭ ጌታም መለሰ ።
ወአኀዘ ይቤሎሙ ዑቁ ኢያስሕቱክሙ ።
እንዳያስቷችሁ አስተውሉ ይላቸውም ጀመረ ።
፮ እስመ ብዙኃን ይመጽኡ በስምየ እንዘ ይብሉ
አነ ውእቱ ክርስቶስ ።
፮ እኔ ክርስቶስ ነኝ እያሉ ብዙ ስዎች በኔ
ስም ይመጣሉና ።
ወያስሕትዎሙ ለብዙኃን ።
ብዙ ሰዎችንም ያስቷቸዋል ።
፯ ወአመ ሰማዕክሙ አፅባዕተ ወድምፀ ጸባዒት
ዑቁ ኢትደንግፁ ።
፯ ሰልፍና የሰልፍንም ድምፅ በሰማችሁ ጊዜ
እንዳትደነግጡ አስተውሉ ።
እስመ ሀለዎ ይኩን ዝንቱ ።
ይህ ይሆን ዘንድ አለውና ።
ወባሕቱ አኮ ሶቤሃ ዘየኃልቅ ።
ነገር ግን ያን ጊዜ የሚፈጸም አይደለም ።
፰ ወይትነሣእ ሕዝብ ዲበ ሕዝብ ።
፰ ሕዝቡም በሕዝቡ ላይ ይነሣል ።
ወነገሥት ዲበ ነገሥት ።
ነገሥት በነገሥት ላይ ።
ወይከውን ድልቅልቅ በበበሔሩ ።
በየሀገሩም መናወጥ ይሆናል ።
ወይመጽእ ረኃብ ።
ረኃብም ይመጣል ።
ወዝንቱ ቀዳሚሁ ለጻዕር ።
ይህም የጻዕር መጀመሪያ ነው ።

፱ ወአንትሙሰ ዑቁ ርእሰክሙ ።
፱ እናንተ ግን ለራሳችሁ አስተውሉ ።
ወይወስዱክሙ አዕዋዳተ ።
ወደ ዐደባባይ ይወስዷችኋል ።
ወይቀሥፉክሙ በመኳርብት ።
በምኲራብም ይገርፏችኋል ።
ወይትባጽሑክሙ ኀበ መላእክት ወነገሥት በእ
ንቲአየ ።
ስለኔ ወዳለቆችም ወደ ነገሥታትም ያደርሷችኋል ።
ከመ ይኩን ስምዓ ላዕሌሆሙ ምስክር ሊሆንባቸው ።

፲ ወለኲሎሙ አሕዛብ ያደሉ ይቀድሙ ይሰ
ብከዋ ለወንጌል ።
፲ ለአሕዛብም ሁሉ አስቀድሞ ወንጌልን ሊያ
ስተምሯቸው ይገባል ።
፲፩ ወሶበሂ ያበጽሑክሙ ኢትቅድሙ ተሐ
ልዩ ዘትብሉ ወዘትነብቡ ። ማቴ፡፲ ፡ ፲፱ ሉቃ፡
፲፪ ፡ ፲፩ ፡ ፳፩ ፡ ፲፬
፲፩ ባደረሷችሁም ጊዜ አስቀድማችሁ የምት
ናገሩትን አታስቡ ።
ዘእንበበከሙ ሶቤሃ ንቡ ።
ያን ጊዜ ያናገራችሁን ተናገሩ ።
እስመ ኢኮንክሙ አንትሙ ዘትነብቡ ።
የምትናገሩት እናንተ አይደላችሁምና ።
ዘእንበለ መንፈስ ቅዱስ ።
መንፈስ ቅዱስ ነው እንጂ ።
፲፪ ወያገብእ እኁው እኁዋሁ ለሞት ።
፲፪ ወንድም ወንድሙን ለሞት አሳልፎ ይሰ
ጠዋል ።
ወአብ ወልዶ ፤ አባትም ልጁን ።
ወውሉድ ይትነሥኡ ላዕለ አዝማዲሆሙ ።
ልጆች ባባቶቻቸው ላይ ይነሣሉ ።
ወይቀትልዎሙ ፤ ይገድሏቸዋል ።
፲፫ ወትከውኑ ጽሉአነ በኀበ ኲሉ በእንተ
ስምየ ።
፲፫ ስለኔ ስም በሁሉ ዘንድ የተጠላችሁ ትሆ
ናላችሁ ።
ወዘሰ አዝለፈ ትዕግሥተ ውእቱ ይድኅን ።
እስከ ፍጻሜ የታገሠ ግን ይድናል ።
፲፬ ወሶበ ርኢክሙ ኃጣሮ ለሙስና ዘይቤ ዳን
ኤል ነቢይ ዘይቀውም ውስተ መካን ቅዱስ ዘያነብብ
ለይለቡ ።

፲፬ ነቢዩ ዳንኤል የተናገረውን የመፍረሱን ርኩሰት ባያችሁ ጊዜ በቅዱስ ቦታ የቆመው አንባቢው ያስተውል ።
ውእተ አሚረ እለ ውስተ ይሁዳ ይጕዩ ውስተ አድባር
ያን ጊዜ በይሁዳ ያሉ ወደተራራ ይሸሹ ።

፲፭ ወዘኒ ውስተ ናኅስ ኢይረድ ውስተ ቤት ።
፲፭ በሰገነትም ያለ ወደቤት አይውረድ ።
ወኢይባእ ይንሣእ ዘኮነ እምቤት ።
ከቤቱም እንዳች ይወስድ ዘንድ አይግባ ።

፲፮ ወዘኒ ገዳመ ሀሎ ኢይትመየጥ ድኅሬሁ ከመ ይንሣእ ልብሶ ።

፲፮ በዱርም ያለ ልብሱን ይወስድ ዘንድ ወደ ኋላው አይመለስ ።

፲፯ ወባሕቱ እሌ ሎን ለፅኑሳት ወለእለ የሐፅና በውእቱ መዋዕል ።

፲፯ ነገር ግን ለፀነሱ በዚያም ወራት ለሚያ ሳድጉ ወዮላቸው ።

፲፰ ወጸልዩ ከመ ኢይኩን ጕያከሙ በክረምት።
፲፰ ሽሽታችሁም በክረምት እንዳይሆን እመ ልከቱ ።

፲፱ እስመ ይከውን ይእተ አሚረ ዐቢይ ሕማም ዘእምእመ ኮነ ዓለም ኢኮነ ከማሁ ።

፲፱ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ እንደሱ ተደርጎ የማያውቅ ታላቅ መከራ ይሆናልና ።
ወእምከመ ፈጠረ እግዚአብሔር ።
እግዚአብሔርም ከፈጠረው ፍጥረት ጀምሮ ።
ወኢይከውንሂ ፤
ከእንግዲህም ወዲህ የማይደረግ ።

፳ ወሶበ አኮ ዘአሕፀሮን እግዚአብሔር ለእማንቱ መዋዕል እምኢድኅነ ኵሉ ዘሥጋ ።

፳ እግዚአብሔርስ ዘመኑን ባያሳጥረው ሥጋ የለበሰ ሁሉ ባልዳነም ነበር ።
ወባሕቱ በእንተ ኅሩያኒሁ እለ ኃረየ እግዚአብሔር
እግዚአብሔር የሐፀራ እማንቱ መዋዕል ።
ነገር ግን እግዚአብሔር ስለ መረጣቸው እኒያ ወራ ቶች ያጥራሉ ።

፳፩ ወይእተ እሚረ እመቦ ዘይቤለከሙ ነዋ ዝየ ሁሎ ክርስቶስ ። ማቴ፡ ፳፬ ፡ ፳፫ ሉቃ ፲፯፡ ፳፫ ፳፩ ፡ ፰ ።

፳፩ ያን ጊዜም ክርስቶስ ከዚህ ነው ።
ወነዋ ከሐከ ።
ወይም ከዚያ ነው ያላችሁ ሰው ቢኖር ።
ኢትእመኑ ፤　　　　አትመኑ ።

፳፪ እስመ ይመጽኡ ሐሳውያነ መሲሕ ።
፳፪ ሐሰተኞች መሲሖች ይነሣሉና ።
ወሐሳውያን ነቢያት ።
የነቢያትም ሐሰተኞች ።

እስመ ይገብሩ ተአምረ ወመንክረ ከመ ያስሕቱ ።
ያስቱ ዘንድ ምልክትና ተአምራት ያደርጋሉ ።
ወሶበሂ ይትከሃሎሙ ለኅሩያኒሆሂ እምአስሐትዎሙ
ቢቻላቸውም የተመረጡትንም ባሳቷቸው ነበር ።

፳፫ ወአንትሙሰ ዑቁ ።
፳፫ እናንተ ግን ዕወቁ ።
ናሁ አቅደምኩ ወነገርኩክሙ ኵሎ ።
እነሆ አስቀድሞ ነገርኋችሁ ።

በእንተ ምጽዋቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው

፳፬ ወባሕቱ ይእተ አሚረ ምስለ ኵሉ ሕማም ፀሐይኒ ይጸልም ኢሳ፡ ፲፫ ፡ ፲ ሕዝ፡ ፴፪፡ ፯ ኢዩኤ፡ ፪፡ ፲
፳፬ ነገር ግን በዚያ ወራት ከዚህ ሁሉ መከራ ጋራ ፀሐይ ትጨልማለች ።
ወወርኀኒ ኢይሁብ ብርሃና ።
ጨረቃም ብርሃኑንም አይሰጥም ።

፳፭ ወከዋክብትኒ ይወድቁ እምሰማይ ።
፳፭ ከዋክብትም ከሰማይ ይወድቃሉ ።
ይትከወስ ኃይለ ሰማያት ።

የሰማያት ኃይልም ይናወጣል ።
፳፮ ወአሜሃ ይሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በደመና ምስለ ኃይል ወብዙኅ ስብሐት ።
፳፮ ያን ጊዜ ከብዙ ምስጋናና ከኃይል ጋራ በደመና ሲመጣ የሰው ልጅ ክርስቶስን ያዩታል ።
፳፯ ወይእተ አሚረ ይፌንዎሙ ለመላእክቲሁ ማቴ፡ ፳፬ ፡ ፴፩ ።
፳፯ ያን ጊዜም መላእክትን ይሰዳቸዋል ።
ወያስተጋብእሙ ለኅሩያኒሁ እም፬ቱ ነፋሳት ።
የተመረጡትን ካራቱ ነፋሳት ይሰበስቧቸዋል ።
ወእምአጽናፈ ምድር እስከ አጽናፈ ሰማይ ፤
ከምድር ዳር እስከ ሰማይ ዳርቻ ።
፳፰ ወእምበለስ አእምሩ እምሳሊሁ ።
፳፰ ምሳሌውንም በበለስ ዕወቁ ።
ወእምከመ ኮነ ዐጽቃ ድኩመ ጫፏ የለመለመ ።
ወሠረጸ ቆጽላ ።
ቅጠሏም የለመለመ እንደሆነ ይትዓወቅ ከመ እል ጸቀ ማዕረር ።
መከር እንደደረሰ ይታወቃል ።
፳፱ ወከማሁ አንትሙኒ እምከመ ርኢክሙ ዘንተ ኵሎ ከመ ኮነ ።
፳፱ እንደዚህም እናንተም ይህን ሁሉ አንዴ ተደረገ ያያችሁ እንደሆነ ።
እእምሩ ከመ በጽሐ ኅበ ኆኅት ።
ወደደጅ እንደደረሰ ዕወቁ ።
፴ አማን እብለከሙ ከመ ኢተኃልፍ ዛቲ ትውልድ ዘእንበለ ይኩን ዝንቱ ኵሉ ።
፴ ይህ ሁሉ ሳይሆን ይህች ትውልድ አታልፍም ብዬ እንዳታልፍ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፴፩ ሰማይ ወምድር የኃልፍ ።

፴፩ ሰማይና ምድር ያልፉል ።
ወቃልየሰ ኢየኃልፍ ።
ቃሌ ግን አያልፍም ።

፴፪ ወበእንተሰ ይእቲ ዕለት ወይእቲ ሰዓት አልቦ ዘየአምራ ።

፴፪ ያችን ቀን ግን ያችንም ሰዓት የሚያውቃት የለም ።
ወኢመላእክተ ሰማይ ።
በሰማይ የሚኖሩ መላእክትም ።
ወኢወልድ ፤ ልጅም ።
ዘእንበለ አብ ባሕቲቱ ።
ከአብ ብቻ በቀር ።
ዑቁ ፤ ተጠበቁ ።

፴፫ ትግሁ ወጸልዩ ። ማቴ፡ ፳፬ ፡ ፵፪ ።
፴፫ ተግታችሁ ጸልዩም ።
እስመ ኢተአምሩ ማዕዜ መዋዕለ ጊዜሁ ።
የጊዜውን ወራት መቼ እንደሆነ አታውቁምና ።

፴፬ እስመ ከመ ብእሲ ዘይነግድ ወየኃድግ ቤቶ
፴፬ ቤቱን ትቶ እንደሚሄድ ሰው ነውና ።
ወይሁቦሙ ግብሮ ለአግብርቲሁ ለለ፩ዱ እምኔሆሙ።
ከባሮቹ ላንዱም ላንዱ ሥራቸውን እንደሚሰጣቸው።
ወይኤዝዞ ለአጻዊኒ ከመ ይትጋህ ።
በረኛውንም እንዲተጋ ያዘዋል ይተጋ ዘንድ እእዝ ሮውን ያዘዋል ።

፴፭ ትግሁ እንከ ፤

፴፭ እንግዲህ ትጉ ።
እስመ ኢተአምሩ ማዕዜ ይመጽእ በዓለ ቤት ።
ባለቤት መቼ እንዲመጣ አታውቁምና ።
አመሂ ሠርከ ።
በሠርክም እንደሆነ ።
ወእመሂ መንፈቀ ሌሊት ።
በዙለ ሌሊትም እንደሆነ ።
ወእመሂ ጊዜ ይነቁ ዶሮሆ ።
ዶሮ ሲጮህም እንደሆነ ።
ወእመሂ ጸቢሐ ።
ማለዳም እንደ ሆነ ፤ ሐተታ ጠርዝና ጠርዙን ይዞ ተናገረ ።

፴፮ ኢይምጽእክሙ ግብተ ወኢይርከብክሙ እንዘ ትነውሙ ።

፴፮ ድንገት እንዳይመጣባችሁ ተኝታችሁም እንዳያገኛችሁ ።

፴፯ ወናሁ እብለክሙ ለኵልክሙ ትግሁ ።
፴፯ እነሆ ለሁላችሁም ትጉብየ እነግራችኋለሁ

ዘከመ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ይቅትልዎ ለኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፲፬

፩ ወእስከ ሰኑይ መዋዕል ይከውን ፋሲካ በዓለ ናዕት ። ማቴ፡ ፳፮ ፡ ፪ ሉቃ ፳፪ ፡ ፩ ።

፩ እስከ ሁለት ቀን ፋሲካ በዓለ ናዕትም ይሆ ናል ።
ወየኅሥሡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ይትአየንዎ ወየአኃዝዎ ወይቅትልዎ ።
የካህናት አለቆችና ጸሮች ተተንኩለው ይዘው ሊገ ሉት ይሹ ጀመር ።

፪ ወይቤሉ አኮ በበዓል ከመ ኢይትሀወኩ ሕዝብ ።

፪ ሕዝቡ እንዳይታወኩ ግን በበዓል አይደለም አሉ ።

በእንተ ዘከመ ረፈቀ በቢታንያ ለምሳሕ

፫ ወእንዘ ሀሎ ቢታንያ በቤተ ስምዖን ዘለምጽ እንዘ ይረፍቅ ። ማቴ፡ ፳፮ ፡ ፮ ዮሐ ፲፪ ፩ ።

፫ በቢታንያ በለምጻሙ በስምዖን ቤት ተቀ ምጦ ሳለ ።
መጽአት ብእሲት ።
ሴት መጣች ።
ወእምጽአት ዕፍረተ ዘአልባስጥሮስ ዘናርዱ ።
የጣፈጠ ናርዶስ የሚባል ሽቱ አመጣች ።
ቅድው ፤ ያማረ ።
ዘዕጹብ ሤጡ ፤
ዋጋው ብዙ የሆነ ። ሐተታ ማቴዎስ ዘቢረሌ ይላል ማርቆስ ዘናርዱ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም የሁለት ቀን ትምህርት የልሳን መለያየት ነው ፤ አንድም ጭቃው የቢረሌ ነውና ማቴዎስ ዘቢረሌ አለ ሥራው የናርድ ነውና ማርቆስ ዘናርዱ አለ፤አንድም ጭቃውም ሥራውም የብርሌ ነውናርዱ የሽቱ ስም ነው ።
ወእኮሰቶ ፤
ነቀነቀችው ፣ ቀላቀለችው አዋሐደችው ።
ወሶጠት ዲበ ርእሱ ፤
በራሱ ላይ አፈሰሰችው ፤
ወቦ እለ ተምዑ ፤
የተቆጡም ሰዎች ነበሩ ።

፬ ወይቤሉ ለምንት ዘመጠነዝ ኃጕል ዘዝ ዕፍረት ።

፬ የዚህ ሽቱ ይህን ያህል ጥፋት ለምንድን ነው አሉ ።

፭ እምኢተክህለኑ ይሠየጥ ዝንቱ ዕፍረት ፈድ ፋደ እምቦ ፻ት ዲናር ወይትወሀብ ለነዳያን ።

፭ ይህ ሽቱ ከሦስት መቶ ወቄት በሚበዛ ተሸጦ ለድሆች ይሰጥ ዘንድ ባልተቻለም ነበር አሉ ።
ወገሠጽዋ ፤ ገሠጹዋትም ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኅድግዋ ለብ
እሲት ወኢታሥርኅዋ ።

፮ ጌታም ተዋት አታድክሟት አለ ሠናየ ግብረ
ገብረት ላዕሌየ ።
በኔ መልካም ሥራ ሠራች ።

፯ ወለነዳያንሰ ዘልፈ ትረክብዎሙ ።

፯ ድኆችንስ ዘወትር በናንተ ዘንድ ታገኙዋ
ቸዋላችሁ ።
ወጊዜ ፈቀድክሙ ታሤንዩ ላዕሌሆሙ ።
በወደዳችሁም ጊዜ ትመጸውቷቸዋላችሁ ፤
ወኪያየሰ አኮ ዘልፈ ዘትረክቡኒ ።
እኔን ግን ዘወትር የምታገኙኝ አይደላችሁም ።

፰ ወዛቲኒ ዘባቲ ገብረት ወአቅደመት ወቀ
ብዓተኒ እንርየ ።

፰ ይህችም አስቀድማ ያደረገችውን እገሬንም
የቀባችኝን ለምቀበርበት አደረገችው ።

፱ አማን እብለክሙ ኀበ ሰበክዋ ለዛቲ ወን
ጌል ውስተ ኵሉ ዓለም ይንግሩ ዘገብረት ዛቲኒ ።

፱ ወንጌሉን በሚያስተምሩበት ይህች ሴት የሠ
ራችውን ይነግሩላታል ።
ወይዜክርዋ ፤
ያስቡታል ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ።

ዘከመ ሤጦ ይሁዳ

፲ ወይሁዳ አስቆሮታዊ ፩ዱ እም፲ቱ ወ፪ቱ
ሖረኀበ ሊቀ ካህናት ከመ ያግብኦ ሎሙ። ማቴ ፳፮፥፲፬

፲ ከሥራ ሁለቱ አንዱ የአስቆሮት ሰው የሚ
ሆን ይሁዳ አሳልፎ ሊሰጣቸው ወደ ሊቀ ካህናት
ዘንድ ሄደ ።

፲፩ ወሰሚዖሙ ተፈሥሑ ።

፲፩ በሰሙም ጊዜ ደስ አላቸው ።
ወተናገርዎ የሀብዎ ፴ ብሩረ ።
ሠላሳ ብር ሊስጡት ተነጋገሩት ።
ወፈቀደ በጽሚት ያግብኦ ሎሙ ።
በስውር አሳልፎ ሊሳጣቸውም ወደደ ።

በእንተ ደኀሪት ድራር ወአስተዳልዎት ።

፲፪ ወአመ ቀዳሚት ዕለት በዓለ መጸለት ፋሲካ
አመ ይጠብሑ ፍሥሐ ። ማቴ ፳፮ ፥ ፲፯ ሉቃ ፳፪ ፥ ፯

፲፪ በጉን በሚያርዱበት ጊዜ በመጀመሪያው
ፋሲካ በቂጣ በዓልም ።
ወይቤልዎ አርዳኢሁ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ
ለከ ፍሥሐ ትብላዕ ።
ደቀ መዛሙርቱ ፋሲካውን ትበላ ዘንድ በየት ብና
ዘጋጅልህ ትወዳለህ አሉት ።

፲፫ ወፈነወ ፪ተ እምአርዳኢሁ ወይቤሎሙ ሑሩ
ሀገረ ዘቅድሜክሙ ።

፲፫ ወደፊታችሁ ካለ አገር ሂዱ ብሎ ደቀ መዛ
ሙርቱን ላከ ።
ወትረክቡ ብእሴ ዘይጸውር ፃሕበ ማይ ፤
የውኃ ማድጋ የተሸከመ ሰው ታገኛላችሁ ።
ወትልውዎ ኀበ ቦአ ።
ወደገባበት ተከተሉት ።

፲፬ ወበልዎ ለበዓለ ቤት ይቤለከ ሊቅ አይቴኑ
ጽርሕ ኀበ እበልዕ ፍሥሐ ምስለ አርዳእየ ።

፲፬ የዚህን ቤት ባለቤት መምህር ከደቀ መዛ
ሙርቱ ጋራ ፋሲካ የምበላበት አዳራሽ ወዴት ነው
ብሎሃል በሉት ።

፲፭ ወውእቱ ያርእየክሙ ጽርሐ ዓቢየ ወንጹፈ
ወርሱየ ።

፲፭ እሱም የተጌጠና የተነጠፈ ታላቅ አዳ
ራሽ ያሳያችኋል ።
ወህየ አስተዳልዉ ለነ ፤
በዚያ አዘጋጁልን ።

፲፮ ወሖሩ አርዳኢሁ ሀገረ ። ማቴ ፳፮ ፥ ፳
ሉቃ ፳፪ ፥ ፲፫ ።

፲፮ ደቀ መዛሙሬቱም ወደ ከተማ ሄዱ ።
ወረከቡ በከመ ይቤሎሙ ።
እንደ ነገራቸው አገኙ ።
ወአስተዳለው በህየ ፍሥሐ ።
ፋሲካውንም በዚያ አዘጋጁ ።

፲፯ ወመስዮ ሖረ ምስለ ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ።

፲፯ ሲመሽ ከሥራ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱ ጋራ
ሄደ ።

ዘከመ ከሠተ ለሐዋርያት ዘያገብኦ

፲፰ ወእንዘ ይረፍቁ ወይበልዑ ይቤሎሙ እግ
ዚእ ኢየሱስ አማን እብለክሙ ፩ዱ እምኔክሙ
ዘይበልዕ ምስሌየ ያገብአኒ ። ዮሐ፲፫ ፥ ፳፩ ።

፲፰ ተቀምጠው ሲበሉ ጌታ ከናንተ አንዱ
ከኔ ጋራ የሚበላው ያሲዘኛል ብየ በውነት እነግ
ራችኋለሁ አላቸው ።

፲፱ ወአኃዙ ይቴክዙ ወየኃዝኑ ወይበሉ በበ ፩
አነኑ እንጋ ውእቱ ።

፲፱ አንዳች እኔ እሆን እያሉ ያዝኑም ጀመር ።

፳ ወአውሥአ ። መለሰ ፤

፳ ወይቤሎሙ ፩ እም ፲ ወ፪ ዘይጸብሕ ምስሌየ
ውስተ መጽብሕየ ።
በገበታ እጁን ከኔ ጋራ ወደ ወጭት የሚጠልቅ
ከሥራ ሁለቱ አንዱ ነው አላቸው ።

፳፩ ወልደ ዕጓለ እመሕያውስ የሐውር በከመ
ጽሑፍ በእንቲአሁ ። መዝ ፵ ፥ ፱ ግብ ፩ ፥ ፲፮

፳፩ የሰው ልጅ ክርስቶስ ግን ስለሱ እንደ
ተጻፈ ይሄዳል ።
ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ ዘእምኔሁ ይት
ሜጠውዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

ነገር ግን የሰው ልጅ ክርስቶስን አሳልፎ ለሚሰጠው ለዚያ ሰው ወዮለት ።
እምኀየሶ ሶበ ኢተወልደ ለውእቱ ብእሲ ።
ለዚያ ሰው ባልተወለደ በተሻለው ነበር ።

ዘከመ ሠርዓ አኰቴተ ቍርባን

፳፪ ወእንዘ ይበልዑ ነሥአ ኅብስተ ባረከ ወፈቀተ ። ማቴ ፳፮ ፣ ፳፯ ።
፳፪ ሲበሉ ኅብስቱን ይዞ ባረከ ቆረሰም ። ወወሀቦሙ ፤ ሰጣቸው ።
ወይቤሎሙ ንሥኡ ዝውእቱ ሥጋየ ።
ይህ ሥጋየ ነው ንሡ አላቸው ።
፳፫ ወነሥአ ጽዋአ፡
፳፫ ጽዋውንም ያዘ ።
ወአእኰተ ወወሀቦሙ ።
አመስግኖም ሰጣቸው
ወይቤሎሙ ንሥኡ
ንሡም አላቸው ።
ወሰትዩ እምኔሁ ኵልክሙ ፡
ሁላችሁም ከሱ ጠጡ ።
፳፬ ወይቤሎሙ ዝውእቱ ደምየ ዘሐዲስ ሥርዓት ዘይትከዓው በእንተ ብዙኃን ።
፳፬ ስለ ብዙ ሰዎች የሚፈስ የሐዲስ ሥርዓት ደሜ ይህ ነው ንሡ አላቸው ።
፳፭ አማን እብለክሙ ኢይሰቲ እምዝንቱ ፍሬ ወይን እስከ እንታክቲ ዕለት አመ እስትዮ ሐዲሰ በመንግሥተ እግዚአብሔር ፤
፳፭ በእግዚአብሔር መንግሥት ታድሼ እስከ ምጠጣበት እስከዚያች ቀን ድረስ ከዚህ ወይን ፍሬ አልጠጣም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

ዘከመ ነደግዎ ሐዋርያት ለኢየሱስ ።

፳፮ ሰቢሖሙ ወአንቢቦሙ ወጽኡ ውስተ ደብረ ዘይት ፤
፳፮ አመስግነውም ወደ ደብረ ዘይት ወጡ።
፳፯ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ኵልክሙ ትክህዱኒ በዛቲ ሌሊት። ዮሐ ፲፮ ፴፪ ዘካር ፲፫ ፯ ።
፳፯ ጌታም በዚች ሌሊት ሁላችሁ ትክዱኛላችሁ አላቸው ።
እስመ ይብል መጽሐፍ እቀትሎ ለኖላዊ ወእዘርዎን ለአባግዒሁ ።
ጠባቂውን እገድለዋለሁ በጎቹንም እበትናቸዋለሁ የሚል ጽሑፍ አለና ።
፳፰ ወእምድኅረ ተንሣእኩ እቀድመክሙ ገሊላ ፤
፳፰ ከተነሣሁም በኋላ ወደገሊላ እቀድማችኋለሁ ።
፳፱ ወይቤሎ ጴጥሮስ ለእመኒ ኵሎሙ ክህዱከ አንሰ ኢይክህደከ ።
፳፱ ጴጥሮስም ሁሉ ቢክዱህ እኔ አልክድህም አለው ።
፴ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለከ አንተ ትክህደኒ ዮም ሥልሰ በዛቲ ሌሊት ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ፪ተ ጊዜ ገ
፴ ጌታም ዶሮ ሳይጮህ ሁለት ጊዜ በዚህች ሌሊት ሦስት ጊዜ ትክህደኛለህ ብዩ በውነት እነግርሃለሁ ። ሐተታ ማቴዎስ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ አለ ፣ ማርቆስ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ክልኤ ጊዜ አለ ፣ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ዶሮው ጊዜው ሳይደርስ በተአምራት ጮኋል። ማቴዎስ የተአምራቱ ትቶ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ አለ ማርቆስ የተአምራቱን ቈጥሮ ክልኤ ጊዜ አለ ። እንድም ዶሮ መጀመሪያ ጮሆ ይዘገያል ኋላ ቀጥሎ ቀጥሎ ይጮሀል ። ማቴዎስ የመጀመሪያውን ትቶ ዶሮ ሳይጮህ አለ ። ማርቆስ የመጀመሪያውን ቈጥሮ ሁለት ጊዜ ሳይጮህ አለ ።
፴፩ ወአፈድፈደ ጴጥሮስ ተኃልፎተ ወትም ክህተ እንዘ ይብል እመኒ ምስሌከ ወኢይክህደከ ።
፴፩ ጴጥሮስም ካንተ ጋራ እሞታለሁ እንጂ አልክድህም ብሎ ነገር ማበርታትንና ትምክህትን አበዛ ።
ወከማሁ ይቤሉ ኵሎሙ ።
ሁሉም እንደሱ አሉ ።

ዘከመ ጸለየ በጌቴሴማን ።

፴፪ ወሖሩ ዐጸደ ወይን እንተ ስማ ጌቴሴማን ማቴ፡፳፮፡፴፮፡ሉቃ ፳፪፡ ፵ ።
፴፪ ጌቴሴማን የሚባል ወደ ወይን ቦታ ሄዱ ወይቤሎሙ ንበሩ ዝየ እስከ አሐውር ከሐ እጼሊ ፤ እጸልይ ዘንድ ወዲያ እስከሄድ ከዚያ ቆዩኝ አላቸው
፴፫ ወነሥኦሙ ለጴጥሮስ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ
፴፫ ያዕቆብና ጴጥሮስ ዮሐንስንም ከሱ ጋራ ወሰዳቸው ።
ወአኀዘ ይትከዝ ወይኅዝን ።
ያዝን ያቀረቅርም ጀመረ ።
፴፬ ወይቤሎሙ ተከዘት ነፍስየ እስከ ለሞት ።
፴፬ ነፍሴ እስክትሞት አዝናለችና ።
ንበሩ ዝየ፡ከዚህ ቆዩ ወትግሁ እንከ፡ትጉም አላቸው።
፴፭ ወእምዝ ተአተተ ሕቀ ወሰገደ ውስተ ምድር ወጸለየ ።
፴፭ ከዚህም በኋላ ጥቂት እልፍ ብሎ ከምድር ሰገደ ጸለየ ።
ከመ ትኅልፍ እምኔሁ ይእቲ ሰዓት ለእመ ይትከሃል ።
የሚቻል እንደሆነ ያች ሰዓት ከሱ ታልፍ ዘንድ ።
፴፮ ወይቤ አባ ወአቡየ ዙሉ ይትከሃለከ አኅልፍ እምኔየ ለዛቲ ጽዋዕ ።

፴፮ አባቴ ሆይ ሁሉ ይቻልሃል ይህችን ጽዋ ከኔ አሳልፋት አለው ።
ወባሕቱ ፈቃደ ዚአከ ይኩን ወአኮ ፈቃደ ዚአየ ።
ነገር ግን ያንተ ፈቃድ ይሁን እንጂ የኔ ፈቃድ አይደለም ።

፴፯ ወገቢአ ረከቦሙ እንዘ ይነውሙ ።
፴፯ መጥቶም ተኝተው አገኛቸው ።
ወይቤሎ ለጴጥሮስ ስምዖን ትነውምኑ ።
ጴጥሮስንም ስምዖን ሆይ ትተኛለህን አለው ።
ወኢትክልኑ ተዓግሦ አሐተ ሰዓተ ።
አንድ ሰዓት መታገሥ አይቻልህምን አለው ።

፴፰ ትግሁ ወጸልዩ ከመ ኢትባኡ ውስተ መንሱት ።

፴፰ ወደ መከራ እንዳትገቡ ትጉ ጸልዩም ።
እስመ መንፈስ ይፈቅድ ወሥጋ ይደክም ።
መንፈስ ይወዳልና ሥጋ ግን የደከመ ነው ።

፴፱ ወሖረ ካዕበ ወጸለየ ወከማሁ ከመ ይቤ ።
፴፱ ሁለተኛም ሂዶ ያኑ ብቻ ጸለየ ።
፵ ወገቢአ ካዕበ ረከቦሙ እንዘ ይነውሙ ።
፵ ዳግመኛም በተመለሰ ጊዜ ተኝተው አገኛቸው ።
እስመ ክቡዳት አዕይንቲሆሙ ወኢየአምሩ ዘይነብቡ ።
ዓይኖቻቸው ከብደው ነበርና የሚናገሩትን አያውቁም ነበርና ።

፵፩ ወመጽአ በሣልስ ወይቤሎሙ ኑሙ እንከሰ ወአዕርፉ ምዕረ ።

፵፩ በሦስተኛውም መጥቶ እንግዲህስ ተኙ አንድ ጊዜም ዕረፉ ።
እስመ ናሁ በጽሐ ጊዜሁ ።
ጊዜው ደርሷልና ።
ወናሁ ያገብእዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ውስተ እደ ኃጥአን ።
እነሆ የሰው ልጅ ክርስቶስ በኃጥአን እጅ ይያዛል ።
፵፪ ተንሥኡ ንሖር ናሁ በጽሐ ዘያገብአኒ ።
፵፪ እነሆ የሚያሲዘኝ ደርሷልና ተነሡ እንሂድ አላቸው ።

## ዘከመ አግብአ ይሁዳ ለኢየሱስ ወዘከመ አኀዝዎ ።

፵፫ ወእንዘ ይትናገሮሙ በጽሐ ይሁዳ አስቆሮታዊ ፩ዱ እም፲ቱ ወ፪ቱ ። ማቴ ፳፮ ፥ ፵፯ ሉቃ ፳፪ ፥ ፵፯ ዮሐ ፲፰ ፫ ።
፵፫ ሲነጋገራቸውም ካሥራ ሁለቱ አንዱ የአስቆሮት ሰው የሚሆን ይሁዳ ደረሰ ።
ወምስሌሁ ብዙኃን ሰብእ ምስለ መጣብሕ ወአብትር እምኀበ ሊቃነ ካህናት ወረበናት ወጸሐፍት ።
ብዙ ሰዎችም ከሱ ጋራ ሾተል ጐመድ ይዘው ከሽማግሎችና ከጸፎች ከካህናት አለቆችም መጡ ።

፵፬ ወወሀቦሙ ትእምርተ ዘያገብኦ ።
፵፬ የሚያሲዘውም ምልክት ሰጣቸው ።
ወይቤሎሙ ዘሰዓምክዎ ውእቱ አኃዝዎ ወአጽንዕዎ ወስድዎ ።
የምስመው እሱ ነውና አጽንታችሁ ይዛችሁ ውሰዱት አላቸው ።

፵፭ ወሶቤሃ መጽአ ኀቤሁ ወይቤሎ ረቢ ወሰዐሞ
፵፭ ያን ጊዜውን ወደሱ መጥቶ መምህር ሆይ ብሎ ሳመው ።

፵፮ ወሰፍሑ እደዊሆሙ ላዕሌሁ ወአኃዝዎ ።
፵፮ እጃቸውንም ዘርግተው ያዙት ።
፵፯ ወመልሐ መጥባሕቶ ፩ዱ እም እለ ምስሌሁ ይቀውሙ ።

፵፯ ከሱ ጋራ ቆመው ካሉት አንዱ ሾተሉን መዘዘ ።
ወዘበጦ ለገብረ ሊቀ ካህናት ።
የሊቀ ካህናቱንም ባሪያ መታው ።
ወመተረ እዝኖ ።
ጆሮውን ቈረጠው ።

፵፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ዘሠራቂኑ ትዴግኑኒ ወጻእክሙ ምስለ መጣብሕ ወአብትር ተአኀዙኒ ።

፵፰ እንደሌባ ልትይዙኝ ብትርና ሰይፍ ይዛችሁ ወጣችሁን አላቸው ።

፵፱ ወትሎ አሚረ ሀሎኩ ምስሌክሙ እሜህር በምኵራብ ።
ዘወትር በምኵራብ ሳስተምር ከናንተ ጋራ አልነበርኩምን ።
ወኢአኃዝክሙኒ ።
አልያዛችሁኝም ።
ወባሕቱ ከመ ይብጻሕ ዘውስተ መጻሕፍት ።
ነገር ግን በመጻሕፍት የተጻፈው ይፈጸም ዘንድ ነው ።
፶ ወኃደግዎ ኵሎሙ አርዳኢሁ ።
፶ ወጕዩ ። ማቴ ፳፮ ፥ ፶፮ ።
ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ ጥለውት ሸሹ ።
፶፩ ወተለዎ ፩ዱ ወሬዛ ዘይትአጸፍ ሰንዱነ ዕራቆ ።
፶፩ ዕርቃኑን በበፍታ የሰወረ አንድ ጕበዝ ተከተለው ።
ሐተታ፥ራሱን አርቆ ፥ አንድም ቅራፍ በፍታ የለበሰ ።
ወአኀዝዎ ወራዙት ።
ጐልማሶች ያዙት ።
፶፪ ወኃደገ ሰንዱኖ ወጐየ ዕራቆ ።
፶፪ በፍታውንም ጥሎ ሸሸ ።

## ዘከመ ቆመ ኢየሱስ በዓውድ

፶፫ ወወሰድዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ኀበ ሊቀ ካህናት ወጸሐፍት ወረበናት ። ማቴ ፳፮ ፥ ፶፯ ሉቃ ፳፪ ፥ ፶፬ ዮሐ ፲፰ ፥ ፲፫ ።

፶፫ ጌታንም ወደ ካህናት አለቃና ወደ ጸሐፎች አመጡት ።

፶፬ ወተለዎ ጴጥሮስ እምርኁቅ እስከ ውሳጤ ሊቀ ካህናት ወነበረ ምስለ ወዓልያኒሆሙ ይስኅን መንገለ በርህ ።

፶፬ ከብላቴኖቻቸው ጋራ የሳቱ ጸዳልወደ ወደ ቅበት በኩል ተቀምጦ እሳት ይሞቅ ነበር ።

፶፭ ወኃሠሡ ሊቃነ ካህናት ወኵሉ ዓውድ ስማዕተ ሐሰት ያስተዋድይዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ከመ ይቅትልዎ ። ማቴ ፳፮ ፥ ፶፱ ።

፶፭ ሊቃነ ካህናት ሸንጎውም ጌታን ይገሉት ዘንድ ሊያካስሱት ይሹት ጀመር ።
ወኃጥኡ ፤
ነውር አጡበት ።
፶፮ ወብዙኃን እለ አስተዋደይዎ ።
፶፮ ያሳጡት ብዙ ናቸው ።
ወኢኃብረ ቃሎሙ ።
ነገራቸው ግን አንድ አልሆነም ።
፶፯ ወቦ እለ ተንሥኡ ስማዕተ ሐሰት ወነበቡ ።
፶፯ በሐሰት ተነሥተው የመሰከሩም የሐሰት ምስክሮችም አሉ ።
፶፰ ወይቤሉ ንሕነ ሰማዕናሁ እንዘ ይብል አነ እነሥቶ ለዝንቱ ቤተ መቅደስ ዘእደ ገብሮ ወበሠሉስ አሐንጽ ካልዕ ዘእደ ኢገብሮ ። ዮሐ ፪ ፤ ፲፱ ።
፶፰ ይህን እጅ የሠራውን ቤተ መቅደስ አፍርሼ በሦስተኛው ቀን ሌላ እጅ ያልሠራው እሠራለሁ ሲል እኛ ሰምተነዋል አሉ ።
፶፱ ወምስለ ዝኒ ኢኃብረ ስምዖሙ ።
፶፱ ከዚህም ጋራ ምስክርነታቸው አንድ አልሆነም ዘእደ ገብሮ ዘእደ ኢገብሮ በማለት ተለያይ ተዋል ።
፷ ወተንሥአ ሊቀ ካህናት ወሐተቶ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
፷ ሊቀ ካህናቱም ቆሞ ጌታን ጠየቀው ።
ወይቤሎ እልቦኑ ዘትሠጠው እንዘ መጠነዝ ያስተ ዋድዩከ ።
ይህን ያህል ሲያሳጡህ የምትመልሰው የለህምን አለው ።
፷፩ ወአርመመ ። ዝም አለ ።

ወኢተሠጥዎ ፡ ወኢምንተኒ ፤
ምንም ምን አልመለሰለትም ።
ወካዕበ ሐተቶ ሊቀ ካህናት ሁለተኛም ሊቀ ካህናቱ ጠየቀው ።
ወይቤሎ አንተኑ ውእቱ ክርስቶስ ወልዱ ለቡሩክ ።
የተባረከው የአብ ልጅ ክርስቶስ አንተ ነህን አለው ።
፷፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፴

፷፪ ጌታም አዎን እኔነኝ አለው ።
ወትሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይነብር በየማነ ኃይል ።
የሰው ልጅ ክርስቶስን በኃይል ቀኝ ተቀምጦ ታዩ ታላችሁ ።
ወይመጽእ በደመና ሰማይ ።
በሰማይ ደመናም ይመጣል ።

፷፫ ወሰጠጠ አልባሲሁ ሊቀ ካህናት ።
፷፫ ሊቀ ካህናቱም ልብሱን ቀደደ ።
ወይቤ ምንተ እንከ ትፈቅዱ ሎቱ ስማዕተ ።
ምን ምስክር ትሹለታላችሁ ።

፷፬ ወናሁ ሰሊክሙ ስማዕክሙ ጽርፈቶ ።
፷፬ እነሆ እናንተ ስድቡን ሰምታችሁታል ።
ምንተ እንከ ትብሉ ።
እንግዲህ ምን ትላላችሁ ።
ወአግብኡ ፍትሐ ኵሎሙ
ሁሉም ፈረዱበት ።
ወይቤሉ ይቅትልዎ ።
ሞት ይገባዋልም አሉ ።
፷፭ ወአኀዙ እምውስቴቶሙ ይውርቅዎ ።
፷፭ ከሳቸውም ወገን ይተፉበትም ጀመር ።
ወጸፍዕዎ ገጾ ፤ ፊቱንም ይጸፉት ።
ወይኰርዕዎ ርእሶ ፤
ራሱንም ይመቱት ጀመር ።
ወይቤልዎ ተነበይ ለነ ክርስቶስ መኑ ውእቱ ዘጸፍዓከ ።
ክርስቶስ ሆይ የመታህ ማነው ይሉት ጀመረ ።
ወኮኑ ወዓልት ይጸፍዕዎ በሕቁሎሳልቱም መላልሰው በጥፊ መቱት ።

በእንተ ክህደተ ጴጥሮስ ።

፷፮ ወእንዘ ሀሎ ጴጥሮስ ታሕተ ውስተ ውሣጤ ዓፀድ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፷፱ ሉቃ ፳፪ ፡ ፶፭ ዮሐ ፲፰ ፡ ፲፯
፷፮ ጴጥሮስም በቅጥሩ ውስጥ ታች ተቀምጦ ሳለ ።
መጽአት አሐቲ ወለት እምእዕማተ ሊቃነ ካህናት ።
ከካህናቱ አለቆች ገረዶች አንዲቱ መጣች ።
፷፯ ወአርአየቶ ለጴጥሮስ ይስኅን ።
፷፯ ጴጥሮስን እሳት ሲሞቅ አየችው ።
ወነጸረት ፤ አስተዋለችውም ።
ወትቤሎ አንተኒ ምስለ ኢየሱስ ገሊላዊ ሀሎከ ።
አንተም ከገሊላዊ ከኢየሱስ ጋራ ነበርክ አለችው ።
፷፰ ወክህደ ወይቤላ ኢየአምር ወኢይጤይቅ ዘትብሊ ።
፷፰ አንቺ የምትዪውን አላውቀውም አላስ ተውለውም ብሎ ካደ ።
ወወፅአ አፍአ ኀበ ጸናፌ ዓፀድ ።
ከቅጥሩም ውጪ ወደ አፍአ ወጣ ።
ወነቀወ ዶርሆ ፤ ዶሮም ጮኸ ።

፷፱ ወርእየቶ ካዕበ ካልእት ወለት ማቴ ፳፮ ፡ ፸፩
፷፱ ዳግመኛ ሌላይቱ ገረድ አየችው ።
ወትቤሎሙ ለዕለ ይቀውሙ ሀየ ዝንቱኒ እምኔሆሙ ውእቱ ።
ከዚያ ቆመው ላሉት ይህም ከሳቸው ወገን ነው አለቻቸው ።

፸ ወክህደ ካዕበ ። ሉቃ ፳፪ ፡ ፶፱ ዮሐ ፲፰ ፡ ፳፭ ።

፸ ሁለተኛ ካደ ።
ወእምድኅረ ሕቀ ካዕበ ይቤልዎ ለጴጥሮስ እለ ይቀውሙ አማን እምኔሆሙ አንተ ።
ጥቂትም ቆይቶ ቆመው ያሉት ሁለተኛ ጴጥሮስን አንተም በእውነት ከሳቸው ወገን ነህ አሉት ።
ወገሊላዊ አንተ ፤ የገሊላም ሰው ነህ ።
ወቃልከ የዓውቀከ ፤
ነገርህም ያስታውቃል ።
፸፩ ወአኀዘ ይትረገም ወይምሀል ።
፸፩ ይምል ይረገምም ጀመር ።
ከመ ኢየአምሮ ለውእቱ ብእሲ ዘትብሉ ።
ያን የምትሉትን ሰው እንዳላውቀው ብሎ ።
፸፪ ወሶቤሃ ነቀወ ካዕበ ዶርሆ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፸፭ ዮሐ ፲፰ ፡ ፳፯ ።
፸፪ ያን ጊዜም ዶሮ ሁለተኛ ጮኸ ።
ወተዘከረ ጴጥሮስ ቃሎ ለእግዚእ ኢየሱስ ዘይቤሎ ሠልሰ ትክህደኒ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ፪ኤ ጊዜ ወበከየ ።
ጴጥሮስም ጌታ ዶሮ ሁለት ጊዜ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ያለውን ቃል አስቦ አለቀሰ ። ማቴዎስ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ይላል ፡ ማርቆስ ሁለት ጊዜ አለ እንደምነው አይለያይም ቢሉ አይለያይም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው አልጮኸም ፡ ማርቆስ ግን ሁለት አለ ማለቱ ማታ በተአምራት ያለጊዜው ጮሆ ነበርና ሁለተኛ ሳይጮህ ሲል ነው ። አንድም ዶሮ መጀመሪያአንድጊዜ ጮሆ ይዘገያል ኋላ ተጥሎ ቀጥሎ ይጮሃል ፤ ማቴዎስ የመጀመሪያውን ትቶ ዶሮ ሳይጮህ አለ ፤ ማርቆስ የመጀመሪያውን ቈጥሮ ሁለተኛ ሲጮህ አለ ።

ዘከመ አቀምዎ ለኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ።

## ምዕራፍ ፲፭

፩ ወሶቤሃ ጸቢሖ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ወረበናት ወጸሐፍት ሕዝብ ወኵሉ ዓውድ፡ማቴ ፳፯፡፩ ሉቃ ፳፫ ፡ ፩ ዮሐ ፲፰ ፡ ፳፰ ።

፩ በነጋም ጊዜ ሽማግሎችና የካህናት አለቆች የሕዝቡም ጸፎች ሸንጎውም ሁሉ ተማከሩ ።
ወሐመድዎ ለኢየሱስ ።
ኢየሱስንም አሠሩት ።
ወወሰድዎ ወመጠውዎ ለጲላጦስ ።
ወሰደውም ለጲላጦስ ሰጡት ።

፪ ወተስእሎ ለጲላጦስ ።
፪ ጲላጦስም ጠየቀው ።
ወይቤሎ አንተኑ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሣቸው አንተን ነህ አለው ።

፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ። ማቴ ፳፯፡፲፩። ሉቃ ፳፫ ፡ ፪ ዮሐ ፲፰ ፡ ፴፫ ።

፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ አንተ ትብል ።
አንተ ትላለህ አለው ።
ወአስተዋደይዎ ሊቃነ ካህናት ብዙኀ ።
የካህናት አለቆችም ብዙ አሳጡት ።
ወውእቱሰ አልቦ ዘአውሥአ ።
እሱ ግን ምንም ምን የመለሰው የለም ።

፬ ወሐተቶ ካዕበ ጲላጦስ ።
፬ ጲላጦስም ሁለተኛ መረመረው ።
ወይቤሎ አልቦኑ ዘትሰጠው እንዘ መጠነዝ ያስተዋድዩከ ።
ይህን ያህል ሲያሳጡህ የምትመልሰው የለህምን አለው ።
፭ ወኢተሰጥዎ እግዚእ ኢየሱስ ወኢምንተኒ
፭ ጌታ ግን ምንም ምን አልመለሰለትም ።
እስከ አንከሮ ጲላጦስ ።
ጲላጦስ እስኪያደንቀው ድረስ ።
ዘከመ አስተዳኀርዎ ለኢየሱስ እምነ በርባን ።
፮ ወሰሰበዓል የሐዩ ሎሙ አሐደ እምነ ሙቁሐን ዘአብደሩ ።
፮ በበዓል በበዓል ከእስሮች የወደዱትን አንድ አንድ ያድንላቸው ነበር ።
፯ ወሀሎ ፩ዱ ዘስሙ በርባን ሙቁሕ ምስለ እለ ሐከክ ወምስለ ቀተልተ ነፍስ ።
፯ ከነፍስ ገዳዮችና ከሽፍቶች ጋራ የታሰረ በርባን የሚሉት አንድ ሰው ነበር ።
፰ ወጸርሑ ሕዝብ ወከልሑ ወሰአሉ ይግበር በከመ ያለምድ ።
፰ እንዳለመደ ያደርግላቸው ዘንድ ጮኸው አስምተው ለመኑ ።
፱ ወአውሥአ ጲላጦስ ።
፱ ጲላጦስም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ትፈቅዱኑ አሕይዎ ለከሙ ለንጉሠ አይሁድ ።
የአይሁድን ንጉሥ ላድንላችሁ ትወዳላችሁን አላቸው ።
፲ እስመ የአምሮሙ ከመ በቅንዓቶሙ አግብእዎ ሊቃነ ካህናት ።
የካህናት አለቆች በቅናታቸው አሳልፈው እንደ ሰጡት ያውቃልና ።

፲፩ ወሊቃነ ካህናትሰ ሆከምዎሙ ለሕዝብ ከመ በርባንሃ ይስአሉ ያሕዩ ሎሙ ።

፲፩ የካህናት አለቆች ግን በርባንን ያድንላቸው ዘንድ እንዲለምኑ ሕዝቡን አነሣሡቸው ።

፲፪ ወካዕበ አውሥአ ጲላጦስ ። ማቴ ፳፯ ፣ ፳፪ ሉቃ ፳፫ ፣ ፲፰ ።

፲፪ ጲላጦስም ሁለተኛ ተናገረ ።
ወይቤሎሙ ምንተ እንከ ትፈቅዱ እረስዮ ለዘተብህለ ንጉሠ አይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሥ የተባለውን ምን ላድርገው ትወዳላችሁ አላቸው ።

፲፫ ወካዕበ ከልሑ ወይቤሉ ስቅሎ ።
፲፫ ዳግመኛም ስቀለው ብለው ጮሁ ።
፲፬ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ምንተ እኩየ ገብረ ።

፲፬ ጲላጦስም ምን ክፉ ሥራ ሠራ አላቸው ።
ወፈድፋደ ጸርሑ ወይቤሉ ስቅሎ ።
ስቀለው ብለው አብዝተው ጮሁ ።

፲፭ ወመከረ ጲላጦስ ይግበር ፈቃዶሙ ለሕዝብ ።

፲፭ ጲላጦስም የሕዝቡን ፈቃድ ሊያደርግ ወደደ ።
ወአሕየወ ሎሙ በርባንሃ ።
በርባንንም አዳነላቸው ።
ወቀሠፎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወወሀቦሙ ይስቅልዎ ።
ጌታንም ገርፎ ሊሰቅሉት ሰጣቸው ።

ዘከመ ተሣለቁ ላዕለ ኢየሱስ

፲፮ ወአብእዎ ሐራ ውሳጤ ዐጸድ ኀበ ምኵናን ። ማቴ ፳፯ ፣ ፳፯ ዮሐ ፲፱ ፣ ፪ ።

፲፮ ጭፍሮች ወደ ፍርድ ዐደባባይ አገቡት ።
ወጸውዑ ኵሎ ሠገራተ ሰጲራ
ሰጲራ የሚባለውን ጭፍራ ጠሩ ።

፲፯ ወአልበስዎ ሜላተ ።
፲፯ ነጭ ሐርም አለበሱት ።
ወጸፈሩ አክሊለ ዘሦክ ወአስተቀጸልዎ ።
የሾህ አክሊል ታተው ደፋለት ።
ወይሳለቅዎ ፤ ዘበቱበት ።

፲፰ ወይቤልዎ በሐ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
፲፰ የአይሁድ ንጉሣቸው ሆይ ደህንነት ላንት ይሁን አሉት ።
፲፱ ወይኰርዕዎ ርእሶ በሀለት ።
፲፱ ራሱንም በዘንግ መቱት ይመቱት ነበር ።
ወይወርቅዎ ፤ ይተፉበትም ነበር ።
ወያስተበርኩ ወይሰግዱ ሎቱ ።
ተንበርክከውም ይሰግዱለት ነበር ።

ዘከመ አጽርዎ መስቀሎ

፳ ወሶበ ተሣለቁ ላዕሌሁ ሰለብዎ ውእተ ሜላተ ወአልበስዎ አልባሲሁ ።

፳ ከዘበቱበትም በኋላ ያን ነጭ ሐር ገፈው ልብሱን አለበሱት ።
ወወሰድዎ ኀበ ይሰቅልዎ ።
ወደሚሰቅሉትም ቦታ ወሰዱት ።

፳፩ ወአበጡ ፩ደ ኃላፌ ፍኖት ስምዖንሃ ቀሬናዌ እትወቶ እምሐቅል ። ማቴ ፳፯ ፣ ፴፪ ። ሉቃ ፳፫ ፣ ፳፮ ።

፳፩ ከዱር ሲገባ ከመንገደኞች አንዱን ከቀራንዮ ሰው ስምዖንን ጕተቱት ።
ወውእቱ አቡሆሙ ለእለ እስክንድሮስ ወለሮፎስ ።
እሱም የሮፎስና የእስክንድሮስ አባት ነው ።
ከመ ይጹር መስቀሎ ።
መስቀሉን ሊሸከም ።

፳፪ ወወሰድዎ ብሔረ ጎልጎታ ዘበትርጓሜሁ ይብልዎ መካነ ቀራንዮ ።

፳፪ በትርጓሜው የራስ ቅል ቦታ ወደሚሉት ወደ ጎልጎታ ወሰዱት ።

፳፫ ወወሀብዎ ይስተይ ወይነ ምሱለ ከርቤ ቱሱሕ ።

፳፫ ከከርቤ ጋራ የተቀላቀለ ወይን ይጠጣ ዘንድ ሰጡት ።
ወአበየ ሰትዮ ፤ አልጠጣም አለ ።

ዘከመ ተሰቅለ ኢየሱስ

፳፬ ወሰቀልዎ
፳፬ ሰቀሉትም ።
ወተአፀው ዲበ አልባሲሁ ።
ማቴ ፳፯ ፣ ፴፭ ። ሉቃ ፳፫ ፣ ፴፬ ። ዮሐ ፲፱ ፣ ፳፫ ።
በልብሱም ዕፃ ተጣጣሉ ።
ወተካፈሉ ዘከመ ይነሥኡ ።
እንደደረሳቸውም ተካፈሉ ።

፳፭ ወ፫ቱ ሰዓት ጊዜ ይሰቅልዎ ።
፳፭ በሰቀሉት ጊዜ ፫ት ሰዓት ነበረ ።
ሐተታ ፣ ማቴዎስ ቀትር ይላል ፣ ማርቆስ ሠለስት አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ፣ ማቴዎስ በንኡስ ቈጥር ቀትር አለ ፣ ማርቆስ በዓቢይ ቈጥሮ ሠለስት አለ ፤ አንድም ሁሉም በንኡስ ቈጥረዋል ፣ የማቴዎስ አይለወጥም ፣ ማርቆስ ቀትሩን ብቻ በንኡስ ቈጥሮ ።
አንድም መስቀሉን በሠለስት አዘጋጅተዋል በቀትር ሰቅለውታል ያዘጋጁበትን ሲያይ ማርቆስ ሠለስት አለ ፤ የሰቀሉበትን ሲያይ ማቴዎስ ቀትር አለ ።
፳፮ ወይብል መጽሐፈ ጌጋዩ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።

፵፪ ዓርብ ሲመሽ ያን ጊዜም የሰንበት መግ ቢያ ነበር ።

፵፫ መጽአ ዮሴፍ እምአርማትያስ ብእሲ ኄር ።
፵፫ ከአርማትያስ ዮሴፍ የሚባል ደግ ሰው መጣ
ወጠቢብ ብልሕ ነበር ።
ወውእቱ ይሴፎ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
እሱም የእግዚአብሔርን መንግሥት ተስፋ ያደርግ ነበር ።
ወተሀበለ ወቦአ ኀበ ጲላጦስ ወሰአለ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ወደ ጲላጦስም ደፍሮ ገብቶ የጌታን ሥጋ ለመነ ።

፵፬ ወአንከረ ጲላጦስ እፎ ሞተ ።
፵፬ ጲላጦስም እንዴት ሞተ ብሎ አደነቀ ።
ወጸውዖ ለሐራዊ ።
ወይቤሎ ወድዓኑ ሞተ ።
የጭፍራውንም አለቃ ጠርቶ ፈጽሞ ሞቷል አለው ።
ወይቤ እወ ሞተ ።
አዎን ሞተ አለው ።

፵፭ ወአእሚሮ በኀበ ሐራዊ ከመ ሞተ አዘዘ ይጸግዎ ለዮሴፍ ሥጋሁ ።

፵፭ እንደሞተም ከጭፍራው አለቃ በተረዳ ጊዜ ሥጋውን ለዮሴፍ ይሰጠው ዘንድ አዘዘ ሐተታ ጲላጦስ ሞተ ብሎ ጠየቀሁ ፤ እወ ሞተ ፤ አዎን ሞተ አለው ። እፎ ሞተ እንዴት ሞተ አለው ። ከመ ከመዝ ግዒሮ ሞተ ። ዓለሙን እንዲህ በታምራት አስጨን ቆት አስጠብቦት ሞተ አለው መሞቱን ዐውቆ ለዮ ሴፍ አውርድ አለው ። አንድም ሐራዊ ሞተ ብሎ ነገረው ። ጲላጦስ ወድአኑ ሞተ ፤ ፈጽሞ ሞተን አለው ። እወ ሞተ ፤ አዎን ሞተ አለው ። ጲላጦስ እንዴት ሞተ ብሎ አድንቆ አውርድ ብሎ አሰናበተው
፵፮ ወተሣየጠ ዮሴፍ ሰንዱናተ
፵፮ ፀፍታም ገዛ ።
ወአውረዶ ወገነዞ በሰንዱናት ።
አውርዶም በፀፍታ ገነዘው ።
ወቀበሮ ውስተ መቃብር ሐዲስ ዘአውቀረ ውስተ ኰኵሕ ባስጠረበውም ደንጊያ ውስጥ ቀበረው ።
ወአንኰርኰረ እብነ ውስተ አፈ መቃብር ።
ደንጊያውንም ከመቃብሩ አፍ ገጠመ ።
፵፯ ማርያም መግደላዊት ወማርያም እመ ዮሳ ርእያ ኀበ ቀበርዎ ።
፵፯ የዮሳ እናት ማርያምና ማርያም መግደላዊት የቀበሩበትን ቦታ ያዩ ነበር ።

በእንተ ትንሣኤሁ ለኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፲፮ ።

፩ ወሶበ ኃለፈት ሰንበት ማርያም መግደላዊት ወማርያም እመ ያዕቆብ ወሰሎሜ ተሣየጣ አፈወ ከመ ይምጽአ ወይቅብዓ ሥጋሁ ፤ ማቴ. ፳፰ ፥ ፩ ። ሉቃ. ፳ ፥ ፩ ። ዮሐ. ፳ ፥ ፩ ።

፩ ሰንበት ባለፈች ጊዜም የያዕቆብ እናት ማር ያምና የመግደላዊቱ ማርያም ሰሎሜም መጥተው ሥጋውን ይቀቡ ዘንድ ሽቱ ገዙ ።

፪ ወሐራ ወእንግሐ ጥቀ ሐዊረ ኀበ መቃብር በእሑድ ሰንበት ።

፪ በመጀመሪያውም ሰንበት ፈጽሞ ማልደው ወደመቃብር ሄዱ ።

፫ ወሶበ ሠረቀ ፀሐይ ይቤላ በበይናቲሆሙ መኑ ይከሥታ ለነ ለእብን እምኆኅተ መቃብር ።
፫ ፀሐይ በወጣች ጊዜም ደንጊያውን ከመቃ ብሩ አፍ ማን ያንሣልናል አሉ ። ሐተታ ደርሰዋል ቢሉ ማን ያንሣልን አልደረሱም ቢሉ ማን ያነ ሣልናል አሉ ።
፬ ወረዊዮን ርእያሁ ለእብን ኀበ አንኰርኰረት ።
፬ ፈጥነውም ሄደው ደንጊያይቱን ተገልብጣ አዩዋት ።
ወዓባይ ይእቲ ጥቀ ፤
እጅግም ታላቅ ነበረች ።
፭ ወበዊኦን ውስተ መቃብር ረከባ ፩ደ ወሬዛ እንዘ ይነብር መንገለ የማን ። ማቴ. ፳፰ ፥ ፩ ። ሉቃ. ፳፬ ፥ ፬ ። ዮሐ ፳ ፥ ፲፪ ።
፭ ወደ መቃብር በገቡም ጊዜ አንድ ጉልማሳ በቀኝ በኩል ተቀምጦ አዩ ።
ወይለብስ አልባሰ ንጹሐ ፤
ነጭ መጎናጠፊያ ለብሶ ።
ወደንገፃ ። ደነገጡም ።
፮ ወይቤሎን መልአክ ኢትደንግፃ ።
፮ አትደንግጡ አላቸው ።
ኢየሱስሃኑ ናዝራዌ ዘተሰቅለ ተኀሥሣ ።
የተሰቀለውን የናዝሬቱን ኢየሱስን ትሻላችሁን ።
ተንሥአ ። ተነሣ ።
ወኢሀሎ ዝየ ። ከዚህስ የለም ወናሁ መካኑ ኀበ ተቀብረ ። እነሆ የተቀበረበት ቦታ ፤
፯ ወባሕቱ ሑራ ንግራሆሙ ለአርዳኢሁ ወለ ጴጥሮስ ከመ ይቀድሞሙ ገሊላ ።
ማር. ፲፬ ፥ ፳፰ ።
፯ ወደገሊላ እንዲቀድማቸው ሂዳችሁ ለጴጥ ሮስና ለደቀ መዛሙርቱ ንገሯቸው ።
ወበህየ ይሬእይዎ በከመ ይቤሎሙ ።
እንደ ነገራቸው በዚያ ያዩታል ፤
፰ ወወፅአ እምነ መቃብር ወጐያ ከመቃብር ወጥተው ሸሹ ፤
፰ እስመ አኀዞን ረዓድ ወድንጋጼ ፤
ድንጋጤና መንቀጥቀጥም ይዟቸው ነበርና ፤
ወኢነገራ ወኢለመኑሂ ።

[illegible] ለማን አልተናገሩም እስመ ፈርሃ ።
ፈርተዋልና ።
[illegible] ዘአዘዛ ለጴጥሮስ ወለእሊአሁ ፈጺሞን
[illegible] ።
[illegible] ብሎ ያዘዘውን ለጴጥሮስ ለወንድሞቹ ነገረው
[illegible] ኋላ ። አንድም ዘአዘዞሙ ለጴጥሮስ ወለ
[illegible] ንገሩ ብሎ ያዘዛ
[illegible] ነገረው [illegible] ኋላ አስተርአዮሙ እግዚ
[illegible] ።
[illegible] ኋላ ታያቸው ።
[illegible] እስከ ዓረብ
[illegible] ለመድ
[illegible]
[illegible]
[illegible] ማለት [illegible] ማለን [illegible]
[illegible] ።

[illegible] አስተርአየ ኢየሱስ ለ[illegible] ።

፱ [illegible] በጽባሕ በእሑድ ሰንበት አስተር
እያ ቅድመ ለማርያም መግደላዊት እንተ እምኔሃ
አውፅአ ሰብዓተ አጋንንተ ። ዮሐ· ፳ ፣ ፲፮ ።

፱ በመጀመሪያው ሰንበት ተነሥቶም ሰባት
አጋንንት ላወጣላት ለማርያም በመጀመሪያ ታያት
ሐተታ ፤ መልክ መልካም ተወዳጅ እኅት ነበረቻት
ወዲህ ወላድ ወዲህ መወደድ ያላት በዚህ ሁሉ ምቀ
ኝነት አድሮባታል ወዲህ መውለድ ወዲህ መወደድ
እያለች በዚህ ምክንያት ሰባት አጋንንት አድረው
ባት ነበር መንፈስ ትዕቢት መንፈስ ፅርፈት ማለት
ስድብ ፣ መንፈስ ቅንዓት መንፈስ ትውዝፍት ማለት
የምንዝር ጌጥ መንፈስ ዝሙት መንፈስ ሐሜት መን
ፈስ ሐሰት ።

፲ ወይእቲ ሖረት ዜነወቶሙ ለእለ ምስሌሁ
ሀለዉ ቀዲሙ እንዘ ይበክዩ ወይላሁ ።

፲ እሷም ሄዳ አስቀድሞ ከሱ ጋራ ሲያለቅሱ
ለነበሩ ነገረቻቸው ።

፲፩ ወእሙንቱሂ ሶበ ሰምዑ ከመ አስተርአያ
ወሕያው ውእቱ ወኢአምንዋ ።
፲፩ እሳቸውም እንደታያት ሕያውም እንደሆን
በሰሙ ጊዜ አላመኑዋትም ።
፲፪ ወእምዝ አስተርአዮሙ ለ፪ቱ እምኔሆሙ
በካልዕ ራዕይ እንዘ የሐውሩ ሐቅለ ። ሉቃ·፳፬፣፲፫ ።
፲፪ ከዚህም በኋላ ከሳቸው ወገን ለሁለቱ
በበረሃ ሲሄዱ ሌላ መስሎ ታያቸው ።
፲፫ ወሖሩ እሙንቱሂ ወዜነዎሙ ለቢጾሙ ።
፲፫ እሳቸውም ሄደው ለባልንጀሮቻቸው ነገሯ
ቸው ።
[illegible]ሙኒ ኢአምንዎሙ
እሳቸውንም አላመኑዋቸውም ።

፲፬ ወእምድኅረዝ ካዕበ እንዘ ይረፍቁ ፲ወ፩ዱ
አስተርአዮሙ
፲፬ ከዚህ በኋላ ዐሥራ አንዱ ተቀምጠው ሲበሉ
ታያቸው ።
ወገሠጾሙ በእንተ ሕጸጸ አሚኖቶሙ ወጽንአ ልቦሙ
ስለ ሃይማኖታቸውም መጉደል ስለ ልቡናቸውም
ጽናት ገሠጻቸው ። አንድም ወግዕዘ ጽንዓ ልቦሙ
ይላል ። የልቡናቸውን ጽናት ነቀፈ ።
እስመ ለእለ ርእይዎ ከመ ተንሥአ ኢአምንዎሙ ።
እንደ ተነሣ ያዩትን አላመኑዋቸውምና ።

ዘከመ ፈነዎሙ ኢየሱስ ለሐዋርያት ።

፲፭ ወይቤሎሙ ሑሩ ወስብኩ ውስተ ኵሉ
ዓለም ወስብኩ ወንጌለ ለኵሉ ፍጥረት ።

፲፭ ወደ ዓለም ሁሉ ሂዱ ወንጌልንም ለሰው
ሁሉ አስተምሩ አላቸው ።

፲፮ ዘአምነ ወዘተጠምቀ ይድኅን ።
፲፮ ያመነም የተጠመቀም ይድናል ወዘሰ ኢአ
ምነ ይደየን ።
ያላመነ ግን ይፈረድበታል ።

፲፯ ወዛቲ ተእምር ለእለ አምኑ በስምየ ትትል
ዎሙ ። ግብ· ፲፯ ፣ ፲፰ ። ፪፥፬ ። ፲ ፣ ፵፩ ፣ ፲፰ ።

፲፯ ይህች ታምራት በስሜ ያመኑትን ትከተላ
ቸዋለች ።
በስመ ዚአየ አጋንንተ ያወፅኡ ።
በኔ ስም አጋንንትን ያወጣሉ ወበካልዕ ልሳን ይት
ናገሩ ሐዲሳተ ።
በሌላ ቋንቋ አዲስ ነገር ይናገራሉ ።

፲፰ ወአራዊተ ምድር ይእኀዙ በእደዊሆሙ ።
ሉቃ ፳፬ ፣ ፲፩ ።

፲፰ አባብ ይይዛሉ ።
ወኢይነክዮሙ ።
ጉዳት አያገኛቸውም ።
ወዘሂ ይቀትል ለእመ በልዑ ወሰትዩ አልቦ ዘየኃሥ
ሞሙ የሚገል ነገርም ቢበሉ ቢጠጡም የሚያገኛ
ቸው ጉዳት የለውም ።
ወዲበ ዱያን እደዊሆሙ ያነብሩ ወይሔይኑ ።
እጃቸውን በበሽተኞች ላይ ይቃጣሉ ያኖራሉም ።
ወእሙንቱሂ ይትፌወሱ ።
እነሳቸውም ይፈወሳሉ ።

በእንተ ዕርገቱ ለኢየሱስ ።

፲፱ ወእግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እምድኅረ
ተናገሮሙ ዓርገ ውስተ ሰማይ ።

፲፱ ጌታ ግን ይህን ካስተማራቸው በኋላ ወደ
ሰማይ ዓረገ ።
ወነበረ በየማነ አቡሁ ።
ባባቱም ቀኝ ተቀመጠ ማለት ባባቱም ዕሪና ኖረ ።

፳ ወወፂኦሙ እሙንቱ ሰበኩ በኵለሄ ።

፳ እሳቸውም ወጥተው በሥፍራው ሁሉ አስተማሩ ።

እንዘ እግዚእ ይረድእ ።

ጌታ እየረዳቸው ።

ወቃሎ ያጸንዕ በተእምር ዘይተሉ ።

ሕጉ ወንጌልንም ቀጥሎ ቀጥሎ በሚደረግ ተአምራት እያስረዳላቸው ።

መልእ ጽሒፈተ ብሥራቱ ለማርቆስ ሐዋርያ ፭ዱ እም ፸ወ ፪ቱ አርድእት ።

ከሰባ ሁለቱ አርድእት አንዱ ማርቆስ የጻፈው ወንጌል ደረሰ ተፈጸመ ።

ወኮነ ጽሒፎ በሀገረ ሮሜ በልሳነ ሮም ዘአፍርንጊ ። በሮማይስጥ ቋንቋ በሮም ሀገር የጻፈው ። ብዙ ሮም አለና ከዚያ ሲለይ ዘአፍርንጊ አለ ። ቤተ ኢየሱስ ቤተ ፈረንሲስ እንዲባል እምድኅረ ዕርገቱ ለእግዚእነ በ፲ወ፩ ዓመት ።

ጌታ ካረገ በኋላ ባሥራ አንድ ዓመት ።

ወበራብዕት ዓመተ መንግሥቱ ለቀላውዴዎስ ቄሣር ቀላውዴዎስ ቄሣር በነገሠ ባራተኛው ዓመት የጻፈው ወስብሐት ለእግዚአብሔር ። እስጀምሮ ላስፈጸመን ለእግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይግባው ።

ኍልቈ ምዕራፍ ዓቢይ ዘወንጌለ ማርቆስ ።

የማርቆስ ወንጌል ዓቢይ ምዕራፍ ቍጥር ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ምዕራፍ | ፩ ። | ቀዳሚሁ ለወንጌለ ኢየሱስ ክርስቶስ | የወንጌል መጀመሪያ ። |
| ም | ፪ ። | ወቦአ ካዕበ ሀገረ ቅፍርናሆም ። | ዳግመኛ ወደቅፍርናሆም ገባ ። |
| ም | ፫ ። | ወቦአ ካዕበ ምኵራበ ። | ዳግመኛ ወደ ምኵራብ ገባ ። |
| ም | ፬ ። | ወአኀዘ ካዕበ ይምሀሮሙ ። | ዳግመኛ ያስተምር ጀመረ ። |
| ም | ፭ ። | ወበጽሑ ማዕዶተ ባሕር ኀበ ብሔረ ጌርጌሴኖን ። | ጌርጌሴኖን ባሕር ማዶ ደረሱ ። |
| ም | ፮ | ወወፂአ እምህየ ቦአ ሀገሮ ። | ከዚያ ወጥቶ አገሩን ገባ ። |
| ም | ፯ | ወተጋብኡ ኀቤሁ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን | ጸሐፍት ፈሪሳውያን ወደሱ ተሰበሰቡ ። |
| ም | ፰ ። | ወይእተ አሚረ ካዕበ ብዙኀ ሰብእ ። | በዚያ ወራት ብዙ ሰው ነበረ ። |
| ም | ፱ ። | ወእመ ሰዱስ ዕለት ነሥአሙ ። | በስድስተኛው ቀን ወሰዳቸው ። |
| ም | ፲ ። | ወተንሥአ ሖረ እምህየ ። | ከዚያ ተነሥቶ ሔደ ። |
| ም | ፲፩ ። | ወአልጺቆሙ ለኢየሩሳሌም ቤተ ፋጌ | ኢየሩሳሌም በደረሱ ጊዜ ። |
| ም | ፲፪ ። | ወአኀዘ ይመስል ሎሙ ። | ይመስልላቸው ጀመረ ። |
| ም | ፲፫ ። | ወወፂአ እምኵራብ ። | ከምኵራብ በወጣ ጊዜ ። |
| ም | ፲፬ ። | ወእስከ ሰኑይ መዋዕል ። | እስከ ሁለት ቀን ። |
| ም | ፲፭ ። | ወሶበ ጸብሐ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ። | በነጋ ጊዜ የካህናት አለቆች መከሩ ። |
| ም | ፲፮ ። | ወኀለፈት ሰንበት ። | ሰንበት ካለፈች በኋላ ። |

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌለ ማርቆስ ። | | የማርቆስ ወንጌል አርእስት ማውጫ |
|---|---|---|
| ዘእንተ ስብከተ ዮሐንስ መጥምቅ ። | ምዕራፍ ፩ ቍጥር ፩ | ዮሐንስ መጥምቅ እንደ አስተማረ ። |
| ዘእንተ ጥምቀት ወተመክሮት ዘኢየሱስ ። | ቍ ፱ | ስለ ጌታ መጠመቅና መፈተን ። |
| በእንተ ዘከመ አኀዘ ኢየሱስ ብክይስ ወይኅረይ ቀደምተ ሐዋርያተ ። | ቍ ፲፬ | ጌታ መጀመሪያ እንደ አስተማረና ሐዋርያትን እንደ መረጠ ። |
| በእንተ ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ በቅፍርናሆም ለዘቦቱ ጋኔን ። | ቍ ፳፩ | ጋኔን ያደረበትን በቅፍርናሆም እንደ አዳነ ። |
| በእንቱ ሐማተ ጴጥሮስ ወካልዓን ሕሙማን እለ ተፈወሱ ። | ቍ ፳፱ | የጴጥሮስ አማትን ሌሎችም በሽተኞች እንደ ዳኑ ። |
| በእንተ ዘከመ ሐይወ መፃጉዕ | ም ፪ ቍ ፩ | መፃጉዕ እንደ ዳነ ። |
| በእንተ ዘከመ ተጸውዓ ሌዊ ። | ቍ ፲፫ | ሌዊ እንደ ተጠራ |
| በእንተ ጾም ዘክርስቲያን ። | ቍ ፲፰ | ስለ ክርስቲያን መጦም ፤ |
| በእንተ ሰዊተ ሥርናይ ወሰንበት | ቍ ፳፫ | ስለ ሥንዴ እሸትና ስለ ሰንበት ። |
| በእንተ ዘየብሰት እዴሁ ። | ም ፫ ቍ ፩ | እጁ ስለ ደረቀች ሰው ፤ |
| በእንተ ካልእን ተእምራት ዘኢየሱስ ። | ቍ ፯ | ጌታ ሌሎችን ታምራት እንዳደረገ ፤ |
| በእንተ ዘከመ ኀረዮሙ ለሐዋርያት ወወሀቦሙ ሥልጣነ በላዕለ አጋንንት ወድውያን ። | ቍ ፲፫ | ጌታ ሐዋርያትን እንደ መረጣቸው በአጋንንትና በበሽተኞችም ላይ ሥልጣን እንደ ሰጣቸው ። |
| ዘእንተ ዘከመ አስተዋደይዎ ለኢየሱስ ከመ ያወፅእ አጋንንተ በብዔል ዜቡል | ቍ ፳፩ | አጋንንትን በብዔል ዜቡል እንዲያወጣ ጌታን እንደ አካሰሱት ። |
| በእንተ አዝማዲሁ ለኢየሱስ | ቍ ፴፩ | ስለ ጌታ ዘመዶች ። |
| በእንተ ምሳሌ ዘራዒ ። | ም ፬ ቍ ፩ | ስለ ዘሪ ምሳሌ ። |
| በእንተ ዘርዕ ወማዕረር ። | ቍ ፳፮ | ስለ ዘርና ስለ መከር ። |
| በእንተ ኅጠተ ሰናፔ ። | ቍ ፴ | ስለ ሰናፍጭ ቅንጣት ። |
| በእንተ ኅድዓተ ማዕበል ። | ቍ ፴፭ | ስለ ማዕበል ጸጥታ ። |
| ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ በብሔረ ጌርጌሴኖን ዘቦቱ ጥቀ እኩያን አጋንንት ። | ም ፭ ቍ ፩ | ጌታ በጌርጌሴኖን ክፉዎች አጋንንት ያደሩበትን እንደ አዳነ ። |
| በእንተ ዘከመ ፈወሳ ኢየሱስ ለእንተ ደም ይውኅዛ ወዘከመ አንሥአ ለወለተ ኢያኢሮስ ። | ምዕራፍ ፭ ቍጥር ፳፩ | ደሟ የሚፈስ ሴትን እንደ አዳነ የኢያኢሮስንም ልጅ እንደ አስነሣት ። |
| በእንተ ዘከመ ሰበከ ኢየሱስ በናዝሬት ። | ም ፮ ቍ ፩ | ጌታ በናዝሬት እንደ አስተማረ ። |
| በእንተ ዘከመ ፈነዎሙ ምሂሮ ለሐዋርያት ይስብኩ ። | ቍ ፯ | ሐዋርያትን አስተምሮ ያስተምሩ ዘንድ እንደሰደዳቸው ። |
| በእንተ ዘከመ ስምዓ ኮነ ዮሐንስ መጥምቅ ። | ቍ ፲፬ | ዮሐንስ መጥምቅ እንደ መሰከረ ። |
| በእንተ ዘከመ ተመይጡ ሐዋርያት ። | ቍ ፴ | ሐዋርያት እንደተመለሱ ። |
| በእንተ ዘከመ አብዝኃ በቀዳሚ ፭ተ ኅብስተ ። | ቍ ፴፬ | መጀመሪያ ፭ እንጀራ እንደ አበረከተ ። |
| ዘእንተ ዘከመ ሖረ በዲበ ማይ | ቍ ፵፰ | በውኃ ላይ እንደ ሔደ ። |
| ዘእንተ ዘከመ ተገብረ መንክራተ በጌንሴሬጥ በገሲሰ ጽንፈ ልብሱ ። | ቍ ፶፮ | በጌንሴሬጥ ልብሱን በመዳሰስ ታምራት እንደተደረገ |

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌለ ማርቆስ ። | | የማርቆስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|
| በእንተ ቀዳማዊ ትእዛዝ ። | ቍ. ፳፰ | ስለ መጀመሪያ ትእዛዝ ። |
| በእንተ ማስያስ ወልደ ዳዊት | ቍ. ፴፭ | ስለ ማስያስ ክርስቶስ የዳዊት ልጅ ። |
| በእንተ መደልዋን ጸሐፍት ። | ቍ. ፴፰ | ስለ ግብዞች ጸሐፊዎች ። |
| በእንተ ዘከመ ወደሳ ለመበለት ነዳይት በውኂቦታ ጸሪቀ ። | ቍ. ፵፩ | ድኀዪቱን ሴት ገንዘቧን በመስጠቷ እንደ አመስገናት ። |
| በእንተ ንስቲተ ቤተ መቅደስ ወኢየሩሳሌም ። ምዕራፍ ፲፫ ፤ ቍጥር ፩ | | ስለ ቤተ መቅደስና ስለ ኢየሩሳሌም መፍረስ ። |
| በእንተ ካልዕት ምጽዓቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው | ቍ. ፳፬ | ስለ ክርስቶስ ሁለተኛ መምጣት ። |
| ዘከመ ተማከሩ ሊቃነ ካህናት ይቅትልዎ ለኢየሱስ ። ምዕ ፲፬ ቍ. ፩ | | ጌታን ሊገሉት ሊቃነ ካህናት እንደ መከሩ ፤ |
| በእንተ ዘከመ ረፈቀ በቢታንያ ለምሳሕ ። | ቍ. ፫ | ጌታ በቢታንያ ለመብል እንደ ተቀመጠ ። |
| በእንተ ዘከመ ሤጦ ይሁዳ ። | ቍ. ፲ | ጌታን ይሁዳ እንደ ሸጠው ። |
| በእንተ ዶኀሪት ድራር ወአስተዳልዎት ። | ቍ. ፲፪ | ሁለተኛ እራት ስለ ማዘጋጀት ። |
| በእንተ ዘከመ ከሠተ ለሐዋርያት ዘያገብእ ። | ቍ. ፲፰ | የሚያሲዘውን ለሐዋርያት እንደ ገለጠላቸው ። |
| በእንተ ዘከመ ሠርዓ አኰቴተ ቍርባን ። | ቍ. ፳፪ | የቍርባንን ምሥጢር እንደ ሠራ ። |
| በእንተ ዘከመ ኀደግዎ ሐዋርያት ለኢየሱስ ። | ቍ. ፳፯ | ሐዋርያት ጌታን ጥለውት እንደ ሸሹ ። |
| ዘከመ ጸለየ በጌቴሴማን ። | ቍ. ፴፪ | በጌቴሴማኒ እንደ ጸለየ ። |
| በእንተ ዘከመ አግብአ ለኢየሱስ ወዘከመ አኀዝዎ ። | ቍ ፵፫ | ጌታን ይሁዳ አሳልፎ እንደ ሰጠው እንደያዙትም ። |
| በእንተ ዘከመ ቆመ ኢየሱስ በዐውድ ። | ቍ. ፶፫ | ጌታ በሸንጎ እንደ ቆመ ። |
| በእንተ ክሕደተ ጴጥሮስ ። | ቍ. ፷፮ | ጴጥሮስ እንደ ካደ ። |
| በእንተ ዘከመ አቀምዎ ለኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ። ምዕ ፲፭ ቍ. ፩ | | ጌታን ከጲላጦስ ፊት እንዳቆሙት ። |
| ዘከመ አስተዶኀርዎ ለኢየሱስ እምነ በርባን ወኰነንዎ | ቍ. ፮ | ጌታን ከበርባን ይልቅ እንደ ረገሙት እንደ ፈረዱበትም ። |
| በእንተ ዘከመ ተሣለቁ ላዕለ ኢየሱስ ። | ቍ. ፲፮ | በጌታ እንደ ዘበቱበት ። |
| በእንተ ዘከመ አጾርዎ መስቀሎ ። | ቍ. ፳ | መስቀሉን እንደ አሸከሙት ። |
| በእንተ ዘከመ ተሰቅለ ኢየሱስ ፤ | ቍ. ፳፬ | ጌታ እንደ ተሰቀለ ። |
| በእንተ ጸዐሩ ወሞቱ ለኢየሱስ ፤ | ቍ. ፴፫ | ስለ ጌታ ጭንቅና ስለ ሞቱ ። |
| በእንተ ዘከመ ተቀብረ ኢየሱስ ፤ | ቍ. ፵፪ | ጌታ እንደ ተቀበረ ። |
| በእንተ ትንሣኤሁ ለኢየሱስ ምዕ ፲፮ ቍ. ፩ | | ስለ ጌታ ትንሣኤ ። |
| በእንተ ዘከመ አስተርአየሙ ኢየሱስ ለብዙኃን ፤ | ቍ. ፱ | ለብዙ ሰዎች እንደ ተገለጠላቸው ። |
| በእንተ ዘከመ ፈነዎሙ ኢየሱስ ለሐዋርያት ። | ቍ. ፲፭ | ጌታ ሐዋርያትን እንደ ሰደዳቸው ። |
| በእንተ ዕርገቱ ለኢየሱስ ። | ቍ. ፲፱ | ጌታ እንዳረገ ። |

## የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል

### ቅዱስ ሉቃስ እንደ ጻፈው ።

ብሥራተ ሉቃስ ወንጌላዊ ፩ እም፳ወ፮ቱ አርድእት ጸሎቱ ወበረከቱ የሃሉ ምስሌነ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ሉቃስ ማለት ዓቃቤ ሥራይ ማለት ነው ቀድሞ ዓቃቤ ሥራይ ዘሥጋ ነበር ኋላ ግን ዐቃቤ ሥራይ ዘነፍስ ሁኑዋልና አንድም ትንሣኤ ማለት ነው ለስብከተ ወንጌል ይፋጠናልና አንድም መበሥር ማለት ነው ብሥራተ መልአክን ይጽፋልና ይህ ቃል የሠለስቱ ምእት ነው ። ጥንተ ነገሩ እንደምን ነው ቢሉ እንደ ማቴዎስ ተርክ ፤ ዕፃ በፃ ብለው ተካፍለው ለማስተማር በሚወጡበት ጊዜ ለዮሐንስ ምድረ ጽርእ ደረሰችው ለሰብአ አርድእት ግን ዕፃ የላቸውም አንዱም ሁለቱም ሁነው እንዱን ሐዋ ርያ አንዱም ሁለቱም ሁነው እንዱን ሐዋርያ ተከት ለው ይሄዳሉ ሉቃስም ዮሐንስን ተከትሎ ሂዶ መቄዶንያ የምትባል አገር ከፍሎ አስተምር ብሎ ሰጥቶታል፡ ከዚያ ገብቶ ጌታ ከፅንስ ጀምሮ ያደረገ ውን ተአምራት ያስተማረውን ትምህርት የሠራ ውን ትሩፋት ቢያስተምራቸው ከአምልኮተ ጣዖት ወደአምልኮተ እግዚአብሔር ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ ፤ተመለሱ አሞኑ ተጠመቁ ትምህርት ካልደረሰበት ለማድረስ ወጥቶ በሚሄድበት ጊዜ መኰንን እስክንድርያ ታኦፊ ይለዋል ባጠገብ ያለች አገር ናት እሱም በሱ ስብከት እምኑዋል ወንጌልን ጻፍልኝ ብሎት በዚህ ምክንያት ይጽፋል አንድም እንዳባትነቱ ከራሱ እንቅቶ ይጽፋል መዋዕለ ጽሕ ፈት ሐተታ እንደ ማቴዎስ ጸሐፍቱም ሁለቱ ከሐ ዋርያት ሁለቱ ከአርድእት ናቸው ሐዋርያት ጨር ሰው እንዲጽፉት ያላደረገ ሁለቱን ከአርድእት ያጻፈ ስለምን ነው ቢሉ ሐተታ እንደ ማቴዎስ ጸሐፍቱ ንስ ከፍ ብሎ አምስት ስድስት ዝቅ ብሎ ሁለት ሦስት ያላደረገ ስለምን ነው ቢሉ ሐተታ እንደ ማቴዎስ ወንጌልሂ ብለህ ተርክ ይህን አርእስት ሠለስቱ ምእት ሰጥተዋል ፤ እንደ ማቴዎስ ተርክ ።

### ምዕራፍ ፩ ።

፩ እስመ ብዙኃን እለ ወጠኑ ይንግሩ ወይም ሀሩ በእንተ ግብር ዘአምኑ በላዕሌነ ።

፪ በከመ መሐሩነ እለ ቀደሙነ ርእዮቶ ወተል እክዎ ለቃሉ ።

፫ ወረትዓኒ ሊተኒ እትልዎ እምጥንቱ ወጥ ዩቀ ኵሎ በበመትልው ።

፬ እጽሐፍ ለከ አእዚዝ ታኦፊል ከመ ታእ ምር ጥዩቀ በእንተ ኵሉ ኃይለ ነገር ትምህርተ ዘተመሀርከ ።

እስመ ብዙኃን እለ እኃዙ ሠሪዓ ዜና ግብር ዘንሕነ ጠየቅናሁ በከመ አይድኡነ እለ ቀደሙነ ወተልእ ክዎ ለቃል ለቃሉም ይላል ሊተኒ ረትዓኒ ካዕበ እጽሐፍ ለከ አእዚዝታ ኦፊላ ከመ ታእምር ኃይለ ነገር ትምህርተ ዘተመሀርከ በአማን ኪያሁ ይላል አጭር አብነት ብዙኃን ያላቸው ማቴዎስና ማር ቆስ ናቸው ። ከእንድ ከወጣ ብዙ ማለት የመጽሐፍ ልማድ ነው ወውእቱ ዘአኀበረ ተሰናዕምተ ኵሉ ዘአኮ ቀሊለ ይረክብ ሰብእ በኅበ ኮኑ አማልክት ብዙኃን ወአጋእዝት ብዙኃን በሰማይ ወበምድር እንዲል ። ሠሪዕ ጽሒፍ ሲል ነው ወወልደ ዕጓለ እመሕያውስ የሐውር በከመ ተሠርዓ በእንቲአሁ እንዲል ዜና ወንጌል ናት ሥነ ዜና ሀለዓለም እንዲል ግብር ተአምራት ነው ።

፩ እኛ የተረዳነው ተአምራቱን የምትናገር ወን ጌልን ሊጽፉ የጀመሩ ብዙ ናቸው እኮን ። በከመ አይድዑነ እለ ቀደሙነ

፪ ከኛ አስቀድሞ የነበሩ እንደ ነገሩን ፣ ወተ ልእክዎ ለቃል አካላዊ ቃልን ያገለገሉት ወወ ልደ ዕጓለ እመሕያውስ ኢመጽአ ከመ ይትለአክዎ ሀእንበለ ዳዕሙ ይትለአክ እንዲል ወተልእክዎ ለቃሉ ይላል ወንጌልን ያስተማሩለት ።ወመጠነ ተልእ ከኒ ሠናየ በኤፌሶን ለሊከ ተአምር እንዲል ። ወን ጌልን ያስተማሩለት አስቀድሞ የነበሩ ሰዎች እንደነ ገሩን ።

፫ ሊተኒ ረትዓኒ ለኒያ ቀናቸው እጽፍልሀ ዘንድ ለኔም ቀናኝ ፣ ፫ኛ ሁኖ ይጽፋልና አንድም ግን ከግን ሰንፎ ብለው ወንጌልን ሊጽፉ የጀመሩ ብዙ ናቸው እኮን ለኒያ አልቀናቸውም ሥላሴ ባራቱ ኪሩቤል እምሳል አድርገውባቸው ሊተሰ ለኔ ግን እጽፍልሀ ዘንድ ቀናኝ አራተኛ ሁኖ ይጽ ፋልና ተራ ሳይሻ አንድም እስከ ብዙኃን መጻሕ ፍተ ሐዲሳትን ሊጽፉ የጀመሩ ብዙ ናቸው እኮን ለኒያ ቀናቸው ። ለኔም ቀናኝ መጽሐፈ ግብረ ሐዋ ርያትን ይጽፋልና አንድም ግን ከግን ሰንፎ ብለው

መጻሕፍተ ሐዲሳትን ሊጽፉ የጀመሩ ብዙ ናቸው እኮን ስኢያ እልቀናቸውም ሥላሴ ምሥጢር ከልባቸው ነገር ካንደበታቸው ብርዕ ከጃቸው እናከና ውንላችሁ ብለዋቸው ሊተስ ለኔ ግን ቀናኝ ሥላሴ ምሥጢር ከልቡናየ ብርዕ ከእጄ ነገር ካንደበቴ እከ ናውነውልኝ ።

እእዚዝ ታእፈላ የተዛወረ ቀለም ነው ፊላታያ ማለት ነው ።

፪ ሥዩም ዜናና የምትሆን መፍቀሬ አምላክ እጽፍልሕ ዘንድ ለኔ ቀናኝ ። ፊላ መፍቀሪ ማለት ነው ። ታእስ ማለት በመ እምላክ ነው ከመ ታእምር ኃይለ ነገር ። ያን እውነተኛ እድርገህ የተማርከውን የወንጌል ምሥጢር ትረዳ ዘንድ ። አን ድም እስመ ብዙኃን እለ እኃዙ ይውጥኑ ወይጽሐፉ ይንግሩ ወይምሀሩ ይግበሩ ወያንብሩ በእንተ ግብር ዘእምኑ በላዕሌነ በእንተ ነገር ዘንሕነ ጠየቅናሁ በከመ አይድኡነ እለ ቀደሙነ ወኮኑ ርእየቶ እምቅድም ወኮኑ እምቅድመ ይርእዩ ዙሎ ዘኮነ ወኮኑ ይርእዩ ዙሎ ዘኮነ ወተልእከዎ ለቃለ ፈቃዱ ለቃለ ፈቃድከ ወፈቀድኩ እትልዎ እምጥንቱ በበመትልው እስመ ኮንኩ እተልዎ ለዙሉ ግብር በዙሉ ግብር ወእጤይቆ በጥይቅና ሊተኒ ረትዓኒ ካዕበ እጽሐፍ ለከ ለእጊዝ ለእኃዚ ታእፈላ ከመ ታእምር ጽድቀ ኃይለ ነገር ትምህርተ ዘተመህርከ በእማን ኪያሁ ይላል ረጅም አብነት በኛ ስብከት ያመኑትን እኛ ወንጌልን የተረዳንበትን ተአምራቱን የምትናገር ወንጌልን ጽፈው አጽፈው ደጉ ሰው ማኅደር ሰፍተው ሊያኖሩ የወደዱ ብዙ ናቸው እኮን ፩ም በኛ ስብከት ያመኑትን ወንጌልን እኛ የተረዳንበትን ተአምራቱን ሊጽፉ የወደዱ ብዙ

ናቸው እኮን ። ይንግሩ ለመጣላቸው
ይምሐሩ ፤ ዙረው ።
ይግበሩ ፥ ለራሳቸው ።
ያንብሩ ለሌላው ።

በከመ አይድኡነ ከኛ አስቀድሞ የነበሩ እንደነገሩን ወኮኑ እምቅድም ርእዮቶ አስቀድሞ ያደሩለት ። ንፈቅድ ንርአዮ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዲል ወኮኑ እምቅድም ይርእዩ ይላል ፥ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር የሚያደርገውን ተአምራት ያዩ ዘንድ ያደሩለት ። ወኮኑ እምቅድመ ይርእዩ ዙሎ ዘኮነ ፣ ሠላሳ ሦስት ዓመት የሚደረገውን ታምራት ሳያዩ ያደሩለት ወተልእከዎ ለቃለ ፈቃዱ ፤ ወዶ የሠራት ።. ለቃለ ፈቃድከ ይላል ወደህ የተቀበልካት ወንጌልን ያስተማሩለት ወፈቀድኩ እትልዎ እምጥንቱ በመትልው በጀመረበት ስጀምር በጨረሰበት ስጨርስ የሚቀድመውን ሳስቀድም የሚከተለውን ሳስከትል በጽፈት ልከተለው ወደድኩ ኀበሂ ዓርገ ደብረ ወኀበሂ ነበረ ወኀበሂ መሐረ ኀበሂ ዓርገ ሐመረ ወኀበሂ ገሠጸ ባሕረ እንዲል ከሁሉ ይልቅ ሉቃስ ተራ ያቀናል ይባላልና እስመ ኮንኩ እተልዎ ለዙሉ ግብር ሥራውን ሁሉ እማርለት ነበርና እንተስ ተለውከ ትምህርተየ እንዲል አንድም በጀመረበት ስጀምር በጨረሰበት ስጨርስ የሚቀድመውን ሳስ ቀድም የሚከተለውን ሳስከትል ልጽፈው ወደድኩ እስመ ኮንኩ እተልዎ በዙሉ ግብር ይላል በሥራው ሁሉ እመስለው እከተለው ነበርና ።
ሊተኒ ረትዓኒ ካዕበ እጽሐፍ ለከ ለእጊዝ በአጋንንት ለመሠልጠን ለእኃዚ ሥልጣና ለምትሆን ላንተ ታያፊላ ሆይ ዳግመኛ እጽፍልሕ ዘንድ ለኔም ቀናኝ። ከመ ታእምር ጽድቀ ኃይለ ነገር ፥ ያን እውነተኛ እድርገህ የተማርከውን የወንጌልን ምሥጢር መረዳትን ታውቅ ዘንድ ።

በከመ አይድዓ ገብርኤል ልደቶ ለዮሐንስ

፭ ወኮነ በመዋዕለ ሄሮድስ ንጉሥ ሀሎ አሐዱ ካህን ዘስሙ ዘካርያስ በመዋዕለ አብያ ፩ ኅጹ ፭፻ ፲። ኮነ ያለውን ሀሎ ብሎ አመጣው ።

፭ ፤ ሄሮድስ ነግሦበት በነበረ ዘመን አብያ ሌቀ ካህናትነት በተሾመበት ወራት ዘካርያስ የሚባል አንድ ካህን ነበር ፥ አብነት ዘአምዘመደ አብያ ይላል ። ከአብያ ዘመዶች ወገንን የሚሆን ዘእምላእካነ ቤተ አብያ ይላል ። ከአብያ ወገን ተሹመው ከሚያገለግሉት ወገን የሚሆን ።
ወይሠርጽ ከመ ሕገ ቤተ አብያ
ከአብያ ወገን እንደሚሠሩት ሥራ የሚሠራ ሐተታ ተራ ካህን ነው ቢሉ የተመቸ ሊቀ ካህናት ነው ቢሉ ምሉና ደግ ሁነው ቅሹመው ነበርና ወብእሲቱኒ እምእዋልደ እሮን
ሚስቱም ከእዋልደ አሮን ወገን ናት ።
ወስማ ኤልሳቤጥ
ስሟም ኤልሳቤጥ ትባል ነበረ ሐተታ የአሮን ሚስት ኤልሳቤጥ ሳለች አሪት ተሠርታለች የዘካርያስ ሚስት ኤልሳቤጥ ሳለች ወንጌል ተሠራች ። በኤልሳቤጥ የተሠራች ሕግ በኤልሳቤጥ አለፈች ለማለት

፮ ወክልኤሆሙ ጻድቃን እሙንቱ በቅድመ እግዚእብሔር ።

፯ እግዚአብሔር ባወቀው ነገር በእግዚአብሔር ዘንድ ሁለቱም ሁሉ ደጋግ ነበሩ ።
ሐተታ እስመ መካን ይእቲ ኤልሳቤጥ ብሎ እንደሚያመጣው ምክንት በኃጢአት አይደለውምን ምክንትስ ኢተውህበ ለብእሲት ዳዕሙ በግብረ እደ ሃትመው ዘእንበለ ውሉድ እንዲል ጻድቃን ማለቱ እንደምን ነው ቢሉ በሌላው እውነት ነው እዷን

ግን መካን ማለቱ እስክትወልድ ድረስ ነውና ።
ወየሐውሩ በኵሉ ትእዛዙ ።
በትእዛዙ ጸንተው ይኖራሉ ወነበቦ ባለው
ወሕጉ
በዘጠኙ ቃላት
ወኵነኔሁ ለእግዚአብሔር ።
በኢታምልክ ጸንተው ይኖራሉ ።
ወንጹሐን እሙንቱ እምኃጢአት ።
ከሩካቤ ንጹሐን ናቸው ።
ሐተታ ይህንስ ኃጢአት አይለውም ቅዱስ ጳውሎስ ክቡር አውስቦ ብሎታል ብሎ ከሌላው ኃጢአት ንጹሐን ናቸው ።

፯ ወአልቦሙ ውሉድ ።
፯ ልጅ አልነበራቸውም ።
እስመ መካን ይእቲ ኤልሳቤጥ
ኤልሳቤጥ መካን ነበረችና ።
ወክልኤሆሙ ልጒቃን እሙንቱ ።
እሷም እሱም አርጅተው ነበርና
ወኃለፈ መዋዕሊሆሙ
የሕፃንነታቸው ዘመን አልፎባቸው ነበርና ።

፰ ወእምዝ እመ ይገብር ግብረ ክህነት በዕብሬቱ ቅድመ እግዚአብሔር ።

፱ በከመ ይገብሩ ካህናት ።

፱ ከዚህ በኋላ ካህናቱ እንደሚሠሩት ሥራ ያለ በቤተ መቅደስ ሁኖ ፥ ተራ ካህን ነው ቢሉ በስሞኑ ሊቀ ካህናት ነው ።

፱ ቢሉ ባመት ፩ ቀን ፥ የክህነት ሥራ በሚሠራበት ጊዜ ። በጽሐ ጊዜ የዐጥን ።
የሚያጥንበት ጊዜ ደረሰ ። ሐተታ ለእግዚአብሔር ሁሉ ፊቱ ሲሆን መሥዋዕት የተሠዋበትን ስሙ የተጠራበትን ቅድመ እግዚአብሔር ይለዋል ።
ወቦአ ቤተ መቅደሱ ለእግዚአብሔር ።
ከቤተ መቅደስ ገባ ። ታሪክ የጥቅምት ጨረቃ ሠርቅ ባደረገች ባሥር ነው ፥ ዕለቱም ዕለተ የሴፍ ነው ፥ ተሰብስበው ይጸልያሉ ። ወበይእቲ ዕለት አሕምምዋ ለነፍስክሙ እንዲል አባቶቻቸው በኮሬብ ዕንላተ ላሕም አቁመው ነበርና ። ሮቤል ካባቱ ቁባት ደርሶ ነበርና አንድም ወንድማቸውን ዮሴፍን ሸጠው በልተው ነበርና በዚህ ሁሉ እዳ አታድርግባቸው ሲሉ ፤

፲ ወኵሎሙ ሕዝብ ሀለዉ በምልአሙ ይጼልዩ በአፍአ በጊዜ ሰዓተ ዕጣን ። ዘፀ.፴፥፯ ፥ ዘሌ. ፲፮፥፲፯ ።

፲ ሕዝብ ሁሉ በሚያጥንበት ጊዜ ተሰብስበው በአፍአ ይጸልዩ ነበር ። ሐተታ ፥ ምን እያሉ ይጸልዩ ነበር ቢሉ በጐ ራዕይ ግለጽለት ስቡን ፀአ ቅርንተ ምሥዋዕ ምላለት እያሉ ስቡ የመላ እንደ ሆነ ዘመነ ጽጋብ ይሆናል የጐደለ እንደሆነ ዘመነ ረኃብ ይሆናል ። አንድም ዓብዩድን ናዳብን ባላወቁት ኃጢአታቸው እንደ ቀሰፍካቸው ባላወቀው ኃጢአቱ አትቅሠፈው እያሉ ።

፲፩ ወአስተርአዮ መልአከ እግዚአብሔር እንዘ ይቀውም መንገለ የማነ ምሥዋዕ በዕጣን ዘበርትዕ እለና ከዚያ ሲለይ ።

፲፩ ዕጣን አለ በመሠውያው ቀኝ በኩል ከእግዚአብሔር የታዘዘ መልአክ ታየው ። ሐተታ ፥ ለሰይጣን ቀኝ የለውም ። መልአክግን የማናዊ ነውና መልአክ እንደሆነ ለማጠየቅ በቀኝ በኩል አለ ፩ም ሰው ሁሉ ወደ የማናዊ ግብር የሚመለስበት ዘመን ደረሰ ሲል ፩ም ሰውን ሁሉ መክሮ አስተምሮ ወደቀኝ የሚመልስ ልጅ ትወልዳለህ ሲል ።

፲፪ ወሶበ ርእዮ ደንገፀ ዘካርያስ
፲፪ ዘካርያስም መልአኩን ባየው ጊዜ ደነገጠ ፍርኃት ወረዓድ ወረደ ላዕሌሁ ፍርኃት ረዓድ አደረበት ፥ ሐተታ ፍርሃት የልቡና ረዓድ የጉልበት ድንጋጤ የናላ ነው ልማድ ቢለወጥበት ከዚህ አስቀድሞ ከምስሐል ከአዕናቍ ቃል ይሰማ ነበር ። እንጂ መልአክ ሊይቶ አያውቅምና ።
አንድም አብዩድን ናዳብን ባላወቁት ኃጢአት እንደ ቀሠፋቸው ባላወቅሁት ኃጢአቴ ሊቀሥፈኝ መጣ ብሎ አንድም እጇም ያስፈራ ነበርና በአፍአ ያሉትን ጨርሶ እኔንም ሊገለኝ መጣ ብሎ ፤

፲፫ ወይቤሎ መልአክ ኢትፍራህ ዘካርያስ
፲፫ መልአኩ ዘካርያስን አትፍራ አለው ። ሐተታ ፥ ፍርኃት አርቆ መናገር ለመልአክ ልማዱ ነውና ፤ ኢትፍራህ ብእሴ ፍትወቶ ዳንኤል ኢትፍርሂ ማርያም እንዲል ፤ እስመ ናሁ ተሰምዓ ጸሎትከ ቅድመ እግዚአብሔር ።

ልጅ ስጠኝ እያለ ይለምን ነበር ቢሉ ልመናህ ተሰምቷልና ብእሲትከ ኤልሳቤጥ ትፀንስ ወትወልድ ለከ ወልደ ።

ሚስትህ ኤልሳቤጥ ወንድ ልጅ ትወልድልሃለች፤ አንድም አሪት የተማረ ነበርና የተቈጠረው ሱባዔ ደረሰ የተነገረው ትንቢት ቀረ እያለ ይጸልይ ነበርና ልመናህም ተሰምቷልና ወብእሲትከኒ ሚስትህም ወንድ ልጅ ትወልድልሃለች አለው ወትሰምዮ ስሞ ዮሐንስ ።

ስሙንም ዮሐንስ ትለዋለህ ዮሐንስ ማለት ፍሥሓ ወኃሤት ማለት ነው ።

፲፬ ወይከውነከ ትፍሥሕተ ወኃሤተ
፲፬ ፈጽሞ ደስ ያሰኝሃል ።
ወብዙኃን ይትፌሥሑ በልደቱ በመወለዱም ብዙ

ሰዎች ደስ ይላቸዋል ወሶበ ሰምዑ አዝማዲሃ ወአ ግዋሪሃ ከመ አዕበየ እግዚአብሔር ሳዕሌሃ ሣህሎ ተፈሥሑ ባቲ እንዲል እንድም በትምህርቱ በት ንቢቱ ደስ ይላቸዋል ።

፲፭ እስመ ዓቢየ ይከውን ውእቱ በቅድመ እግ ዚአብሔር ።

፲፭ በእግዚአብሔር ዘንድ ደግ ይባላልና ።
ኢይሰቲ ወይነ ወሜስ ።
የወይን ጠጅ የማር ጠጅ አይጠጣም ። ሐተታ የማር ጠጅስ በሀገራቸው እጅግም ያህል ብሎ ጥሩ ጠጅ ጉሽ ጠጅ አይጠጣም ኢዘያሰክር ። አረቄ
ወኢዘኢያሰክር ።
ቡን አይጠጣም ።
ይመልእ ላዕሌሁ መንፈስ ቅዱስ እምከርሠ እሙ ከናቱ ማኅፀን ጀምሮ መንፈስ ቅዱስ ተመልቶ ይኖራል ።

፲፮ ወለብዙኃን እምደቂቀ እስራኤል ይመይጦሙ ኀበ እግዚአብሔር አምላኮሙ ።

፲፮ መክሮ አስተምሮ ከእስራኤል ወገን ብዙ ሰዎችን ከአምልኮተ ጣዖት ወደ አምልኮተ እግዚአ ብሔር ይመልሳቸዋል ።

፲፯ ወውእቱ የሐውር ቅድሜሁ ። በመንፈስ ቅዱስ ሚልክ ፬ ፣ ፮ ፣ ማቴ ፣ ፲፩ ፣ ፳፬ ።

፲፯ በፊት በፊት ይሄዳል ማለት በመንፈስ ቅዱስ ተቃኝቶ መንፈቅ ተቀድሞ ያስተምራል ።
ወበኃይለ ኤልያስ ።

በኤልያስ ግብር ጸንቶ ይኖራል ። እንድም በመን ፈስ ቅዱስ ኃይለ ኤልያስ ኤልያስ ተቃኝቶበት በሚኖር በመንፈስ ቅዱስ ተቃኝቶ ይኖራል ።
ከመ ይሚጥ ልበ አበው ኀበ ውሉድ ።
የአበው የነአብርሃምን ዕውቀት ወደ ውሉድ ወደ ሐዋርያት ይመልስ ዘንድ ።

ወሕሊና ከሀድያን ኀበ አእምሮ ጻድቃን ።
የከሀድያን የነ አብርሃምን አእምሮ ወደ ጻድቃን ወደ ሐዋርያት አእምሮ ይመልስ ዘንድ ሐተታ ከሀድያን አላቸው በቀደ መ ግብራቸው እንድም የአበው የጸ ሐፍት ፈሪሳውያን ዕውቀት ወደ ውሉድ ወደ ሐዋ ርያት ዕውቀት ይመልስ ዘንድ ፣ የከሀድያን የፈ ሪሳውያንን አእምሮ ወደ ውሉድ ወደ ሐዋርያት አእምሮ ይመልስ ዘንድ አሁን የተመቸ ።
ከመ ይሥራዕ ሕገ ።
ሥራት ይሠራ ዘንድ ።
ወሕዝበ ዘድልው ለእግዚአብሔር ።
ሕዝቡን መክሮ አስተምሮ ለእግዚአብሔር ማኅ ደር ለ መሆን የበቁ ያደርግ ዘንድ ።

፲፰ ወይቤሎ ዘካርያስ በምንት አአምር ከመ ይከውን ዝንቱ ኵሉ ።

፲፰ ዘካርያስም ይህ ሁሉ እንዲደረግ በምን ዐውቀዋለሁ አለው ሐተታ ምልክት ሽቶ እስመ አይሁድኒ ተአምረ ይሴዓሉ እንዲል እንድም ተጠ ራጥሮ ። ናሁ አነ ልሂቅ ።
እነሆ እኔ አርጅቻለሁ ።
ወብእሲትየኒ ኃለፈ መዋዕሊሃ የሷም የሕፃንነቷ ዘመን አልፏዋል ።

፲፱ ወተሰጥዎ መልአክ ።
፲፱ መልአኩም መለሰ ።

ወይቤሎ አነ ውእቱ ገብርኤል ዘእቀውም ቅድመ እግዚአብሔር ዘተፈናኩ ኀቤከ እንግርከ ወእዜንከ ዘንቱን ልደቱን ልንግርህ መዳንተ የተላኩሁ የእግ ዚአብሔር ባለሟል የምሆን እኔ ገብርኤል ነኝ አለው ። ሐተታ የእግዚአብሔር ባለሟል ያይ ደለ ሰይጣን ሐሰት ይናገራል እንጂ የእግዚአብሔር ባለሟል የምሆን እኔ ሐሰት እናገራለሁን ለማለት እንዲህ አለ ። ሐተታ በምን ያውቀዋል ቢሉ በመ ጽሐፍ በሄኖክ በዳንኤል ሲመለከት ለምዶታልና።

፳ ወናሁ ትከውን በሐመ ።
፳ ምልክት ሽቶ ላለው ለዚህ ምልክት ድዳ ትሆናለህ ። ወትስእን ነቢበ እስከ እመ ይከውንዝንቱ ይህ እስኪደረግ ድረስ አትናገርም ።
እስመ ኢአመንከኒ ነገርየ ዘይከውን ወይትፌጸም በዕድሜሁ በጊዜው ጊዜ የሚደረግ ነገሬን አልተ ቀበልኸኝምና ። እንድም ተጠራጥሮ ላለው የተ ግሣጽ አነጋገር ።
እመ ኢአመንከኒሰ ።
በጊዜው ጊዜ የሚደረግ ነገሬንስ ካልተቀበልከኝ ድዳሁን አትናገር አለው ።

፳፩ ወሀለዉ ሕዝብ ይጼልዩ ወይጸንሕዎ ለዘካርያስ ።
፳፩ ሕዝቡ ግን ይመጣል እያሉ እየጠበቁት ይጸልዩለት ነበር ።
ወአንከሩ ።
አደነቁ ራዕይ በስቶበትን ይሆን አረጋዊ ነውና ወድቆ የሚያነሣው አጥቶ ይሆን አብዩድን ናዳብን ባላወቁት ኃጢአታቸው እንደ ቀሰፋቸው ባላወ ቀው ኃጢአቱ ቀሥፎት ይሆን እያሉ
እስመ ጐንደየ ውስተ ቤተ መቅደስ ።
ቤተ መቅደስ ከገባ ብዙ ሰዓት ሁኖታልና ።
፳፪ ወወፂኦ ኀቤሆሙ እፎአ ስእነ ተናግሮቶሙ
፳፪ ወደነሱ በወጣ ጊዜ መናገር ተሳነው ።
ወአእመሩ ከመቦ ዘአስተርአዮ ውስተ ቤተ መቅደስ በቤተ መቅደስ ሳለ የታየው እንዳለ ዐወቁ የታየው እስ አሉ ።

ወነበረ ከማሁ እንዶ በሀም ውእቱ ።
ወኮን በሀመ ወሰአን ነቢበ እንዳለው ድዳ ሁኖ ኖረ ።
ወይኤምርሙ በእዴሁ ።
ተርታውን ነገር በእጁ እየጠቀሰ ያሳያቸው ነበር እንድም አይነተኛውን እየጻፈ ስምየን የሚባል ተወራጅ ሹሞላቸው ኖረ ።

፳፫ ወእምዝ ፈጺሞ መዋዕለ ዕብሬቱ አተወ ቤቶ ።

፳፫ ሊቀ ካህናት ነው ቢሉ በዓመት አንድ ቀን አጥኖ ከከተማ ቤቱ ገባ ። ተራ ካህን ነው ቢሉ ሰሞኑን ፈጽሞ ዓርገ ደብረ ዘይት ይላል ደብረ ዘይት ወዳለ ቤቱ ገባ ።

፳፬ ወእምድኅረ ከልኤ መዋዕል ፀንሰት ኤልሳቤጥ ብእሲቱ ።

፳፬ ከሁለት ቀን በኋላ ኤልሳቤጥ ፀነሰች ። ሐተታ ስለ ክብረ ዕጣን ሁለት ቀን ኑሮ ተገናኝቷታል ። ዛሬም ሕጋውያን ስለ ሥጋው ደሙ ሁለት ቀን ኑረው መገናኘት ይገባቸዋል ።

፳፭ ወከበተት ዕንባ ኃምስተ አውራኃ እንዘ ትብል ከመዝኑ ረሰየኒ እግዚአብሐር አመ ሐውፆ ሐወፀኒ በዝንቱ መዋዕል ያዕትት ዝንጓጔየ እምሰብእ

፳፭ በዚህ ወራት ስድቤን ከሰው ያርቅልኝ ዘንድ እግዚአብሐር በረድኤት በጐበኘኝ ጊዜ እን ዲህ አደረገኝ ብላ አምስት ወር ፅንሷን ሰወረች ። ሐተታ ፥ በዶግ ሴት ልማድ ዳግመኛ ይህች ባልቴት የበላችው ቂጣ ቢነፋት ፀነሰኩ ትላለች ባሏት ነበርና ምን እያሉ ይሰድቧት ነበር ቢሉ ዕጹተ ማኅፀን ዶብ ስተ እጥባዕት ኀጥእተ በረከት ምልእተ መርገም የበቅሎ ዘመድ ቢወልዷት እንጂ እትወልድ እያሉ ይሰድቧት ነበርና ።
በእንተ ዘአብሠራ ለማርያም ወበእንተ ሥጋዌሁ ለቃል ።

፳፮ ወበሳድስ ወርኅ ተፈነወ ገብርኤል መል አከ እምኀበ እግዚአብሐር ኀበ አሐቲ ሀገር ዘገሊላ እንተ ስማ ናዝሬት ።

፳፮ ወከበተት ፅንሳ ፭ተ አውራኃ ብሎ ነበርና በስድስተኛው ወር መልአኩ ገብርኤል የገሊላ ክፍል ዕፃ ወደምትሆን ናዝሬት ወደምትባል አገር ከእግ ዚአብሐር ዘንድ ታዞ ሄደ ።

፳፯ ኀበ ድንግል እንተ ተፍኅረት ለብእሲ ዘስሙ ዮሴፍ ዘእምቤተ ዳዊት ።

፳፯ ከዳዊት ወገን ለተወለደ ዮሴፍ ለሚባል ሰው ወደታጨች ወዳንዲት ድንግል ።ሐተታ ብዙ ገሊላ አለና ከዚያ ሲለይ እንተ ስማ ናዝሬት ብዙ ደናግል አሉና እንተ ተፍኅረት ለብእሲ ዘስሙ ዮሴፍ ብዙ ዮሴፍ አለና ከዚያ ሲለይ ዘእምቤተ ዳዊት አለ ። ወስማ ለይእቲ ድንግል ማርያም ።

ያችም ብላቴና ማርያም ትባላለች ታሪክ ነገረ ማር ያም የተፍኀርስ ነገር እንደምን ነው ቢሉ ተክታ በጥሪቃ የሚባሉ ባለጸጎች ባልና ሚስት ነበሩ ባለጸግነታቸውም የወርቅ የዕንቍ የወንድ ባሪያ የሴት ባሪያ የፈረስ የበቅሎ የላም የበግ የፍየል ይህ ቀራ ቸው የማይባሉ ነገር ግን ልጅ አልነበራቸውም ከዕለታት ባንድ ቀን ከዕቃ ቤት ገብቶ ዕቃውን አይቶ ቴክታ ካንች በቀር የምወደው እንደሌለኝ አምላከ እስራኤል ያውቃል ነገር ግን ልጅ የለንም አላት ። ለልጅማ እኔ ምንድነኝ ወደ እግዚአብሐር እናመልክት እንጂ አለችው እመለከቱ ፤ ነጭ እን ቦሳ ከማኅፀንዋ ስትወጣ ። እንቦሳዋ እንቦሳ ስትወ ልድ እስከ ስድስት ድረስ ፯ተኛይቱ ጨረቃ ጨረ ቃይቱ ፀሐይ ስትወልድ አይታ ነገረችው ፥ በዘመ ናቸው መተርጕመ ሕልም አለና ሄደህ አስተርጕመህ ና አለችው ሄዶ ቢነግረው ደግ ልጅ ትወልዱ ይሆ ናል አለው ። ተመልሶ መጣ ምን አለህ አለችው ልጅ ትወልዱ ይሆናል አለኝ አላት ። የጨረቃይ ቱንና የፀሐዩንስ ጊዜ ይተርጕመው እንጂ አልተተ ረጐመም አለችው እንዲሀ ሁነው ሲኖሩ ፀነሰች ወለደችም ስሟንም ሄኤሜን አለቻት ረከብኩ ስእ ለትየ ማለት ነው ሄኤሜን ደርዲዕን ደርዲዕ ቶናህን ቶናህ ሲካርን ፥ ሲካር ሄርሜላን ሄርሜላ ሐናን ወለደ ሐና ከነገደ ይሁዳ የተወለደ ኢያቄም የሚ ባል ሰው አግብታ መካን ሁና ስትኖር ወዳጅ ባል ንጀራ እለቻት ዛሬ ከቤተ እግዚአብሐር ሄጂ እጅ ልነሣ እወዳለሁ ነገር ግን ልብስ የለኝም እንጂ አለቻት የኔ ልብስ ብዙ አለልሽ አንዱን ለብሰሽ ሂጂ አለቻት ምን አልባት በዝሙት ያመጣሽው እንዳይ ሆን አለቻት እግዚአብሐር በምን ምክንያት ነው ልጅ የነሣሽ እያልኩ ሳዝንልሽ እኖር ነበር ለካ ብት ዕቢትሽ ነው አለቻት ነገሩም አልቀረም ተውሳ ለብሳ እጅነሥታ ስትመለስ አርጋብ ከመንገድ ሁነው ከል ጆቻቸው ጋራ ሲጫወቱ አይታ ለሁሉ ልጅ ሰጥተ ኸዋል ሐናን ደንጊያ ብለህ ፈጥረሃታልን ብላ አል ቅሳ ተመለሰች በዚህ ሌሊት ጸዓዳ ርግብ ስባቱን ስማያት ሰንጥቃ መጥታ በማኅፀንዋ ስታድር ለኢያ ቄም የፀምር መታጠቂያ ሲያስታጥቁት የብርሃን በትር ሲያሲዙት ዓይታ ነገረችው እሱም እኔም እንጂ ከደጃችን ያለች ዛፍ ለምልማ አብባ አፍርታ ፍጥረት ሁሉ ሲመገባት አየሁ ብሎ ነገራት ። ከዚህ በኋላ እመቤታችን ተፀነሰች ።

ሮቤል የሚባል ዘመዷም ወዳጅዋም ቢሉ ሞተ ትወደው ነበርና ያልጋውን ሸንኮር ይዛ ስታስቅስ የሞተው ተነሥቶ ሰላም ለኪ ኦ እምኔውቱ ለፀሐየ ጽድቅ ለዘገብረ ሰማየ ወምድረ ብሎ ሰመተርጐመ ሕልም ያልሆነለትን ተርጕሞ አርፏል ። አይሁድ ይህን ሰምተው ምቀኝነት ኦደረባቸው ፣ ቀድሞ ከኔህ ወገን ዳዊት ሰሎሞን እየተወለዱ አርባ አርባ ዘመን ገዙን ዛሬ ደግሞ ከኔህ የሚወለድ እንደምን ያለ ይሆን ብለው ቀኑባቸው ኋላ እመቤታችን ተወ ለደች ሦስት ዓመት ሲሆናት መዋዕለ ጥብ ሲፈ ጸም የብፅዓት ልጅ ናትና ወስደው ለካህናት ሰጡ ካህናቱም አክብረው ተቀብለው የምግቧን ነገር እንዴት እናደርጋለን ሲሉ ፣ መልአኩ ፋኑኤል ሰማያዊ ኅብስት ሰማያዊ ጽዋ ይዞ ወረደ ዘካርያስ የኔ ሀብት ነው ብሎ ሊቀበል ሄደ ሽቅብ ይዞት ወጣ ሲመለስ ይወርዳል ፣ ሁሉም የኛ ሀብት ነው እያሉ ቢሄዱ ሽቅብ እየያዘው እየወጣ የማይሆን ሆነ የዚች ብላቴና ሀብት እንደሆነ ከሰው ለይተሽ አኑረሻት ነይ አሏት ። ከሰው ለይታ አኑራት ብትሄድ ከም ድር ሦስት ክንድ ተሰንዝር ከፍ አድርጎ ከንፉን ጋርዶ መግቧት ዓረገ ። በዚህ ሁሉ ምቀኝነት አድሮ ባቸዋል ። የምግቧስ ነገር ከተያዘልን ብለው ከቤተ መቅደስ አኖሯት ። ሴቲት እንጣላታለን እያሉ ይመ ጣሉ የቤተ መቅደሱ ቅጽር እሳት እየሆነ ይመልሳቸዋል

መጥቁል የሚባል መሠርይ አለ እንዲህ ያለችጠላት ተነሥታብናለችናአጥፋልንብለው ብዙ ወርቅ ብዙ ግምጃ ብዙ ከብት ሰጡት ወርቁን ብረት ብሩን ብርት አደረገችው ። ግምጃውን ብል በላው ደመ ነፍስ ያላቸው ሁሉ አልቀው አድረዋል ። እንዲህ ያለች ናት ሐሰት መሰሎኝ ብሎ ምስት መቶ ልቡ ሳነ ሥጋ አጋንንት በምስሓብ ስቦ እንዲህ ያለች ጠላት ተነሥታብናለችና አጥፉልኝ አላቸው ፣ እን ተማ ወዳጃችን ስትለን ሰማዩን ምድር ምድሩን ሰማይ አድርጉ ብትለን ይሆንልን የለምን ብለው ተሰብስበው መጡ ። መልአኩ ቅዱስ ገብርኤል ከመንገድ ቆይቶ ብሰይፍ አርዶ አርዶ ፈጅቷቸዋል በቤተ መቅደስ ዐሥራ ሁለት ዓመት ትኖራለች ፣ ከዚያ ሦስት ዐሥራ አምስት ዓመት ይሆናል ። አይሁድ ስምቀኝነት እያርቋምና ይህች ብላቴና መጠን አንስት አደረሰች ቤተ መቅደስ ታሳድፍብ ናለች ትውጣልን አሉት ዘካርያስን ሊቀ ካህናቱ እሱ ነውና እንደምን ትሆኝ አላት ወደ እግዚአብ ሔር አመልክትልኝ ኦለችው ቢያመለክት ከነገደ ይሁዳ ሚስቶቻቸው የሞቱባቸውን ሰዎች በትር ሰብስበህ ከቤተ መቅደስ አግብተህ ጸልይበት ምል ክት እገልጽልሃለሁ አለው ። ቢሰበስብ ሽህ ከመ ጠኝ መቶ ሰማንያ አምስት ሆነ ለሁለት ሽህ ዐሥራ አምስት የጎደለው ማለት ነው ያን ከቤተ መቅደስ አግብቶ ቢያወጣው ከዮሴፍ በትር አዮሴፍ ዕቀባ ለማርያም የሚል ተቀርጾ ተገኝቷል ። ርግብም መጥታ ከራሱ ላይ አርፋበታለች ፣ ዕጣም ቢያ ወጡ ለሱ ወጥቷል እንደ ሦስት ምስክር ያም ሆነ ያም ሆነ ከእግዚአብሔር አገኝተን የሰጠንህን ከእ ግዚአብሔር አግኝተን እስከናስናብትህ ወስደህ ጠብ ቃት አትንካ ብለው ሰጡት የተፍገረ ነገር ይህ ነው ። ማርያም ማለት መርህ ለመንግሥተ ሰማይ ማለት ነው ። ምእመናንን እየመራች ገነት መንግ ሥተ ሰማይ ታገባለችና ። አንድም ፍጽምት ማለት ነው ለጊዜው መልክ ከደም ግባት አስተባብራ ይዛ ተገኝታለች ። ፍጻሜው ግን ንጽሐ ሥጋ ንጽሐ ነፍስ ንጽሐ ልቡና አንድ አድርጋ ይዛ ተገኝታለችና አንድም ጸጋ ወሀብት ማለት ነው ለጊዜው ለናት ላባቷ ጸጋ ሀብት ሁና ተሰጥታለች ። ፍጻሜው ግን ለሁላችን ተሰጥታለችና ። አንድም ልዕልት ማለት ነው አርያም ማለት ልዑል ማለት እንደሆነ እመ ቤታችንንም መትሕተ ፈጣሪ መልዕልተ ፍጡራን ይላታልና ። ተፈሥሒ ቤተ ይሁዳ ወተሐሠዪ ቤተ እስራኤል ተሰአኪተ እግዚአብሔር ወሰብእ ማኅ በረ መሃይምናን ወሕዝብ ማለት ነው ። አንድም ማሪሃም ማለት እግዝእተ ብዙኃን ማለት ነው አብርሃም ማለት አበ ብዙኃን ማለት እንደሆነ ያንም ዘበዕብራይስጢ እንጂ ይለዋል ብሎ ማርያም ማለት ትሉ እግእዝተ ብዙኃን ማለት ነው ።

፴፰ ወቦአ መልአክ ኀቤሃ

፴፰ መልአኩ እሷ ወዳለችበት ቤት ገባ የቦታ አንድም ባሕርዩዋን መስሰላት መስሎ ታያት ። ወይቤላ ተፈሥሒ ፍሥሕት አምልእተ ጸጋ እግዚ አብሔር ምስሌኪ ።

እግዚአብሔር ከሥጋሽ ሥጋ ከነፍስሽ ነፍስ ነሥቶ አንድ አካል አንድ ባሕርይ ይሆናልና በትንቢተ ነቢያት በመላእክት ተልእኮ ደስ ያለሽ ምልእተ ክብር ሆይ ደስ ይበልሽ አላት ።

ወቡርክት አንቲ እምአንስት ።

ከሴቶች ተለይተሽ መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌለብሽ ነሽ ።

፴፱ ወርእያ ደንገፀት እምቃሉ ።

፴፱ መልኩን አይታ ድምፁን ሰምታ ደነ ገፀች ። አንድም ርእያ ቅሉ ሰሚዓ ሲል ነው ወር እዮ ሕልመ አቡሁ ገብአ ማቴሳላ እንዲል ። ድም ፁን ሰምታ ደነገጠች ።

ወኀለየት ወትቤ አፎኑ ዘከመዝ እንጋ አምኃ ይትአ ምኑ እንዴት እንዲህ ያለ ሰላምታ እንደምን ይቀ በላሉ ብላ አስባ ተናገረች ። ሐተታ ፣ እናቴን ሄዋ ንን ያሳተ ሰይጣን ሊያስተኝ መጥቷል ብላ ።

፴ ወይቤላ መልአክ ኢትፍርሂ ማርያም ።
፴ መልአኩም ማርያም አይዞሽ አትፍሪ አላት ሐተታ ፤ ለመልአክ ፍርኃት አርቆ መናገር ልማድ ነውና ። ኢትፍራህ ብእሴ ፍትወት ዳንኤል ኢትፍራህ ዘካርያስ እንዲል ።
እስመ ረከብኪ ሞገሰ በኀበ እግዚአብሔር ።
በእግዚአብሔር ዘንድ ባለሟልነትን አግኝተሻልና

፴፩ ወናሁ ትፀንሲ ወትወልዲ ወልደ ። ኢሳ ፯ ፤ ፲፬ ሉቃ ፡ ፱ ፤ ፳፩

፴፩ እነሆ ትፀንሻለሽ ወንድ ልጅም ትወልጃለሽ ።
ወትሰምዪዮ ስሞ ኢየሱስ ።
ስሙንም ኢየሱስ ትይዋለሽ

፴፪ ውእቱ ዓቢይ ። ዳን. ፯ ፤ ፲፬ ።
፴፪ እሱ ዓቢይ እግዚአብሔር ነው
ወይሰመይ ወልደ እግዚአብሔር ልዑል ።
የልዑል የእግዚአብሔር አብ የባሕርይ ልጅ ይባላል
ወይሁቦ እግዚአብሔር መንበረ ዳዊት አቡሁ ። እግዚአብሔር አብ ያባቱን የዳዊትን ዙፋን ይሰጠዋል ፡ ሐተታ ፤ ይህማ የተነገረ ለሰሎሞን አይደለም ቢሉ ለጊዜው ለሰሎሞን ቢሆን ፍጻሜው ለጌታ ነውና ። አንድም ሰሎሞን በግዘፍ በነገሠባቸው ጌታ በርቀት ይነግሥባቸዋልና አንድም የጌታ መንግሥቱ መንበርከ እግዚኦ ለዓለመ ዓለም ብሎ በተናገረለት ሥልጣን ነውና አንድም ስምዒ ወለትየ ወርእዪ ወአጽምዒ ብሎ መንበር አድርጎ በተናገረለት በምእመናን ላይ ነውና አንድም ነገሠ መባሉ ቅሉ በሥጋ ዳዊት ነውና ዲበ መንበረ ዳዊት ትፀንእ መንግሥቱ እንዲል ።

፴፫ ወይነግሥ ለቤተ ያዕቆብ ለዓለም ።
፴፫ በያዕቆብ ወገን ለዘለዓለም ሠልጥኖ ይኖራል ።
ወአልቦ ማኅለቅት ለመንግሥቱ ።
ለጌትነቱ ፍጻሜ የለውም ።
ወርኢኩ በራዕየ ሌሊት ወመጽአ ከመ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ወበጽሐ ኀበ ብሉየ መዋዕል ወተውህበ ሎቱ መንግሥት ወምኵናን መንግሥቱኒ መንግሥት ዘለኵሉ ዓለም ወአልቦ ማኅለቅት ለመንግሥቱ እንዲል ። ታሪክ ዘፍ ፳፬ ፡ ፩ ። እግዚአብሔር ሥራውን ያለ ምክንያት አይሠራውም ለአብርሃም ኢያውብር የሚባል ዘመድ ሎሌ ነበረው በሚሞትበት ጊዜ አስጠርቶ ልጄን ይስሐቅን ሶርያ ወርደህ ከዘመዶቼ ወገን አጋባው እንጂ ከአዋልደ ከነዓን እንዳታጋባው ማል እጄን ጽፋ ጉልበቴን ምታ አለው እጄን ጽፋ ማለቱ የሰጠኸኝ አይባረክልኝ በል ሲል ነው ። ጉልበቴን ምታ ማለቱ የወለድኩት አይባረክልኝ በል ሲል ነው ። እሱም ጠንቅቆ ይምላል ያች የማመጣት ብላቴና አልመጣም ያለች እንደሆነ ወደ ነበርክበት እሱን ይገድው ልሒድን አለው ዑቅ ኢታግብእ ለወልድየሰ ባሕቱ ዘሐፀነኒ ወሴሰየኒ ይፈኑ ለከ መልአኮ እግዚአብሔር መንገድህን ያቃናልህል አምጥተህ አጋባው እንጂ እሱንስ አትውሰደው አለው ።

ከቃው መልከሙን መርጦ ዐሥር ግመል ጭኖ ሄደ ወደማታ ከውኃ ዳር አርፎ ያወጣ ያወርድ ጀመር ውሃ ከሚቀዱት ሴቶች ከጌታዬ ዘመዶች ወገን ሁና መልከ ከደም ግባት አስተባብራ የያዘች ሕፃን ሁና ውሃ አጠጭኝ ብያት አጠጥታኝ ለግመሎቼም የምታጠጣልኝ ሁና ኪያሃ አስተዳሉከ ለገብርከ ይስሐቅ ባልኩ ነበር እያለ ሲያወጣ ሲያወርድ ወእምቅድመ ያኅልቅ ተናግሮ ይላል ሐልዮ ሲል ነው ይህን ተናግሮ ሳይፈጽም ርብቃ ባጭር ታጥቃ ማድጋ ነጥቃ መጣች ። ቀድታ በምትሄድበት ጊዜ ወሃ አጠጭኝ አላት ቀድታ አጠጣችው ለግመሎችህ ላጠጣልህን አለችው ይሁን አለ እየቀዳች አጠጣችለት አስተያየቷን አረጋገጡን ይመለከታል የማንሽ ልጅ አላት ። ሜልካ ለናኮር የወለደችለት የባቱኤል ልጅ ነኝ አለችው ። ከቤትሽ ማደርያ አይገኝምን አላት ምንታጥቶ አንተ የምትበላው ዳቦ የምትጠጣው ጠጅ የምትተኛበት አልጋው ለግመሎችህ ጋጡ ገፈራው ተርፏል አለችው ።

ወእምዝ ረወዩ አግማሊሁ ነሥአ ኢያውብር አዕኑገ ዘወርቅ እንዲል ፤ ያሥር ወቄት ለሁለቱ እጆቿዋ አምባር የሁለት ወቄት ለሁለቱ ጆሮቿዋ ጉትቻ አስጊጦ ሰደዳት ላባ የሚባል ሰሱ ወንድም አላት ማን ሰጠሽ አላት እንዲህ ያለ ሰው አስጊጦ ሰደደኝ አለችው ። እንደሷ የሚያገኝ መስሎት ሄደ ።

አንተን ያህል ሰው ከዚህ ምን አንርሃል አንተ የምትበላው ዳቦ የምትጠጣው ጠጅ የምትተኛበት አልጋው ምንጣፉ ለግመሎችህ ጋጡ ገፈራው ተርፎ ከቤት ገብተህ እህል ቅምሰህ ውሃ ጠጥተህ አታርፍምን ብሎ ይዞት ሄደ ከገባ በኋላ እግርህን ታጥበህ ዕረፍ አሉት ። ጌታዬ የላከኝን ሳልናገር ሌላ ሥራ አልሠራም አለ ።

የንጉሥ መልክተኛ የታዘዘውን ሳያደርግ ሌላ ሥራ እንዳይሠራ በል ተናገር አሉት ፤ እሱም ጌታዬ አብርሃምን እልቆ አክብሮታል ካረጀ በኋላ የወለደው የሚወደው ልጅ አለው ከአዋልደ ሶርያ እንጂ ከአዋልደ ከነዓን እንዳታገባው ብሎ አምሎኛል ገንዘብ ይገድ መጥቼ ከወሀ ዳር ዐርፌ ሳወጣ ሳወርድ ይህች ብላቴና መጥች እንደምታዩት አስጊጬ ሰደድኳት ለጌታዬ ልጅ ሚስት ልትሆን ስጡኝ እናንተም ገንዘባችሁን ተቀበሉኝ አላቸው ።

እነሱም ንሕነስ ኢንክል ተናገር ኢ ሠናየ ወኢ እኩየ አሉት ። ነገር ወስኑልኝ ቁረጡልኝ እንጂ እኔማ ቀኝስ ግራስ ብል ምን አጥቼ አለ ። አማጭ ስል ማጼ የበቅሎ ክበድ የሐር ገመድ አለኝ ይላልና ይሁን ተቀመጥ አሉት አደረ ። ቢነጋ አሰናብቱኝ ገንዘባችሁን ተቀበሉኝ ልጅቷንም ስጡኝ አለ ። ዐሥር ቀን ትረፍ አሉት ኢታስተድኀሩኒ እግዚ አብሔር ነገሬን አቅንቶልኝ ሳለ አታስናክሉኝ አላ ቸው ባይሆን እሷን እንጠይቃት ብለው ጠየቋት እሄዳለሁ አለች ገንዘቡን ሰጥቶ ይዞ መጣ ይስሐቅ ወንበዴ እንዳይጣላቸው ብሎ መንገድ አላፊ መስሎ ይሰልላል አራምዳ አይታ ያማነው አለችው የም ትሄጅለት የጌታዬ ልጅ ነው አላት ።

ተራ ልብስ ለብሳ ነበርና አውርዱኝ ብላ አጊጣ ቆየች ይዟቸው ሂደ ል ይህ ሁሉ ምሳሌ ነው አብር ሃም የእግዚአብሔር አብ ኢየውብር የቅዱስ ገብር ኤል ይስሐቅ የመለኮት ርብቃ የትስብእት ፤ ዐሥሩ ወቄት ያሥሩ ቃላት ሁለቱ ወቄት የፍቅረ ቢጽና የፍቅረ እግዚአብሔር አንድም ፪ቱ ተፈሥሒ ፍሥ ሕት ኦ ምልእተ ጸጋ ቡርክት አንቲ እምአንስት ወቡሩክ ፍሬ ከርሥኪ ያለው ፤ ዐሥሩ እፎኑ ከመ ዝኑ እንጋ ካለው ጀምሮ ወአልቦ ማኅለቅት ለመ ንግሥቱ እስካለው ዓሥር ይሆናል የዚህ ምሳሌ ። ሳድስ ወርኅ ያለውም በስድስተኛው ሽህ ሲል ነው እንኳን በወር በዕለት ይመስለዋል ። በሐሙስ ዕለት ወበመንፈቀ ሌሊት እትወለድ እምወለተ ወለትከ እንዲል ።

፴፬ ትቤሎ ማርያም ለመልአክ እፎኑ ይከ ውነኒ ዝንቱ እንዘ ኢየአምር ብእሴ ።

፴፬ ወንድ ሳላውቅ መፅነስ መውለድ እንደ ምን ይሆንልኛል ፤ እምአይቴ ረከብከ ዘከመዝ ብሥ ራተ ዘእንበለ ምት እምድንግል ፅንስተ ወዘእንበለ ዘርእ እምድር ዕትወተ እንዲል ፤ ምድር ያለ ዘርዕ ታፈራ ዘንድ ሴት ያለወንድ ትፀንስ ዘንድ እንዲህ ያለ የምሥራች ከማን አገኘኸው አለችው እንዲህ ማለቷ ነገሩን ሽታው አይደለም ጥንቱን እንደምን ይሆንልኛል ነገሩን አላደርገውም ስትል ነው እንጂ ዘንተ ትቤ ድንግል በእንተ ዘኢዓርገ ሕሊና ዕጓለ እመሕያው ውስተ ልባ እንዲል ።

፴፭ አውሥአ መልአክ

፴፭ መልአኩም መለሰ

ወይቤላ መንፈስ እግዚአብሔር ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ ። ያንችማ ፅንስ መቼ እንደ ሌሎች ሴቶች ፅንስ ነዋ መንፈስ ቅዱስ ያድርብሻል ።

ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ ።

ኃይለ ልዑል ወልድ ሥጋሽን ይለብሳል አንድም መንፈስ ቅዱስ ያድርብሻል ኃይለ ልዑል ወልድ ከሦስቱ ግብራት ይከለክልሻል ወውእቱኒ ንጹሕ እምሠለስቱ ግብራት እለ ሥሩዓት በዕጓለ እመሕያው እንዲል ።

ወዘኒ ይትወለድ እምኔኪ ቅዱስ ውእቱ ።

ካንች የሚወለደውም ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ ተብለው ከሚመስገኑ ከሦስቱ ቅዱስ አንዱ ቅዱስ ነው ።

ወይሰመይ ወልደ እግዚአብሔር ልዑል ።

የልዑል እግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ ይባላል ።

፴፮ ወናሁ ኤልሳቤጥኒ እንተ ንምአዝማድኪ ይእቲኒ ፀንሰት ወረከበት ወልደ በልህቃቲሃ ወበ ርስእቲሃ ።

፴፮ ከዘመዶችሽ ወገን የምትሆን ኤልሳቤጥ ስንኳ በፍጹም እርጅናዋ ልጅ አግኝታ ፀንሳለች ። ሐተታ ፤ ኤልሳቤጥ ስንኳ ማለቱ ስለ ምን ነው ቢሉ እመቤታችን ምንም በድንግልና ቢሆን ሙቀት ልምላሜ አልተለያትም ። ኤልሳቤጥ ግን ምንም በዘር በሩካቤ ቢሆን ሙቀት ልምላሜ ተለይቷት ነበርና ። ይህማ ሙቀት ልምላሜ ሳለ በድንድልና እንዲወልዱ ፤ ሙቀት ልምላሜ ከተለየ በኋላ በዘር በሩካቤ እንዲወልዱ የሚያደርግ እሱ አይደለምን ብሎ መጽሐፍ ያለበትን ማፅናት ልማድ ነውና እን ዲህ አለ ። አንድም ከዘመዶችሽ ወገን የምትሆን ኤልሳ ቤጥ በል ።

ወናሁ ሣድስ ዝንቱ ወርኅ ለእንተ ይብልዋ መካን ።

መካን ለሚሏት ለኤልሳቤጥ ከፀነሰች እነሆ ይህ ወር ስድስተኛ ነው ።

፴፯ እስመ አልቦ ነገር ዘይስእኖ ለእግዚአ ብሔር ።

፴፯ ሙቀት ልምላሜ ሳለ እንበለ ዘርእ እን ዲወልዱ ቢያደርግ ለእግዚአብሔር የሚሳነው ነገር የለምና መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላእሌኪ ላለው ። አንድም ሙቀት ልምላሜ ከተለየ በኋላ በዘር በሩ ካቤ እንዲወልዱ ቢያደርግ የሚሳነው ነገር የለምና ወናሁ ኤልሳቤጥኒ ላለው ።

፴፰ ትቤሎ ማርያም ለመልአክ ነየ አመተ እግዚአብሔር ይኩነኒ በከመ ትቤለኒ ።

፴፰ እንዲህ ባላት ጊዜ እመቤታችን ለመል አኩ የእግዚአብሔር ገረዱ እነሆ አለሁ እንዳልከ ይሁንልኝ አለችው በዚህ ጊዜ ቃሏን ምክንያት አድ ርጎ አካላዊ ቃል በማኅፀኑዋ ተቀርጹዋል ። ሐተታ እንደ እደ ፀሐፊ ሥልጣነ እግዚአብሔር እንደ ብርአ ፀሐፊ የመንፈስ ቅዱስ በቀንዱ ያለ ቀለም የሌሎች ሴቶች ባሕርይ በብርዑ ያለ ቀለም የእመቤታችን ባሕርይ ምሳሌ እስትንፋሱ የመንፈስ ቅዱስ አልወርድ ሲለው እፍ እያለ ያወርደዋል ፤ የፈጠረ የከፈለ ያዋሐደ መንፈስ ቅዱስ ነውና ምሥጢሩ የአካላዊ ቃል ቀለሙ የትስብዕት ረቂቅ

ምሥጢር ከልቡና ሳይለይ በቀለም ገዝፎ እንዲታይ ፣ ረቂቅ አካላዊ ቃልም ከአብ አንድነት ሳይለይ በሥጋ ገዝፎ ታይቷል ። አንድም ወሀየንተ እድዘዝየ ያግኅድ ከመ እግዝእትነ ማርያም ይእቲ ይሳል ብሎ እንደ እደ ጸሐፌ ይኩንኒ ያለችው የቃሏ ምሳሌ ሐረ ወኅሰፈ እምኃቤሃ መልአክ ።
የቦታ ላለው እሷ ካለችበት ሄደ ባሕርይዋን መስለላት ላለው ተሰወራት ።

በእንተ ብጽሐት ኀበ ኤልሳቤጥ

፴፱ ወተንሥአት ማርያም ፍጡነ በውእቱ መዋዕል ወሖረት ደወለ ዓይነ ከርም ።

፴፱ እመቤታችን በዚያ ወራት ፈጥና ደጋ ደጋውን ሄደች አንድም ጮቄ ጮቄውን የክረምት ግብር ባለበት ጉም በሚሰብበት ዝናም በሚዘንብበት ለተክል የሚያስ ጡት ወሀ በሚሄድበት በስርጥ ጉዳና ሄደች ። ሐተታ ስለ ሦስት ነገር ትሄዳለች ኤልሳቤጥ ፀ ሰች ብሏታልና የኤልሳቤጥን ፅንስ ለመረዳት ዘካርያስ ታመመ ብላዋታልና ለመጠየቅ ፣ ምስክር ሦስት ለማድረግ መልአኩ መስክሯል ፣ ዮሐንስ በማኅፀን የሚሰግድ ነው ፣ ኤልሳቤጥም እሙ ለእግዚእየ የምትል ናትና ።

ወበጽሐት ሀገረ ዳዊት ዘይሁዳ ።
ይሁዳ ከሚባል አገር ደረሰች ።

፵ ወቦአት ቤተ ዘካርያስ ወአምኃታ ለኤልሳቤጥ

፵ ከዘካርያስ ቤት ገብታ ኤልሳቤጥን እንዴት ነሽ አለቻት ወሶበ ሰምዓት ኤልሳቤጥ ቃላ ለማርያም እንዘ ትትኣምኃ ኦንፈርዓፀ እጓል በውስተ ከርሣ እመቤታችን እንዴት ነሽ ስትላት ኤልሳቤጥ በሰማች ጊዜ በማኅፀኗዋ ያለ ብላቴና ሰገደ ሐተታ ፣ ሐዋርያት በሲኖዶስ ሰገደ ብለውታል ። ያሬድም ሰገደ ብሎታል ።

፵፩ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ ኤልሳቤጥ

፵፩ በኤልሳቤጥ መንፈስ ቅዱስ አደረባት ቀለ ይቷትን ያውቃል ሥራ አሰራት ሲል ነው ።

፵፪ ፣ ወከልሐት በዓቢይ ቃል ።

፵፪ ቃሏን ከፍ አድርጋ ኦስምታ ተናገረች ። ወትቤ ቡርክት አንቲ እምአንስት ።
ከሴቶች ተለይተሽ መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌላብሽ በረከተ ሥጋ በረከተ ነፍስ እያማለድሽ የምታሰጭ ነሽ ።
ወቡሩክ ፍሬ ከርሥኪ ።
የማኅፀንሽም ፍሬ መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌለበት በረከተ ሥጋ በረከተ ነፍስ የሚያድል ነው ።

፵፫ ወምንትኑ አነ ከመ ትምጽኢ ኀቤየ እሙ ለእግዚእየ ።

፵፫ የጌታዬ እናቱ እመቤቴ ወደኔ ትመጭ ዘንድ እኔ ምንድነኝ ፣ ስልማዱ ገረድ ወደ እመቤቷ ትሄዳለች እንጂ እመቤት ወደ ገረዷዋ ትመጣለችን አለቻት ።

፵፬ እስመ ናሁ ሶበ ሰማዕኩ እንዘ ትትአምኂ እንፈርዓጸ እጓል በውስተ ከርሥየ በፍሥሐ ወበኃሤት ።

፵፬ እንዴት ነሽ ስትዪኝ በሰማሁ ጊዜ በማኅፀኔ ያለ ብላቴና ደስ ብሎት ሰግዷልና ።

፵፭ ወብፅዕት እንቲ እንተ ተአምኒ ከመ ይከውን ቃለ ዘነገሩኪ እምኀበ እግዚአብሔር ።

፵፭ ከእግዚአብሔር አግኝተው የነገሩሽን ነገር እንዲደረግ የምታምኚ አንድም ከመ ይከውን ቃል ከእግዚአብሔር አግኝተው የነገሩሽ ነገር እንዲደረግ የምታምኚ አንቺ ንፅሕት ክብርት ነሽ ። ሐተታ መጽሐፍ ስም ካልጠራ ማብዛት ልማዱ ነውና የነገራት አንድ ገብርኤል ሲሆን አብዝታ ተናገረች በተአምኖ አመ ነገርዎ ለኖኅ በእንተ ዘኢያስተርኢ ግብር ዘኀቡዕ ፈርሃ እንዲል ፣ የነገረው አንድ ሱርያል ሲሆን ።

፵፮ ወትቤ ማርያም ታዓብዮ ነፍስየ ለእግዚአብሔር ።

፵፮ እመቤታችን ሰውነቴ እግዚአብሔርን ታከብረዋለች ።

፵፯ ወትትኃሠይ መንፈስየ በአምላኪየ ወመድኃኒየ ።

፵፯ ልቡናዬም በፈጣሪዬ በመድኃኒቴ አምና ደስ ይላታል አለች ። ሐተታ ፣ ከምን አድኑዋታል ቢሉ ከንዴተ ህላዌ ከልማደ አንስት ።
እሰመ ርእየ ሕማማ ለአመቱ የገረዱን የሔዋንን መከራዋን አይቷልና ። አንድም ትሕትናዋን በእግረ እጋንንት መረገጧን አይቷልና አንድም የኔን የገረዱን ትሕትናዩን አይቷልና ። ሐተታ ይህስ እንደምን ነው ቢሉ መጽሐፈ ኢሳይያስ ስትመለከት ። ናሁ ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ከሚለው አንቀጽ ብትደርስ ድንግልና እያላት ምነው እኔ በሆንኩ አላለችም እንዲህ ካለችዩቱስ ከጊዜዋ ደርሼ ወጥቼ ወርጄ አገልግያት ብላ ተመኝታለች እንጂ ኃዘኔን ሰምቷልና ምን እያለች ታዝን ነበረ ቢሉ የተቆጠረው ሱባኤ ደረሰ የተነገረው ትንቢት ቀረ እያለች ታዝን ነበረ ።

፵፰ ናሁ እምይእዜሰ ያስተበፅዑኒ ኵሉ ትውልድ ።

፵፰ ከንግዲህስ ወዲህ ትውልድ ሁሉ ያመሰ
ግኑኛል ፡፡ ሐተታ ባንድ መልአክና ባንዲት ባል
ቴት ቃል ብቻ ተመስግኘ እቀራለሁን ትውልደ
ሴም ትውልደ ካም ትውልደ ያፌት ሁሉ ያመሰግ
ኑኛል ስትል እንዲህ አለች ዙሉ አለ ከዚህ የወጣ
ትውልድ የለምና ፡፡ አንድም ፍጥረት ሲል ነው ፡፡
አራት ዘለደት እንዲል ፍጥረት ሁሉ ያመሰግኑኛል፡፡

፵፱ እስመ ገብረ ሊተ ኃይለ ዓቢያተ ፡፡
፵፱ ደግ ነገር ሥራ ሠርቶልኛልና
ሐተታ ፤ አብ ቢሉ ልጁን ወልድ ቢሉ አካሉን በጎ
ቱም ድንግልና ፀንሼ በጎቱም ድንግልና እንድወል
ደው አድርጎኛልና
ወቅዱስ ስሙ ፡፡
ይህን ያደረገልኝ ስሙ ልዩ ነው ፡፡ ሐተታ አብ
ይባላል እንጂ ወልድ መንፈስ ቅዱስ አይባልም
ወልድ ይባላል እንጂ አብ መንፈስቅዱስ አይባልም፤
መንፈስ ቅዱስ ይባላል እንጂ አብ ወልድ አይባልም

፶ ወምሕረቱ ለትውልደ ትውልድ
፶ ይቅርታውም ለልጅ ልጅ ነው ለእለ
ይፈርሁዎ ፡፡
ያው ግን ለሚያመልኩት ለሚፈሩት ፤ ሐተታ አባቷ
ዳዊት ሣህሉሰ ለእግዚአብሔር እምዓለም ወእስከ
ለዓለም ዲበ እለ ይፈርህዎ ብሎ ነበርና ከዚያ አያ
ይዛ እንዲህ አለች ፡፡

፶፩ ወገብረ ኃይለ በመዝራዕቱ ፡፡ ኢሳ . ፶፩ ፡ ፱፡፡
፶፩ አብ ቢሉ በልጁ ፡፡ ወልድ ቢሉ በሥል
ጣኑ ድጋግ ተአምራት አደረገ ፡፡
ወዘረዎሙ ለእለ ያዓብዩ ሕሊና ልቦሙ ፡፡
ትዕቢተኞች ጸሐፍት ፈሪሳውያንን አጋንንትን በተ
ናቸው ፡፡

፶፪ ወነሠቶሙ ለኃያላን እመናብርቲሆሙ ፡፡
፶፪ ኃያላን ጸሐፍት ፈሪሳውያንን ከሹመታ
ቸው ሻራቸው ከልዕልናቸው አዋረዳቸው አንድም
ኃያላን አጋንንትን ከማደሪያቸው ከሰው ለያቸው
አዕበዮሙ ለትሑታን ፡፡
ትሑታን ሐዋርያትን ዐሥራት በኵራት ቀዳምያት
ሰጥቶ ትሑታን ነፍሳትን ልዕልና ነፍስ ሰጥቶ
አከበራቸው ፡፡

፶፫ ወአጽገቦሙ እምበረከቱ ለርሁባን ፡፡ ፩ ነገ
፪ ፭ ፡፡ መዝ . ፴፫ ፡ ፲
፶፫ ዓሣ ሰጋሪ ልብደ ሠሪ የነበሩ ርሁባን
ሐዋርያትን ዐሥራት በኵራት ቀዳምያት ሰጥቶ
አጸገባቸው ርሁባን ነፍሳትን ሥጋውን ደሙን ልጅ
ነትን ሰጥቶ ደስ አሰኛቸው ፡፡
ወፈነዎሙ ዕራቆሙ ለብዑላን ዐሥራት በኵራት
ቀዳምያት ተቀብለው ይኖሩ የነበሩ ጸሐፍት ፈሪ
ሳውያንን ባዶ እጃቸውን ሰደዳቸው ብዑላን አጋንን
ትን ባዶቸውን ሰደዳቸው ፡፡

፶፬ ወተወክፎ ለእስራኤል ቍልዔሁ ፡፡
፶፬ እንዲህ አድርጎም እሥራኤል ዘሥጋን ተዋ
ሐደ ኀበ ያዕቆብ ኀድረ ወኀበ እስራኤል ተዋረሲ
እንዲል ፡፡

፶፭ ወተዘከረ ሣህሎ ዘይቤሎሙ ለአበዊነ ለአ
ብርሃም ወለዘርዑ እስከ ለዓለም ፡፡ ዘፍ ፲፯ ፡ ፱ መዝ
፻፴፩ ፡ ፪ ፡፡ ኢሳ. ፵፩ ፡ ፰ ፡፡

፶፭ ላባቶቻችን ለአብርሃም ለይስሐቅ ለያዕ
ቆብ የነገራቸውን ይቅርታውን እስከ ዘለዓለም አሰበ፡፡
፶፮ ወነበረት ማርያም ኀቤሃ መጠነ ሠለስቱ
አውራኅ ፡፡
፶፮ እመቤታችን ሦስት ወር ከኤልሳቤጥ ዘንድ
ኖረች ፡፡
ወእምድኅሬሁ አተወት ቤታ ከሦስት ወር በኋላ
ወደ ቤቷ ተመለሰች ፡፡

በእንተ ልደተ ዮሐንስ መጥምቅ ፡፡

፶፯ ወበጽሐ ዐርኃ ለኤልሳቤጥ ከመ ትለድ፤
፶፯ ኤልሳቤጥ ልጅ የምትወልድበት ጊዜው
ደረሰ ፤ ሐተታ ፤ ከዚያ ኑራ ቢሆን የመለኮት እናት
ተልእኮ ባገኘች ነበርና ፤ ይህማ እንዳይሆን ጌታ
የመጣው ለትሕትና ነው እንጅ ለልዕልና ነውን
ብሎ እመቤታችን ነማናዊት በተ መቅደስ ነችና
ኀርስ ርስሐት እንዳያገኛት ፡፡
ወወለደት ወልደ ፡፡
ወንድ ልጅ ወለደች ፡፡
፶፰ ወሰምዑ ሰምዑ አዝማዲሃ ወአግዋሪሃ ከመ
አዕበየ እግዚአብሔር ሣህሎ ላዕሌሃ ፡፡
፶፰ ጐረቤቶቿና ዘመዶቿ እግዚአብሔር ይቅ
ርታውን እንዳበዛላት ማለት ልጅ እንደሰጣት በሰሙ
ጊዜ ፡፡
ተፈሥሑ ላቲ ፡፡
በሷ ደስ አላቸው፡፡አንድም ምስሌሃ ከሷ ጋራ እንደሷ
ደስ አላቸው ፡፡ ሐተታ ፤ በትምህርቱ በትንቢቱ
ደስ ያሰኛቸዋልና ፡፡
፶፱ ወእምዝ እመ ሰሙን ዕለት መጽኡ ይግ
ዝርዎ ለሕፃን ፡፡
፶፱ ከዚህ በኋላ በስምንተኛው ቀን ሊገዝ
ሩት መጡ የሌቀ ካህናት ልጅ ነውና አክብረው
ሊገዝሩት መጡ አለ ፡፡ ሌሎቹን ግን እያመጡላ
ቸው ይገዝሩ ነበር ፡፡ ሐተታ ወይም ዝቅ ብሎ
ቢሆን ሰ ነቱ ልሕሉሕ ይሆናል ወይም ከፍ ብሎ
ቢሆን ሰውነቱ ያጠናል ይሰማዋልና አማካይ ቀን
ሽተው ፡፡ ምስጢሩ ግን የሰምንቱ ብሔረ አሪት ምግ
ብና ሲፈጸም ግዝረተ ነፍስ የሰምንቱ ሺህ ምግብና
ሲፈጸም ግዝረተ ሥጋ ሶሰው እንዲሰጠው ለማጠየቅ
ወይሰምይዎ በስመ አቡሁ ዘካርያስ ፡፡
ባባቱ ስም ዘካርያስ ይሉት ዘንድ ፡፡ ሐተታ እኛ
ዛሬ ለወንድ ልጅ ባርባ ቀን ለሴት ልጅ በሰማንያ

ቀን በዕለተ ጥምቀት ስም እንድናወጣ እነሱም በዕ ለተ ግዝረት ስም ያወጡ ነበርና ።

፷ ወአውሥአት እሙ
፷ እናቱም መለሰች
ወትቤ አልቦ ። አይሆንም
አላ ዮሐንስ ይሰመይ ስሙ ።
ስሙ ዮሐንስ ይባል እንጂ አለች ።

፷፩ ወይቤልዋ አልቦ እምአዝማድኪ ዘከማሁ ስሙ ።

፷፩ ከዘመዶችሽ ወገን እንዲህ ያለ ስም የለ እንደምን ይሆናል አሏት ።

፷፪ ወቀጸብዎ ለአቡሁ
፷፪ አባቱን ጠቀሱት
ወይቤልዎ መነ ትፈቅድ ይሰምይዎ ።
ሴት ብታውቅ በወንድ ያልቅ ነውና ማን ቢሉት ትወዳለህ አሉት ።

፷፫ ወስአለ ሰውሐ ። ሉቃ ፩ ፲፫
፷፫ ዓይኑ ዓ ነው ያሉ እንደሆነ ጻፈ አልፋው አ ነው ያሉ እንደሆነ ብር ቀርጻችሁ ብራና ደምጣ ችሁ ቀለም በጥብጣችሁ ስጡኝ ብሎ ለመነ ።

ወጸሐፈ እንዘ ይብል ዮሐንስ ይሰመይ ስሙ ስሙ ዮሐንስ ይባል ብሎ ጻፈ ።

ዮሐንስ ይሰመይ ስምንቱን ቀለም ጽፎ ከዚህ በኋላ ተናግሯል ሰው ሁሉ የስምንቱ ብሔረ አሪት የስ ምንቱ ሽህ ምግብና ሲፈጸም በልሳነ ነፍስ እንዲናገር ያጠይቃል አንድም ዮሐንስ ይሰመይ ስሙ ብሎ ፲ን ጽፎ ተናግሯል ያሥሩ ቃላት ምግብና ሲፈጸም ሰው ሁሉ በልሳነ ነፍስ እንዲናገር ያጠይቃል ።

፷፬ ወአንከሩ ኵሎሙ ።
፷፬ ሁሉም አደነቁ ።
ወከሠተ አፉሁ ወነበበ ።
አንደበቱ ረቶ ተናገረ ።
ወባረኮ ለእግዚአብሔር ።
እሱም እግዚአብሔርን አመሰገነ ። ሐተታ ከዚህ ጊዜ ያደረሰኸኝ ብሎ ።
፷፭ ወኮነ ፍርሃት ላዕለ ኵሉ ሰብእ ዘውእቱ ብሔር ወላዕለ ኵሉ ደወለ ይሁዳ ።
፷፭ በይሁዳና በዚያ አገር ባሉ ሰዎች ሁሉ የአንክሮ ፍርሃት አደረባቸው ።
ወተናገርዎ ለዝንቱ ነገር ላዕለ ኵሉ ደወለ ይሁዳ።
በይሁዳ አውራጃ ሁሉ ይህን ነገር ተጫወቱት ።
፷፮ ወዓቀብዎ በልቦሙ እለ ሰምዕዎ
፷፮ የሰሙት ሁሉ በልቡናቸው አስተዋሉት።
ወእሙሰ ተዓቅብ ዘንተ ኵሎ ነገረ ወትወድዮ ውስተ ልባ እንዲል ።
ወይቤሉ ምንትኑ ይከውን እምዝንቱ ሕፃን ።

ከዚህ ሕፃን የተነሣ ምን ይሆን አንድም ይህ ብላ ቴና እንደምን ያለ ይሆን እንደ ኖኅ አበ አንጋድ እንደ ሙሴ ጠላት ይገድል ባሕር ይከፍል ደመና ይጋርድ መና ያወርድ እንደ ኢያሱ በረድ ያዘንም ፀሐይ ያቆም እንደ ጌዴዎን ጸምር ይዘረጋ ጠል ያወርድ እንደ ኤልያስ ሰማይ ይለጉም እሳት ያዘንም ይሆን አሉ ።
እስመ እደ እግዚአብሔር ላዕሌሁ ።
የእግዚአብሔር ኃይል አድሮበታልና ።

፷፯ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ ዘካርያስ አቡሁ ።

፷፯ በዘካርያስ መንፈስ ቅዱስ አደረበት ። ሐተታ ተለይቶትን ያውቃል ቢሉ ሥራ አሠራው ሲል ነው ።
ተነበየ ወይቤ ። ተነበየ ብሎ አንድ እርእስት ይቤ ብሎ ፪ት እርእስት ተናገረ ፣ለሁለቱም ያመጣል ፣

፷፰ ይትባረክ እግዚአብሔር አምላከ እስራ ኤል ዘተሣሀለነ ወገብረ መድኃኒተ ለሕዝበ ዚአሁ መዝ ፻፲፥ ፲፪ ።

፷፰ ይቅር ያለን ለወገኖቹ ደኅንነትን ያደረ ገልን የእስራኤል ፈጣሪ እግዚአብሔር ይከበር ይመ ስገን ብሎ ተናገረ ።

፷፱ አንሥአ ለነ ቀርነ መድኃኒትነ እምቤተ ዳዊት ገብሩ ። መዝ ፤ ፻፴፩ ፥ ፲፰ ።

፷፱ ከባለሟሉ ከዳዊት ወገን የምንድንበት ክር ስቶስን ያሥነሣልን ። ሐተታ ፤ ቀርን ሾለው እንስ ሳት በቀንዳቸው ድል እንዲያደርጉ ምእመናንም በሱ አጋንንትን መናፍቃንን ድል ይነሱበታልና ብከ ንወግዖሙ ለኵሎሙ ፀርነ እንዲል አንድም አራት ሽቱ አምስተኛ በዘይት አጣፍጠው በቀንድ አድርገው ያኖራሉ መንግሥት የሚገባቸው ከቤተ ይሁዳ የተወለዱ ቀኝ እካላቸውን ተቀብተው መን ግሥትን ። ክህነት የሚገባቸው ከቤተ ሌዊ የተወለዱ ቀኝ አካላቸውን ተቀብተው ክህነትን እጅ ያደር ጋሉ እሱም እንደ አራት ሽቱ አራቱን ባሕርያተ ሥጋ እንደ አምስተኛ ዘይት ባሕርየ ነፍስን ነሥቶ ክህነትን መንግሥትን ሶሬሱ ገንዘብ አድርጎ ለም እመናን የሚያድል ሁኗልና

፸ በከመ ነበበ በአፈ ነቢያቲሁ ቅዱሳን እለ እምዓለም ኤር ፳፫ ፡ ፮ ።

፸ እለ እምሰብእ እለ እምጥንት ሲል ነው ከሰው ወገን በሚሆኑ ከጥንት በነበሩ ንፁዳን ፣ ከቡራን በሚሆኑ በነቢያት አድሮ እንደተናገረ ።

፸፩ ከመ ያድኅነነ እምእደ ፀርነ ።
፸፩ ከጠላቶቻችን እጅ ያድነን ዘንድ ።

ወእምእደ ኵሎሙ እለ ይጸልዑነ ።
ከሚጠሉንም ሁሉ እጅ ማለት ከአኩያት ፍትወ ታት ኃጣውእ ያድነን ዘንድ ።ሐተታ የሚያጣሉን ስለሆነ ይጸልዑነ አለ ።

፸፪ ከመ ይግበር ሣህሎ ምስለ አበዊነ ።
፸፪ ላባቶቻችን ያደረገውን ላባቶቻችን እን ዳደረገላቸው ከባቶቻችን ጋራ ይቅርታውን ያደርግ ዘንድ ።
ወከመ ይዘክር ኪዳኖ ቅዱሰ ዕሩዕ መሐላውን ያስብ ዘንድ

፸፫ መሐላሁ ዘመሐለ ለአብርሃም አቡነ ።
ዘፍ ፳፪፣፲፯ ፣ ኤር ፴፩፣፴፫ ፣ዕብ ፩፣፲፫ ።

፸፫ መሐላውም ላባታችን ለአብርሃም የማ ለው ነው ።

፸፬ ከመ የሀበነ በዘኢንፈርሀ እምእደ ፀርነ።
፸፬ በጠላቶቻችን በአጋንንት እጅ የተወረወ ረው ጦር የተጣለው ጠ‹ ር ያገኘናል ብለን በማ ንፈራ ገንዘብ የማንፈራበትን ሥጋውን ደሙን ልጅ ነትን ይሰጠን ዘንድ ።

፸፭ ያድኅነነ ናምልኮ በጽድቅ ወበርትዕ ።
፸፭ በጽድቀ አሚን ጸንተን በንጽሐ ጠባይዕ ሁነን እናምነው ዘንድ ። አንድም በወንጌል በአ ራት ሁነን እናምልከው ያድነን ።
በቅድሜሁ ።
እሉ ባለበት ዘመን ምስት ዓመት ከምስት ወር ።
ወበኵሉ መዋዕሊነ ።
እኛ ባለንበትም ዘመን ሁሉ አንድም በቅድሜሁ በኵሉ መዋዕሊነ ፣እሱ ባወቀው ባለንበት ዘመን ሁሉ አምልከነው ያድነን ዘንድ ።

፸፮ ወአንተኒ ሕፃን ነቢየ ልዑል ትሰመይ ።
ሚል ፬፣፫ ሉቃ ፩፣፲፯ ።

፸፮ ይቤ ለለው ጨርሶ ተነበየ ላለው እመጣ አንተም ብላቴና ልዑል እግዚአብሔር የሾመህ መም ህር ትባላለህ ።
እስመ ተሐውር ቅድመ እግዚአብሔር ከመ ትጺሕ ፍኖቶ መንገድ ልትጸርግ በእግዚአብሔር ፊት ትሔ ዳለህ ማለት ሰውን ከኃጢአት ከጣዖት ትለይ ዘንድ መንፈቅ ተቀድመህ ታስተምራለህና ።

፸፯ ከመ ተሀቦሙ ያእምሩ መድኃኒቶሙ ።
፸፯ ተሀቦሙ መድኃኒቶሙ ያእምሩ መድኃ ኒቶሙ ብለሕ ግጠም መድኃኒታቸው ክርስቶስን ነዋ በግዕ ብለህ ትዳርጋቸው ዘንድ ። ያእምሩ ሊያውቁ አንድም መድኃኒታቸው ክርስቶስን ሊያውቁ ታስ ተምራቸው ዘንድ ።

፸፰ በዘይትኃደግ ሎሙ ኃጢአቶሙ በሣህሉ ወበምሕረቱ ለአምላክነ ለዘሐወፀነ እምአርያም ዘካ ፫፣፱ ፣ ሚል ፬ ፣ ፪ ።

፸፰ ለና ለ አንድ ወገን ከአርያም ወርዶ በኃ በኘን በፈጣሪያችን ይቅርታና ቸርነት ኃጢአታ ቸውን በሚስረይላቸው ገንዘብ ይስረይላቸው ዘንድ፤

፸፱ ወሠረቀ ከመ ያርዕዮሙ ብርሃኖ ለእለ ይነ ብሩ ውስተ ጽልሙት ወጽላሎተ ሞት ።

፸፱ በድንቁርና በቀቢጸ ተስፋ ላሉ ዕውቀ ትን ይገልጽ ዘንድ ተወለደ ።
ከመ ያርትዕ እገሪነ ውስተ ፍኖተ ሰላም ።
እግረ ሕሊናችንን ወደወንጌል ጎዳና ያቃናልን ዘንድ

፹ ወልኅቀ ሕፃን ።
ብላቴናው አደገ ።

፹ ወፀንዐ በመንፈስ ቅዱስ ።
በመንፈስ ቅዱስ ጸና ። ሐተታ ልጅ የሚያሳድግ ብቻ ጣቢታ አይደለም ኃይል እልኀቂተ ኵሉ አለ ችና ጸንዓ በመንፈስ ቅዱስ አለ ።
ወነበረ ኀቅለ እስከ እመ ያገይሥዎ ኀበ እሥራኤል ምክራቸው አስተምራቸው ብ/ው ሥላሴ ወደ እሥ ራኤል በመምህርነት እስኪያማልዱት ድረስ አን ድም እስራኤል ምክረን አስተምረን ብለው በመ ምሕርነት እስኪማልዱት ድረስ በበረሃ ኖረ ። አን ድም እስከ እመ ያስተርኢ ሎሙ ለ'ሥራኤል ይላል አብነትለእሥራኤል በመምህርነት እስኪ ገለጽ ድረስ በበረሃ ኖረ ።

## በእንተ ልደተ ኢየሱስ ።

### ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወኮነ በውእቱ መዋዕል ወፅአ ትእዛዝ እም ኀበ አውግሥጦስ ቄሣር ከመ ይጸሐፍ ኵሉ ዓለም።

፩ ኮነ ያለውን ወጽአ ብሎ አመጣው ሰው ሁሉ ከግብር ይቈጠር ዘንድ በዚያ ወራት ከአውግ ሥጦስ ቄሣር ትእዛዝ ወጣ ጸሐፊዮ ለውእቱ ብእሲ ከመ ዘሞተ እንዲል ። ሐተታ ፣ አውግሥጦስ ማለት ሠጣጤ ከርሥ ቄሣር ማለት ጸዳል ማለት ነው ይህስ እንዳይሆን ጌታ በዘመኑ ተወዷል ብሎ አውግሥጦስ ማለት ፀዳል ማለት ነው ። ቄሣር ማለት ሠጣጤ ከርሥ ማለት ነው ። ታሪክ የሮም ንጉሥ ካንድ ጕልማሳ ሚስት ያለ ፈቃዷ ደረሰባት ባሏን ትወድ ነበርና ያለ ፈቃዴ ደረሰብኝ ብላ ታንቃ ሞተች ፣ ወንድሞቹዋ እኅታችን የሞተች እንጂ በሱ ምክንያት ነው ብለው ከቤተ ጣዖት ገብቶ ሲወጣ ሸምቀው ገደሉት ኋላ ሕዝቡ እሱስ እሷስ የሞቱ አንድ ሰው ብናሠለጥን አይደለም ብለው ነገር የሚወስኑላቸው መቶ ሃያ ባውላ ሹመ ዋል ከመቶ ሃያው ባውላ ያንዱ ባውላ ሚስት ፀንሳ ሳለች በምትወልድበት ጊዜ ሞተች ገንዘው እንቀ ብራለን ሲሉ ፅንስ ተንቀሳቀሰ ሕያውን ከምውት ጋር እንቀብራለን ብለው ሆዷን ቀደው አወጡት

አደገ ኃያል ምሑረ ጸብእ ሆነ እኔህን ሁሉ አጥ
ፍቶ ነግሷል እንድም ኃይለኛ ጠላች ተነሥቶባቸው
አጥፋልንና እናነግሥሃስን ብለውት አጥፍቶላቸው
አንግሠውታል ፨ ከባውላው ወገን ስለ ተወለደ
ብልዮስ ቄሣር ብለውታል ፤ ብልዮስ ቄሣር ጋብዮስ
ቄሣርን ጋብዮስ ቄሣር አውግሥጦስ ቄሣርን ፤ ይወ
ልዳል ይህ ሦስተኛ ቄሣር ነው ፨

፪ ወውእቱ ጸሐፍ ቀዳሚ ፨

፪ ይህ ቍጽር መጀመሪያ ነው ፨
አመ ቄሬኔዎስ መስፍን ለሶርያ ቄሬኔዎስ ለሶርያ
ደጃዝማች ተሹሞ በነበረ ጊዜ እንድም ወውእቱ
ጸሐፈ ቀዳሚ ይላል አብነት አሱ መጀመሪያ ቈጠረ፨

፫ ወሖረ ኵሉ ሰብእ ይጸሐፍ በበ ሀገሩ ፨

፫ ሰው ሁሉ በየሀገሩ ከግብር ይቈጠር ዘንድ
ሔደ ፨

፬ ወዓርገ ዮሴፍኒ እምገሊላ እምሀገረ ናዝ
ሬት መንገለ ይሁዳ ኀበ ሀገረ ዳዊት እንተ ስማ ቤተ
ልሔም ፨ ፩ ነገ ፳፮ ሚክ ፭ ፤ ፪ ፤ ማቴ ፤ ፪፤ ፮፨

፬ ዮሴፍም ናዝሬት ከምትባል ሀገር ከገሊላ
ቤተ ልሔም ወደምትባል የዳዊት ሀገር ወደ ምት
ሆን ወደ ይሁዳ ወጣ ፨
እስመ ውእቱ ኮነ እምቤተ ዳዊት ውእቱ ፨
ከዳዊት ወገን ነውና ፨
ወእምአዝማደ ቤቱ ውእቱ ፨
ከዘመዶቹ ወገን ነውና ፨

፭ ወሖረ ይጸሐፍ ምስለ ማርያም እንተ ፈኃሩ
ሎቱ እንዘ ፅንስት ይእቲ ፨
ሖረ ምስለ ማርያም ይጸሐፍ ምስለ ማርያም ብለህ
ግጠም ፨

፭ ከጮኛው ከመቤታችን ጋራ ጸንሳ ሳለች
ይቈጠር ዘንድ ሄደ ፨

፮ ወእምዝ እንዘ ሀሎዉ ህየ በጽሐ ዕለተ
ወሊዶታ ፨

፮ ከዚህ በኋላ በዚያ ሳሉ የምትወልድበት
ጊዜ ደረሰ ፨

፯ ወወለደት ወልደ ዘበኵራ ፨

፯ የበኵር ልጅዋን ወለደች ፨
ወአሠረቶ መንኮብያቲሁ ፨
አውራ ጣቱን አሠረችው ሐተታ ፤ያጸናዋልና ፤
ምትሐት እንዳይደለ ለማጠየቅ እንድም በዛራ ልማድ
እንድም ዮሴፍ ኒቆዲሞስ እንዲሀ አድርገው ይገ
ንዙሃል ስትል ፨
ወአስከበቶ ውስተ ጎል ፨
በበረት አኖረችው እስመ አልቦሙ መካን ለማኅ
ደሮሙ ብሎ እንዲያመጣው ቦታ የላቸውምና እን
ድም ላሕምኒ አእመረ ዘአጥረዮ እድግኒ ምቅግሀ
ይላል ፤ እህያ ላህም አምኃ አስትንፋስን ገበሩ የሚል
ነው ፤ እስተማወቅዎ እስትንፋስ እድግ ወላህም
በመዋዕለ ቍር እንዲል ፨
ወጠብለሎቶ በአጽርቅት ፨
በጨርቅ ጠቀለለችው ብታጣ እንድም ምትሐት
እንዳይደለ ለማጠየቅ ፨ እንድም ዮሴፍ ኒቆዲሞስ
በድርብ በፍታ እንዲሀ ይገንዙሃል ስትል እንድም
ከሀናት ዕለት ዕለት ሥጋህን ይጠቀልሉታል ስትል
እስመ አልቦሙ መካን ውስተ ማኅደሮሙ ፨
ለማደሪያቸው ቦታ አልነበራቸውምና አስከበቶ ላለው

፰ ወሀለው ናሎት ውስተ ውእቱ ብሔር ይተ
ግሑ ወይሄልው

፰ በዚያ ሀገር ተግተው የሚጠብቁ ጠባቆች
ነበሩ ፨
ወየዓቅቡ መራዕዪሆሙ ሌሊተ በበዕብሬቶሙ ፨
በየፈረቃቸው ተግተው መንጋቸውን የሚጠብቁ ፤
ሐተታ ቀዳማይ አካች ካልዓይ አካች ሣልሳይ
አካች ፨ ራብዓይ አካች እንዲሉ ዐሥራ ሁለቱን
ሰዓተ መዓልት ካራት ተካፍለው ይጠብቃሉ ሦስት
ሦስት ይደርሳቸዋልና በበዕብሬቶሙ አለ ፨

፱ ወናሁ ቆመ መልአከ እግዚአብሔር ኀቤ
ሆሙ ፨

፱ እነሆ ከእግዚአብሔር የታዘዘ መልአክ ባጠ
ገባቸው ቆመ ፨
ወስብሐተ እግዚአብሔር ሠረቀ ላዕሌሆሙ ፨
ከቤተ ልሔም እሳቸው እስካሉበት ድረስ ባሕረ
ብርሃን ፈሰሰላቸው እንድም በረቀ ይላል አልፎ
አልፎ እንደ መስቀል መብራት ቦግ ቦግ ብሎ ታየ፨
ወፈርሁ ዓቢየ ፍርሃተ ፨
ፈጽመው ፈሩ ፨

፲ ወይቤሎሙ መልአክ ኢትፍርሁ ፨

፲ መልአኩ እይዟችሁ አትፍሩ አላቸው ፨
እስመ ናሁ እዜንወክሙ ዐቢየ ዜና ዘይከውን ፍሥሐ
ለክሙ ወላኵሉ ሕዝብ ፨
ሐተታ ለመልአኩ ፍርሃት አርቆ መናገር ልማድ
ነው ኢትፍራህ ዘካርያስ እንዲል ፨ እናንተን ስውንም
ሁሉ ደስ የሚያሰኝ ነገር እነግራችኋለሁ ፨

፲፩ እስመ ናሁ ተወልደ ለክሙ ዮም መድኅን
ዘውእቱ ክርስቶስ እግዚእ ቡሩክ በሀገረ ዳዊት ፨

፲፩ መርገመ ሥጋ መርገመ ነፍስ የሌለበት
በረከተ ሥጋ በረከተ ነፍስ የሚያድል የዓለም መድ
ኃኒት የሚሆን የባሕርይ አምላክ ክርስቶስ በዳዊት
ከተማ በዳዊት ባሕርይ ተወልዷልና ፨

፲፪ ወከመዝ ትእምርቱ ለክሙ ፨

፲፪ ምልክቱ ይህ ነው ፨
ትረክቡ ሕፃነ አሱረ መንኮብያቲሁ ፨
ሕፃኑ አውራ ጣቱን ታስሮ ወጥብሉለ በአጽርቅት
በጨርቅ ተጠቅሎ ፨

ወስኩብ ውስተ ጎል ፤
በበረት ተኛሎ ታገኙታላችሁ ።

፲፫ ወግብተ መጽኡ ምስለ ውእቱ መልአክ ብዙኃን ሐራ ሰማይ ።

፲፫ ከዚያ መልአክ ጋራ ብዙ መላእክት ነጉደው ሲመጡ ተሰሙ ።
ይሴብሕዎ ለእግዚአብሔር ።
እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ።

፲፬ ወይብሉ ስብሐት ለእግዚአብሔር በሰማያት
፲፬ አምላክ ለሆነ ሥጋ ከሥላሴ ጋራ ባንድነት ምስጋና ይገባዋል ወሰላም በምድር ለዕጓለ እመሕያው ሥምረቱ ።
የሰው ግዕዛኑ ይሰጥው ዘንድ በምድርም ዕርቅ ተወጠነ እያሉ ፩ም ስብሐት ለእግዚአብሔር እያልክ መልስ ንባብ አትሻ አምላክ ሰው ሆነ ።
ወሰላም በምድር
ሰው አምላክ ሆነ እያሉ ።
ሥምረቱ ለሰብእ ።
የሰው ፍቅር አገብሮት አምላክ ሰው ቢሆን ሰው አምላክ ሆነ ላሰው ። አንድም ስብሐት ለእግዚአብሔር በሰማያት በመላእክት ዘንድ ምስጋና ተደረገ በቦታቸው በልዕልናቸው ሰማያት አላቸው ። ወሰላም በምድር ወደቂቀ አዳም ዘንድ አንድነት ሆነ ። የም አሐዱ መርዔተ ኮኑ መላእክት ወሰብእ ከመ ይሰብሕዎ ለክርስቶስ በቃለ አሚን እንዲል መላእክት ከኖሎት ኖሎት ከመላእክት ጋራ አንድ ሁነው አመስግነዋልና ለዕጓለ እመሕያው ሥምረቱ የሰው ፍቅር አገብሮት አምላክ ሰው ቢሆን የሁለቱም መፍቻ ።

፲፭ ወእምዝ ዓሪጎሙ መላእክት እምኅቤሆሙ ውስተ ሰማይ ።
፲፭ መላእክት ከሳቸው ተለይተው ወደሰማይ ከወጡ በኋላ ።
ይቤሉ እሙንቱ ሰብእ ኖሎት ንሑር እስከ ቤተ ልሔም ።
እነዚያ ጠባቆች እስከ ቤተ ልሔም ድረስ እንሂድ። ወናእምር ዘንተ ነገረ ዘአርአየነ እግዚአብሔር ። እግዚአብሔር የገለጸልንን ነገር እንወቅ አሉ ። ሐተታ ከዚያ መልአክ አለ ከዚህ እግዚአብሔር አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም መልአክ ካለበት እግዚአብሔር እግዚአብሔር ካለበት መልአክ አይለይምና ።
፲፮ ወሖሩ ፍጡነ ።
፲፮ ፈጥነው ሄዱ ።
ወረከብዎሙ ለማርያም ወለዮሴፍ ።
ዮሴፍንና እመቤታችንን
ወሕፃንኒ ይሰክብ ውስተ ጎል ሕፃኑም በጎል ተኝቶ አገኙዋቸው ።

፲፯ ወርእዮሙ አእመሩ ከመ በእንተ ሕፃን ዘነገርዎሙ ።

፲፯ አይተው የነገሯቸው ስለ ሕፃኑ እንደ ሆነ አወቁ ።

፲፰ ወኵሎሙ እለ ሰምዑ አንከሩ ዘነገርዎሙ ኖሎት ።

፲፰ መላእክት የነገሯቸው ኖሎት አይተው ። እንድም የነገሯቸው ኖሎት አይተው እንድም ኖሎት የነገሯቸው ሌሎች ሰምተው አደነቁ ።

፲፱ ወማርያምሰ ተዓቀብ ዘንተ ኵሎ ነገረ ወትወድዮ ውስተ ልባ ።
፲፱ እመቤታችን ግን ይህን ነገር ታስተውለው ነበር በልቡናዋም ታኖረው ነበር ።
፳ ወተመይጡ ኖሎት እንዘ ይሴብሕዎ ወየአኵትዎ ለእግዚአብሔር በእንተ ኵሉ ዘርእዩ ወሰምዑ ዘከመ ይቤልዎሙ ።
፳ እንደ ነገሯቸው ስላዩት ስለሰሙት ነገር ሁሉ እግዚአብሔርን እያመሰገኑት ጠባቆች ተመለሱ ። እንዲህ ያለ ምሥጢር የገለጽክልን ተመስገን እያሉ ።

ዘከመ ተገዝረ ኢየሱስ ወዘከመ አቀምዎ ውስተ ቤተ መቅደስ ።

፳፩ ወአመ ተፈጸመ ሰሙነ ዕለት ወሰድዎ ለሕፃን ከመ ይግዝርዎ ዘፀ. ፲፫፥፲፪ ዘሌዋ. ፲፪፥፫ ማቴ ፩፥፳፩ ሉቃ ፩፥፴፩ ።
በስምንተኛው ቀን ሊገዝሩት ወሰዱት ።
ወሰመይዎ ስሞ ኢየሱስ በከመ ሰመዮ መልአክ እምቅድመ ትፅንሶ በከርሣ ።
መልአኩ ሳትጸንሰው ኢየሱስ ትዪዋለሽ ብሎ እንደ ተናገረ ስሙንም ኢየሱስ ይሉት ዘንድ ። ሐተታ ዮሐንስን የሊቀ ካህናት ልጅ ነው ብለው አክብረው ሊገዝሩት መጡ አለ ፤ ጌታ ግን መምጣቱ ለትሕትና ነው እንጂ ለልዕልና አይደለምና ወሰዱት አለ ፤ ሃይማኖተ አበው ዝንቱ ዘተገዝረ እመ ሳምን ዕለት ዝንቱ ዘገዘርዎ በሥርዓተ ሕፃናት ይላል ስንክሣር አልተገዘረም አለ ። እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ስንክሣር ምን ቁም ነገር ነው ነገር እንደ ሃይማኖተ አበው ነው ፤ ይህስ ስንክሣርን መንቀፍ ሃይማኖተ አበውንም መንቀፍ ነው መላሻቸው አንድ ነው ብሎ ገዛሪው ምላጭ ይዞ ቀርቧል ወዳጄ ልትገዝረኝ መጣህ ቢለው ምላጩ እንደ ሰም ቀልጦበታል ከዕለተ ዓርብ አስቀድሞ ደሙ አይፈስምና እሱ በተአምራት ተገዝሯል ሃይማኖተ አበው መገዘሩን ሲያይ ተገዘረ አለ ። ስንክሣር በገዛሪ እጅ አለመገዘሩን ሲያይ አልተገዘረም አለ ።
፳፪ ወአመ ተፈጸመ ዕድሜ ንጽሖሙ ዘሌ ፲፪ ፩ ዘፀ ፲፫፥፪ ዘኍ ፰፥፲፯ ።

፳፪ ከሕርስ ደም የሚነጹበት ቀን በደረስ ጊዜ ሐተታ ፥ በሌሎች ሴቶች ልማድ መናገር ነው እንጂ በመቤታችንስ ይህ ሁሉ የለባትም አንድም ከስው የሚለዩበት ቀን በተፈጸመ ጊዜ ለወንድ ባርባ ቀን ለሴት በስማንያ ቀን ።
በከመ ሕገ ሙሴ ወሰድዎ ኢየሩሳሌም ያቅምዎ ቅድመ እግዚአብሔር ።
ከእግዚአብሔር ፊት ሊያቆሙት ማለት እንደ ኦሪት ሥርዓት አጅ ያስነሱት ዘንድ ወደ ቤተ መቅደስ ወሰዱት ።

፳፫ በከመ ጽሑፍ ውስተ ሕገ እግዚአብሔር ኵሉ ተባዕት ዘይፈትሕ ማኅፀነ እሙ ቅዱሰ ይስመይ ለእግዚአብሔር ።

፳፫ በኵር ሁኖ የሚወለደው ሁሉ የእግዚአብሔር ልዩ አገልጋይ ይባላል ተብሎ በኦሪት እንደ ተጻፈ ። ሐተታ ፊታሒውስ አባቱ ነው መገለጫውን ሲያይ እንዲህ አለ እንጂ ።

፳፬ ወከመ ያብኡ መሥዋዕተ በከመ ተብህለ ውስተ ሕገ እግዚአብሔር ።

፳፬ በኦሪት እንደ ተነገረ ስለ እሱ መሥዋዕት ያቀርቡለት ዘንድ ።
ዘውገ ማዕነቅ ።
የዋኖስ ወገን ቡላል ፥ የቡላል ወገን ዋኖስ አንድም ሁለት ቡላል ሁለት ዋኖስ ዘውገ እልባስ እንዲል ።
ወእመ አኮ ከልኤቲ ዕጐለ ርግብ ።
ይህም ባይገኝ ሁለት ርግብ ሊሠውለት ሐተታ ፥ አንዱን ሠውቶ ውሃ በብርት አድርጎ ደሟን ይቀበለዋል ባንዲቱ እየነከረ ይረጭባታልእስሚዛ እንዶድ አውባን ቅጠል የተጐነጐነ ሐር ጽሕመ ጠሊ ጨምሮ ይረጭበታል ኋላ ፈትቶ ከበረሐ ወስዶ ይጥላታል የተሰዋችዪቱ የጽድቅ የወንጌል ያልተሠዋችዪቱ የኦሪት የኃጢአት ምሳሌ ።

፳፭ ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ በኢየሩሳሌም ዘስሙ ስምዖን ።

፳፭ በኢየሩሳሌም ስምዖን የሚባል አንድ ሰው ነበረ ።
ወውእቱ ጻድቅ ።
እሱም ደግ ።
ወየዋህ ።
ቅን ኃዳጌ በቀል ነበረ ።
ወይሴፈው ይርአይ ፍሥሓሆሙ ወመድኃኒቶሙ ለእሥራኤል ።
የእሥራኤልን ድኅነት ያይ ዘንድ ተስፋ ያደርግ ነበረ ።
ወመንፈስ ቅዱስ ላዕሌሁ ።
መንፈስ ቅዱስ አድሮበታል ያደረበት ነበር ።

፳፮ ወአርአዮ መንፈስ ቅዱስ ከመ ኢይመውት ዘእንበለ ይርአይ መሲሐ ለእግዚአብሔር ።

፳፮ እግዚአብሔር በተዋሕዶ ያከበረው ወልድን ሳያይ እንዳይሞት መንፈስ ቅዱስ ነግሮት ነበር ።

ታሪክ ፤ በጥሊሞስ የሚባል ገናና ንጉሥ ነበረ ከገናንነቱ የተነሣ ይህን ዓለም እንደ ሰም አቅልጦ እንደ ገል ቀጥቅጦ ገዝቶታል ያገሩን ሁሉ ቋንቋ ያውቅ ነበር ። ምን ቀረኝ ብሎ ጠየቀ ብዙ ጥበብ ብዙ ምሳሌ ያለባቸው አርባ ስድስቱ መጻሕፍተ ብሉያት ቀርተውሃል አሉት በዚያ ወራት በእሥራኤል ሠልጥኖባቸዋልና ጸሐፍቱንም መጻሕፍቱንም ስደዱልኝ ብሎ ላከ አርባ ስድስቱን መጻሕፍተ ብሉያት ሰባ ሁለት ጸሐፍት አድርገው ሰደዱለት ሁለቱ ከመንገድ ሙተው ቀርተዋል ለሰባው የሚላካቸው አንድ አንድ ብላቴና እያደረገ ለሁለት ለሁለት እንዳንድ ድንኳን ሰጣቸው ሠላሳ አምስት ይሆናል ታናናሹን እንዳንድ ደጋጉን ለሁለት ለሁለት የዕብራይስጡን በጽርዕ ቋንቋ ጻፉ ብሎ ሰጣቸው ።

መጽሐፈ ኢሳይያስ ለስምዖን ደረሰው ።ሲጽፍ ናሁ ድንግል ትፀንስ ወትወልድ ወልደ ከሚለው አንቀጽ ደረሰ ። ድንግል በድንግልና ትጸንሳለች በድንግልና ትወልዳለች ብዬ ብጽፍ ስንኳን የአሕዛብ ንጉሥ የእሥራኤልስ ንጉሥ ቢሆን ይቀበለኛል ብሎ ወለት ትጸንስ ብሎ ጻፈ ። እንቅልፍ መጥቶበት ተኝቶ ቢነቃ ወለትን ፍቆ ድንግልን ጽፎ አገኘ ። ድንግልን ፍቆ ወለት ብሎ ጻፈ ። ሁለተኛ እንቅልፍ መጥቶበት ተኛ ቢነቃ ወለትን ፍቆ ድንግልን ጽፎ አገኘው ድንግልን ፍቶ ወለትን ጽፎ ሦስተኛ እንቅልፍ መጥቶበት ተኛ ቢነቃ ወለትን ፍቆ ድንግልን ጽፎ አገኘው ። እፍቃለሁ ሲል ኢትመውት ዘእንበለ ትርአይ መሲሐ ለእግዚአብሔር ብሎ ይህን ነግሮታል እንዲህ መሆኑ ስለምን ነው ቢሉ ውስጡ ጥበበ እግዚአብሔር ነው ። በዕብራይስጥ የተጻፉትን ዓላውያን የሚያቃጽሏቸው ናቸውና ።

በዕብራይስጥ የተጻፉት ሲጠፉ በጽርዕ የተጻፉት እንዲገኙ አድርጓል ። ዘመኑ አምስት መቶ ነው ያሉ እንደሆነ ይህን ሲጽፍ ሁለት መቶ አምሳ ሁለት ነበር ይህን ከጻፈ በኋላ ሁለት መቶ አምሳ ኖሯል ሦስት መቶ ነው ያሉ እንደሆነ ይህን ሲጽፍ መቶ አምሳ ሁኖት ነበር ይህን ከጻፈ በኋላ መቶ አምሳ ዘመን ኖሯል ። መምር ኤስድርስ ግን ይህን ሲጽፍ ያስራምስት ዓመት ብላቴና ነበር ብሏል ።

፳፯ ወወሰዶ መንፈስ ምኵራብ ፤
፳፯ ካልጋ ተጣብቆ ሲኖር መንፈስ ቅዱስ አንሣሥቶ አጸናንቶ ወደምኵራብ ወሰደው ወሶበ አብዕም አዝማዲሁ ለሕፃን እግዚእ ኢየሱስ ከመ ይግበሩ ሎቱ ዘበሕጉ ።

በአረት እንደ ታዘዘ ያደርጉለት ዘንድ ብላቴናውን ዮሴፍና እመቤታችን ወደ ቤተ መቅደስ ባገቡት ጊዜ ።

፳፰ ተወክፎ ውእቱኒ ወአንበሮ ውስተ ሕፃኑ
፳፰ እሱ ተቀብሎ አቀፈው ።
ወባረኮ ለእግዚአብሔር ።
ከዚህ ጊዜ ያደረሰከኝ ከደዌዬ የፈወስከኝ ብሎ እግዚአብሔርን አመሰገነው ።

፳፱ ወይቤ ይእዜ ትሥዕሮ ለገብርከ ።
፳፱ በታቀፈው ጊዜ ታድኗል ወደኸው እንደሆን ከዚህ ላኑርህ አለው ባሪህን ዛሬ በሞት ታስናብተዋለህ ትሥዕሮ ልታሰናብተው ይገባል ሠዓሮ አስናብተው በሰላም ።
ፃር ጋር ሳይፀናብኝ በሽማግሌ ፃር ጋር ይፀናልና።

፴ እግዚእ በከመ አዘዝከ ።

፴ ስሚው አብ ነው ያሉ እንደ ሆነ አቤቱ ኢትመውት ዘእንበለ ትርአይ መሲሖ ለእግዚአብሔር ብለህ እንደ ተናገርከ ።

፴፩ እስመ ርእያ አዕይንትየ አድኅኖተከ ።
ዘአስተዳሎከ ቅድመ ኵሉ ሕዝብከ ።

፴፩ ለወገኖችህ ፊት ያዘጋጀኸውን አድኅኖትህ ወልድን አይቻለሁና ።

እንድም ሦስት አመት ከሦስት ወር ከሚያዩት አስቀድሞ ያዘጋጀኸው አድኅኖትህ ወልድን አይቻለሁና እንድም ስሚው ወልድ ነው ያሉ እንደሆን ።
በከመ አዘዝከ ።
መሬት አንተ ብለህ እንደተናገርከ ይህ የሁሉ ነው በወገኖችህ ፊት ያዘጋጀኸውን አድኅኖትህን አይቻለሁና እንድም ሦስትም ዓመት ከሦስት ወር ከሚያዩት ተአምራት አስቀድሞ ያዘጋጀኸውን አድኅኖትኸን አይቻለሁና ።

፴፪ ከመ ትከሥት ብርሃነ ለአሕዛብ ።

፴፪ ለአሕዛብ ትንቢትን ተሰፋን ትገልጽ ዘንድ፤
ወክብረ ለሕዝብከ እሥራኤል ።
ለእሥራኤል ሃይማኖትን ልጅነትን ትገልጽ ዘንድ ። ሐተታ እንዲህ ማለት ማካፈል አይደለም በወንጌል ካመኑ በኋላ ሁሉም በሁሉ ያሉ ናቸው የሌለ የሌላቸውን ሰጥቶ መናገር ነው እንጂ ።

፴፫ ወዮሴፍስ ወእሙ ያነክሩ በእንተ ዘነበበ ላዕሌሁ ።

፴፫ እመቤታችንና ዮሴፍ ግን ስለሚናገረው ነገር የሚናገረውን ነገር ያደንቃሉ ። ሐተታ ይህ አረጋዊ ፀንቶ እንዲህ ያለ ነገር ይናገራል ብለው ። እንድም ስለዚህ ሕፃን እንዲህ ይናገራል ብለው ስጌታ ስለሚናገረው አደነቁ ።

፴፬ ወባረኮሙ ስምዖን ።
፴፬ ስምዖን መረቃቸው ። ኢሳ ፰ ፲፬ ሮሜ ፱ ፴፪ ፩ ጴጥ ፪ ፯ ወይቤላ ለእሙ ማርያም ናሁ ዝንቱ ሕፃን ሥዩም ለድቀቶሙ ወለተንሥኦቶሙ ለብዙኃን እምውስተ እሥራኤል እናቱን ማርያም ሆይ ይህ ሕፃን ከእሥራኤል ወገን ለብዙ ሰዎች ለልማታቸው ለጥፋታቸውም ንቡር ድልው ነው ።
ወለትእምርት በዘይትወቀሱ በሚፈረድባቸው ገንዘብ ይፈረድባቸው ዘንድ ።

፴፭ ወለኪሰ ይበውእ ውስተ ነፍስኪ ኵናት ኑፋቄ ።

፴፭ ባንቺ ግን ባንቺም እንደ ጦር የሚከፍል ኃዘን በልብሽ ያድራልና አንድም ወለነፍስ አንተ ትበውእ ኵናት ይላል ጸብነት የጌታ ሞት እንደ ጦር የምትሰማ ኃዘን ናት ። አንድም ወለነፍስ አንተ ትበውእ ውስተ ኵናት ይላል አብነት በጥጦስ ጦር ለምትከበብ ለአይሁድ ሰውነት ለልማታቸውም ለጥፋታቸውም ንቡር ድልው ነው ማለት የተዘጋጀ ነው ።
ከመ ይከሥት ሕሊና ልቦሙ ለብዙኃን ።
የብዙ ሰዎችን ሐሊና ይገልጽ ዘንድ ማለት የምእመናን ልቡና በደስታ ይገልጽ ዘንድ

፴፮ ወሀለወት ሐና ነቢይት ወለተ ፋኑኤል እንተ እምነገደ አሴር ።

፴፮ ከነገደ አሴር የተወለደች የፋኑኤል ልጅ ሐና የምትባል ነቢይት ነበረች ።
ወኃለፈ መዋዕሊሃ ።
የሕፃንነቷ ዘመን አልፏል ።
ወምስለ ምታስ ነበረት ስብዓተ ክረምተ እምድኅረ ነበረት በድንግልናሃ ።
በድንግልና ዐሥራ አምስት ዓመት ከኖረች በኋላ ባል አግብታ ሰባት ዓመት ኖረች ።
፴፯ ወኮነት መአስብተ ሰማንያ ወአርባዕተ ክረምተ ።
፴፯ ሰማንያ አራት ዓመት ፈት ሁና ኖረች ። ሐተታ መላው መቶ ስድስት ዓመት ይሆናል በጐ የበላች ባልቴት ናት ።
ወኢትወፅእ እምኵራብ መዓልተ ወሌሊተ እንዘ ትትቀነይ በጾም ወበጸሎት ።
በጾም በጸሎት ተወስና እግዚአብሔርን ስታገለግል በመዓልትም በሌሊትም ከምኵራብ አትወጣም ነበር ። ሕገ ሥጋ ጠፍቶላታል ቢሉ የተመቸ አል ከፋላትም ቢሉ እየወጣች እየገባች ።
፴፰ ወተንሥአት ሶቤሃ ወገነየት ።
፴፰ ፈጥና ተነሥታ አመነች ።
ወእእኰተቶ ለእግዚአብሔር ፤ እግዚአብሔርን አመሰገነችው ። ወነገረት በእንቲአሁ ለኵሎሙ እለ ይሴፈው መድኃኒታ ለኢየሩሳሌም ።

የኢየሩሳሌምን ድኅነት ተስፋ ለሚያደርጉ ሁሉ የብላቴናውን ነገር ተናገረች ።

በእንተ ኢየሱስ ሕፃን ።

፴፱ ወፈጺሞሙ ኵሎ ዘበሕገ ኦሪት አተው ገሊላ ሀገሮሙ ናዝሬተ ።

፴፱ በኦሪት የታዘዘውን በዓል አከብረው ከጨ ረሱ በኋላ ወደ ሀገራቸው ተመለሱ ።

፵ ወልሕቀ ሕፃን ።
፵ ሕፃኑ አደገ ።
ወፀንዓ በመንፈስ ቅዱስ ። የሚያሳድግ ብቻ ማቢታ አይደለም ኃይል አልጎቈተ ኵሉ አለችና በመንፈስ ቅዱስ ጸና ።
ወምሉአ ጥበበ ጥበብን ተመልቶ ።
ወፍጹም በጸጋ እግዚአብሔር ዘላዕሌሁ ።
የእግዚአብሔር ጸጋ በርሱ ነበረች ማለት በርትዓተ መለያልይ አደገ አንድም ወምሉአ ጥበበ ጥበብ መንፈሳዊን ተመልቶ ወበጸጋ ልሕቃንሰ በአካል ዘሥጋ ነፍሱን ትበርሀ በጥበብ ወበጸጋ ዝኒ ከመ አዳም ቀዳማዊ ባለው አደገ ።

ዘከመ ረፈቀ ኢየሱስ ማእከለ ሊቃውንት ።

፵፩ ወየሐውሩ አዝማዲሁ ኢየሩሳሌም ለለዓመት ለበዓለ ፋሲካ ። ዘፀ ፳፫ ፣ ፲፭፡ዘዳ ፲፯ ፪ ።

፵፩ እመቤታችንና ዮሴፍ ባመት ባመት በዓል ለማክበር ኢየሩሳሌም ይሄዱ ነበር ።

፵፪ ወአመ ኮኖ ፍጹመ ሎቱ ፲ቱ ወ፪ቱ ክረምቱ
፵፪ ዐሥራሁለት ዓመት ሲመላው ዓርጉ ለበ ዓል ኢየሩሳሌም በከመ ያለምዱ ።
እንዳለመዱ በዓለ ፋሲካውን ለማክበር ኢየሩሳሌም ወጡ ።

፵፫ ወሠሊጦሙ ግብሮሙ አተው ገሊላ ሀገሮሙ
፵፫ በዓሉን ካከበሩ በኋላ ወደሀገራቸው ተመለሱ ወሕፃንስ ኢየሱስ ነበረ ኢየሩሳሌም ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ግን በኢየሩሳሌም ቀረ። ነበረ ውስተ ገሊላ እንዲል ተርፈ ሲል ወኢያእመሩ ዮሴፍ ወእሙ እመቤታችንና ዮሴፍ ግን እንደቀረ ዐላወቁም ።

፵፬ ወይመስሎሙ ከመ ዘበፍኖት ሀሎ ምስለ ሰብእ ።

፵፬ በፊት ከሄዱ ሰዎች ጋራ ያለ መስሏቸው ነበር ። ሐተታ ያገኘው ሁሉ ይነጣጠቀው ነበርና፤ ወበጺሖሙ ኃሠሥዎ በዕለታ ኅበ አዝማዲሁ ወኅበ እለ የአምርዎ ። በደረሱም ጊዜ ከዘመዶ ቹና ከሚያውቁት ዘንድ ዕለቱን ፈለጉት ።
ወኢረከብዎ ። እላገኙትም ።

፵፭ ወሶቤ ኢረከብዎ ተሠውጡ ኢየሩሳሌም እንዘ የኃሥሥዎ ።

፵፭ ባያገኙት እየፈለጉ ወደኢየሩሳሌም ተመ ለሱ ።

ወእምዝ በሣልስታ ረከብዎ

፵፮ እንዘ ይነብር በማእከለ ሊቃናት
፵፮ ከዚህ በኋላ በሦስተኛው ቀን በሊቃነ ካህ ናት መካከል ተቀምጦ አገኙት ።
ወያጸምዮሙ ።
ሲሰማቸው ።
ወይሴአሎሙ ።
ሲጠይቃቸው እንድም ያጸምዮሙ አጥብቅ ሲያሰ ማቸው ሲጠይቃቸው ፣

፵፯ ወያነክርዎ ኵሎሙ እለ ሰምዑ ጥበቦ ወአውሥኦቶ ።

፵፯ ጥያቄውን ምላሹን የሰሙ ሁሉ ያደንቁት ነበር ።

፵፰ ወሶበ ርእይዎ ደንገፁ ፣

፵፰ ባዩት ጊዜም ደነገጡ ልጅ ከሽማግሌ መካከል ተቀምጦ ሲያፈችል ቢገኝ ያስደነግጣልና ወትቤሎ እሙ ወልድየ ለምንት ከመዝ ረሰይከነ፤ እናቱ እመቤታችን ልጄ ለምን እንዲህ አደረግኸን፥ አስመ ናሁ አቡከኒ ወአነኒ ሠራሕነ እንዘ ነሐሥሥከ። አኔና ዮሴፍ ስንፈልግህ ደከምን አለችው ።

፵፱ ወይቤሎሙ ለምንት ተሐሥሡኒ ።
፵፱ ለምን ትፈልጉኛላችሁ ።
ኢያአመርክሙኑ ከመ ይደልወኒ እሀሉ ውስተ ዘአ ቡየ ቤት ባባቴ ቤት በዚህ ዓለም በምልአት መኖር እንዲገባኝ እላወቃችሁምን ። አንድም በቤተ መቅ ደስ መኖር እንዲገባኝ አታውቁምን አላቸው ።

፶ ወእሙንቱስ ኢለበው ቃሎ ዘይቤሎሙ ።
፶ እሳቸው ግን በምልአት ያላቸውን ነገር አላስተዋሉትም ነበር ዮሴፍን ሲያይ ነው እንጂ አመቤታችንስ ታውቃለች ።

፶፩ ወሖረ ወወረደ ምስሌሆሙ ናዝሬተ ።
፶፩ ከሳቸው ጋራ ወደናዝሬት ሄደ ።
ወኮነ ይትኤዘዝ ሎሙ ።
ያገለግላቸው ነበር ።
ወእሙስ ተዓቅብ ዘንተ ኵሎ ነገረ ።
እመቤታችን ግን ይህን ሁሉ ነገር ታስተውለው ነበር ወትወድዮ ውስተ ልባ ።
በልቡናዋ ታኖረው ነበር ።

፶፪ ወእግዚእ ኢየሱስ ልህቀ ።
፶፪ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አደገ ።
ወዐብየ በጥበብ ወምከር ።
በጥበብ ጠባይዓዊ በምክር ጠባይዓዊ ። አንድም በጥበብ መንፈሳዊ በምክር መንፈሳዊ ።
ወበጸጋ ። በርትዓተ መለያልይ ልሀቃ ንሰ በአካል ዘሥጋ ነፍሱኒ ትበርሀ በጥበብ ወበ ጸጋ ባለውም አደገ ።

በኀበ እግዚአብሔር ወበኀበ ሰብእ ።            በእግ
ዚአብሔርም ዘንድ በሰውም ዘንድ ማለት ፍቅረ
ቢጽንና ፍቅረ እግዚአብሔርን ይዞ አደገ ።

በእንተ ስብከት ዘዮሐንስ መጥምቅ

ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወአመ ፲ቱ ወኃምስቱ ዓመተ መንግሥቱ
ለጢባርዮስ ቄሣር ፤

፩ ጢባርዮስ ቄሣር በነገሠ ባ፲፭ ዓመት ።
ሐተታ ከአውግሥጦስ ቄሣር ፲፭ ዓመት ያመጣል
ከጢባርዮስ ቄሣር ፲፭ በ፴ ዘመን ተጠመቀ ለማ
ለት እንዲህ አለ ፥ የቍጥር መጽሐፍ አውግስጦስ
ቄሣር በነገሠ ባ፵፪ ዓመት ተወለደ ይላል ።
ቅዱስ ቄርሎስ አውግስጦስ በነገሠ በ፲፰ ዓመት ተወ
ለደ ይላል ወንጌል ፲፭ ዓመት ያመጣል አለ ። አይ
ጣላም ቢሉ አይጣላም ። የአውግስጦስ ቄሣር መላ
ዘመነ መንግሥቱ ፶፯ ነው ። በነገሠ በ፵፪ ዘመን
ጌታ ተወልዷል ፲፭ና ፵፭ ፶፯ ይሆናል ። ቄርሎስ
፲፰ አለ በነገሠ በ፳፬ ዘመን ንጉሠ ነገሥትነት ደር
ሷል ንጉሠ ነገሥትነት ከደረበ ጀምሮ ቈጥሮ ፲፰
አለ ። ፳፬ና ፲፰ ፵፪ ይሆናል አይጣላም ።
እንዘ ጲላጦስ ጲንጤናዊ መልአከ ይሁዳ ።
የጴንጤን ሰው ጲላጦስ በይሁዳ ተሹሞ ሳለ
በተሾመ ጊዜ ወሄሮድስ ንጉሥ ላዕለ ገሊላ ።
ሄሮድስ በገሊላ ነግሦ ሳለ በነገሠ ጊዜ ።
ወፊልጶስ እኍሁ መልአከ ኤጡርያስ ።
ወንድሙ ፊልጶስ በኤጡርያስ ነግሦ ሳለ በነገሠ ጊዜ።
ወስብሔረ ጥራኮኒዶስ ።
በጥራኮኒዶስም ተሹሞ ሳለ በተሾመ ጊዜ ።
ወሊላንዮ እንተ ስብላኒስ ። ሊላንዮ በሰብላኒስ
ተሹሞ ሳለ በተሾመ ጊዜ ፥ ሊሳንዮ ሀቢ እንተ ሳብ
ላኔስ ይላል ሊሳንዮ ሀቢ በስብላኒስ ተሾሞ ሳለ
በተሾመ ጊዜ ፤ ፊልጶስ ባራቱ አህጉር ተሹሟል ።
አንድም መልስ ላዕለ ራብዕት እዴሃ ለይሁዳ ይላል
አብነት ጲላጦስ በይሁዳ በርቦዋ ተሹሞ ሳለ በተ
ሾመ ጊዜ ፥ ሄሮድስ በገሊላ በርቦዋ ተሹሞ ሳለ በተ
ሾመ ጊዜ ወፊልጶስ እኍሁ ላዕለ ራብዕተ እዴሃ
ለኢጡርያስ ።

ወንድሙ ፊልጶስ በኢጡርያስ በርቦዋ ተሹሞ ሳለ
በተሾመ ጊዜ ወሊሳንዮ ሀቢ ላዕለ ራብዕተ እዴሃ
ለሰብላኒስ ።
ሊሳንዮስ ሀቢ በስብላኒስ በርቦዋ ተሹሞ ሳለ በተ
ሾመ ጊዜ አንዱን አገር ካራት እየተካፈሉ ተሹመ
ውታል ። ላዕለ መንፈቀ መንፈቃ ይላል አብነት
ትርጓሜው አይለወጥም ።

፪ ወአመ ሐና ወቀያፋ ሊቃነ ካህናት ።
፪ ሐና ቀያፋ ሊቃነ ካህናትነት ተሹመው
ሳሉ በተሾሙ ጊዜ ሐተታ ። ሊቀ ካህናቱ አንድ
አይደለም ቢሉ ምሉና ዱግ ሁነው ተሹመውታል ።
መጽአ ቃለ እግዚአብሔር ላዕለ ዮሐንስ ወልደ ዘካ
ርያስ በገዳም ።
ከዘካርያስ ልጅ ከዮሐንስ ዘንድ በገዳም ሳለ ውጣ
አስተምር የሚል ቃል ተሰማ ።

፫ ወሖረ አድያመ ዮርዳኖስ ወሰበከ ጥምቀተ
ለንስሐ በዘይት ኀደገ ኃጢአት ። ማቴ ፡ ፫ ፩ ማር፡፩፡፬

፫ ኃጢአት በሚሰረይ ገንዘብ ይሰረይ ዘንድ
በዮርዳኖስ ዙሪያ እየዞረ ለንስሐ ጥምቀትን አስተማረ

፬ በከመ ይብል ቃለ መጽሐፈ ኢሳይያስ ነቢይ
ኢሳ፡ ፵ ፫ ዮሐ፡ ፩፡ ፳፫ ።

፬ የነቢዩ የኢሳይያስ መጽሐፍ እንደ ተናገረ
ዘይቤ ናሁ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብክ በገዳም ዘይብል
ጺሑአ ፍኖቶ ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርን መንገድ አዘጋጁ ።
ወአርዩ መጽያሕቶ ።
ጥርጊያውንም አስተካከሉ የሚል ያዋጅ ነጋሪ ቃል
እነሆ በገዳም አለ የሚል ።

፭ ኵሉ ማዕምቅ ይምላእ ።
፭ ጎድጓዳው ሁሉ ይምላ ።
ወኵሉ ደብር ወወግር ይትሐት ተራራው ኰረብ
ታው ሁሉ ይናድ ዝቅ ይበል ።
ወይኩን መብእስ መጽያሕተ ርቱዓ ።
ስንካላው መንገድ ጽርጊያ ይሁን ።
ወይእሪ ፍኖት መብእስ ።
ስንካላው ይተካከል ።
ወይርአይ ኵሉ ዘነፍስ አድኅኖቶ ለእግዚአብሔር።
ሥጋዊ ደማዊ ሰው ሁሉ የእግዚአብሔርን ማዳን
ይይ ይወቅ ሐተታ ንጉሥ በወጣበት ጊዜ ጕድጓዳው
መልቶ ሥሩ ተነቅሎ ደንጊያው ተለቅሞ ለፈረስ
ለሠረገላ እንዲመች ተደልድሎ ይቆያልና በዚያ ግሥ
እንዲህ አለ ። ይህም አልቀረም ዘሩባቤል ከፋርስ
ከባቢሎን በወጣ ጊዜ ይህ ሁሉ ተደርጓል ። አንድም
ኵሉ ማዕምቅ እያልክ መልስ ። ተስፋ ያልያዘ ልቡና
ተስፋ ይያዝ ።
ወኵሉ ወግር ። ጣዖታዊ ልቡና ጣዖቱን ይተው ።
ወይኩን መብእስ በጣዖት በኃጢአት የተሰናከለ
ሰው ሁሉ ንጹሕ ይሁን ወይዕሪ ፍኖት መብእስ
ሰው ሁሉ አንድ ወገን ሁኖ በሕገ ኦሪት ለእግዚ
አብሔር ይገዛ ።

፮ ወይርአይ ኵሉ ዘነፍስ ።
፮ ሰው ሁሉ ሚጠተ ሥጋውን ይይ ፥ አንድም
ኵሉ ማዕምቅ ትሩፋን ከባቢሎን ይውጡ ።
ወኵሉ ወግር ። ባቢሎናውያን ይዋረዱ ከዚህ በላይ
አይለወጥም ። አንድም ኵሉ ማዕምቅ ሐዋርያት
ልዕልና ነፍስ ያግኙ ። ወኵሉ ወግር ። ጸሐፍት ፈሪ
ሳውያን ይዋረዱ ። ወይኩን መብእስ በኃጢአት

የተሰናከለ ሰው ሁሉ ንጹሕ ይሁን ። ወይዕሪ ፍኖት መብእስ ። ሰው ሁሉ አንድ ወገን ሁኖ በሕገ ወንጌል ለእግዚአብሔር ይገዛ ወይርአይ ኵሉ ዘነፍስ ። ሥጋዊ ደማዊ ሰው ሁሉ ሚጠተ ነፍሱን ይወቅ ፤ አንድም ኵሉ ማዕምቅ ነፍሳት ይውጡ ወኵሉ ደብር ። ኢጋንንት ይዋረዱ ከዚህ በታች አይለወጥም አንድም ኵሉ ማዕምቅ ። ተስፋ ያልያዘ ልቡና ተስፋ ይያዝ ፣ ወኵሉ ደብር ። በምክረ ርእሱ በፈቃደ ርእሱ የሚኖር ሰው ሁሉ በምክረ ካህን ይኑር ወይኩን መብእስ ፤ በኃጢአት የተሰናከለ ሰውነት ንጹሕ ይሁን ። ወይዕሪ ፍኖት መብእስ ፣ ሰው ሁሉ አንድ ወገን ሁኖ በሕገ ወንጌል ለእግዚአብሔር ይገዛ ። ወይርአይ ኵሉ ዘነፍስ ። ሥጋዊ ደማዊ ሰው ሁሉ እድኅኖተ እግዚአብሔር ወልድ በእምሳለ ኀብስት እንዲሰጥ እንዲሠዋ ይወቅ ሲሰጥ ሲሠዋ ያስተውል ።

፯ ወይቤሎሙ ዮሐንስ ለሕዝብ እለ መጽኡ ኀቤሁ ያጥምቆሙ ኦ ትውልደ ሰበድዓት መኑ ነገረክሙ ታምሥጡ እመቅሠፍት ዘይመጽእ።ማቴ ፫፡፯

፯ ዮሐንስም ሊያጠምቃቸው የመጡትን ሕዝቡን እናንት የጉበና ልጆች ከሚመጣው መቅሠፍት ትድኑ ዘንድ ማን ነገራችሁ አላቸው ። ሐተታ ማቴዎስ ትውልደ አራዊተ ምድር ይላል ። ሉቃስ ትወልደ ሰበድዓት አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም የሁለት ቀን ትምህርት የልሳን መለያየት ነው ። አንድም ማቴዎስ የወል ስማቸውን ሉቃስ የጉልማ ስማቸውን ተናገረ ። አንድም የሰበድዓት ኅብሩ ብዙ እንደሆነ ቤተ አይሁድም ብዙ ኃጢአት ይሠራሉና ።

፰ ግበሩ እንከ ፍሬ ዘይደልወክሙ ለንስሐ ።
፰ ለማመን የሚያበቃችሁን ሥራ ሥሩ ።
ወኢይምሰልክሙ በብሂለ ዘትብሉ ሀሎ አቡነ አብርሃም ። አብርሃም አባታችን ነው በማለት አይምሰላችሁ ።
እብለክሙ ከመ ይክል እግዚአብሔር አንሥኦ ውሉድ ለአብርሃም እምእላንቱ እዕባን ።
እግዚአብሔር ከነዚህ ደንጊያች ለአብርሃም ልጅ መተካት ይቻለዋል ብዬ እነግራችኋለሁ ።

፱ እስመ ወድአ ተሠይመ ጉድብ ኀበ ጉንደ ዕፀው ።
፱ ገጀሞ በዛፎች ሥር ላይ ፈጽሞ ተቃጥቷልና ። ሐተታ ማቴዎስ ማኅፄ ይላል ከዚህ ጉድብ አለ እንደ ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም የሁለት ቀን ትምህርት የልሳን መለያየት ነው ። አንድም ሥራው የገጀሞ ነውና ሉቃስ ጕድብ አለ ኦልቆር ጥለት ቢል አዙሮ ከላይ እንደ ምሳር አድርጐ ይሠራዋልና ያን ሲያይ ማቴዎስ ማኅፄ አለ ።
ወኵሉ ዕፅ ዘኢይፈሪ ፍሬ ሠናየ ይገዘምዎ ወውስተ እሳት ይወድይዎ ።
መልካም ፍሬ የማያፈራውን ዕንጨት ሁሉ ቆርጠው ከእሳት ይጥሉታል ።

፲ ወተስአልዎ ሕዝብ ወይቤልዎ ምንተ ንግበር
፲ ሕዝቡ ምን እናድርግ ብለው ጠየቁት ።
፲፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ዘቦ ክልኤ ልብስ ክዳናት የሀብ ለዘአልቦ ።

፲፩ ሁለት ልብስ ያለው መጐናጸፊያን ለሌለው ይስጥ ።
ወዘሂ እክል ቦ ከማሁ ለይግበር ።
እህል ያለውም ለሌለው ይስጥ ብሎ መለሰላቸው ።

፲፪ ወመጽኡ መጸብሐንሂ ያጠምቆሙ ።
፲፪ ቀራጮችም ሊያጠምቃቸው መጡ ።
ወተስአልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ምንተ ንግበር ።
መሀምር ምን እናድርግ ብለው ጠየቁት ።

፲፫ ወይቤሎሙ አልቦ ፍድፋዴ ዘትገብሩ እም ዘተአዘዝክሙ ።

፲፫ ከታዘዛችሁት አትርፋችሁ አትሥሩ አላቸው
፲፬ ወተስአልዎ ሐራሂ ወይቤልዎ ንሕነኬ ምንተ ንግበር ።

፲፬ ጭፍሮችም እኛስ ምን እናድርግ ብለው ጠየቁት ።
ወይቤሎሙ ኢትትዓገሉ ወኢመነሂ ።
ማንንም ማንን አትበድሉ ።
ወኢትሂዱ ። አትቀሙ
ወንበሩ በበሲሳይክሙ ።
ደመወዛችሁ ይብቃችሁ አላቸው ።
፲፭ ወሐለዩ ኵሉ ሕዝብ በልቦሙ ወመሰሎሙ ዮሐንስ ከመ ውእቱ ክርስቶስ ።
፲፭ ሕዝቡም ዮሐንስ ክርስቶስ እንደሆነ በልቡናቸው አሰቡ ።
፲፮ ወአውሥአ ዮሐንስ ወይቤሎሙ ለኵሎሙ አንሰ አጠምቀክሙ በማይ ።
፲፮ ዮሐንስም እኔስ በውሃ አጠምቃችኋለሁ ወይመጽእ ዘይጸንዓኒ ዘኢይደልወኒ እፍታሕ ቶታን አሣዕኒሁ ። ማቴ ፫ ፲፩ ማር ፩ ፰ ዮሐ ፩ ፳፮ ግብ ፩ ፭ የጫማውን ማዘቢያ እፈታ ዘንድ የማይገባኝ ከኔ የሚበረታ ግን ይመጣል ብሎ መለሰላቸው ሐተታ፣ እጹር ማቴዎስ እድንን ማርቆስ እፍታሕ ሉቃስ መገናኛው ዮሐንስ ። እንዲህ ግን ስለሆነ እንድን ይቀድማል እፍታሕ ይከተላል እጹር መጨረሻ ነው ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ።
ወውእቱ ያጠምቀክሙ በመንፈስ ቅዱስ ወበእሳት።
እሱ በመንፈስ ቅዱስ በእሳት ያጠምቃችኋል ።
፲፯ ዘመስሔ ውስተ እዴሁ ወያነጽሕ ዐውደ እክሉ ።
፲፯ የእህሉን አውድማ የሚያጸራበት መንሽ በጁ ነው ።

ወያስተጋብእ ሥርናዮ ውስተ መዛግብቲሁ ።
ሥንዴውን በጎተራ ይሰበስባል ወኃሠርሰ ያውዒ
በእሳት ዘኢይጠፍዕ ።
ገለባውን ግን በማይጠፋ እሳት ያቃጥለዋል ።

፲፰ ወቦ ባዕድኒ ብዙኀ ዘመሀሮሙ ለሕዝብ
፲፰ ለሕዝቡ ያስተማራቸው ሌላም ብዙ አለ ።
ወባዕደኒ ብዙኃ መሐሮሙ ይላል ። ሌላ ትምህርት
ንም አስተማራቸው አለ ጻገም ሕግን ።
ወገሠጾሙ ።
ይመክራቸው ነበር ።

ዘከመ ተሞቅሐ ዮሐንስ መጥምቅ ።

፲፱ ወኮነ ዮሐንስ ይጌሥጾ ለሄሮድስ ።
፲፱ ዮሐንስ ሄሮድስን ይገሥጸው ነበር ።
ወይዘልፎ በእንተ ሄሮድያዳ ብእሲተ ፊልጶስ እኁሁ።
ማቴ ፲፬ ፬ ማር ፮ ፲፯ ።
በወንድሙ በፊልጶስ ሚስት በሄሮድያዳ ምክንያት
ይዘልፈው ነበር ።
ወበእንተ ኵሉ እኩይ ዘገብረ ሄሮድስ ።
ሄሮድስ ስለሚሠራው ክፉ ነገር ሁሉ ይገሥጸው
ነበር ። ሐተታ ሰውሮ ነፍስ ሳያስገድል አይውልም
ነበር ። አንድም ግብረ ሰዶም ይሠራ ነበር ።

፳ ወዓዲ ወሰከ ።
፳ ሄሮድስ በኃጢአት ላይ ኃጢአት ጨመረ
እንበይነ ዝኒ ተቀየሞ ለዮሐንስ ወዓፀዎ ውስተ
ቤተ ሞቅሕ ።
ስለዚህ ነገር ዮሐንስን ሳይዘልፈኝ አይቀርም ብሎ
ተቀይሞ አጋዘው ። እንበይነ ዝኒቂም ስለዚህ ቂም
አጋዘው አንድም ዮሐንስ በዘለፋ ላይ ዘለፋ ጨመረ
ስለዚህ ተቀየመው አጋዘው ተቀይሞ አጋዘው ስለ
ዚህ ቂም አጋዘው ።

በእንተ ጥምቀት ዘኢየሱስ ።

፳፩ ወእምድኅረ ተጠምቁ ኵሉ ሕዝብ ተጠ
ምቀ እግዚእ ኢየሱስኒ ። ማቴ ፫ ፲፫ ። ማር ፩ ፲፱ ።
ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፴፪ ።

፳፩ ሕዝብ ሁሉ ከተጠመቁ በኋላ ጌታችን
ኢየሱስ ክርስቶስም ተጠመቀ ። ሐተታ ጌታ ፊት
ተጠምቆ ሕዝቡ በኋላ ተጠምቀው ቢሆን አሪት
አላለፈችም ባንድነትም ተጠምቆ በሆነ ተቀላቅላ
ትሠራለች ባሉ ነበርና ።

፳፪ ወእንዘ ይጼሊ ተርኅወ ሰማይ ማቴ ፡ ፫
፲፯ ። ሉቃ ፱ ፴፭ ። ፪ ጴጥ ፩ ፡ ፲፯ ።

፳፪ ሲጸልይ ሰማይ ተከፈተ ። ወወረደ መን
ፈስ ቅዱስ በአምሳለ ሥጋ ርእየተ ርግብ ጸዓዳ ።
መንፈስ ቅዱስ መልክአ ርግብ ባለው ባሕርይ
አምሳል ወረደ ወመጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል
አንተ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ።
የምወድህ ልጄ አንተ ነህ የሚል ድምፅ መጣ ።
ወኪያከ ሠመርኩ ።
ደስታዬን ላይብህ የመረጥኩህ ።

በእንተ መጽሐፈ ትውልድ ዘኢየሱስ ።

፳፫ ወየአክል ሠላሳ ክረምቱ ለእግዚእ ኢየ
ሱስ ።

፳፫ ጌታ በተጠመቀ ጊዜ ሠላሳ ዘመን ሆኖ
ነበር ።

ወይመስሎሙ ወልደ ዮሴፍ ውእቱ ።
ምንም አንተ ውእቱ ወልድየ ብሎ ቢመሰክርለት
ለሳቸው ። የዮሴፍ ልጅ ይመስላቸው ነበር የዮሴፍ
ልጅ ነው ይሉ ነበር ።

፳፬ ወልደ ኤሊ      የኤሊ ልጅ ።
፳፬ ወልደ ማቲ ።
የማቲ ልጅ ። ማቴዎስ ዮሴፍን ወልደ ማትያን
ወልደ ያዕቆብ ይለዋል ። ከዚህ ሉቃስ ወልደ ኤሊ
ወልደ ማቲ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ
አይጣላም ። ለዳዊት ናታን ሰሎሞን የሚባሉ ልጆች
ነበሩት ማቴዎስ በሰሎሞን የወረደውን ቈጠረ ።
ሉቃስ በናታን የወረደውን ቈጠረ ። ያውስ ቢሆን
ላንድ ሰው ሁለት አባት አለውን ብሎ ማቴዎስ
በልደት ሥጋዊ ቈጥሮ ሉቃስ በልደት ሕጋዊ ቈጥሮ
ማቲ ሹሻን አግብቶ ኤሊን ወልዶ ይሞታል ።
ማትያን እሷን አግብቶ ያዕቆብን ይወልዳል ኤሊና
ያዕቆብ ወንድማማች ናቸው ኤሊ ታላቅ ነው ታላቅ
ባለ ታናሽ አያገባምና ለኤሊ ሚስት አጋቡት እሱ
ልጅ ሳይወልድ ሞተ ። አቅም ዘርዓ ለአኁከ ብለው
ለያዕቆብ አጋቡት እሷን አግብቶ ዮሴፍን ይወልዳ
ልና። አንድም የጌታ ልደቱ እንደ ማቴዎስ በልደት
ሥጋዊ ። እንደ ሉቃስ በልደት ሕጋዊ አይደለምና
ተለያይተው ቈጠሩ ።
ወልደ ኤሊ ።      የኤሊ ልጅ
ወልደ ሜልኪ ።
የሜልኪ ልጅ ።
ወልደ ዮና ።      የዮና ልጅ
ወልደ ዮሴፍ ።      የዮሴፍ ልጅ

፳፭ ወልደ ማታትዩ ።
፳፭ የማታትዩ ልጅ ።
ወልደ አሞጽ ። የአሞጽ ልጅ
ወልደ ናሆም ። የናሆም ልጅ
ወልደ ኤስሎም ።
የኤስሎም ልጅ ።
ወልደ ናጌ ።      የናጌ ልጅ
፳፮ ወልደ ማአት ። የማአት ልጅ
ወልደ ማታትዩ ።
የማታትዩ ልጅ ።
ወልደ ሴሜይ ።      የሴሜይ ልጅ
ወልደ ዮሴፍ ።      የዮሴፍ ልጅ
ወልደ ዮዳ ።      የዮዳ ልጅ

፳፯ ወልደ ዮናን ። የዮና ልጅ ።
ወልደ ሬስ ። የሬስ ልጅ
ወልደ ዘሩባቤል ፤
የዘሩባቤል ልጅ ደግ ሰውነውና ደግነቱን ሲያይ ዘሩባቤልን አነሳው መንግሥት ከተለያየ በኋላ አሥራሁለቱን ነገድ አንድ አድርጎ ነግሦአልና ወያዕቆብስ ያስተኤሪ ንግሠ እንዲል ።
ወልደ ሰላትያል ።
የሰላትያል ልጅ ።
ወልደ ኔሪ ፤ የኔሪ ልጅ

፳፰ ወልደ ሜልኪ ፤

፳፰ የሜልኪ ልጅ ማቴዎስ ሰላትያልን ወለደ ኢኮንያን ወልደ ኤልያቄም ይለዋል ። ሉቃስ ወልደ ኔሪ ወልደ ሜልኪ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ለዳዊት ናታን ሰሎሞን የሚባሉ ልጆች ነበሩት ማቴዎስ በሰሎሞን የወረደውን ሉቃስ በናታን የወረደውን ቈጥሮ ነው ። ያውስ ቢሆን ላንድ ሰው ሁለት አባት አለውን ብሎ ማቴዎስ በልደት ሥጋዊ ሉቃስ በልደት ሕጋዊ ቈጥሮ እንዲህ አለ ። አንድም ሜልኪ ነጋሪን ሽታ ወለተ ኤልትማልም ዘኢየሩሳሌምን አግብቶ ኔሪን ወልዶ ይሞታል ። ኤልያቄም እሷን አግብቶ ኢኮንያንን ይወልዳል ። ሜሪና ኢኮንያን ወንድማማች ናቸው ኔሪ ታላቅ ነው ። ታላቅ ሳለ ታናሽ አያገባምና ለኔሪ ሚስት አጋቡት ልጅ ሳይወልድ ሞተ አቅም ዘርዓ ለእኁከ ብለው አጋቡት ኢኮንያን እሷን አግብቶ ሰላትያልን ይወልዳል ። አንድም የጌታ ልያቱ እንደ ማቴዎስ በልደት ሥጋዊ እንደ ሉቃስ በልደት ሕጋዊ አይደለምና ተለያይተው ቈጠሩ ።
ወልደ ሐዲ ፣ የሐዲ ልጅ
ወልደ ዮሳ ። የዮሳ ልጅ
ወልደ ቆሳም ፣ የቆሳም ልጅ
ወልደ ኤልሞዳም ።
የኤልሞዳም ልጅ ።
ወልደ ኤር ፣ የኤር ልጅ

፳፱ ወልደ ዮሴዕ ፣ የዮሴዕ ልጅ
ወልደ አልዓዛር የአልዓዛር ልጅ
ወልደ ማጣት የማጣት ልጅ
ወልደ ሌዊ ። የሌዊ ልጅ
፴ ወልደ ስምዖን ፤
፴ የስምዖን ልጅ ።
ወልደ ይሁዳ ። የይሁዳ ልጅ ፤
ወልደ ዮሴፍ ። የዮሴፍ ልጅ
ወልደ ዮናን ፣ የዮናን ልጅ ፤

ወልደ ኤልያቄም ።
የኤልያቄም ልጅ ።

፴፩ ወልደ ሜልያ ፣ የሜልያ ልጅ
ወልደ ማይናን ።
የማይናን ልጅ ፤
ወልደ ማጣት ፣ የማጣት ልጅ
ወልደ ናታን ። የናታን ልጅ
ወልደ ዳዊት ።
የዳዊት ልጅ ። ዳዊት መገናኛ

፴፪ ወልደ ዕሤይ ፣ የዕሤይ ልጅ
ወልደ ኢዮቤድ ።
የኢዮቤድ ልጅ ።
ወልደ ቡኤዝ ፤ የቡኤዝ ልጅ
ወልደ ሰልሞን ። የሰልሞን ልጅ
ወልደ ነአሶን ፣ የነአሶን ልጅ

፴፫ ወልደ አሚናዳብ ።
፴፫ የአሚናዳብ ልጅ ፣
ወልደ አራም ፣ የአራም ልጅ
ወልደ አርኒ ።
የአርኒ ልጅ ። አርኒ ትርፍ ነው
ወልደ ኤስሮም ።
የኤስሮም ልጅ ።
ወልደ ፋሬስ ። የፋሬስ ልጅ
ወልደ ይሁዳ ። የይሁዳ ልጅ

፴፬ ወልደ ያዕቆብ ፣ የያዕቆብ ልጅ
ወልደ ይስሐቅ ።
የይስሐቅ ልጅ።
ወልደ አብርሃም ።
የአብርሃም ልጅ ።
ወልደ ናኮር ፣ የናኮር ልጅ

፴፭ ወልደ ሴሩህ ። የሴሩህ ልጅ
፴፭ ወልደ ራግው ፣ የራግው ልጅ
ወልደ ፋሌቅ ፣ የፋሌቅ ልጅ
ወልደ ኤቦር ። የኤቦር ልጅ
ወልደ ሳላ ። የሳላ ልጅ

፴፮ ወልደ ቃይንም ።
፴፮ የቃይንም ልጅ ።
ወልደ አርፋስክድ ።
የአርፋስክድ ልጅ ።
ወልደ ሴም ። የሴም ልጅ
ወልደ ኖህ ። የኖኅ ልጅ
ወልደ ላሜህ ፣ የላሜህ ልጅ
፴፯ ወልደ ማቱሳላ ፣
፴፯ የማቱሳላ ልጅ ፣
ወልደ ሄኖክ ። የሄኖክ ልጅ
ወልደ ያሬድ ፣ የያሬድ ልጅ
ወልደ መላልኤል ።

የመላልኤል ልጅ ።
ወልደ ቃይናን ፣
የቃይናን ልጅ ።

፴፰ ወልደ ሄኖስ ።የሄኖስ ልጅ
ወልደ ሴት ። የሴት ልጅ
ወልደ አዳም ። የአዳም ልጅ
ወልደ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር ልጅ ፤ እያወራረሰ መጥቶ አዳምን ወልደ እግዚአብሔር አለ ፍጥረተ እግዚአብሔር ሲል ነው ፣ አሪት ዘልደት እንዲል አዳም ዘእምእግዚአብሔር አዳም ዘእግዚአብሔር ይላል አብነት ። እንድም ወልድ ወልድ ያለ ውንለጌታ የስጡ እንደሆነ እኒህ ሁሉ አባቶች ናቸውና ። ሐተታ በምን ይመስለዋልና አዳምን ወልደ እግዚአብሔር አለው ቢሉ አዳም በኃጢአቱ ሰውን ሁሉ እንዳስጐዳ ጌታም በትሩፋቱ ሰውን ሁሉ በማጽደቁ ይመስለዋልና ። ሰባ ሰባት ትውልድ ቈጠረ ማየ አይኅ ከላይ በሰባት ዓይነት ቍልቍል ወርዷልና ከታች በሰባ ዓይነት ሽቅብ ፈልቋል ፣ በሰባ ሰባት ትውልድ የመጣውን ፍዳ መርገም ለማጥፋት እንደመጣ ለማጠየቅ ። ማቴዎስ ቍልቍል ሉቃስ ሽቅብ ቈጠረ የሥጋን እምላክን መሆን የአምላክን ሰው መሆን ለመናገር ። እንድም ማቴዎስ ርደቱን ሉቃስ ዕርገቱን ተናገረ ።

በእንተ ተመክሮት ዘኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፬ ።

፩ ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ እግዚእ ኢየሱስ ወተመይጠ እምዮርዳኖስ ማቴ፡፬፡፩ ማር ፡ ፩ ፲፪ ።

፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መንፈስ ቅዱስ መልቶበት ማለት የባሕርይ ልጅነቱን ከመንፈስ ቅዱስ አስመስክሮ ከዮርዳኖስ ተመለሰ ።
ወወሰዶ መንፈስ ገዳመ ።
መንፈስ ፈቃዱ ወደገዳም አወጣው ።

፪ እርብዓ መዓልተ ወአርብዓ ሌሊተ ያሜክሮ ሰይጣን ።

፪ አርባ ሌሊትና አርባ መዓልት ከሰይጣን ይፈታተን ነበር ፣
ኢበልዓ ወኢሰትየ ምንተኒ በውእቶን መዋዕል በዚያ ወራት ምንም ምን አልበላም አልጠጣም ።
ወተፈጸሞን እማንቱ መዋዕለ ርኅበ ።
አርባው ቀን ከተፈጸመ በኋላ ተራበ ።

፫ ወይቤሎ ሰይጣን እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ በል ከመ ዝንቱ እብን ይኩን ኅብስተ

፫ ሰይጣንም የእግዚአብሔርስ ልጅ ከሆንክ ይህ ደንጊያ እንጀራ ይሆን ዘንድ እዘዝ አለው

፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ዘዳግ፡ ፰፡፫፡ ማቴ፡ ፬፡፬ ።

፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ጽሑፍ ዘይብል አኮ በኅብስት ከመ ዘየሐዩ ሰብእ ሰው በእንጀራ ብቻ እንዳይድን ተጽፏል። አላ በኵሉ ቃል ዘይወጽእ እምአፉሁ ለእግዚአብሔር ።
እግዚአብሔር በተናገረው ነገር ሁሉ ይድናል እንጂ አለው ማቴዎስ አላ አእባን ይላል ሉቃስ ዝንቱ እብን አለ እንደ ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ሁለት ይዞ ቀርቧል ፣ ሉቃስ አንድ ማለቱ ለመንገርከበቃ ብሎ ። እንድም ሁለት ደንጊያ ይዞ ቀርቦ አንዱን ላንተ አንዱን ለኔ ዳቦ አድርገህ እንብላ ብሎታል ዝም አለ ለኔስ ይቅርብኝ አንተ ጾንቶብሃልና ዳቦ አድርገህ ብላ ብሎታል ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ።

፭ ወአዕረጎ ሰይጣን ውስተ ደብር ነዋህ
፭ ሰይጣን ወደረጅም ተራራ አወጣው ።
ወአርአዮ መንግሥታተ ኵሉዓለም ከመ ወኢምንትኒ፡ የዓለሙን ሁሉ ግዛት በዓይነት ቅጽበት አሳየው።

፮ ወይቤሎ ሰይጣን ዘንተ ኵሉ ምኵናነ ለከ እሁበከ ።

፮ ይህን ሁሉ ግዛት ላንተ እሰጥሃለሁ ።
ወዘንተኒ ክብረ ። ፤
ይህንም ክብር ።
እስመ ሊተ ተውህበ ፤
ለኔ ተሰጥቷልና ፤
ወለዘፈቀድኩ እሁቦ ።
እኔ ለወደድኩት እሰጠዋለሁ ።

፯ ወእምከመ ሰገድከ ሊተ አንተ ቅድሜየ ለከ ይኩንከ ኵሉ ።

፯ ለኔ ብትሰግድልኝ ሁሉም ላንተ ይሆንልሃል አለው ።

፰ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ። ዘዳግ ፮ ፡ ፲፫ ፲ ፡ ፳ ።

፰ ጌታም መለሰ ፤
ወይቤሎ ሑር እምድኅሬየ ሰይጣን ።
ሰይጣን ወግድ ከኋላየ ።
ጽሑፍ ለእግዚአብሔር አምላክከ ትስግድ ።
ለፈጣሪህ ለእግዚአብሔር ትሰግድ ዘንድ ።
ወኪያሁ ባሕቲቶ ታምልክ ።
እሱንም ብቻ ታመልክ ዘንድ ተጽፏል አለው ።
፱ ወወሰዶ ኢየሩሳሌም ።
፱ ወደ ኢየሩሳሌም አወጣው ።
ዲበ ርእሰ ማዕዘንተ ቤተ መቅደስ ።
ከምኵራብ ምሕዋሩ ጫፍ አቆመው ።

ወይቤሎ እመሰ ወልደ እግዚአብሔር አንተ ረድ ለሊከ እምዝየ ወተወረዉ ።
የእግዚአብሔርስ ልጅ ከሆንኽ ራስህን ከዚህ ወደ ታች ወርውር ።

፲ እስመ ጽሑፍ ዘይብል ከመ ለመላእክቲሁ ይኤዝዞሙ በእንቲአከ ከመ ይዕቀቡከ ። መዝ. ፺ ፡ ፲፩

፲ ይጠብቁህ ዘንድ ስላንተ መላእክትን እን ዲያዛቸው ተጽፏልና ።

፲፩ ወበእደዊሆሙ ያነሥኡከ ።
፲፩ በእጃቸው ያነሡሃል ።
ከመ ኢትትዓቀፍ በእብን እግርከ ።
እግርህ በደንጊያ እንዳይሰናከል ።

፲፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፪ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ጽሑፍ ዘይብል ኢታመክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ ። ዘዳ. ፮ ፡ ፲፮
አምላክህን አትፈታተነው ተብሏል አለው ። ሐተታ ማቴዎስ ተራራን በመጨረሻ ያደርጋል ፤ ሉቃስ ቤተ መቅደስን በመጨረሻ አደረገ ፤ አንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ተራራ ነው መጨረሻ ሉቃስ ቤተ መቅደስን መጨ ረሻ ማድረጉ ኀበሂ ዓርገ ወኀበሂ ነበረ ወኀበሂ መሐረ እንዲል ። ከሁሉ ይልቅ ሉቃስ ተራ ያቀናል ይባላልና የተራራ ነገር አንድ ወገን ይሁን ብሎ ቤተ መቅደስን መጨረሻ አደረገ እንጂ ፤ ይህስ በምን ይታወቃል ቢሉ ሑር እምድኅሬየ ያለው በተራራ ነው ከዚህ በኋላ አይመለስም ፤ ይህስ እን ዳይሆን ሰይጣንና ውሻ ተመላላሽ ነው ብሎ ፤ ትራፍ እንተ ትቄንጽ እንዲል ፤ ከሁሉ ይልቅ የትዕቢት ጾር ይጸናል ቅዱሳንም ከበቁ በኋላ በትዕቢታቸው ይዋረዳሉ የትዕቢት ጾር ሳይቀር አሶ ፋሁላችሁ ለማሰት ቤተ መቅደስን መጨረሻ አያረገ ።

፲፫ ወፈጺሞ ሰይጣን አመክሮተ በኵሉ ኃይሉ ኀደጎ እስከ ጊዜሁ ።

፲፫ ሰይጣን በሁሉ ከተፈታተነው በኋላ እስከ ጊዜው ተወው ።
በዕለተ ዓርብ በአይሁድ ሥጋው ሁኖ እስኪያስቅለው አይደርስበትም ።
ዘከመእኀዘ ኢየሱስ ይሰብክ በገሊላ ።

፲፬ ወተመይጠ እግዚእ ኢየሱስ በኃይለ መን ፈስ ቅዱስ ወሖረ ገሊላ ። ማቴ. ፬ ፡ ፲፪ ማር ፩ ፡ ፲

፲፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በመንፈስ ቅዱስ ድል ነሥቶ ወደ ገሊላ ተመለሰ ።
ወተሰምዓ ነገሩ ውስተ ኵሉ በሐውርት ።
ተአምራቱም በየሀገሩ ተሰማ ።

፲፭ ወይሜህሮሙ በኵሉ ምኵራባቲሆሙ ።
፲፭ በየጉባኤያቸውም ያስተምራቸው ነበር ።
ወያነክሩ ምሕሮቶ ።
ትምርቱንም ያደንቁ ነበር ።
ወይሴብሕዎ ፤ አመሰገኑት
ወኵሉ ያከብሮ ፤ ሁሉ ያከብረዋል ።

ዘከመ ሰበከ ኢየሱስ በናዝሬት

፲፮ ወሖረ ናዝሬት ኀበ ተሐፅነ ። ማቴ.፲፫ ፡ ፶፬ ማር.፮ ፡ ፩ ዮሐ. ፬ ፡ ፵፬

፲፮ ወዳደገበት ወደ ናዝሬት ሄደ ወቦአ ምኵ ራበ በዕለተ ሰንበት በከመ ያለምዶ ።
እንዳለመደ ቅዳሜ ወደምኵራብ ገባ ።
ወተንሥአ ያንብብ ፤ ሊያነብ ተነሣ ።

፲፯ ወወሀብዎ መጽሐፈ ኢሳይያስ ። ማቴ. ፲፫ ፡ ፶፬ ማር.፮ ፡ ፩ ዮሐ.፬ ፡ ፵፬

፲፯ መጽሐፈ ኢሳይያስ ሰጡት ። አንድም አንብብ ብለው መጽሐፈ ኢሳይያስ ሰጡት ሊያነብ ተነሣ ።

፲፰ ወከሢቶ መጽሐፈ ረከበ መካነ ኀበ ጽሑፍ ዘይብል መንፈሰ እግዚአብሔር ላዕሌየ ዘበእንቲአሁ ቀብዐኒ ። ኢሳ. ፷፩ ፡ ፩

፲፰ ወደፊት እዜንዎሙ ብሎ የሚያመጣውን ዘበእንቲአሁ ብሎ አጸፈ መጽሐፉን ገልጾ ባለ ማስ ተማር በኔ ህ ል ው ና ባለ መንፈስ ቅዱስ ያዋሐ ደኝ እግዚአብሔር እዜንዎሙ ለነዳያን ፈነወኒ ፤ ነዳያንን አስተምራቸው ዘንድ ላከኝ ከሚልአንቀጽ ደ ረሰ እንድምመንፈስዘዚአየበህላዌ ለሊሁ ኃደረ ላዕሌየ ብሎ ሳዊሮስ ዘእንጾኪያ ተርጕሞታልና ብሎ የባሕ ርይ ሕይወቱ መንፈስ ቅዱስ በኔ ህልው ነው ፤ ወዘ በእንቲአሁ ቀብዐኒ ስለ ማስተማርም ያዋሐደኝ መንፈስ ቅዱስ ነዳያንን አስተምራቸው ዘንድ ላከኝ የሚል አንቀጽ አገኘ ከሚል አንቀጽ ደረሰ ።

፲፱ እሰብክ ሎሙ ግዕዛነ ለፂዉዋን ።
፲፱ የሥጋ ምርኮኞችን በተአምራት የነፍስ ምርኮኞችን በትምህርት አስተምር ዘንድ ።
ወእስተፍሥሖሙ ለኅዙናን ።
ኅዙናን ሥጋን በተአምራት ኅዙናን ነፍስን በትም ህርት ደስ አሰኛቸው ዘንድ ።
ወእንግሮሙ ለግፉዓን ።
በሥጋ የተጠቁትን በተአምራት በነፍስ የተጠቁትን በትምህርት አደናቸው ዘንድ ።
እፍትሖሙ ለሙቁሐን ።
በሥጋ የታሰሩትን በተአምራት በነፍስ የታሰሩትን በትምህርት እፈታቸው ዘንድ ።
ወእፈውሶሙ ለቁሱላን ።

ቁስላን ሥጋን በተአምራት ቁስላን ነፍስን በትም ሀርት አድናቸው ዘንድ ።
ወእሰብከ ሎሙ ዓመተ እግዚአብሔር ኅሪተ ።
በተመረጸች በእግዚአብሔር ቀን ማለት ሦስት ዓመት ወዘኮነ መዋዕለ ።
ሦስቱን ወር አስተምር ዘንድ ፤ አንድም ዘመነ ሥጋ ዌን ወዘኮነ መዋዕለ ፤ መዋዕለ ንስሐን አስተምር ዘንድ ሾመኝ የሚል አንቀጽ አገኘ ከሚል አንቀጽ ደረሰ ።

፳ ወከደኖ መጽሐፈ ወመጠዎ ለላእክ ወነበረ ።
፳ መጽሐፉን አጥፎ ለቃቤቱ ሰጥቶት ተቀመጠ
ወእንሥኡ አዕይንቲሆሙ ኵሎሙ እለ ሀለዉ ውስተ ምኵራብ ወነጸርዎ ።
በምኵራብ ያሉ ሁሉ ዓይናቸውን አቅንተው አዩት ።

፳፩ ወአኀዘ ይቤሎሙ ዮም በጽሐ ቃለ ዝንቱ መጽሐፍ ወተፈጸመ ውስተ እዘኒክሙ ።

፳፩ የዚህ መጽሐፍ ነገር ገና ዛሬ በጆሯችሁ ደረሰ ተፈጸመ እያለ ይነግራቸው ጀመረ ።
ወእንዘ ይመስል ሎሙ ይላል ፤ እንግርሙ እፍት ሆሙ እፈውሶሙ አስተፍሥሖሙ የተባሉ እኔ ነኝ ግፉዓን ሙቁሓን ቍሱላን ኅዙናን የተባላችሁ እናንተ ናችሁ እያለ እየመሰለ የሚተረጉምላቸው ጀመረ

፳፪ ወኵሎሙ ሰምዕዎ ወአንከርዎ ምግባረ ቃሉ ወማዕምረ አፉሁ ።
፳፪ የተከናወነ ቃሉን ማለት እስከድንቅ እንዲ ናውና መናገሩን ሰምተው አደነቁ ።
ወይቤሉ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልደ ዮሴፍ ።
ይህ የዮሴፍ ልጅ አይደለምን አሉ ።

፳፫ ወይቤሎሙ ቦኑ ትብሉኒ ዛተ ምሳሌ ዓቃቤ ሥራይ ፈውስ ርእሰከ ።
፳፫ እስም በውኑ ባለመድኃኒት ራስክን አድን ትሉኛላችሁ ፤ አንድም ራስህን ቤተ እስራኤልን አድን ትሉኛላችሁ ፤ አንድም ረድ እስኩ እመበቀልከ ትሉኛላችሁ ።
ኵሎ ዘሰማዕነ ዘገበርከ በቅፍርናሆም ግበር በዝየኒ በሀገርከ በቅፍርናሆም የሠራኸውን እንደሰማነው በዚህም በሀገርህ አድርግ ትሉኛላችሁ አላቸው ።
፳፬ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ ኢይከብር ነቢይ በሀገሩ ።
፳፬ ነቢይ በሀገሩ አይከብርም ብዬ እነግራች ኋለሁ ።

፳፭ አማን እብለክሙ ብዙኃት መበለታት ሀለዋ በውስተ እስራኤል በመዋዕለ ኤልያስ ነቢይ አመ ተዐፅወ ሰማይ ፫ተ ዓመተ ወ፮ተ አውራኃ እስከ ኮነ ረኃብ ዓቢይ ውስተ ኵሉ ምድር ።
፫ ነገሥት ፲፰ ፥ ፱
፳፭ ዝናብ ሳይዘንብ ሁሉ ረኃብ ጸንቶባቸው ድርቅ ሰማይ በተዘጋ ጊዜ ማለት ዝናም ለዘር ጠል ለመከር እንዳይሰጥ ሦስት ዓመት ከስድስት ወር በተከለከለ ጊዜ በነቢዩ በኤልያስ ዘመን ብዙ ባልቴቶች እንደ ነበሩ ።

፳፮ ወኢተፈነወ ኤልያስ ኀበ አሐቲ እምኔሆን ፪ ነገ. ፭ ፥ ፲፬

፳፮ ኤልያስም ከነርሱ ወደ አንዲቱ እንዳልተላከ፤ ዘእንበለ ብእሲት መበለት ዘሀለወት በሰራጵታ ዘሲዶና ።
በሲዶና ክፍል በሰራጵታ ወዳለችው ሴት እንደ ተላከ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ።

፳፯ ወብዙኃን እለ ለምጽ ሀለዉ በውስተ እስራኤል አመ መዋዕለ ኤልሳዕ ነቢይ ።

፳፯ በኤልሳዕ ዘመን በእስራኤል ዘንድ ብዙ ለምጻሞች ነበሩ ።
ወኢንጽሐ አሐዱሂ እምኔሆሙ ዘእንበለ ንዕማን ሶርያዊ ከሶርያዊ ሰው ከንዕማን በቀር ከነርሱ አንዱ ስንኳ አልነጻም ።

፳፰ ወተምዑ ኵሎሙ እለ ሀለዉ በምኵራብ ሰሚዖሙ ዘንተ ።

፳፰ በጉባኤ ያሉ ሁሉ ይህን ሁሉ ሰምተው ተቆጡ ። ሐተታ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልደ ዮሴፍ ቢሉት ቦኑ ትብሉኒ ዘልክሙ ዛተ ምሳሌ ዓቃቤ ሥራይ ፈውስ ርእሰከ ብሎ አማን አማን እብለክሙ ኢይከብር ነቢይ በሀገሩ ይላቸዋል ፤ እንድናከብርህ ኵሎ ዘሰማዕነ ዘገበርከ በቅፍርናሆም ግበር በዝየኒ በሀገርከ ይሉታል ።
አማን እብለክሙ ብዙኃት መበለታት ወብዙኃን እለ ለምጽ ይላቸዋል ፤ አንድም አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልደ ዮሴፍ ቢሉት አማን እብለክሙ ኢይከብር ነቢይ በሀገሩ ብሎ ቦኑ ትብሉኒ ዛተ ምሳሌ፤ ዓቃቤ ሥራይ ፈውስ ርእሰከ ይላቸዋል እኋቸውም ኵሎ ዘሰማዕነ ዘገበርከ በቅፍርናሆም ይሉታል እማን እብለክሙ ብዙኃት መበለታት ሀለዋ ወብዙኃን እለ ለምጽ ሀለዉ ይላቸዋል ፤ አንድም እማን እብለ ክሙ ብዙኃት መበለታት ሀለዋ ወኢተፈነወ ኀበ አሐቲ እምኔሆን ፤ ወብዙኃን እለ ለምጽ ሀለዉ ወኢንጽሐ አሐዱሂ ዘእንበለ ንዕማን ቢላቸው ፤ ወተምዑ ኵሎሙ እለ ሀለዉ በምኵራብ ሰሚዖሙ ዘንተ ።
ዛሬስ በሴት በለምጻም ይመስለን ጀመረ ብለው ተቆጥተው ፤
አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ወልደ ዮሴፍ ይሉታል ፤ ቦኑ ትብሉኒ ዛተ ምሳሌ ዓቃቤ ሥራይ ፈውስ ርእሰከ ይላቸዋል ፤ ኵሎ ዘገበርከ በቅፍርናሆም ግበር በዝየኒ ይሉታል ፤ አማን እብለክሙ ኢይከብር ነቢይ በሀገሩ ብሎ ይጨርሳል ።

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስምዖንን አትፍራ አይዞህ
እምይእዜሰ ሰብአ ታሤግር ።
ከእንግዲህስ ወዲህ ሰው የምታጠምድ የምታስተምር
ትሆናለህ አለው ።

፲፩ ወአውፅኡ አሕማሪሆሙ ውስተ ምድር ።
፲፩ መርከቦቻቸውን ከየብስ አውጥተው ።
ወኃደጉ ኵሎ ወተለውዎ ።
ሁሉን ትተው ለጊዜው በእግር ተከተሉት ፍጻሜው
በግብር መሰሉት ማቴዎስ ከባሕር ተጠሩ ያላል
ሉቃስ ከወደብ ተጠሩ አለ እንደምን ነው አይጣላም
ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ሉቃስ
እንዲህ ማለቱ ወደቡ አያይዞ ከባሕር የሚያደርስ
ስለሆነ ፤ እንድም ነገር እንደ ሉቃስ ነው ከወደብ
ተጠርተዋል ወወዓሉ ኀቤሁ እስከ ዐሥርቱ ሰዓት
እንዲል ሲማሩ ውለው ተመልሰዋል ሁለተኛ
እንደ ማቴዎስ ከባሕር ተጠርተዋል የፊተኛውን
ሉቃስ የኋለኛውን ማቴዎስ ጻፉ ነገር እንደ ሉቃስ
ነው ፤ ጌታ ያልተቀመጠባት መርከብ የእሪት የኃ
ጢአት ፤ ጌታ የተቀመጠባት መርከብ የጽድቅ የወ
ንጌል ምሳሌ ።

ዘከመ አሕየዎሙ ኢየሱስ ለለምጻዊ ወለመጻጉዕ።

፲፪ ወኮነ እንዘ ሀሎ ውስተ አሐቲ ሀገር መጽአ
ብእሲ ዘለምጽ ኵለንታሁ ማቴ. ፰፥፪ ማር. ፩፥፵።

፲፪ ባንድ አገር ተቀምጦ ሳለ ሁለንተናውን
ለምጽ የያዘው ሰው መጣ ።
ወሶበ ርእዮ ለእግዚእ ኢየሱስ ሰገደ በገጹ ወአስተ
ብቍዖ ።
ጌታን ባየው ጊዜም ግንባሩን መሬት አስነክቶ ማለ
ደው ።
ወይቤሎ እግዚኦ እመሰ ፈቀድከ ትክል አንጽሖትየ ።
አቤቱ ከወደድከስ እኔን ማዳን ይቻልሃል አለው ።

፲፫ ወሰፍሐ እዴሁ ወገሠሦ ።
፲፫ እጁን ዘርግቶ ዳሰሰው ።
ወይቤሎ እፈቅድ ንጻሕ ።
መዳንህን እውዳለሁ ዳን አለው ።
ወኃደጎ ለምጹ ሶቤሃ ።
ያን ጊዜውንም የለምጹ ደዌ ተወው ።

፲፬ ወአዘዞ ወከልኦ ኢይንግር ወኢለመኑሂ
ወይቤሎ ሖር አፍትን ርእሰከ ለካህን ዘሌ.፲፬.፬ ።

፲፬ ራስህን ለካህን አስመርምር ።
ወአብእ መባአ በእንተ ዘነጻሕከ በከመ አዘዘ ሙሴ ።
ከለምጽሕ ስለ ዳንክ ሙሴ እንዳዘዘ መባሕን ስጥ
እንጂ ለማንም ለማን አትናገር አለው ፤ ከመ ይኩን
ስምዓ ላዕሌሆሙ ምስክር ሊሆንባቸው ።

፲፭ ወተሰምዓ ነገሩ ፈድፋደ ።
፲፭ ነገሩም ፈጽሞ ተሰማ ።
ወመጽኡ ኀቤሁ ብዙኃን ሰብእ ይስምዕዎ ።
ብዙ ሰዎችም ሊሰሙት ወደሱ መጡ ።
ወይትፈወሱ እምደዌሆሙ ።
ከደዌያቸውም ይፈወሱ ዘንድ ።

፲፮ ወውእቱሰ ይወፅእ ገዳመ ወይጼሊ በህየ ።
፲፮ እሱ ግን ወደ ገዳም ወጥቶ ይጸልይ ነበር ።

፲፯ ወእምዝ ኮነ በአሐቲ ዕለት እመዋዕል
እንዘ ሀሎ ይሜህሮሙ ወይነብሩ ፈሪሳውያን ወሊቃ
ናተ ኦሪት እለ መጽኡ እምገሊላ ወእምኵሉ አህጉረ
ይሁዳ ወእምኢየሩሳሌም ።

፲፯ ከዕለታትም ባንድ ቀን ከኢየሩሳሌምና
ከገሊላ ከየሀገሩም ሁሉ የመጡ የኦሪት መምህራንና
ፈሪሳውያን ከዚያ ተቀምጠው ሳሉ ያስተምር ነበር ።
ወኃይለ እግዚአብሔር ውእቱ በዘይፌውስ ።
በሚፈውሳቸውም ገንዘብ ይፈውሳቸው ዘንድ የእ
ግዚአብሔር ኃይል ነበር ።

፲፰ ወአምጽኡ ኀቤሁ ብእሴ መፃጉዓ እንዘ
ይጸውርዎ ፬ቱ ዕደው በዓራት ። ማቴ.፱፥፪ ማር.፪፥፫፡

፲፰ አንድ ሽባ አራት ሰዎች ባልጋ ተሸክመው
አመጡት ።
ወፈቀዱ ያብእዎ ኀቤሁ ይፈውሶ ።
ሊያድነው ወደሱ ያቀርቡት ዘንድ ወደዱ ።

፲፱ ወኃጥኡ እንተ ኀበ ያበውእዎ ኀበ እግዚእ
ኢየሱስ እስመ ጽድቅ ሰብእ ።

፲፱ ሰው ስለበዛ እንደሚያገቡት አጡ ።
ወዓርጉ ናሕሰ ወነሠቱ ጠፈረ ወአውረድዎ ምስለ
ዓራት ውስተ ቤት ።
ከሰገነት ላይ ወጥተው ጠፈሩን አፍርሰው ከናልጋው
አውርደው ከቤት አገቡት ።
ቅድሜሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታ ካለበት ።

፳ ወርእዮ ሃይማኖቶሙ ወይቤሎ ለውእቱ
ብእሲ ድውይ ትኅድገ ለከ ኃጢአትከ ።

፳ ሃይማኖታቸውን አይቶ ያንን የታመመ ሰው
ኃጢአትህ ተሰርዮልሃል አለው ።

፳፩ ወአንዙ የኀልዩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን
ወይቤሉ ምንትኑ ዝንቱ ዘይነብብ ጽርፈተ ።

፳፩ ጸሐፍት ፈሪሳውያን አሰበው ይህ ስድብ
የሚናገር ማነው መኑ ዘይክል ኃዲገ ኃጢአት ዘእ
ንበለ ፩ እግዚአብሔር ባሕቲቱ ።
ከብቻው ካንድ እግዚአብሔር በቀር ኃጢአት ማስ
ተስረይ የሚቻለው ማነው ሌላ ።

፳፪ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ዘይሄልዩ
ወይቤሎሙ ምንተ አኩየ ተሐልዩ በልብክሙ ።

፳፪ ጌታም የሚያስቡትን አውቆባቸው በል ቦቻሁ ለምን ክፉ ታስባላችሁ ።

፳፫ ምንት ይቀልል እምብሂለ ተኅደገ ለከ ኃጢአትከ ወእምብሂለ ተንሥእ ወጹር ዓራተከ ወሑር ።

[illegible] ፳፬ ተንሥተህ አልጋህን ተሸከመህ ሂድ ከማ [illegible] ኃጢአትህ ተሰረየልህ ከማለት ማን ይቀላል [illegible] ።

፳፬ ከመ ታእምሩ ወትለብዉ ከመ ብውህ ሉቱ [illegible] ዕጓለ እመሕያው ይኅድግ ኃጢአተ በዲበ ምድር ።

፳፭ [illegible] እንዲ [illegible] ተነሣ [illegible] ተነሥቶ [illegible] ወደቤትህ [illegible]

፳፮ ወተንሥአ ሶቤሃ ወነሥአ ዓራቶ ዘዲ [illegible] ወአተወ ቤቶ እንዘ [illegible] ለእግዚአብሔር ።

[illegible] አልጋ ተሸ [illegible] በሬዎቻቸው ሄደ ።
[illegible] ።
[illegible] ።
[illegible] ለእግዚአብሔር ።
[illegible] አመሰገኑ ።
[illegible] ።
[illegible] ።
[illegible] ።
[illegible] ለሌዊ ።

[illegible] እምህየ ርእየ ብእሴ መጸ [illegible] እንዘ ይነብር ኀበ ምጽባሕ ማቴ [illegible] ።
[illegible] ከዚያ ወጥቶ ሲሄድ ሌዊ የሚ [illegible] ተቀምጦ አየ ።
[illegible] ።

[illegible] ወተለዎ ።
[illegible] ተከተለው ።
[illegible] ኀቢየ ምሳሐ በቤቱ ።
[illegible] በቤቱ ታላቅ ምሳ አቀረ [illegible]

[illegible] ምስሌሁ መጸብሐን [illegible] ምስሌሆሙ ።

ከሱ ጋራ ለምሳ የተቀመጡ ብዙ ሰዎች መጸብሐ ሐንና ኃጥአንም ነበሩ ።
ወባዕዳንኒ ብዙኃን ምስሌሆሙ ሌሎችም ብዙ ሰዎች ።

፴ ወአንጐርጐሩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ላዕሌሁ ።

፴ ጸሐፍት ፈሪሳውያንም በሱ ተቆጡ ።
ወይቤልዎሙ ለአርዳኢሁ ለምንት ትበልዑ ወትሰ ትዩ ምስለ ኃጥአን ወመጸብሐን ።
ደቀ መዛሙርቱን ከቀራጮች ጋራ ስምን ትበላላ ችሁ ትጠጣላችሁ አሏቸው ። ሐተታ ማቴዎስ ለም ንት ይበልዕ ሊቅክሙ አሏቸው ይላል ከዚህ ሉቃስ ለምንት ትበልዑ አሏቸው አለ ። እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ ማቴዎስ መም ራችሁ ከመጸብሐን ጋራ ለምን ይበላል ብለዋቸዋል ሳይመልሱ ዝም ቢሉ እሱስ ሥርዓት ዐፍራሽ ነው እናንተ ለምን ትበላላችሁ ብለዋቸዋል ። አንድም እንደ ሉቃስ ለምን ትበላላችሁ ብለው ጠይቀዋ ቸዋል ፤ ዝም አሉ እናንተስ ዐላዋቆች ናችሁ ፤ እረ ዐዋቂ ነኝ የሚለው ያ ለምን ይበላል ብለዋቸዋል የፊተኛውን ማቴዎስ የኋለኛውን ሉቃስ ጻፉ ።

፴፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ሕሙማን ይፈቅድዎ ለዓቃቤ ሥራይ ።
ባለመድኃኒትን ድውያን ይሹታል ።
ወአኮ ጥዑያን ።
ጤነኞች ግን አይሹትም ።

፴፪ ኢመጻእኩ እጸውዕ ጻድቃነ ።
፴፪ ጻድቃንን ልጠራ አልመጣሁም ።
አላ ኃጥአነ ለንስሐ ።
ኃጥአንን ወደ ንስሐ ልጠራ ነው እንጂ ።

፴፫ ወይቤልዎ ለምንት አርዳኢሁ ለዮሐንስ ጽኑዐ ይጸውሙ ።

፴፫ የዮሐንስ ደቀ መዛሙርቱ ብዙ ይጾማሉ ።
ወጸሎተ ይገብሩ ።
ጸሎትም ይጸልያሉ ።
ወከማሁ እስኪ ፈሪሳውያን ።
እንደዚሁ የፈሪሳውያንም ደቀ መዛሙርት ይጾማሉ ።
ወአርዳኢከሰ እሊአከ ይበልዑ ወይሰትዩ ።
ያንተ ደቀ መዛሙርት ግን ለምን ይበላሉ ይጠጣሉ አሉት ።

፴፬ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢይክሉ ደቂቀ ለመርዓዊ ጸዊመ እንዘ ሀሎ መርዓዊ ምስሌ ሆሙ ።

፴፬ ሙሽራ ከሳቸው ጋራ ሳለ የሙሽራ ሚዜ ዎች መጾም አይቻላቸውም ።

፴፫ ወባሕቱ ይመጽእ መዋዕል አመ ፡ ይነ ሥእዎ ለመርዓዊ እምኔሆሙ ።

፴፫ ነገር ግን ሙሽራው ከነሱ የሚለይበት ጊዜ ይመጣል ።
ወይእተ አሚረ ይጸውሙ ።
ያንጊዜ ይጾማሉ ።

፴፬ ወይቤሎሙ ምሳሌ ።
፴፬ በምሳሌ ነገራቸው ።
አልቦ ዘይጠቅብ ግምደ ድርግሃ ልብሰ ውስተ ስጠት ብሉይ ።
ያዲስ ልብስቁራጭ ባረጀ ልብስ የሚጠቅም የለም።
ወእመ አኮሰ ይሠጥጦ ሐዲስ ለብሉይ ።
ያለዚያ ግን አዲሱ አሮጌውን ይቀደዋል ።
ወኢየአሪ ምስለ ብሉይ ወኢይሰነአው ።
አይሰማማውም ።

፴፭ ወአልቦ ዘይወዲ ወይነ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ብሉይ ።

፴፭ ጉሽ ጠጅ ባዲስ ራዋት የሚሾም የለም ።

ወእመ አኮሰ ዝቁሂ ይነቅዕ ። ያለዚያ ረዋቱ ይቀደዳል ወይኑሂ ይትከዓው ። ወይኑም ይፈሳል ። ወዝቁሂ ይትኀጉል ። ራዋቱም ይቀደዳል ።

፴፮ ወለወይንሰ ሐዲስ ውስተ ዝቅ ሐዲስ ይወድይዎ ።

፴፮ ጉሹን ጠጅ ግን ባዲስ ራዋት ይሾሙታል ወይትዓቀቡ በበይናቲሆሙ ።
እርስ በርሳቸውም ይጠባበቃሉ ።

፴፱ ወአልቦ ዘይስቲ ጸአፈ ሐዲስ እንዘ ይፈ ቅድ ከራሜ ።

፴፱ ጥሩ ጠጅ ሊጠጣ ወዶ ሳለ ጉሽ ጠጅ የሚ ጠጣ የለም ።
እስመ ይኄይስ ካራሚ እምሐዲስ ።
ከጉሹ ጥሩው ይሻላልና ፤ እንደዚህም ሁሉ ወንጌልን ሊማር ወዶ ሳለ ኦሪትን የሚማር የለም እስመ ይኄ ይስ ፤ ከአሪት ወንጌል ትበልጣለችና ። ሐተታ ጉሽ ጠጅ አላት ኦሪትን ይህ ጉሽ ጠጅ ሲጠጡት ለጊዜው ደስ ያሰኛል ከሆድ ገብቶ አይሰማማም ሲጠጡት ደስ እንዲያሰኝ ፤ ኦሪትም ለእም ዓቀብከ ኦሪተከ ትበ ልዕ ከራሜ ከራሚከ ወይሰፍፍ ማኅበብተ ወይንከ ወትሬኢ ውሉደ ውሉድከ እስከ ሣልስ ወራብዕ ትው ልድ ስትል ደስ ታሰኛለች ፤ ጉሽ ጠጅ ከሆድ ገብቶ እንዳይሰማማ ኦሪትም በሞት ጊዜ ከርደተ ገሃነም አታድንም ፤ ጥሩ ጠጅ አላት ወንጌልን ፤ ጥሩ ጠጅ ሲጠጡት ይከብዳል ይገርማል ከሆድ ከገባ በኋላ ገብቶ ይሰማማል ። ወንጌልም በዚሁ ጸፍአከ መል ታሕቴከ እንተ የማን ሚጥ ሎቱ ካልዕታ ወለዘሂ ይፈቅድ ይትዓገልከ መልበስከ ኅድግ ሎቱ ክዳንከሂ ወለዘሂ አበጠከ ፩ደ ምዕራፈ ሑር ምስሌሁ ወአብ ጽሕ ሎቱ ፪ኤ ምዕራፈ ስትል ትገርማለች ከሆድ ከገባ በኋላ እንዲስማማ ርደተ ገሃነም የለባትምና ። አንድም አልቦ ዘይስቲ ከራሜ እንዘ ይፈቅድ ጸዐፈ ። አፍለኛውን ሊጠጣ ወዶ ሳለ መጻጻ የሚጠጣ የለም ። እስመ ይብል ይኄይስ ሐዲስ እምነ ከራሚ ፤ ከመጻጻ አፍለኛው ይሻላል ይላል ። እንደዚሁም ሁሉ ወንጌ ልን ሊማር ወዶ ሳለ ኦሪትን የሚማር የለም ከኦሪት ወንጌል ትበልጣለች ይላልና ኦሪትን መጻጻ አላት አስቀድማ ተሠርታለችና ወንጌልን አፍለኛ አላት በኋላ ተሠርታለችና ።

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ በእንተ
ሰዊት ወዕለተ ሰንበት ።

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወእምዝ ካዕበ ወፈረ እግዚእ ኢየሱስ ማዕከለ ገራውህ በሰንበት ።

፩ ከዚህ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሰን በት በእርሻ መካከል ሄደ ።
ወመሐዉ አርዳኢሁ ሰዊተ ወሐሰዩ በእደዊሆሙ ወበልዑ ። ደቀ መዛሙርቱ እሸት እየቆረጡ እያሹ ይበሉ ጀመር ።

፪ ወይቤልዎሙ ፈሪሳውያን ለምንትኑ ትገብሩ ዘኢይከውን ለገቢር በሰንበት ።

፪ ፈሪሳውያን በሰንበት ለመሥራት የማይገባ ሥራ ለምን ትሠራላችሁ አሏቸው ።
ሐተታ ፤ ማቴዎስ ርኢ ዘይገብሩ አርዳኢከ ብለው ጠየቁት ይላል ። ሉቃስ ለምንት ትገብሩ አሏቸው አለ ። እንደምን ነው አይለያይም ቢሉ አይለያይም ። ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ርኢ ዘይገብሩ አርዳኢከ። ብለው ጠይቀውታል ። ዝም አላቸው ለምንት ትገ ብሩ ብለው እነሱን ጠይቀዋቸዋል ። የፊተኛውን ማቴዎስ የኋለኛውን ሉቃስ ጽፈዋል ። አንድም ነገር እንደ ሉቃስ ነው ፤ ለምንት ትገብሩ ብለው እነ ሱን ጠይቀዋቸዋል ። ዝም ቢሏቸው ባይመልሱላ ቸው ርኢ ዘይገብሩ ብለው እሱን ጠይቀውታል እሱ ይመልስላቸዋል ።

፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ኢያንበብክሙኑ ዘገብረ ዳዊት አመ ርኅበ። ዳዊት በተራበ ጊዜ ያደረገውን አላነበባችሁምን ። ውእቱሂ እርሱም ወእለ ምስሌሁ ። ከሱም ጋራ ያሉት

፬ ዘከመ ቦአ ቤተ እግዚአብሔር ወነሥአ ኅብ ስተ ቍርባን ።

፬ ከቤተ እግዚአብሔር ገብቶ የሚሠሩትን መሥዋዕት እንደ ወሰደ ።
ወበልዓ ውእቱኒ ። እሱም እንደ በላ ። ወወሀቦሙ ለእለ ምስሌሁ ዘኢይከውኖሙ ለበሊዕ ።
ከሱም ጋራ ላሉ ለመብላት የማይገባቸውን እንደ ሰጣቸው ። ዘእንበለ ለካህናት ለባሕቲቶሙ ለካህናት ብቻ ይገባቸዋል እንጂ ።

፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ውእቱ ለሰንበት ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፭ የሰንበት ጌታዋም ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ነው አላቸው ።

ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ ለዘየብሰት እዴሁ ።

፮ ወእምዝ በካልዕት ሰንበት ቦአ ምኵራብ ወመሀሮሙ ።

፮ ከዚህ በኋላ በሁለተኛው ሰንበት ከምኵራብ ገብቶ አስተማራቸው ።

፮ ወሀሎ ብእሲ ዘየብሰት እዴሁ እንተ የማን ።
፮ ቀኝ እጁ የሰለለች ሰው ነበር ወይትዓቀብዎ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ለእመ ይፌውስ በሰንበት ።
ጸሐፍት ፈሪሳውያን በሰንበት ይፈውሰው እንደሆነ ብለው ይጠባበቁት ነበር ።
ከመ ይረክቡ ምክንያተ ዘያስተዋድይዎ ።
የሚያማልሉት ነገር ያማሉት ዘንድ ምክንያት ያገኙበት ዘንድ ።

፰ ወውእቱሰ የአምሮሙ ዘይሔልዩ ።
፰ እሱ ግን የሚያስቡትን ያውቅባቸው ነበር ።
ወይቤሎ ለውእቱ ብእሲ ተንሥእ ወቁም ማዕከለ ።
ያንንም ሰው አለው ተነሥተህ ቁም ።
ወተንሥአ ወቆመ ።
ተነሥቶ ቆመ ።

፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እሴእለክሙ ወምንት ውእቱ ዘይደሉ ዘይከውን በሰንበት ።
፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በሰንበት የሚገባውን እጠይቃችኋለሁ ።
ገቢረ ሠናይኑ ፡ አው ገቢረ እከይኑ ።
መልካም መሥራት ነው ። ወይስ ክፉ መሥራት ።
አሕይዎ ነፍስኑ። ሙሢመ ቀቲል ነፍስ ማዳን ነውን ።
ወይስ ነፍስ መግደል ነው የሚገባው አላቸው ።
፲ ወአርመሙ ። ዝም አሉ ወነጸሮ ኵሎሙ በመዓት ይቤሎ ለውእቱ ብእሲ ስፋሕ እዴከ ።
፲ እነሱንም በመዓት አይቶ እጅህን ዘርጋ አለው ወሰፍሐ ።           እጁን ዘረጋ ።
ወሐይወት እዴሁ ከመ ካልእታ እንደ ግራዪቱ ሆነች
፲፩ ወእሙንቱሰ የአብዱ ፈድፋደ ።
፲፩ እነሱ ግን እጅግ ተናደዱ ።

ወተማከሩ በበይናቲሆሙ ዘከመ ይሬስይዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታን እንደሚያደርጉት እርስ በርሳቸው ተማከሩ ።

ዘከመ ሰመዮሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሐዋርያት ።

፲፪ ወእምዝ ኮነ በውእቱ መዋዕል ዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ደብር ይጼሊ ።

፲፪ በዚያ ወራት ሊጸልይ ወደ ተራራ ወጣ ።
ወያሌሊ በጸሎት ኀበ እግዚአብሔር ።
ያስተበቍዕ ሲል ነው። ወደ እግዚአብሔር በመጸለይ ይተጋ ዘንድ ።

፲፫ ወጸቢሖ ጸውዖሙ ለአርዳኢሁ ማቴ ፡ ፲፩ ፡ ማር ፡ ፫ ፡ ፲፫ ።

፲፫ በነጋም ጊዜ ደቀ መዛሙርቱን ጠራቸው።
ወኀረየ እምውስቴቶሙ ዐሠርተ ወክልኤተ ወሰመዮሙ ሐዋርያተ ።
ከነሱም ዐሥራ ሁለቱን መርጦ ሐዋርያት አላቸው
፲፬ ስምዖን ዘተሰምየ ጴጥሮስ ።
፲፬ ጴጥሮስ የተባለ ስምዖን ።
ወእንድርያስ እኁሁ ።    ወንድሙ እንድርያስ ፤
ወያዕቆብ ።    ያዕቆብም ።
ወዮሐንስ ።    ዮሐንስም
ወፊልጶስ ።    ፊልጶስም
ወበርተሎሜዎስ ።    በርተሎሜዎስም ።

፲፭ ወማቴዎስ ።    ማቴዎስም
፲፭ ወቶማስ ።    ቶማስም
ወያዕቆብ ወልደ እልፍዮስ ።
የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብም ።

፲፮ ወስምዖን ቀናዒ ።
፲፮ ቀናዒ የሚባለው ስምዖን ።
ወይሁዳ ዘያዕቆብ ።
የያዕቆብ ወንድም ይሁዳ ።
ወይሁዳ አስቆሮታዊ ዘአኀዎ ወዘአግብኦ ።
ከድቶ ያስያዘው የአስቆሮት ሰው ይሁዳም ናቸው ።

፲፯ ወወረደ ምስሌሆሙ ወቆመ ውስተ መካን ርሒብ ።

፲፯ ከርሳቸው ጋራም ወርዶ በሰፊ ቦታ ቆመ ።
ወብዙኃን ሰብእ እምአርዳኢሁ ።
ከደቀ መዛሙርቱም ወገን ብዙ ሰዎች ነበሩ ።
ወብዙኃን ጥቀ እምሕዝብ ።
ከሕዝቡም ወገን እጅግ ብዙ ሰዎች ።
ዘእምኵሉ ይሁዳ ።
ከይሁዳ አውራጃ ሁሉ የመጡ ።
ወእምኢየሩሳሌም ወእምጢሮስ ወሲዶና ።
ከኢየሩሳሌምና ከጢሮስና ከሲዶና ።

ወእምጢሮስ ወሲዶና እለ መጽኡ ይስምዕዎ ወይትፈወሱ እምደዌሆሙ ።
ከጢሮስና ከሲዶና ሊሰሙት ከደዌያቸውም ሊፈወሱ የመጡ ።

፲፰ ወእለሂ ኢጋንንት እኩያን ፤
፲፰ የክፉዎች አጋንንት ያደሩባቸውም ይድኑ ነበር ።

፲፱ ወኵሎሙ አሕዛብ ይፈቅዱ ይግሥሥዎ ።
፲፱ ሕዝቡ ሁሉ ሊዳስሱት ይሹ ነበር ።
እስመ ኃይል ይወፅእ እምኔሁ ።
ኃይል ከሱ ትወጣ ነበርና ።
ወያሐይዎሙ ለኵሎሙ ፤
ሁሉንም ይፈውሳቸው ነበር ።

በእንተ ሰብከት በውስተ ደብር ወበእንተ ብፁዓን ።

፳ ወውእቱሰ አንሥአ አእይንቲሁ ኀበ አርዳኢሁ ፡ ማቴ፡፭ ፡ ፩ ።

፳ እሱ ግን ወደ ደቀ መዛሙርቱ ዓይኑን አንሥቶ ።
ወይቤሎሙ ብፁዓን አንትሙ ነዳያን ።
ድሆች ብፁዓን ናችሁ ።
እስመ ለክሙ ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
መንግሥት ሰማያት የናንተ ናትና ።

፳፩ ብፁዓን እለ ትርኅቡ ይእዜ ፡ ማቴ፡፭፡፮ ።
ዛሬ የምትራቡ ብፁዓን ናችሁ ።

፳፩ እስመ ትጸግቡ ። ትጸግባላችሁና ።
ብፁዓን እለ ትበክዩ ይእዜ ።
ዛሬ የምታለቅሱ የተመሰገናችሁ ናችሁ ።
እስመ ትስሕቁ ። ደስ ይላችኋልና ።

፳፪ ብፁዓን አንትሙ ሶበ ይጸልዑክሙ ሰብእ።
፳፪ እናንተም ሰዎች ቢጠሏችሁ የተመሰገናችሁ ናችሁ ።
ወይፈልጡክሙ ። ቢለዩዋችሁ ።
ወይሰድዱክሙ ። ከሀገራችሁ ቢያሰጧችሁ ።
ወይጼዕሉክሙ ። ቢሰድቧችሁ ።
ወያወፅኡ ለክሙ ስመ እኩየ በእንተ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
በወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ስለ አመናችሁ ክፉ ስም ቢያወጡላችሁ ።

፳፫ ተፈሥሑ ወተሐሠዩ ይእተ አሚረ ።
፳፫ በዚያን ጊዜ ደስ ይበላችሁ ።
ወእንፈርዐጹ ኃሤትም አድርጉ ።
እስመ ብዙኅ ዕሤትክሙ በሰማያት ።
ዋጋችሁ በሰማይ ብዙ ነውና ።
እስመከማሁ ረሰይዎሙ ለነቢያት ቀደምትአበዊሆሙ።
ባባቶቻቸው በነቢያት እንዲህ ያደርጉ ነበርና ።

፳፬ ወባሕቱ አሌ ለክሙ አብዕልት ።
ሲራ፡፴፩፡ ፰ አሞ. ፮ ፡ ፩ ።

፳፬ እናንተ ባለጸጎች ወዮላችሁ ።
እስመ ሰለጥክሙ ትፍሥሕትክሙ ።
ሐተታ ሉቃስ አጸፋ ይጽፋል ደስታችሁን ጨርሳችኋልና ።

፳፭ አሌ ለክሙ እለ ትጸግቡ ይእዜ ። ኢሳ ፷፭ ፡ ፲፫ ።

፳፭ ዛሬ የምትጸግቡ ወዮላችሁ ።
እስመ ትርኅቡ ። ትራባላችሁና ።
አሌ ለክሙ እለ ትስሕቁ ይእዜ ።
ዛሬ የምትስቁ ወዮላችሁ ።
እስመ ትበክዩ ወትላህዉ ። ታለቅሳላችሁና ።

፳፮ አሌ ለክሙ ሶበ ሠናየ ይብል ሰብእ ላዕሌክሙ ወይዌድሱክሙ ።

፳፮ ሰው ቢያመሰግናችሁ ወዮላችሁ ።
እስመ ከማሁ ረሰይዎሙ ለነቢያተ ሐሰት አበዊሆሙ ነቢያተ ሐሰት ።
አባቶቻችሁን ሰላም ሳይኖር ሰላም እያሉ በሐሰት ጐድተዋቸዋልና በሐሰት ቢያመሰግኑዋችሁ ወዮላችሁ ።
አንድም ለነቢየተ ሐሰት አበዊክሙ ሰው በውዳሴ ከንቱ ቢያመሰግናችሁ ወዮላችሁ ። ቀድሞ አባቶቻችሁን ነቢየተ ሐሰትን ሕግ መጠበቁ ሳይኖር ሕግ ጠባቆች እያሉ ጐድተዋቸዋልና ሰው በውዳሴ ከንቱ ቢያመሰግናችሁ ወዮላችሁ ። አንድም ቅጽል አድርገው ነቢየተ ሐሰት አባቶቻችሁን በሐሰት ጐድተዋቸዋልና ሰው በሐሰት ቢያመሰግናችሁ ወዮላችሁ ።

፳፯ ወለክሙሰ እለ ትሰምዑኒ እብለክሙ አፍቅሩ ጸላእተክሙ ። ማቴ ፡ ፭ ፡ ፵፬ ።

፳፯ ለምትሰሙኝ ለናንተ ግን ጠላታችሁን ውደዱ እላችኋለሁ ።
ወግበሩ ሠናየ ለእለ ይፀርሩክሙ ።
ለሚጠሏችሁም መልካም አድርጉ ።

፳፰ ወደኃርዎሙ ለእለ ይረግሙክሙ ።
፳፰ የሚረግሟችሁን መርቁ ።
ወጸልዩ ለእለ ይትኤገሉክሙ ።
ለሚበድሏችሁም ለምኑ ።

፳፱ ወለዘሂ ጸፍአከ መልታሕቴከ ሚጥ ሎቱ ካልዕታሂ ። ማቴ ፡ ፭ ፡ ፴፱ ፩ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፯ ።

፳፱ ፊትህን ለጸፋህም ሁለተኛውን መልሰለት ።
ወለዘሂ ነሥአከ ፡ ልብሰከ ፡ ከደንከሂ ኢትክልኦ ።
መጐናጸፊያህን ለወሰደብህም ቀሚስህን አትንሣው።

፴ ለኵሉ ለዘሰአለከ ሀብ ።
፴ ለለመነህ ሁሉ ስጥ ።
ወለእመሂ ሂደከ ንዋየከ ኢትክልኦ ።
የሚቀማሕንም እትከልከለው ።

፴፩ ወበከመ ትፈቅዱ ይግበሩ ለክሙ ሰብአ ከማሁ ግበሩ ሎሙ አንትሙ ፡ ጦቢ ፬ ፤ ፲፮ ማቴ.፯.፲፪

፴፩ ሰው ሊያደርግላችሁ የምትወዱትን እናን ተም እንዲሁ አድርጉላቸው ።

፴፪ ወእመሰ ዳዕሙ ዘአፍቀረክሙ አፍቀር ክሙ ምንትኑ ዕሤትክሙ ።

፴፪ የወደዳችሁንም ብቻ ከወደዳችሁ ዋጋችሁ ምንድነው ።
ኃጥአንሂ ዘሰ ይገብሩ ።
ይህንስ ኃጥአንም ያደርጉታል ።

፴፫ ወእመኒ አሠነይክሙ ለእለ ያሤንዩ ለክሙ ምንትኑ እንከ ዕሤትክሙ ።

፴፫ መልካም ለሚያደርጉላችሁስ መልካም ብታደርጉ ምንድነው ዋጋችሁ ።
ኃጥአንሂ ከማሁሰ ይገብሩ ።
እንደዚሁስ ኃጥአንም ያደርጋሉ ።

፴፬ ወእመኒ ለቃሕክሙ እምኀበ ዘትሴፈው ትትፈደዩ እምኔሁ ምንትኑ እንከ ዕሤትክሙ ። ዘዳግ ፲፭፥፰ ማቴ ፡ ፭ ፤ ፵፪ ።

፴፬ እንዲመልሱላችሁ ተስፋ ለምታደርጉዋ ቸው የምታበድሩ ከሆነ ዋጋችሁ ምንድነው ። እስመ ኃጥአንሂ ይሌቅሕዎሙ ለኃጥአን ከመ ይትፈ ደይዎሙ ዕሩየ ።

ያበደሩትን ሊወስዱ ኃጥአንም ለኃጥአን ያበ ድሩዋቸዋልና ።

፴፭ ወይእዜኒ አፍቅሩ ጸላእተክሙ ።
፴፭ አሁንም ጠላታችሁን ውደዱ ።
ወአሠንዩ ሎሙ ፤
መልካም አድርጉላቸው ፤
ወለቅሑ እንዘ ኢትሴፈው ትትፈደዩ ፤
እንከፈላለን ብላችሁ ተስፋ ሳታደርጉ አበድሩ ፤
ወይከውን ብዙኀ ዕሤትክሙ ፤
ዋጋችሁ ብዙ ይሆናልና ።
ወትከውኑ ውሉደ ልዑል ።
የልዑልም ልጅ ትሆናላችሁ ።

እስመ ውእቱ ኄር ላዕለ ኤራን ወላዕለ እኩያን ።
እሱ ለክፉዎም ለበጐውም ቸር ነውና ።

፴፮ ወኩኑ መሓርያነ ከመ አቡክሙ ሰማያዊ መሐሪ ውእቱ ።

፴፮ ሰማያዊ አባታችሁ ርኅሩኅ እንደሆነ እናን ተም የምትራሩ ሁኑ ።

፴፯ ኢትኰንኑ ። ማቴ.፯፥፩ ።
፴፯ አትፈራረዱም ።
ወኢትትኴነኑ ። ... አትቆርቆሩም ...

ኢትግፍዑ ።         አትበድሉ ።
ወኢይግፍዑክሙ ።     አይበድሏችሁ ፡
ኅድጉ ፤            ተው ፤
ወየኃድጉ ለክሙ ፤     ይተውላችኋል ።

፴፰ ሀቡ ወይትወሀበክሙ ፡ ማቴ.፯ ፡ ፪. ማር ፬፥ ፳፬ ።

፴፰ ስጡ ይሰጣችኋል ።
መስፈርተ ሠናየ ንኑኀ ወምሉአ ወዝኅዙኃ ።
በመልካም መስፈሪያ መልተው ፡ ንኑኀ ። ደርበብ አድርገው ። ምሉእ መልተው ።
ወዝኅዙኃ ጠብ ጠብ ሲል ።
ይሁቡክሙ ውስተ ሕፅንክሙ በብብታችሁ ማለት ሰውረው ይሰጡችኋል ። እንድም ሥራውን በሥስት ወገን ይሠሩታል በወጣኒነት በማእከላዊነት በፍጹ ምነት ክብሩንም በዚያው ልክ ይወርሱታልና ። እንድም በዚህ ዓለም በገነት አንድ ወገን በደብረ ጽዮን በመንግሥተ ሰማያት ይወርሱታልና ።
ወበመስፈርት ዘሰፈርክሙ ይሰፍሩ ለክሙ ።
በምትሰፍሩበትም መስፈሪያ ይሰፍሩላችኋል ።

በአንተ ካልዓን ትእዛዛት ።

፴፱ ወመሰለ ሎሙ ።
፴፱ ምሳሌ መሰለላቸው ፡
ወይቤሎሙ ይክል ዕውር ለዕውር መሪሐ ።
ዕውር ዕውርን ሊመራው ይቻለዋልን ።

፵ አኮኑ ክልኤሆሙ ይወድቁ ውስተ ግብ ፡ ማቴ. ፲፥ ፳፬ ዮሐ. ፲፫፥ ፲፮ ።

፵ ሁለቱ ክጉድጓድ ይወድቁ የለምን አላቸው። አንድ አርእስት አልቦ ረድዕ ዘየዓቢ እምን ሊቁ ከመ ምህሩ የሚበልጥ ደቀ መዝሙር የለም ሁለት አርእስት ተናገረ ለሁለቱም ያመጣል ፡ መጠኑ ለኵሉ ይኩን ከመ ሊቁ ።
የሁሉም መጠኑ እንደ መምህሩ ይሁን ።

፵፩ ምንተኑ ትሬኢ ኃሠረ ዘውስተ ዓይነ ቢጽከ ። ማቴ. ፯ ፡ ፫ ።

፵፩ በወንድምህ ዓይን ጉድፍ ስምን ታያለህ ። ሐተታ ዕውር ላለው ወኢትሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዓይንከ ።
ባንተ ዓይን ያለውን ምሰሶ አታስተውለውም ።

፵፪ ወእፎ ትብሎ ለቢጽከ ተዓገሥ እትኅየ እውፅእ ኃሠረ እምውስተ ዓይንከ ።

፵፪ ወንድምህን ክዓይንህ ያለውን ጉድፍ አወጣ ዘንድ ተወኝ እንደምን ትለዋለህ ።
ወአንተሰ ኢትሬኢ ሠርዌ ዘውስተ ዓይንከ ።
ባንተ ዓይን ያለውን ምሰሶ አታስተውለውም ።
ወእምዝ ትኔጽር ታውፅእ ኃሠረ እምዓይነ ቢጽከ ።

ከዚህ ፀኋላ በወንድምህ ዓይን ያለውን ጉድፍ ለማ
ውጣት ትችላለህ ።

፵፫ እልቦ ዕፅ ሠናይ ዘይፈሪ ፍሬ እኩየ ፣ ማቴ
፯ ፣ ፲፰ ፲፱ ፥ ፴፫ ።

፵፫ እልቦ ረድዕ ላለው ። ክፉ ፍሬ የሚያፈራ
መልካም ዕንጨት የለም ።
ወእልቦ ዕፅ እኩይ ዘይፈሪ ፍሬ ሠናየ ።
መልካም ፍሬ የሚያፈራ ክፉ ዕንጨት የለም ።

፵፬ ወኵሉ ዕፅ እምፍሬሁ ይትዓወቅ ።
፵፬ ዕንጨትም ሁሉ በፍሬው ይታወቃል ።
ወኢየዓርሩ በለስ እምዓሥዋክ ።
ከሾህ በለስን አይሰበስቡም ።
ወኢይቀስሙ አስካለ እምእሜከላ ።
ከደንደርም ወይኑን አይለቅሙም ።

፵፭ ኄር ብእሲ እምሠናይ መዝገበ ልቡ ያወ
ፅእ ለሠናይት ።

፵፭ ቸር ሰው ከቸር ልቡ መዝገብ ቸርነቱን
ያወጣል ።
ወእኩይ ብእሲ እምእኩይ መዝገበ ልቡ ያወፅእ ለእኪት
ክፉ ሰው ግን ከክፉ ልቡ ሣጥን ከፉ ነገርን ያወጣል ።
እስመ እምተረፈ ልብ ይነብብ አፍ ።
አፍ ከልብ የተረፈውን ይናገራልና ።

፵፮ ለምንት ትብሉኒ እግዚእ እግዚእ ። ማቴ
፯ ፣ ፳፩ ። ሮሜ ፪ ፣ ፲ ፣ ፫ ያዕ ፩ ፥ ፳፪ ።

፵፮ ለምን አቤቱ አቤቱ ትሉኛላችሁ ።
ወኢትገብሩ ዘእቤለክሙ ።
የምነግራችሁን አትሠሩትም ።

፵፯ ኵሉ ዘይመጽእ ኀቤየ ይሰምዓኒ ቃልየ
ወይገብሮን እርእየክሙ ዘይመስል ።

፵፯ ወደኔ የሚመጣ ነገሬን ሰምቶ የሚሠራው
ሁሉ የሚመስለውን አሳያችኋለሁ ።

፵፰ ይመስል ብእሴ ጠቢብ ዘሐነጸ ቤቶ ወከረየ
ወአዕመቀ ወሣረረ መሠረቶ ዲበ ኰኵሕ ።

፵፰ አጥብቆ ቆፍሮ መሠረቱን ከጭንጫ ላይ
መሥርቶ ቤቱን የሚሠራን ብልህ ሰውን ይመስላል ።
ወብዙኃን አፍላግ መጺአሙ ገፍዕዎ ወሐይዝት
ለውእቱ ቤት ።

ብዙ ጐርፍ በፈሰሰ ጊዜ ፈሳሾች ያንን ቤት ገፉት ።
ወኢክህሉ አንቀልቅሎቶ ።
አላናወጡትም ።
እስመ ዲበ ኰኵሕ ተሣረረ ።
ከጭንጫ ላይ ተመሥርቷልና ።

፵፱ ወዘሰ ይሰምዓኒ ቃልየ ወኢይገብሮ ይመ
ስል ብእሴ ዘሐነጸ ቤቶ መልዕልተ ምድር ዘእንበለ
መሠረት ።

፵፱ ቃሌን ሰምቶ የማይሠራው ግን ሳይመሠ
ርት ቤቱን በምድር ላይ የሚሠራ ሰውን ይመስላል ።
ወገፍዕዎ ወሐይዝት ። ፈሳሾች ገፉት ።
ወወድቀ ሶቤሃ ። ያንጊዜውን ወደቀ ።
ወኮነ ድቀቱ ዓቢየ ። መውደቁም ታላቅ ሆነ ።

በእንተ ወዓሊ ዘመስፍን ።

ምዕራፍ ፯ ።

፩ ወፈጺሞ ነገሮቶሙ ቃሎ ለሕዝብ ቦአ
ቅፍርናሆም ። ማቴ ፰ ፣ ፭ ።

፩ ትምህርቱን ለሕዝቡ ነግሮ ከፈጸመ በኋላ
ወደ ቅፍርናሆም ገባ ።

፪ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ መስፍን ።
፪ አንድ ሾም ነበር ።
ወገብሩ ይደዊ ። ባሪያው ታሞ ነበር ።
ወአልጸቀ ይሙት ። ሊሞት ቀርቦ ነበር ።
ወክቡር ውእቱ በኀቤሁ ። ያውም ባለሟሉ ነው ።

፫ ወሰሚዖ በእንተ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ይመ
ጽእ ለእከ ኀቤሁ ረበናተ አይሁድ ።

፫ ጌታችን ኢየሱስ እንደ መጣ ወሬ በሰማ
ጊዜም የአይሁድን ሽማግሌዎች ላከ ።
ያስተበቊዕዎ ከመ ይምጻእ ወያሕዩ ሎቱ ገብሮ ።
ባሪያውን እንዲያድንለት ይለምኑት ዘንድ ።

፬ ወመጽኡ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወአስተብቍ
ዕዎ ።

፬ ወደ ጌታ መጥተው ለመኑት ።
ወይቤልዎ ነዓ ፍጡነ ረድ ።
ፈጥነህ ውረድ ።
እስመ ይደልዎ ትግበር ም ስሌሁ ዘንተ ።
ሎቱ ሲል ነው ። ግበር ምስሌነ እንዲል ። ይህን ልታ
ደርግለት ይገባዋልና ።

፭ እስመ ያፈቅር ሕዝበነ ።
፭ ወገኖቻችንን ይወዳልና ።
ወምኵራበነኒ ውእቱ ሐነጸ ለነ ።
እሱ የጸሎት ቤት ሰርቶልናልና ። ሐተታ ካርባ
ስምንቱ ምኵራብ አንዱን ሰርቶላቸዋል ። አንድም
አልፎ አልፎ የፈረሰውን መጠቀም ነው ። ማቴ
ዎስ ወልዱ ይላል ሉቃስ ገብሩ አለ እንደምን ነው
አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር ። እንደ ማቴዎስ
ነው ልጁ ነው ሉቃስ ገብሩ አለ ክቤተ ሰብእ ወልዶ
ታልና ። አንድም ሉቃስ ገብሩ ማለቱ ባለሟሉ ሲል

ነው ፡፡ ኢዮብ ገብርየ ሙሴ ገበርየ እንዲል ፤ ማቴዎስ
እሱ ሄዶ ተናገረ ይላል ፡፡ ሉቃስ ረባናትን ላከ አለ
እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ነገር እንደ
ማቴዎስ ነው እሱ ሄዶ ተናግሯል ዝም ቢለው ባይመ
ልስለት እኔንስ ዝም አለኝ እናንተ ሄዳችሁ ንገሩት
ቢላቸው ሂደው ተናግረዋልና ይህን ተካፍለው ጽፈ
ዋል ፡፡ አንድም ነገር እንደ ሉቃስ ሄዳችሁ ንገሩልኝ
ብሎ ሰዲቸዋል ኋላ ተከትሎ ሄዶ ተናግሯል ባሬ
አማላጅ የላከ ሰው ተከትሎ ሄዶ ነገሩን እንዲናገር
ይህን ተካፍለው ጽፈዋል ፡፡

፮ ወሖረ እግዚእ ኢየሱስ ምስሌሆሙ ፡፡ ማቴ ፤ ፰፥፰ ፡፡

፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ከነሱ ጋራ ሄዶ ፡፡
ወአልጺቆ ኀበ ቤቱ ለውእቱ መስፍን ለአከ አዕርከ
ቲሁ ውእቱ መስፍን ኀቤሁ እንዘ ይብል እግዚኦ ኢት
ጻሙ ፡፡
ወደቤቱ ሊገባ በቀረበ ጊዜ አቤቱ አትድከም ብሎ
ወዳጆቹን ወደ ጌታ ላከ ፡፡
እስመ ኢይደልወኒ ከመ ትባዕ ታሕተ ጠፈረ ቤትየ ፡፡
ከቤቴ ጠፈር በታች ትገባ ዘንድ አይገባኝምና ፡፡

፯ ወለልየ ኢይደልወኒ እምጻእ ኀቤከ ፡፡
፯ እኔም ወዳንተ ልመጣ የማይገባኝ ነኝ ፡፡
ወባሕቱ አዝዝ በቃልከ ፡፡
ነገር ግን በቃልህ እዘዝ ፡፡
ወየሐዩ ቍልዔየ ፡፡
ብላቴናየም ይድናልና አለው ፡፡

፰ እስመ አነሂ ብእሲ መኰንን አነ ፡፡
፰ እኔም እንጂ ገዢ ነኝ ፡፡
ወብየ ወዓልት ፡፡
ቶኀዝሮች አሉኝ ፡፡
ወዕብሎ ለዝ ሑር ወየሐውር ፡፡
ይህን ሂድ እለዋለሁ ይሄዳል ፡፡
ወለካልዑኒ ነዓ ወይመጽእ ፡፡
ሌላውንም ና ፤ እለዋለሁ ይመጣል ፡፡
ወለገብርየኒ ግበር ከመዝ ወይገብር ፡፡
ባሪያዬንም እንዲህ አድርግ እለዋለሁ ያደርጋል አለው

፱ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ዘንተ አምኒሁ
አንከረ ፡፡

፱ ጌታም ይህን በሰማ ጊዜ አደነቀ ፡፡
ወተመይጦ ይቤሎሙ ለሕዝብ እለ ተለውዎ አማን
እብለክሙ ኢረከብኩ ዘከመዝ ሃይማኖተ በውስተ
እስራኤል ፡፡
ወይከተሉትም ተመልሶ በእስራኤል ዘንድ እን
ዲህ ያለ እምነት አላገኘሁም ብየ በውነት እነግራ
ችኋለሁ አላቸው ፡፡

፲ ወአተውዎሙ እለ ተፈነዉ ረከብዎ ለቍልዑ
በዘሐይወ ፡፡

፲ የተላኩት ስተመለሱ ጊዜ ልጁን ድና አገኙት

፲፩ ወበሳኒታ ሖረ ሀገረ እንተ ስማ ናይን ፡፡

፲፩ በነጋው ናይን ወደምትባል አገር ሄደ ፡፡
ወሖሩ ምስሌሁ አርዳኢሁ ፡፡
ደቀ መዛሙርቱ ተከትለውት ሄዱ ፡፡
ወሕዝብኒ ብዙኅ ፡፡
ብዙ ሰዎች ተከትለውት ሄዱ ፡፡

፲፪ ወበጺሖ ኀበ አንቀጸ ሀገር ናሁ ረከበ ቀበረ
ዕውረ ዘወልደ ብእሲት መበለት ፡፡

፲፪ ከከተማው በር ሊገባ በቀረበ ጊዜ ያንዲት
ድኃ ልጅ በቃሬዛ ተሸከመውት ሰዎች አገኘ ቀበረ
ዕውረ ምውት ዕውረ ይላል አስከሬን ቃሬዛ የተሸ
ከሙ ሰዎች አገኘ ፡፡
ወውእቱ ዋሕድ ለእሙ ፡፡
እሱም ለናቱ አንድ ልጅ ነበር ፡፡
ወብዙኃን ሰብአ ሀገር ሀለዉ ምስሌሃ ፡፡
ብዙ ሰዎችም ከሷ ጋራ ነበሩ ፡፡

፲፫ ወሶበ ርእያ እግዚእነ መሐራ ወትሣሃላ
ላዕሌሃ ፡፡

፲፫ ጌታም ባያት ጊዜ አዘነላት ይቅር አላትም ፡፡
ወይቤላ ኢትብክዪ ፡፡
አታልቅሽ አላት ፡፡
ወቀርበ ወአኀዘ ነፍቆ ፡
ቀርቦ ቃሬዛውን ያልጋውን ሸንኮሩን ያዘ ንፍቅ
ይላል ነፍስ የተለየችው አስከሬኑን ያዘ ፡፡

፲፬ ወቆሙ እለ ይጸውርዎ ፡፡

፲፬ የተሸከሙት አውርደውት ቆሙ ፡፡
ወይቤሎ ለከ እብለከ ወሬዛ ተንሥእ ፡፡
አንተ ጐበዝ ተነሥ እልሃለሁ አለው ፡፡

፲፭ ወተንሥአ ወነበረ ውእቱ በድን ፡፡

፲፭ ያም በድን ተነሥቶ ተቀመጠ ፡፡
ወተናገረ ርቱዓ ፡፡
አቃንቶ ተናገረ ፡፡
ወአወፈዮ ለእሙ ፡፡
እሱን ለሷ ሰጠው ይርዳሽ ያጥባሽ ብሎ ወአወፈያ
ይላል እሱን ሰጣት ርዳት አጥባት ብሎ ፡፡

፲፮ ወፈርሁ ኵሎሙ ፡፡ ሉቃ ፭፥፳፮ ፤ ፲-፱፥፵፥ ሐ ፩፥፲፩
፲፮ ሁሉም ፍርሃት ያዛቸው ፡፡
ወሰብሕዎ ለእግዚአብሔር ፡፡
እግዚአብሔርን አመሰገኑት
ወይቤሉ ዓቢይ ነቢይ ተንሥአ ለነ ፡፡
ታላቅ ነቢይ ተነሣልን አሉ ፡፡
ወተሣሃሎሙ እግዚአብሔር ለሕዝቡ ፡፡
እግዚአብሔር ወገኖቹን ይቅር ብሏልና ፡፡

በእንተ ኢየሱስ ወበእንተ አርድዕተ ዮሐንስ መጥምቅ

፲፯ ወተሰምዓ ዝንቱ ነገር በኵሉ በሐውርተ ይሁዳ ።

፲፯ ይህ ነገር በይሁዳ አገር ሁሉ ተሰማ ።
ወበኵሉ በሐውርቲሃ ።
ባውራጃዋም ሁሉ ።

፲፰ ወነገርዎ አርድዕቲሁ ለዮሐንስ ዘንተ ኵሎ ነገረ ።

፲፰ ይህንም ሁሉ ነገር ደቀ መዛሙርቱ ለዮሐንስ ነገሩት ።

፲፱ ወጸውዓ ዮሐንስ ፪ተ እምአርዳኢሁ ። ማቴ ፲፩ ፪

፲፱ ዮሐንስም ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ጠርቶ ።
ወለአኮሙ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።
ወደጌታ ላካቸው ።
እንዘ ይብል አንተኑአ ዘይመጽእ ።
ይመጣል የምንለው አንተ ነህን ።
ወሚመ ቦኑ ካልዕ ዘንሴፎ ።
ወይም ተስፋ የምናደርገው ሌላ አለን ብሎ ።

፳ ወበጺሖሙ አለ ለአኮሙ ኀቤሁ ይቤልዎ ዮሐንስ መጥምቅ ለአከነ ወይቤ አንተኑአ ዘይመጽእ ወቦኑ ካልዕ ዘንሴፎ ።

፳ ወደሱ የተላኩትም ሰዎች በደረሱ ጊዜ ይመጣል የምንለው አንተ ነህ ወይም ሌላ ነው ብሎ ዮሐንስ ወደንተ ልኮናል አሉት ።

፳፩ ወፈወሶሙ ለብዙኃን ሶቤሃ እምአደዊሆሙ ወእምሕማሞሙ ።

፳፩ በዚያን ጊዜም ብዙ ሰዎችን ከጭንቅ ደዌያቸው ፈወሳቸው ወእምእጋንንት እኩያን ።
ከክፉ አጋንንትም ።
ወለብዙኃን ዕውራን ጸገዎሙ ይርአዩ ።
ለብዙ ዕውራንም ያዩ ዘንድ ብርሃንን ሰጣቸው

፳፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ፡ኢሳ ፴፭፡፭-፮ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ሑሩ ንግርዎ ለዮሐንስ ዘሰማዕክሙ ወዘርኢክሙ ።

፳፪ ሂዱችሁ ያያችሁትን የሰማችሁትን ለዮሐንስ ንገሩት ።
ዕውራን ይሬእዩ ።
ዕውራን ያያሉ ።
ወስቡራን የሐውሩ ።
አንካሶችም ይሄዳሉ ።
ወእለ ለምጽ ይነጽሑ ።
ለምጻሞችም ይነጻሉ ።
ወጽሙማንሂ ይሰምዑ ።
የደንቆሩም ይሰማሉ ።
ወምውታንሂ ይትነሥኡ ።
የሞቱትም ይነሣሉ ።
ወነዳያንሂ ይዜነዉ ወይትፌሥሑ ።
የተቸገሩትም ይከብራሉ ደስ ይላቸዋል ።

፳፫ ወብፁዕ ዘኢይትዐቀፍ ብየ ።
፳፫ በኔም የማይጠራጠር የተመሰገነ ነው ።

ዘከመ ወደሶ ኢየሱስ ለዮሐንስ መጥምቅ ።

፳፬ ወኃሊፎሙ አርዳኢሁ ለዮሐንስ አኀዘ ይበሎሙ ለሕዝብ በእንተ ዮሐንስ መጥምቅ ።

፳፬ የዮሐንስ መልክተኞች በሄዱ ጊዜ የዮሐንስ መጥምቅን ነገር ለሕዝቡ ይነግራቸው ጀመረ ።
ምንተኑመ ወፃእክሙ ገዳመ ትርአዩ ።
በምድረ በዳ ምን ልታዩ ወጥታችኋል ።
ብርዓኑ ዘይትሐወስ እምነፋስ ።
ነፋስ የሚያንቀሳቅሰው ሸንበቆን ነው ።

፳፭ ወምንተኑመ ወፃእክሙ ትርአዩ ።

፳፭ ነገር ግን ምን ልታዩ ወጥታችኋል ።
ብእሴኑ ዘርሱይ በቀጠንተ አልባስ ።
ቀጭን ልብስ የለበሰ ሰውን ልታዩ ወጥታችኋል ።
ናሁ እለሰ ርሱያን በአልባሰ ክብር ውስተ አብያተ ነገሥት ሀለዉ ።
የክብር ልብስ የለበሱ ግን እንደሆኑ ከነገሥታት ቤት አሉ ።

፳፮ ወምንተኑመ ወፃእክሙ ትርአዩ ።

፳፮ ወይስ ምን ልታዩ ወጥታችኋል ነቢዩን ነቢይን ነው ።
አወ እብለክሙ የዓቢ እምነቢይ ።
አዎን ከነቢይ ይበልጣል ብዬ እነግራችኋለሁ ።

፳፯ ዝንቱ ውእቱ ዘበእንቲአሁ ተጽሕፈ ናሁ አነ እፌኑ መልአኪየ ቅድመ ገጽከ ዘይጼይሕ ፍኖተከ ቅድሜከ ። ሚል ፫ ፩ ማቴ ፲፩ ፲ ማር ፩ ፪ ።

፳፯ መንገድህን በፊትህ የሚጠርግ መልክተኛዬን በፊትህ እልካለሁ ተብሎ የተነገረለት ይህ ነው ።

፳፰ አማን እብለክሙ ኢይትነሣእ እምትውልደ አንስት ዘየዓቢ እምዮሐንስ መጥምቅ ወኢመኑሂ ።

፳፰ ከሴቶች ከሚወለዱ ወገን ከዮሐንስ የሚበልጥ ማንም ማን እንደሌለ በውነት እነግራችኋለሁ ።
፳፰ ወበመንግሥተ ሰማያትሰ ዘይንእስ የዓብዮ።
፳፰ በመንግሥተ ሰማያት ግን ታናሹ ከሱ ይበልጣል ።

ወሰሚዖሙ ኵሎሙ ሕዝብ ወመጸብሐን አጽደቅዎ ለእግዚአብሔር ።
ሕዝቡ ሁሉ ቀራጮችም ነገሩን ሰምተው እውነት ነው አሉ ።
እስመ ተጠምቁ ጥምቀተ ዮሐንስ ።
በዮሐንስ ጥምቀት ተጠምቀው ነበረና ።

፴ ወፈሪሳውያንሰ ወጸሐፍተ ሕግ ዓለዉ ትእዛዘ እግዚአብሔር ።

፴ ፈሪሳውያንና የሕግ ጸሐፊዎች ግን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ አፈረሱ ።
እስመ ኢተጠምቁ በኀቤሁ ።
በሱ ዘንድ አልተጠመቁምና ።

፴፩ በምንት አስተማስሎሙ ለሰብእ ዛቲ ትውልድ ። ማቴ ፲፩ ፣ ፲፮ ።

፴፩ የዚችን ትውልድ ሰዎች በምን እመስላቸዋለሁ ።
ወመኑ ይመስሉ ።
ማንን ይመስላሉ ።

፴፪ ይመስሉ ደቂቀ እለ ይነብሩ ውስተ ምስያጥ ።
፴፪ በገበያው ተቀምጠው ።
ወይጼውዑ ቢጸሙ ።
ባልንጀሮቻቸውን ጠርተው ፤
ወይቤልዎሙ ኃለይነ ለክሙ ወኢዘፈንክሙ ።
የዘፈን ዜማ ቀነቀንላችሁ አልዘፈናችሁም ።
አስቆቀውነኪ ለክሙ ወኢበከይክሙ ።
አለቀስንላችሁ አላለቀሳችሁም የሚሉ ብላቴኖችን ይመስላሉ ።

፴፫ እስመ መጽአ ዮሐንስ መጥምቅ ኢይበልዕ እክለ ወኢይሰቲ ወይነ ። ማቴ ፫ ፣ ፬ ማር ፩ ፣ ፮

፴፫ ዮሐንስ መጥምቅ እህል ሳይበላ ጠጅ ሳይ ጠጣ መጥቷልና ።
ወትቤልዎ ጋኔን ቦቱ ።
ጋኔን አድሮበታል አላችሁት ።

፴፬ ወመጽአ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ይበልዕ ወይሰቲ ።

፴፬ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ግን እየበላ እየጠጣ መጣ ።
ወትቤሉ ነዋ ብእሲ በላዒ ወሰታዪ ወይን ።
እነሆ የሚበላ ጠጅም የሚጠጣ ሰው ።
እርከ መጸብሐን ወኃጥአን ።
የቀራጮችና የኃጥአን ወዳጅ አላችሁት ።

፴፭ ወጸድቀት ጥበብ እምኵሉ ውሉዳ ።
፴፭ ጥበብ ወልድ ከልጆችዋ ሁሉ ይልቅ ከበረች

በአንተ ፈሪሳዊ ወኃጥዕት ብእሲት ፤

ወእንዘ ሀሎ እግዚእ ኢየሱስ ዘየ ይቤሎ አሐዱ እምነፈሪሳውያን ከመ ይምሳሕ በኀቤሁ ።

በሱ ዘንድ ምሳ ይበላ ዘንድ ከፈሪሳውያን አንዱ ለመነው ።

፴፮ ወቦአ ቤተ ፈሪሳዊ ወረፈቀ ።
፴፮ ከፈሪሳዊ ቤት ገብቶም ተቀመጠ ።
፴፯ ወመጽአት ብእሲት ኃጥዕት እምሰብአ ይእቲ ሀገር እእሚራ ከመ ይመስሕ ውስተ ቤተ ፈሪሳዊ ወተማየጠት ዕፍረተ ዘአልባበጥሮስ ። ማቴ ፣ ፳፮ ፣ ፯ ማር ፣ ፲፬ ፣ ፫ ዮሐ ፣ ፲፪ ፣ ፪ ።

፴፯ በዚያ አገር ካሉ ሰዎች ኃጢአተኛ ሴት ከፈሪሳዊ ቤት እንዲበላ ባወቀች ጊዜ የደቀቀ የጣፈጠ ሽቱ ገዝታ መጣች ።

፴፰ ወቆመት ድኅሬሁ ኀበ እገሪሁ ።
፴፰ ከወደኋላው በእግሩ አጠገብ ቆመች ። ሐተታ ጌታ እንደ ግብጻውያን አቀማመጥ እግሩን ወደኋላው አድርጎ ተቀመጦ ነበርና ። አንድም ወንበሩ እንደ አፍርንጆች ወንበር እግር ወደኋላ የሚያደርግ ነው ። አንድም ወደ እግሩ ለማለፍ በኋላው ቆመች ።
ወበከየት ወአርሐሰት እገሪሁ በአንብዓ ።
እያለቀሰች እግሩን በዕንባዋ አጠበችው ።
ወትመዘምዝ በስእርተ ርእሳ ።
በራሷ ጠጕርም አበሰችው ።
ወትስእም እገሪሁ ፤
እግሩንም ትስመው ነበር ።
ወትቀብዖ ዕፍረተ ፤
ሽቱም ትቀባው ነበር ።

፴፱ ወርእዮ ፈሪሳዊ ዘጸውዖ ሐለየ በልቡ ።
፴፱ የጠራው ፈሪሳዊ አይቶ በልቡ አሰበ ።
ወይቤ ሶበሁ ነቢይ ውእቱ ዝንቱ ።
ይህ ነቢይማ ቢሆን ።
እምኢያእመረ ከመ ኃጢአት ዛቲ ብእሲት እንተ ትገሥሥ ።
ይህች የምትዳስሰው ኃጥእት እንደሆነች ባላወቀም ነበር ብሎ ተናገረ ።

፵ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፵ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰ ።
ወይቤሎ ስምዖን በምዖን ብየ ዘእብለከ ።
ስምዖን ሆይ የማስፈረድህ ነገር አለኝ አለው ።
ወይቤሎ እ ሊቅ በል ።
መምህር ሆይ ተናገር አለው ።

፵፩ ወይቤሎ ክልኤቱ ይፈድዩ ለአሐዱ በዓለ እዳ ።

፵፩ ላንድ ሰው ሁለት ባለዳች አሉት ።
አሐዱ ይፈድዮ ኃምስተ ምእተ ዲናረ ።
አንዱ አምስት መቶ ወቄት ይከፍላል ።

ወካልዑኒ ሃምሳ ።
ሁለተኛውም አምሳ ወቄት ይከፍለዋል ።

፵፪ ወኃጢአሙ ዘይፈድዩዎ ኀደገ ሎሙ ለከ ልኤሆሙ ።

፵፪ የሚከፍሉት ባያገኙ ለሁለቱም ተወላቸው።
፵፫ መኑ እንከ ርቱዕ ፈድፋደ ያፈቅሮ እም ኔሆሙ ።

፵፫ ከነሱ ማናቸው አብልጦ ሊወደው ይገበዋል አለው ።
ወተሠጥወ ስምዖን ።
ስምዖንም መለሰ ።
ወይቤ እብለከ ዘብዙኀ ኃደገ ሎቱ ።
ፍረድስ ካልኸኝ አምስት መቶ ወቄት የተወለት አብልጦ ሊወደው ይገባዋል አለው ።
ወይቤሎ ስምዖን ሠናየ ፈታሕከ ።
ስምዖን ሆይ መልካም ፈረድህ ።
እሙነ ፈታሕከ ።
እውነት ፈረድህ አለው ።

፵፬ ወተመይጠ ኀበ ይእቲ ብእሲት ።
፵፬ ወደዚያች ሴት ተመለሰ ።
ወይቤሎ ለስምዖን ትሬኢያኑ ለዛቲ ብእሲት ።
ስምዖንን ይህችን ሴት ታያታለህን አለው ።
ቦእኩ ቤተከ ።
አቤትህ ገባሁ ።
ወኢወሀብከኒ ማየ ጥቀ ለእገርየ ።
ለእግሬ ውኃ እንኳን አልሰጠኸኝም ።
ወይእቲሰ በከየት ወበአንብዓ አርሐሰተኒ እገርየ ።
ይህች ግን ለለቀሰች በእንባዋ እግሬን አጠበች ።
ሐተታ ትእምርተ ንስሐ ነው ።
ወበሰዕርተ ርእሳ መዘመዘተኒ በሬቢ ጸጕርዋ አደ ፈችኝ ። ሐተታ ትእምርተ ትሕትና ነው ።

፵፭ ወሑንተሰ ኢቀአማኀከኒ ።
፵፭ አንተስ አፎ አልነሣኸኝም ።
ወይእቲሰ እምጊዜ ቦእኩ ኢያንተገት ስዒመ እገርየ ።
እሷ ግን ከገባሁ ጀምሮ አምጊዜ ቦእት ከገባች ጀምሮ እግሬን ተመሳም አላቋረጠችም ሐተታ ትእምርተ ፍቅር ነው ።

፵፮ ወአንተሰ ኢቀባዕከኒ ቅብዐ ርእስየ ።
፵፮ ዘይት ሲል ነው ። አንተስ ዘይት ቀብተህ አልቀባኸኝም ።
ወይእቲሰ ዕፍረተ ቀብዓተኒ እገርየ ።
እሷ ግን እግሬን ሽቱ ቀባችኝ ። ሐተታ ትእምርተ አክብሮ ሽቱ ከዘይት እንዲበልጥ በዚህ ይታወቃል ።

፵፯ ወበእንተዝ እብለከ ተኀደገ ኃጢአታ ብዙኅ
፵፯ ስለዚህ ነገር ብዙ ኃጢአቷ ቀረላት ብዬ እነግርሃለሁ ።
እስመ ብዙኀ አፍቀረተኒ ።

ብዙ ወደደችኝና ።
ወዘሰ ውኁደ አፍቀረኒ ውኁድ ኃጢአት ይትኃደግ ሎቱ ።
ጥቂት የሚወደኝ ጥቂት ኃጢአት ይወርድለታል ።

፵፰ ወይቤላ ለይእቲ ብእሲት ተኀደገ ለኪ ኃጢአትኪ ። ማቴ ፱ ፣ ፪ ።

፵፰ አሁንም ኃጢአትሽ ቀርቶልሻል አላት ። ሐተታ አሁን ብዙኀ አፍቀረተኒ አለ ። ሽቱ የተገዛ በት እምስት መቶ ወቄት ነውና ። አሁን ውኁደ አፍቀረኒ አለ ምሳው የተገዛ ባምሳ ወቄት ነውና ። አሁን ብዙኀ ኃጢአታ አላት ዘማ ናትና ። አሁን ውኁድ ኃጢአቱ አለ ጽሐፍት ፈሪሳውያን ምንም ውዳሴ ከንቱ ቢያስቀርባቸው ዓሥሩን ቃላት አንጠብቃለን ባዮች ናቸውና ።

፵፱ ወአኀዙ አለ ይረፍቁ ይበሉ በበይናቲሆሙ መኑ ውእቱ ዝንቱ ዘየኀድግ ኃጢአተ ።

፵፱ ለመብላ የተቀመጡት ይህ ኃጢአትን ይቅር የሚል ማነው አሉ ።
፶ ወይቤላ ለይእቲ ብእሲት ሃይማኖትኪ አሕየ ወተኪ እትዊ በሰላም ።
ሃይማኖትሽ አድኖሻልና በፍቅር ሂጂ አላት ።

ዘከመ ዖደ ኢየሱስ አህጕረ ገሊላ ።

ምዕራፍ ፰ ።

፩ ወእምዝ በሳኒታ አንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ አህጉር ወአእፃዳት ።

፩ ከዚህ በኋላ በነጋው በየሀገሩና በመንደሩ ተመላለሰ ።
ወሰበከ ሎሙ ።
ሰበከላቸው ።
ወመሐሮሙ በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
ስለ እግዚአብሔር መንግሥትም አስተማራቸው ።
ወምስሌሁ ዓሠርቱ ወክልኤቱ አርዳኢሁ ።
ዐሥራሁለቱም ከሱ ጋራ ነበሩ ።

፪ ወአንስትኒ እለ አሕየዎን እም እኩያት አጋንንት ወእምደዌሆን ። ማር ፲፯ ፣ ፱ ።

፪ ከክፉ አጋንንትና ከደዌያቸው የፈወሳቸውም ሴቶች ።
ወእማንቱ ማርያም እንተ ይብልዋ መግደላዊት እንተ ወፅኡ አጋንንት ወፅአ እምኔሃ ።
ሰባት አጋንንት የወጡላት መግደላዊት የሚሏት ማርያም ።

፫ ወዮሐና ብእሲቱ ኩዛ መጋቤሁ ለሄሮድስ ።
፫ የሄሮድስ መጋቢ የኩዛ ሚስቱ ዮሐና ።

ወሶስና ወካልዓትሂ ብዙኃት እለ ተልእክዎ በንዋዮን ።
በገንዘባቸው ያገለገሉት ማለት በሕዋላቃቸው ንጽ
ሕናን ይዘው ያገለገሉት ሌሎችም ብዙ ሴቶችና ሶስ
ናም ነበሩ ። ዘበእንተ ንዋይየ ተቀደሰት ሊተ ነፍስየ
እንዲል ።

በእንተ ምሳሌ ዘዘራኢ ።

፬ ወእንዘ ያጸምዕዎ ዙሎሙ ሕዝብ ።
፬ ሕዝቡም ሁሉ ሲሰሙት ።
ወእለሂ መጽኡ ኀቤሁ እምዙሉ አህጉር ።
ከየሀገሩም የመጡ አሉ ።
ይቤሎሙ ምሳሌ እንተ ከመዝ ።
እንዲህ ያለ ምሳሌ ነገራቸው ።

፭ ወፈረ ዘይዘርዕ ከመ ይዝራዕ ።
ዘርዖ ። ማቴ ፲፫ ፡ ፫ ማር ፬ ፡ ፫

፭ የሚዘራ ገበሬ ዘሩን ሊዘራ ወጣ ።
ወእንዘ ይዘርዕ ቦ ዘወድቀ ውስተ ፍኖት ።
ሲዘራም ከመንገድ የወደቀ ዘር አለ ።
ወመጽኡ ወኬድዎ ሰብእ ወበልዑ አዕዋፈ ሰማይ ።
ሰዎች መጥተው የረገጡት የሰማይ ወፎችም የበሉት ።

፮ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ኰኵሕ ።
፮ ከጭንጫም የወደቀ ዘር አለ ።
ወበቊሎ የብሰ በጊዜሃ ።
በበቀለ ጊዜም ፈጥኖ የደረቀ ።
እስመ አልቦ ሥርው ።
ሥር የለውምና ።

፯ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ሦክ ።
፯ ከሾህ ውስጥ የወደቀ አለ ።
ወበቊሎ ጠበቆ ሦክ ።
በበቀለም ጊዜ እሾህ አንቆ የያዘው ።

፰ ወቦ ዘወድቀ ውስተ ምድር ሠናይት ።
፰ በመልካም ምድር የወደቀም አለ ።
ወሶበ በቊለሂ ፈረየ ምእተ ምክዕቢተ ።
በበቀለም ጊዜ መቶ ዕጽፍ አፈራ ።
ወዘንተ ብሂሎ ይቤሎሙ ዘቦ ዕዝን ሰሚዓ ለይስማዕ ።
ይህን ተናግሮ ሰሚ ጆሮ ያለው ይስማ አላቸው ።

፱ ወተስእልዎ አርዳኢሁ ።
፱ ደቀ መዛሙርቱ ጠየቁት ።
ወይቤልዎ ምንትኑ ይእቲ ዛቲ ምሳሌ ።
ይህች ምሳሌ ምንድናት አሉት ።

፲ ወይቤሎሙ ለክሙ ተውህበ ታእምሩ ምሥ
ጢራ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ። ኢሳ ፮ ፡ ፱
ማቴ ፲፫ ፡ ፲፬ ማር ፬ ፡ ፲፪ ዮሐ ፲፪ ፡ ፵ ግብ
፳፰ ፡ ፳፮ ሮሜ ፲፩ ፡ ፰

፲ የእግዚአብሔርን መንግሥት ምሥጢር
ማወቅ ለናንተ ተሰጥቷል ።
ወለእልክቱሰ በምሳሌ ።
ለቀሩት ግን በምሳሌ ።
ከመ ርእዮሙኒ ኢይርእዩ ።
አይተው እንዳያዩ ።
ወሰሚዖሙኒ ኢይሰምዑ ።
ሰምተው እንዳይሰሙ ።
ወኢይለብዉ ።
እንዳያስተውሉም ።

፲፩ ወከመዝ ምሳሌሃ ።
፲፩ ምሳሌውም ይህ ነው ።
ዘርዕሰ ቃለ እግዚአብሔር ውእቱ ።
ዘሩም ቃለ እግዚአብሔር ነው ።

፲፪ ወዘሰ ውስተ ፍኖት ወድቀ እሉ እሙንቱ
እለ ይሰምዑ ቃለ ።

፲፪ በመንገድ የወደቀውንም ዘር ነገር የሚሰሙ ፤
ወይመጽእ ሰይጣን ወይነሥእ ለቃል እምልቦሙ
ከመ ኢይእመኑ ወኢይሕየዉ ።
አምነው እንዳይድኑ ሰይጣን መጥቶ ነገሩን ከልቡ
ናቸው የሚወስድባቸው ናቸው ።

፲፫ ወዘሰ ውስተ ኰኵሕ ወድቀ ።
፲፫ በጭንጫ የተዘራውም ።
ወሰሚዖሙ ይትዌከፍዎ በፍሥሐ ።
በሰሙ ጊዜም ነገሩን ደስ ብሏቸው የሚቀበሉ ።
ወባሕቱ ሥርው አልቦሙ ሶቤሃ ዳእሙ የአምኑ ።
ነገር ግን ለጊዜው ያምናሉ እንጂ መሠረት የላቸው
ምና ።
ወእምከመ ተመንደቡ የዓልዉ ።
በመከራ በተጨነቁ ጊዜ ይክዳሉ ።

፲፬ ወዘሰ ውስተ ሦክ ወድቀ ።
፲፬ ከሾህ ውስጥ የወደቀውም ።
እሉ እሙንቱ እለ ይሰምዑ ቃለ ወሕሊና ብዕል ።
እኒህም ነገሩን ሰምተው የባለጠግነት አሳብ ።
ወትካዘ መንበርት ።
የመኖሪያ መቍርቈር ።
ወሐውዘ ተድላ ወፈጊዕ ያጠውቆሙ ወኢይገብሩ
ፍሬ ።
የተድላ የደስታም መጣፈጥ አስጨንቆቸው የማይ
ሠሩት ናቸው ።

፲፭ ወዘሰ ውስተ ምድር ሠናይት ።
፲፭ ከመልካም የተዘራው ግን ፤
እሉ እሙንቱ እለ ይሰምዑ ቃለ በሠናይ ልብ ወያዐ
ቅብዎ ወይትዐገሡ
ነገሩን በበጐ ልቡና ሰምተው የሚያስተውሉ
ወያከብርዎ የሚጠብቁ
ወይፈርዩ ። የሚያፈሩናቸው

፲፮ ወአልቦ ዘያኀቱ ማኅቶተ ወይከድና ንዋየ
ወያንብራ ታሕተ ዓራት ። ማቴ ፭ ፲፭ ማር ፬፥፳፩።

፲፮ መብራት አብርቶ በዕቃ ከድኖ ከአልጋ በታች
የሚያኖር የለም ።
ዘእንበለ ዲበ ተቅዋማ ።
ከመቅረዟ ላይ ነው እንጂ ።
ከመ ፡ ይርአዩ ብርሃነ እለ ያንሶሰዉ ።
የሚመላለሱ ብርሃንን ያዩ ዘንድ ።

፲፯ ወአልቦ ኅቡእ ዘኢይትከሠት ። ማቴ ፲ ፡ ፳፮ ማር ፡ ፬ ፡ ፳፪ ።

፲፯ የማይገለጥ የተሸሸገ የለም ።
ወአልቦ ክዱን ዘኢያስተርኢ ።
የማይታይ የተሰወረ የለም ።
ወገሃደ ይከውን ።
ይገለጣል እንጂ ።

፲፰ ወአእምሩ እንከ ይእዜ ዘከመ ትሰምዑ ።
ማቴ ፡ ፲፫ ፡ ፲፪ ።

፲፰ እንግዲህ እንዴት እንደምትሰሙት አስተውሉ ።
እስመ ለዘቦ ይሁብዎ ወይዌስክዎ ።
ላለው ይሰጡታል ይጨምሩለታል ።
ወለዘሰ አልቦ እስኪ ቦ የሃይድዎ ።
የሌለውን ግን ያለውን ይቀሙታል ።

በእንተ አኃዊሁ ለኢየሱስ ።

፲፱ ወመጽኡ ኀቤሁ እሙ ወአኃዊሁ ። ማቴ ፡
፲፪ ፡ ፵፮ ማር ፫ ፡ ፴፪ ።
፲፱ እናቱና ወንድሞቹ ወደሱ መጡ ።
ወስእኑ ረኪቦቶ እስመ ጽፉቅ ሰብእ ።
ሰው ስለበዛ እሱን ማግኘት ተሳናቸው ።
፳ ወይቤልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እምከ ወአ
ኃዊከ አፍአ ይቀውሙ ።
፳ እናትህና ወንድሞችህ ከውጭ ቁመዋል ።
ወይፈቅዱ ይርአዩከ ።
ሊያዩህ ይወዳሉ ብለው ነገሩት ።
ወአውሥአ ። እሱም መለስ ።
፳፩ ወይቤሎሙ እምየ ወአኃውየ እለ ይሰምዑ
ቃለ እግዚአብሐር ወይገብርዎ ።
፳፩ እናቴም ወንድሞቼም የእግዚአብሔርን
ነገር ሰምተው የሚያደርጉት ናቸው ።

በእንተ ዓድፃተ ባሕር ።

፳፪ ወኮነ በአሐቲ ዕለት ዓርገ ውስተ ሐመር
ውእቱ ወአርዳኢሁ ።
፳፪ ከዕለታት ባንድ ቀን እሱም ደቀ መዛሙ
ርቱም ወደ መርከብ ወጡ ።
ወይቤሎሙ ንዑ ንዕዱ ማዕዶተ ቀላይ ።
ኑ ወደ ወንዝ ማዶ እንሂድ አላቸው ።
ወሖሩ ። ሔዱ ።

፳፫ ወእንዘ የሐውሩ ኖመ ።
፳፫ ሲሄዱ ጌታ ተኛ ።
ወመጽአ ነፋሱ አውሎ ውስተ ባሕር ።
አውሎ ነፋስ መጣ ።
ወመልአ ማየ ሐመርሙ ።
መርከባቸውን ውኃ መላው ።
ወተመንደቡ ። ተጨነቁ ።

፳፬ ወሖሩ ኀቤሁ ወአንቅሕዎ ።
፳፬ ሄደውም ቀሰቀሱት ።
ወይቤልዎ ኦ ሊቅ አድኅነነ ከመ ኢንሙት ።
መምህር ሆይ እንዳንሞት አድነን አሉት ።
ወተንሥአ ወገሠጾሙ ለነፋሳትኒ ወለማዕበለ ባሕርኒ ።
ተነሥቶ ነፋሱንም ማዕበሉንም ገሰጻቸው ።
ወአርመሙ ። ዝም አሉ ።
ወኮነ ዛሕነ ዓቢየ ።
ታላቅ ጸጥታ ሆነ ።

፳፭ ወይቤሎሙ አይቴ ሃይማኖትክሙ ።
፳፭ ሃይማኖታችሁ የታል አላቸው ።
ወፈርሁ ። ፈሩ ።
ወአንከሩ ። አደነቁም ።
ወይቤሉ በበይናቲሆሙ መኑ እንጋ ዘይትኤዘዙ
ሎቱ ባሕርኒ ወነፋሳትኒ ።
ውኃና ነፋስ የሚታዘዙለት ይህ ማነው እንጃ አሉ ።

ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ በብሔረ ጌርጌሴኖን
ለዘቦቱ ጋኔን ።

፳፮ ወእምዝ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ቢሐመር
ሀገረ ጌርጌሴኖን በአንጻረ ማዕዶተ ገሊላ ።

፳፮ በገሊላ ማዶ አንጻር ወዳለች ወደ ጌር
ጌሴኖን ሄደ ።

፳፯ ወወሪዶሙ ምድረ ተቀበሎ ብእሲ ዘጋ
ኔን ወዒአ እምሀገር ።

፳፯ ከመርከቡ በወረዱ ጊዜም ጋኔን ያደ
ረበት ሰው ተቀበለው ።
ወጕንዱይ መዋዕል እምዘኢለብሰ ልብሶ ።
ከብዙ ዘመን ጀምሮ ልብስ አይለብስም ነበር ።
ወኢቦአ ቤተ ።
ከቤትም ገብቶ አያውቅም ነበር ።
ዳዕሙ ይነብር ውስተ መቃብር ።
በመቃብር ይኖር ነበር እንጂ ።

፳፰ ወሶበ ርእዮ ለእግዚእ ኢየሱስ ከልሐ
ወሮጸ ወሰገደ ሎቱ ።

፴፱ ወይቤሎ ተመየጥ ቤተከ ወዜኑ ዘገብረ ለከ እግዚአብሔር የሠ
ራልህን ሥራ ሁሉ ንገር ብሎ አሰናበተው ።
ወሖረ ውስተ ኵሉ አህጉር ወነገረ ኵሎ ዘገብረ ሎቱ
እግዚእ ኢየሱስ ክርስቶስ።
ያደረገለትን ሁሉ ተናገረ ።

፵ ወሶበ ተመይጠ እግዚእ ኢየሱስ ተቀበልዎ
ሕዝብ ኅቡረ ።

፵ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በተመለሰ ጊዜም
ሕዝቡ ሁሉ ተቀበሉት ።
እስመ ኮኑ ኵሎሙ ይጸንሕዎ ።
ሁሉም ይጠብቁት ነበርና ።
ፀእንተ ወለተ ኢያኢሮስ ወበእንተ ደም ዘይውኅዝ ።

፵፩ ወመጽአ ብእሲ ዘስሙ ኢያኢሮስ ፤ ማቴ
፱ ፲፰ ማር፡፭ ፳፪ ።

፵፩ ኢያኢሮስ የሚባል ሰው መጣ ፤
ወውእቱ መጋቤ ምኵራብ ።
እሱም የጉባኤ አለቃ ነበር ።
ወሰገደ ሎቱ ታሕተ እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ከጌታ እግር በታች ሰገደ ።

፵፪ ወአስተብቍዖ ይባእ ቤቶ ።
፵፪ ከቤቱም ይገባ ዘንድ ማለደው ።
እስመ ቦቱ አሐቲ ወለት ።
አንዲት ልጅ ነበረችውና ።
ዘ፲ቱ ወ፪ቱ ክረምታ ።
ዐሥራ ሁለት ዘመን ሁንዋት ነበር ።
ወይእቲ አልጸቀት ትሙት ።
እሷም ልትሞት ቀርባ ነበር ።
ወእምዝ እንዘ የሐውር ምስሌሁ እግዚእ ኢየሱስ
ይትጋፍዕዎ ሰብእ ።
ከዚያ በኋላ ጌታ ከሱ ጋራ ሲሄድ ሰዎች ይገፉት ነበር

፵፫ ወመጽአት ብእሲት እንተ ደም ይውኅዛ
እም፲ቱ ወ፪ቱ ክረምት ።

፵፫ ካሥራ ሁለት ዓመት ጀምሮ ደም የሚፈሳት
ሴትም መጣች ወአሕለቀት ንዋያ ለዓቀብተ ሥራይ
ገንዘቧንም ሁሉ ለባለመድኃኒት ሰጥታ ጨርሳ ነበር
ወአልቦ ዘክህለ ፈውሶታ ።
ሊያድናት የተቻለው የለም ።

፵፬ ወቀርበት ወቆመት እንተ ድኅሬሁ ለእግዚእ
ኢየሱስ ።

፵፬ ቀርባ በጌታችን በኢየሱስ ኋላ ቆመች ፤
ወገሠሠት ጽንፈ ልብሱ ።
የልብሱን ጫፍም ዳሰሰች ።
ወቆመ ሶቤሃ ውኅዘተ ደማ ።
የደሟ ጉርፍ ያንጊዜውን ቆመ ።

፵፭ ወይቤ እግዚእ ኢየሱስ መኑ ገሠሠኒ ።
፵፭ ጌታችን ኢየሱስክርስቶስም የዳሰሰኝማነው
አለ ።
ወክህዱ ኵሎሙ ።
ሁሉም ካዱ ።

፵፮ ወይቤልዎ ጴጥሮስ ወእለሂ ምስሌሁ ፡ ሊቅ
አኮኑ ሰብእ ይጣወቅ ወይጸዓቅ ።

፵፮ ጴጥሮስና ከሱ ጋራ የነበሩ መምህር ሆይ
ሰው ይጋፋ ይጨናነቅ የለምን ።
ወትብል ፡ መኑ ገሠሠ ልብስየ ።
ልብሴን ማን ዳሰሰው ትለናለህ አሉት ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ቦ ዘገሠሠኒ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም የዳሰሰኝ አለ ።
እስመ አነ አእምር ከመ ኃይል ወፅአ እምኔየ ።
ኃይል ከኔ እንደወጣ አውቃለሁና አላቸው ።

፵፯ ወርእያ ይእቲ ብእሲት ከመ ኢተከብተ
ላቲ ርዕደት ።

፵፯ ያችም ሴት እንዳልተሰወረላት ባየች ጊዜ
ተንቀጠቀጠች ።
ወሖረት ወሰገደት ሎቱ ።
ሄዳ ሰገደችለት ።
ወነገረት በቅድመ ኵሉ ሕዝብ በእንተ አይ ግብር
ዘቀርበት ኀቤሁ ወገሠሠት ጽንፈ ልብሱ ዘከመ
ሐይወት ሶቤሃ ።
ስለማናቸውም ሥራ ቀርባ የልብሱን ጫፍ ዳሰሳ
ያን ጊዜውንም ፈጥና እንደዳነች በሕዝቡ ሁሉ
ፊት ተናገረች ።

፵፰ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ እመኒ ወለትየ
ሃይማኖትኪ አሕየወተኪ ።

፵፰ ልጄ ሆይ ሃይማኖትሽ አድኖሻልና
እመኝ አላት ።
እትዊ በሰላም ። በደህና ሂጂ አላት ።

፵፱ ወእንዘ ዘንተ ይትናገር መጽአ አሐዱ
እምቤተ መጋቤ ምኵራብ ወይቤሎ ወለትከሰ ሞተት።

፵፱ ይኸን ሲናገር ከጉባኤው ሹም ቤት አንድ
ሰው መጥቶ ልጅህ ሞታለች አለው ።
ወኢታጻምዎ እንከ ለሊቅ ።
እንግዲህ መምህርን አታድክመው ።

፶ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ይቤሎ ለመጋቤ
ምኵራብ ኢትፍራህ ዳዕሙ ተአመን ።

፶ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ይህን በሰማ
ጊዜ እመን እንጂ አትፍራ አለው ።
ወለትከሰ ተሐዩ ።
ልጅህም ትድናለች አለው ።

፶፩ ወበጺሖ ቤተ ከልዓ [illegible] ይ ኢይባእ ምስሌሁ ወኢመንሂ ።

፶፩ ከቤት በገባ ጊዜም ከሱ ጋር ማንም ማን እንዳይገባ ከለከለ ።
ዘእንበለ ጴጥሮስ ወያዕቆብ ወዮሐንስ ወአቡሃ ወእማ ለሕፃን ።
ከጴጥሮስ ከያዕቆብ ከዮሐንስ ከብላቴናዪቱ እናትና አባት በቀር ።

፶፪ ወኵሎሙ ይበክዩ ወያስቆቅዉ ።
፶፪ ሁሉም ያለቅሱላታል ያለቅሱላታል ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢትብክዩ ሕፃንሰ ኢሞተት አላ ትነውም ።
ጌታም ብላቴናይቱ ተኝታለች እንጂ አልሞተችምና አታልቅሱ አላቸው ።

፶፫ [illegible] ወሰሐቅዎ [illegible] ።
[illegible]
[illegible] እንደ ሞተች ዐውቀዋልና ።

፶፬ ወአውፅአ ኵሎ አፍአ ወአኀዛ እዴሃ ።
፶፬ ሰውን አስወጥቶ እጇን ይዞ እንዲህ አለ ።
[illegible] ወይቤላ ተንሥኢ ወለትየ ።
[illegible] ተነሺ [illegible]

፶፭ ወሶበሃ ገብአ ነፍሳ ።
፶፭ ያን ጊዜውንም ነፍሷ ገባች ።
ወተሠውጠ መንፈሳ ሳዕሌሃ ።
መንፈሷም ተመለሰ ።
ወተንሥአት ሶቤሃ ።
ያን ጊዜውንም ተነሣች ።
ወአዘዘ የሀብዋ ዘትበልዕ ።
የምትበላውን ስጧት አለ ።

፶፮ ወደንገፁ አቡሃ ወእማ ።
፶፮ አባት እናቷም አደነቁ ።
ወከልኦሙ ኢይንገሩ ወኢለመኑሂ ዘኮነ ።
የተደረገውን ለማንም ለማን እንዳይናገሩ ከለከላቸው ።

ዘከመ መሐሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ለሐዋርያት ወበእንተ ተፈንዎቶሙ ።

ምዕራፍ ፱ ።

፩ ወጸውዖሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ። ማቴ ፲፥፩ ማር ፫፥፲፭ ።

፩ ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት ጠራ ።
ወወሀቦሙ ኃይለ ወሥልጣነ ።
ኃይልን [illegible]
ወአብሖሙ ላዕለ ኵሉ አጋንንት ።
በአጋንንትም ላይ ሁሉ አሠለጠናቸው ።
ያሕይዉ ድውያነ ።
ድውያንን ይፈውሱ ዘንድ ።

፪ ወፈነዎሙ ይስብኩ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፪ የእግዚአብሔርን መንግሥት ያስተምሩ ዘንድ ወይፈውሱ ድውያነ ።
ድውያንንም ይፈውሱ ዘንድ ላካቸው ።
ወከሎሙ ሕሙማነ ።
የታመሙትንም ሁሉ ።

፫ ወይቤሎሙ ኢትንሥኡ ለፍኖት ወኢምንተ ። ማቴ ፲፥፱ ማር ፮፥፰ ።

፫ ለመንገድ ምንም ምን አትያዙ ።

| | |
|---|---|
| ኢበትረ ። | በትርም ቢሆን ። |
| ወኢጽፍነተ ። | የስንቅ አቀማጫም ። |
| ወኢእክለ ። | ስንቅም ። |
| ወኢወርቀ ። | ወርቅም ቢሆን ። |
| ወኢክልኤተ ክዳናተ ። | |

ሁለት ልብስም ቢሆን ።

፬ ወቤተ ኀበ቞እከሙ ህየ ንበሩ ።
፬ በገባችሁበትም ቤት ኑሩ ።
ወኢትፃዑ እምህየ እስከ ትወፅኡ ።
እስከትሄዱ ከዚያ አትውጡ ።

፭ ወዘሰ ኢተወከፈከሙ ወኢሰምዐክሙ እምይእቲ ሀገር ንግፉ ፀበለ እገሪክሙ ። ግብ ፲፫፥፶፩ ።

፭ የማይቀበላችሁን ግን ከዚያ አገር ወጥታችሁ የእግራችሁን ትቢያ አርግፉ ።
ከመ ይኩን ስምዐ ላዕሌሆሙ ።
መፈረሪያ ይሆንባቸው ዘንድ ።

፮ ወወፂኦሙ ሐዋርያት አዱ አህጉረ እድያም ።
፮ በወጡም ጊዜ በየሀገሩ አውራጃ ዞሩ ።
ወሰበኩ ወፈወሱ በኵለሄ ።
ድውይ እየፈወሱ ባራቱ ማዕዘን ዞረው አስተማሩ ።

በእንተ ሐልዮተ ሄሮድስ ላዕለ ኢየሱስ ።

፯ ወሰምዐ ሄሮድስ ንጉሥ ኵሎ ዘኮነ ። ማቴ ፲፬፥፩ ማር ፮፥፲፬ ።

፯ ንጉሡ ሄሮድስ የሆነውንም ሁሉ ሰማ ።
ዘከመ ገብረ ። ያደረገውን ።
ወየኃሥእ ዘይብል ። የሚለውንም አጣ ።
እስመ ቦ እለ ይብሉ ዮሐንስ ተንሥአ እሙታን ዮሐንስ ከሙታን ተነሣ የሚሉ አሉና ።

፲፯ ወአቅረቡ ወበልዑ ወጸግቡ ኵሎሙ ።
፲፯ ሁሉም በልተው ጠገቡ ።
ወዘአግንሙ ዘተርፈ ፍተታት መልአ ፲ተወ፪ተ መሳይምተ ምሉእነ ።
ያነሡት የቀረው ቁራሽ ዐሥራ ሁለት መሶብ መላ ።

በእንተ እምነተ ጴጥሮስ ወበእንተ ትንቢት ዘሕማማት ።

፲፰ ወእንዘ ይጼሊ በባሕቲቱ ። ማቴ፣፲፮ ፣ ፲፫ ማር፣ ፰ ፣ ፳፯

፲፰ በብቻው ሲጸልይ ።
ወእርዳኢሁኒ ምስሌሁ ።
ደቀ መዛሙርቱ ከሱ ጋራ ሳለ
ተስእሎሙ ወይቤሎሙ መነ ይብሉኒ ሰብእ ።
ሰው ማን ይሉኛል ብሎ ጠየቃቸው ።

፲፱ ወተሰጥውዎ ወይቤልዎ ቦ እለ ይብሉከ ዮሐንስሃ መጥምቀ ።

፲፱ ዮሐንስ መጥምቅ ነው ይሉሃል ብለው መለሱለት ።
ወቦ እለ ይብሉከ ኤልያስሃ ።
ኤልያስ ነው የሚሉህም አሉ ።
ወቦ እለ ይብሉከ አሐዱ እምነቢያት ቀደምት ተንሥአ
ከቀደሙ ነቢያት አንዱ ተነሣ ያሉም አሉ አሉት ።

፳ ወእውሥአ ወይቤሎሙ አንትሙ መነ ትብሉኒ ።

፳ እናንተ ማን ትሉኛላችሁ ።
ወተሰጥዎ ጴጥሮስ ።
ጴጥሮስ መለሰ ።
ወይቤሎ አንተ ውእቱ መሲሑ ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር ልጅ አንተ ነህ አለው ።

፳፩ ወገሠጾሙ ።
፳፩ ገሠጻቸው ።
ወከልዖሙ ኢይንግሩ ዘንተ ወኢለመኑሂ እምሰብእ ።
ይህን ለማንም ለማን እንዳይናገሩ ከለከላቸው ።

፳፪ ወይቤሎሙ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለእመሕያው ብዙኃ ያሐምምዎ ። ማቴ፣፲፮ ፣ ፳፩ ማር ፰ ፣ ፴፫

፳፪ ለሰው ልጅ ክርስቶስ ብዙ መከራ ይቀበል ዘንድ አለው ።
ወያመክርዎ ረበናት ወሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ።
የካህናት አለቆችና ሽማግሌዎች ጸሐፎችም በመከራ ይፈትኑት ዘንድ ።
ወይቀትልዎ ። ይገድሉታል ።
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛውም ቀን ይነሣል ።

በእንተ ክሒደ ርእስ ለክርስቲያን ።

፳፫ ወይቤሎሙ ለኵሎሙ ዘይፈቅድ ይትልወኒ ይጽልእ ለንፍሱ ። ማቴ ፣ ፲፥፴፰፲፮ ፣ ፳፬ ፣ ማር፣ ፰ ፣ ፴፬ ሉቃ ፣ ፲፬ ፣ ፳፯ ዮሐ፣ ፲፪ ፣ ፳፭ ።

፳፫ በኋላዬ ሊከተለኝ የሻ ሰው ሰውነቱን ይካድ።
ወያጥብዕ ወይንሣእ መስቀለ ሞቱ ወኵሎ ዕለተ ይትልወኒ ፤
ጨክኖ የሞቱን መስቀልም ይዞ ዕለት ዕለት ይከተለኝ ።

፳፬ ወዘሰ ይፈቅድ ያድኅና ለንፍሱ ይገድፋ ።
፳፬ ሰውነቱን ሊያድናት የወደደ ያጣታል ።
ወዘሰ ገደፋ ለንፍሱ በእንቲአየ ያድኅና ።
ስለኔ ሰውነቱን የጣላት ነፍሱን ያድናታል ።

፳፭ ወምንተ ይበቍዖ ለሰብእ ለእመ ኵሎ ዓለመ ረብሐ ወንፍሶ ኀጕለ ።

፳፭ በነፍሱ ከጠፋ ዓለሙን ሁሉ ቢገዛ ለሰው ምን ይረባዋል ።
ወለዘኒ ኃፈረኒ ። በኔ ያፈረ
ወኃፈረ ቃልየ ። በነገሬ ያፈረ ሰው ።

፳፮ የኃፍሮ ሎቱኒ ወልደ ዕጓለእመሕያው አመ ይመጽእ በስብሐቲሁ ወበስብሐተ አቡሁ ። ማቴ ፣ ፲ ፣ ፴፫ ማር፣ ፰ ፣ ፴፰

፳፮ በክብር ባባቱም ክብር በመጣ ጊዜ የሰው ልጅም ክርስቶስ ያፍረዋል ።
ወምስለ ቅዱሳን መላእክቲሁ ። ፪፣ጢሞ፣ ፪፣ ፲፪
በቅዱሳን መላእክት ምስጋናም በመጣ ጊዜ ።

፳፯ አማን አማን እብለክሙ ሀለዉ እምእለ ይቀወሙ ዝየ እለ ኢይጥዕምዎ ለሞት እስከ ይሬእይዎ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳፯ ከዚህ ቆመው ካሉት የእግዚአብሔርን መንግሥት እስኪያዩ ድረስ የማይሞቱ አሉ ብየ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፳፰ ወእምድኅረ ዝንቱ ነገር አመ ሳምንት ዕለት ነሥኦሙ እግዚእ ኢየሱስ ለጴጥሮስ ወለያዕቆብ ወለዮሐንስ ወዓርገ ደብረ ከመ ይጼሊ ። ማቴ ፣ ፲፯ ፣ ፩ ማር ፱ ፣ ፩ ።

፳፰ ከዚህ በኋላም በስምንተኛው ቀን ያዕቆብንና ጴጥሮስን ዮሐንስንም ይዟቸው ይጸልይ ዘንድ ወደ ተራራ ወጣ ።

፳፱ ወእንዘ ይጼሊ ተወለጠ ርዕየተ ገጹ ።
፳፱ ሲጸልይም የፊቱ መልክ ተለወጠ ።
ወአልባሲሁኒ ፃዕደወ ።
ልብሱም ነጭ ሆነ ።
ወበረቀ ከመ መብረቅ ።

ተብለጨለጨም ። ሐተታ ማቴዎስ ፯ ይላል ማርቆስ ስድስት ይላል ሉቃስ ስምንት አለ ።እንደ ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ማቴዎስ ከወጡበትና ከወረዱበት አንዱን አውጥቶ ሰባት አለ ። ማርቆስ ሁሉቱንም አውጥቶ ስድስት አለ ሉቃስ ሁለቱንም አግብቶ ስምንት አለ ። አንድም የማቴዎስ የሉቃስ አይለወጥም የማርቆስ የብተት ነው እኛ ስምንት ስንል አንድ ይላሉ ዐሥር ስንል ሦስት ዐሥራ ሦስት ስንል ስድስት ይላሉና አንድም ማቴዎስ አይለወጥም ማርቆስም አይለወጥም የብተት ነው ሉቃስ ስምንች ማለቱ ሰባት ሲል ነው ። ንዒ ኀቤነ ለለሰሙኑ እእምሮ ከመ ግብር ዘበእንተ ጾም ዓቢይ ከመ ውእቱ ሰሙንቱ ሰሙን ውእቱ እንዲል ።

፴ ወናሁ መጽኡ ክልኤቱ ዕደው ።
፴ እነሆ ሁለት ሰዎች መጡ ።
እንዘ ይትናገሩ ምስሌሁ ።
ከሱም ጋራ ይነጋገሩ ነበር ።

፴፩ እሉ እሙንቱ ሙሴ ወኤልያስ ።
፴፩ እሊህ ሙሴ ኤልያስ ናቸው ።
አለ አስተርአዩ በስብሐት ።
በክብር የተገለጹ ።
ወነገሩ ስብሐቲሁ ዘሀለዎ ይኩን በኢየሩሳሌም ።
በኢየሩሳሌም ይደረግ ዘንድ ያለውን መከራውን የተናገሩ አፈወርቅ ይትባረክ እግዚአብሔር ዘሰመዮ ሕማማተ ወልዱ ክብረ ወስብሐተ እንዲል ። እኛ የምንከብርበት ስለሆነ መከራውን ክብር ስብሐት ይለዋል ።
ወፀአቶሂ ።
ወደ ኢየሩሳሌም መውጣቱንም የተናገሩ ። አንድም ወደመስቀል መውጣቱን በኢየሩሳሌም ይደረግ ዘንድ ያለው ታምራቱን የተናገሩ እሊህ ናቸው ።

፴፪ ወፀአቶሂ ረከበ ጴጥሮስሃ ወእለሂ ምስሌሁ ክቡዳን አዕይንቲሆሙ በድቃስ ።

፴፪ ጌታ ከስዋሬው በተገለጸ ጊዜ ጴጥሮስን ወንድሞቹንም ደንግጠው አገኘ ። አንድም ኦውጣን አውጣን አሉ ስለ ወጡ ግን ጴጥሮስን ወንድሞቹን በጽኑ ዕንቅልፍ ተይዘው አገኛቸው ።
ወነቂሆሙ ርእዩ ስብሐቲሁ ።
በነቁም ጊዜ ክብሩን አዩ ።
ወእደውኒ ክልኤቱ እለ ይቀውሙ ምስሌሁ ።
ከሱ ጋራ ቁመው የነበሩትም ሁለቱ ሰዎች ።

፴፫ ወእምዝ ሶበ ፈቀዱ ይትሌለዩ እምኔሁ ይቤሎ ጴጥሮስ ለእግዚእ ኢየሱስ ሊቅ ንንበር ዝየ ።

፴፫ ከዚህ በኋላ ተለይተውት በሄዱ ጊዜ ጴጥሮስ ጌታን መምህር ከዚህ ልንኖር ይገባናል አለው ።
ወንግበር ሠለስተ ሰቃልወ ።
ሦስት ማደሪያም ልንሠራ ።
አሐዱ ለከ ። አንዱን ላንተ ።
ወአሐደ ለሙሴ ። አንዱን ለሙሴ
ወአሐደ ለኤልያስ ። አንዱን ለኤልያስ ።
ወኢየአምር ዘይብል ።
የሚናገረውንም አያውቀውም ነበር ።

፴፬ ወዘንተ ብሂሎ ጸለሎሙ ደመና ።
፴፬ ይህንም ሲናገር ደመና ጋረዳቸው ።
ወቦበ ቦኡ ውስተ ደመና ፈርሁ ።
ከደመናው ውስጥ በገቡ ጊዜ ፈሩ ።

፴፭ ወመጽአ ቃል እምውስተ ደመና ዘይብል ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ዘአፈቅር ወሎቱ ስምዕዎ ።

፴፭ ከደመናው የመረጥኩት ልጄ ይህ ነውና እሱን ስሙት የሚል ቃል ተሰማ ።

፴፮ ወመጺኦ ቃል ረከብዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ባሕቲቶ ።

፴፮ ድምፅ ከተሰማ በኋላ ጌታ ብቻውን ተገኘ ።
ወእሙንቱሰ አርመሙ ።
እነሱ ግን ዝም አሉ ።
ወኢነገሩ ለመኑሂ ዘርእዩ ወሰምዑ ይእተ አሚረ ።
በዚያን ጊዜ ያዩትን የሰሙትን ለማንም ለማን አል ተናገሩም ።

ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ ለዘያንገረግሮ ጋኔን ።

፴፯ ወእምዝ በሳኒታ ዕለት እንዘ ይወርዱ እምደብር ።

፴፯ ከዚህም በኋላ በነጋው ከተራራ ሲወርዱ ።
ተቀበልዎ ሕዝብ ብዙኃን ።
ብዙ ሰዎችም ተቀበሉት ።

፴፰ ወአውየወ አሐዱ ብእሲ በማእከለ ሕዝብ ።
ማቴ ፡ ፲፯ ፡ ፲፬ ማር ፱ ፡ ፲፯ ።

፴፰ አንድ ሰው በሕዝብ መካከል ጮኸ ።
ወይቤሎ ኦ ሊቅ ብቍዓኒ ።
መምህር ሆይ በጅ በለኝ ።
ረዓይ ሊተ ወልድየ ።
ልጄን እድንልኝ ።
እስመ አሐዱ ሊተ ውእቱ ።
ለኔ አንድ ነውና ።

፴፱ ወናሁ እኩይ ጋኔን የሐይዶንዮ ።
፴፱ እነሆ ጋኔን ቀምቶኛል ።
ወያዌግቦ ።
ያስፈራራዋል ያስደነግጠዋል ።
ወታዌግበከሙ ዕለት እኪት ትንዲል ።
ወይነጽሖ ። ይጥለዋል ።
ወያስተራግዖ ። ያራግጠዋል ።

ወያሲውዖ ፤ ያስለግገዋል ።
ወእም ዕፁብ የኃድጎ ቀጥቂጦ ።
በጭንቅ ቀጥቅጦ ይተወዋል ።

፵ ወአስተብቍዕክዎሙ ለአርዳኢከ ከመ
ያውፅእዎ ።

፵ ደቀ መዛሙርትህንም ያወጡት ዘንድ ለመ
ንኋቸው ።
ወስእንዎ ፈውሶቶ ወአውፅኦቶ ።
ማዳን ተሳናቸው ።

፵፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፵፩ ጌታም መለሰ ።
ወይቤ እትውልድ ዕሉት እንተ አልባቲ ሃይማኖት ።
እናንተ ሃይማኖት የሌላችሁ ዓመፀኛ ትውልድ ።
እስከ ማእዜኑ እሄሉ ምስሌክሙ ።
እስከ ፡ መቼ ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ።
ወእስከ ማዕዜኑ እትዔገሠክሙ
እስከ መቼስ እታገሣችኋለሁ ብሎ ።
አምጽእ ዝየ ለወልድከ ።
ልጅህን ወዲህ አምጣው አለው ።

፵፪ ወእንዘ ያመጽእ ነጽሖ ጋኔኑ ።
፵፪ ሲያመጣው ጋኔኑ ጣለው ።
ወአስተራገፆ ። አራገጠው ።

፵፪ ወገሠጾ እግዚእ ኢየሱስ ለውእቱ ጋኔን
እኩይ ።

፵፪ ጌታም ያን ክፉ ጋኔን ገሠጸው ።
ወአሕየዎ ለውእቱ ወልድ ።
ያንንም ልጅ አዳነው ።
ወመጠዎ ወአወፈዮ ለአቡሁ
ለአባቱም ሰጠው ።

በእንተ ዘተናገረ ኢየሱስ አቅዲሞ ነገረ ሞቱ ።

፵፫ ወአንከሩ ኵሎሙ እምዕበዩ ለእግዚአብ
ሔር ።

፵፫ እግዚአብሔር ካደረገለት ታምራት
የተነሣ ፤ እምዕበዮሙ ካደረገላቸው ታምራት
በዕበዩ ባደረገለት ታምራት በዕበዮሙ ባደረገላቸው
ታምራት በበዕበዩ በየተደረገለት ታምራት ። በበዕ
በዮሙ በየተደረገላቸው ታምራት ። በይነ ዕበዩ ስለ
ተደረገለት ታምራት በይነ ዕበዮሙ ስለ አደረገላ
ቸው ተአምራት አደነቁ ።
ወእንዘ እሙንቱ ያነክሩ በእንተ ፡ ኵሉ ዘገብረ እግ
ዚእ ኢየሱስ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ አንትሙ ደይዎ
ለዝንቱ ነገር ውስተ ልብክሙ ።
ጌታ ስለአደረገው ነገር ሁሉ እሱን ሲያደንቁ ደቀ
መዛሙርቱን እናንተስ ይህን ነገር በልቡናችሁ አኑ
ሩት አላቸው ።

እስመ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለእመሕያው ይግባእ ውስተ
እደ ሰብእ ።
ለሰው ልጅ በሰው እጅ ይሰጥ ዘንድ አለውና ።

፵፭ ወኢለበውዎ ለዝንቱ ነገር ።
፵፭ ይህን ነገር አላስተዋሉትም ነበር ።
እስመ ስውር ውእቱ እምኔሆሙ ።
ይህ ነገር ተሰውሯቸው ነበርና ።
ከመ ኢይንሀኩ ።
እንዳያዝኑ ብእሲ ኢመዋቲ ዘአእመረ ሀኬከ እንዲል ።
ወይፈርህዎ ተጠይቆቶ በእንተ ዝንቱ ነገር ።
ስለዚህም ነገር እሱን መጠየቅ ይፈሩ ነበር ።

ዘከመ ይደልዎ ለክርስቲያን ትሕትና
ወተአግሦተ ቢጽ ።

፵፮ ወሀለዩ በበይናቲሆሙ እንዘ ይብሉ መኑ
የዓቢ እምኔሆሙ ። ማቴ፲፰ ፡ ፩ ማር ፱ ፡ ፴፫

፵፮ ከርሳቸው ማንኛቸው እንዲበልጥ እርስ
በርሳቸው አሰቡ ።

፵፯ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ዘይሄልዩ
በልቦሙ ።

፵፯ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም በልባቸው
ያሰቡትን ዐውቆባቸው ።
ነሥአ ሕፃነ ወዓቀሞ በማዕከሎሙ ።
ሕፃን ወሰዶ በመካከላቸው አቆመው ።

፵፰ ወይቤሎሙ ዘተወክፈ ዘመጠነዝ ሕፃን
በስምየ ኪያየ ተወክፈ ።

፵፰ ይህን ሕፃን በስሜ የተቀበለ ሁሉ እኔን
ተቀበለ ።
ወዘሰ ኪያየ ተወክፈ ተወክፎ ለዘፈነወኒ ።
እኔን የተቀበለም አባቴን ተቀበለ አላቸው ።
እስመ ዘአትሐተ ርእሶ እምኵሉ ውእቱ የዓቢ ።
ራሱን ያዋረደ ከሁሉ ይበልጣልና ።

፵፱ ወአውሥአ ዮሐንስ ።
፵፱ ዮሐንስ መለሰ ።
ወይቤሎ ሊቅ ቦ ዘርኢነ ፩ደ ብእሴ እንዘ ያወፅእ
አጋንንተ በስምከ ወከላዕናሁ ።
መምህር ሆይ በስምህ ጋኔን ሲያወጣ አንድ ሰው
አግኝተን የከለከልነው አለ አለው ።
እስመ ኢተለወከ ምስሌነ ።
ከኛ ጋራ አልተከተለህምና ።

፶ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢትከልዕዎ ።

፶ ጌታም አትከልክሉት አላቸው ።
እስመ እምከመ ኢኮነ ዕድውክሙ ቢጽክሙ ዘም
ስሌክሙ ውእቱ ።
ባለጋራችሁ ካልሆነ ከናንተ ጋራ ነው ፡

ዘከመ ተሰደ ኢየሱስ እምሰማርያ ።

፶፩ ወተፈጺሞ መዋዕለ ዕርገቱ እንጸረ ገጾ ለሐዊር መንገለ ገጸ ኢየሩሳሌም ።

፶፩ ወደ ደብረ ታቦር የሚወጣበት በኤፍሬም ዕጣ የሚኖርበት ቀን በተፈጸመ ጊዜ ። አንድም ወደ ኢየሩሳሌም ወደመስቀል የሚወጣበት ቀን በደረሰ ጊዜ ወደ ኢየሩሳሌም ለመሄድ ፊቱን መለሰ ።

፶፪ ወፈነወ ሐዋርያተ ቅድመ ገጹ እለ ይዜንዉ ።

፶፪ መጥን አሰናዱ ብሎ ሐዋርያትን በፊቱ ላከ
ወሐዊሮሙ ቦኡ ሀገረ ሳምር ።
ሂደው ወደ ሳምራውያን አገር ገቡ ።
ከመ ያስተዳልዉ ።
መጥን ያሰናዱለት ዘንድ ።

፶፫ ወኢተወከፍዎሙ ።
፶፫ አልተቀበሏቸውም ።
እስመ ርሑው ውጉሉፍ ገጹ ለኢየሩሳሌም ።
ፊቱን ወደ ኢየሩሳሌም አቅንቶ ነበርና ፣ ሐተታ የፍቅር ነው ምነው በኛ በኩል ያልመጣ ብለው ።

፶፬ ወርእዮሙ አርዳኢሁ ያዕቆብ ወዮሐንስ ዘንተ ።

፶፬ ደቀ መዛርቶቹ ያዕቆብና ዮሐንስ ይኸን አይተው ።
ይቤልዎ ሊቅ ንፈቅድ ትበል ይረድ እሳት እምሰማይ ወያጥፍእሙ በከመ ገብረ ኤልያስ ።
መምህር ሆይ ኤልያስ ሁለት ጊዜ እሳት ከሰማይ አውርዶ አምሳ እምሳውን ጭፍራ ከነአለቆቻቸው እንደአቃጠላቸው እሳት ከሰማይ እውርደህ ልታቃጥላቸው እንወዳለን አሉት ።

፶፭ ወተመይጦ ገሠጾሙ እግዚእ እየሱስ ።
፶፭ ተመልሶ ተቆጣቸው ። የቦታም ከመዓት ወደምኅረት ተመልሶ ።
ወይቤሎሙ ኢያእመርክሙኑ መጠና ሰነፍስከሙ። የሰውነታችሁን መጠን እታውቁምን ማለት እኔ ብታገኙችሁ ነው እንጂ እናንተስ ከነዚያን ልዩ ናችሁ አላቸው ። አንድም ዘአይ መንፈስ አንትሙ የሚል አብነት ይገኛል የማን ሀብት ወገን ናችሁ ሀብተ ርትዕ ያለው ኤልያስ ሁለት ጊዜ እሳት ከሰማይ አውርዶ ሁለቱን አለቆች ካምሳ ካምሳ ጭፍራ ጋራ አስፈጃቸው ። እናንተማ ሀብተ ትሩፋት ያለኝ የኔ ወገን አይደላችሁምን። አንድም የማን መምህር ደቀ መዛሙርት ናችሁ ሀብተ ርትዕ ያለው የኤልያስ ደቀ መዝሙር ኤልሳዕ ሁለት ድባት እሥነሥቶ አርባ ሁለት ሕፃናት አስፈጀ ። እናንተ ሀብተ ትሩፋት ያለኝ የኔ ደቀ መዛሙርት አይደላችሁምን ።

፶፮ እስመ ኢመጽአ ወልደ ዕጓለ እምሕያው ከመ ያጥፍዕ ነፍሳተ ሰብእ ዘእንበለ ከመ ያድኅን ዘተኀጉለ ። ማ፣ቴ፲፰፣፲፩ ማር፣፱፣፴፫ ።

፶፮ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ሊያድን ነው እንጂ ሊያጠፋ አልመጣምና ።
ወሖሩ ካልዕተ ሀገረ ።
ወደሌላም አገር ሄዱ ።

ዘከመ ይደሉ በዓይ ተሊዎተ ኢየሱስ ።

፶፯ ወእምዝ እንዘ የሐውሩ በፍኖት ይቤሎ አሐዱ ሊቅ እትሉከኑ ኀበ ሖርከ ።

፶፯ ከዚህ በኋላ ሲሄዱ አንድ ሰው መምህር ሆይ ልከተልህን አሰው ።

፶፰ ወይቤሎ ኢየሱስ ለቆናጽልኒ ግበብ ቦሙ ማቴ ፰፣፰ ።

፶፰ ጌታም ለቀበሮዎች ጉድጓድ አላቸው ።
ወለአዕዋፈ ሰማይኒ ምጽላል ቦሙ ።
ለዎፎችም ማረፊያ አላቸው ።
ለወልደ ዕጓለ እመሕያውሰ አልቦቱ ኀበ ያሰምክ ርእሶ ።
ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ግን ራሱን ለሚያስጠጋበት የለውም አለው ።

፶፱ ወይቤሎ ካልዑኒ እትሉከኑ እግዚኦ ።
፶፱ ሌላውም እቤቱ ልከተልህን አለው ።
ወባሕቱ አብሐኒ እሑር ቅድመ እቅብሮ ለአቡየ ።
ነገር ግን አስቀድሜ ሄጄ አባቴን እቀብር ዘንድ አሰናብተኝ እለው ።

፷ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ኅድጎሙ ለምውታን ይቅብሩ ምውታኒሆሙ ።

፷ ጌታም ሙታንን ተዋቸው ሙታናቸውን ይቅበሩ ።
ወአንተሰ ሑር ወሰብክ መንግሥተ እግዚአብሔር።
አንተስ ሂደህ የእግዚአብሔርን መንግሥት አስተምር አለው

፷፩ ወይቤሎ ሣልሱኒ እትሉከኑ እግዚኦ ።
፷፩ ሦስተኛው ሌላውም ልከተልህን አለው፤
ወባሕቱ አብሐኒ እሑር እሥራዕ ዡሎ ሰብአ ቤትየ ወእምጸእ ።
ነገር ግን ቤተ ሰዎቼን እሠራ ዘንድ ማለት በዚህ ዋሉ በዚህ እደሩ ብዬ ልምጣ ። አንድም እሰነአል ይላል ተሰናብቼ ልምጣ አለው ።

፷፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አልቦ ዘይእኅዝ ዕርፈ ወየሐርስ ድኅሪተ ወይክውን ድልወ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ።

፷፪ ጌታም ዕርፍ ይዞ ወደኋላው የሚያርስ የለም እለው ከመነኑም በኋላ ወደ ዓለም የሚመለስ የለም ።
እስመ ርትዕት ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር መንግሥት የቀናች ናት ማለት ወደ ፊት ናት

በእንተ ተፈንዎተ ዘሐዋርያት ቀዳማውያን ።

ምዕራፍ ፲ ።

፩ ወእምዝ አርአየ እግዚእነ ካልዓነ ሰብአ ።
፩ ፸ ኃረየም ይላል ። ከዚህም በኋላ ጌታችን ሰብዓ አርድዕትን መረጠ ።
ወፈነዎሙ በበክልኤቱ ቅድመ ገጹ ፤
ሁለት ሁለቱንም በፊቱ ላካቸው ፤
ውስተ ኵሉ አህጉር ።
በየሀገሩ ሁሉ ፤
ወበሐውርት ኀበ ሀለዎ ይባእ ፤
ይገባበት ዘንድ በያለውም አውራጃ ሁሉ ።
ኀበ ሀለዎሙ ይባእሙ ፤
ጌታ ይገባቸው ዘንድ ወዳላቸው አህጉር ፣ ኀበ ሀለዎሙ ይባኡ ፣ ሐዋርያት ይገቡባቸው ዘንድ ወዳላቸው ።
ሀበ ሀለዎሙ ይባዕዎሙ ።
ሐዋርያት ይገቡባቸው ዘንድ ወዳለው አህጉር ።
፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ማዕረሩሰ ብዙኅ ። ማቴ፡፱፡፴ ።
፪ ጌታም መከሩ ብዙ ነው አላቸው ።
ወገባሩ ኅዳጥ ።
ሠራተኞች ግን ጥቂት ናቸው ።
ሰእልዎ እንከ ለበዓለ ማዕረር ከመ ይፈነው ወይፈኑ ገባረ ለማዕረሩ ።
ለመከሩ ሠራተኞችን ያክል ዘንድ ባለመከሩን ለምኑት አላቸው ።

፫ ሑሩ ናሁ እፌንወክሙ ከመ አባግዕ ማዕከለ ተኵላት ። ማቴ፡፲፡፲፮ ።
፫ እነሆ እንደ በግ ተኵላ ወዳለበት እልካችኋለሁና ሂዱ አላቸው ።
፬ ወኢትጹሩ ቍናማተ ፤
፬ ከረጢት አትያዙ ።
ወኢጽፍነተ ፤ ስልቻም ።
ወኢአሣዕነ ። ጫማም ።
ወኢምንተኒ ።
ምንም ምን አትያዙ ።
ወኢተአምኁ ወኢመነኒ በፍኖት ።
በመንገድ ለማንም ለማን ሰላምታ አትስጡ

፭ ወኀበ በጽሕክሙ ቤተ ቅድሙ በሉ ሰላም ለሰብአ ዝንቱ ቤት ።

፭ ከገባችሁበት ቤት አስቀድማችሁ ለዚህ ቤት ሰዎች ሰላም በሉ ።

፮ ወእመቦ ህየ ወልደ ሰላም ያዕርፍ ሰላምክሙ ላዕሌሁ ።

፮ ከዚያም የሰላም ልጅ ቢኖር ሰላማችሁ ይደርበት ።
ወእመ አኮሰ ይገብእ ሰላምክሙ ላዕሌክሙ ።
ባይኖርም ሰላማችሁ ወደእናንተ ይመለስ ።

፯ ወውእተ ቤተ ንበሩ ። ዘዳግ፡፳፬፡፲፬፡ማቴ፡፲፡፲፡ ፩ ፡፲፪ ፩ጢሞ፡፭ ፡ ፲፰ ።

፯ ከገባችሁበት ቤት ኑሩ ።
ብልዑ ወስትዩ ዘእምኀቤሆሙ ።
በርላቸው ዘንድ የተገኘውን ብሉ ጠጡ ።
እስመ ይደልዎ አስቡ ለዘይትቀነይ ።
ለሠራተኛ ዋጋው ይገባዋልና
ወኢትትፋለሱ እምቤት ውስተ ቤት ።
ካንዱ ቤት ወደአንዱ ቤት አትሂዱ ።

፰ ወሀገረኒ እንተ ኀበ ቦእክሙ ወተወክፉክሙ ሰብእ ይእቲ ሀገር ።

፰ ከገባችሁበት ከተቀበሏችሁም አገር ።
ብልዑ ዘአቅረቡ ለክሙ ።
ያቀረቡላችሁን ብሉ ።

፱ ወፈውሱ ድዉያነ እለ ውስቴታ ።
፱ ያሉትን ድውያንንም ፈውሱ ።
ወበልዎሙ ቀርበት መንግሥተ እግዚአብሔር ኀቤክሙ ።
የእግዚአብሔር መንግሥትም ወደናንተ ቀርባለች በሏቸው ።

፲ ወእየኒ ሀገረ ኀበ ቦእክሙ ወኢተወክፉክሙ ሰብእ ይእቲ ሀገር ወፃእክሙ ውስተ መርኅባ ።

፲ ከገባችሁበት ካልተቀበሏችሁ አገር ግን ወደ ዐደባባይ ወጥታችሁ ።
ንግፉ ፀበለ እገሪክሙ እንዘ ትብሉ ።
የእግራችሁን ትቢያ አራግፉ ።

፲፩ ወፀበለክሙኒ ዘተለወነ እምሀገርክሙ ንነግፍ ለክሙ ።

፲፩ ከሀገራችሁ የተጣበቀብንን ትቢያ ስንኳን እራገፍንላችሁ ብላችሁ ።
ወባሕቱ ዘንተ አእምሩ ከመ ቀርበት መንግሥተ እግዚአብሔር ላዕሌክሙ ።

ነገር ግን የእግዚአብሔር መንግሥት ለእናንተ እንደ ቀረበች ይህንም ዕወቁ ።

፲፪ እብለከሙ ሰዶም ትኄይስ ወትረክብ ሣህለ ፈድፋደ እምይእቲ ሀገር በዕለተ ደይን ፤

፲፪ ክዚያችም አገር ይልቅ በፍርድ ቀን ሰዶም ትሻላለች ይቅርታንም ታገኛለች ብየ እነግራችኋለሁ ።

፲፫ አሌ ለኪ ኮራዚ ። ማቴ ፲፩፡፳፩ ።
፲፫ ኮራዚ ሆይ ወዮልሽ ፤
አሌ ለኪ ቤተ ሳይዳ ፤
ቤተ ሳይዳ ሆይ ወዮልሽ ፤
ሶበሰ በጢሮስ ወበሲዶና ተገብረ ኃይል ዘተገብረ በውስቴትክን እምትካት ፤
በናንተ የተደረገው ኃይል በሲዶናና በጢሮስ ተደ ርጎስ ቢሆን ።
ሠቀ እምለብሱ ። ማቅ በለበሱ ነበር ።

ወውስተ ሐመድ እምነበሩ ፤ ወእምነሥሑ ።
በአመድ በተቀመጡ ንስሐም በገቡ ነበር ።

፲፬ ወባሕቱ ጢሮስ ወሲዶና ይረክባ ሣህለ ፈድፋደ እምኔክን በዕለተ ደይን ፤

፲፬ ነገር ግን በፍርድ ቀን ከናንተ ይልቅ ጢሮስና ሲዶና ይቅርታን ያገኛሉ ።

፲፭ ወአንቲኒ ቅፍርናሆም እመ ተለአልኪ እስከ ሰማይ ሀለወኪ ትረዲ ውስተ ሲኦል ።

፲፭ አንች ቅፍርናሆም እስከ ሰማይ ከፍ ከፍ ብትዪ እስከ ሲኦል ትወርጃለሽ ።

፲፮ ዘኪያከሙ ሰምዓ ኪያየ ሰምዓ ማቴ.፲፡ዮሐ.፲፫፡ ፳ ።

፲፮ እናንተን የሰማ እኔን ሰማ ።
ወዘለክሙ አበየ ሊተ አበየ ።
እናንተን እምቢ ያለ እኔን እምቢ አለ ።
ወዘሊተ አበየ አበየ ለዘፈነወኒ ።
እኔን እምቢ ያለ የላከኝን አባቴን እምቢ አለ ።
ወዘሊተ ሰምዓ ሰምዖ ለዘፈነወኒ ።
እኔን የሰማ የላከኝን አባቴንም ሰማ ።

ዘከመ ተመይጡ እምዘተፈነዉ ።

፲፯ ወተመይጡ እልኩቱ ሰብእ እለ ተፈነዉ እንዘ ይትፌሥሑ ወይቤሉ እግዚኦ አጋንንትኒ ገረሩ ለነ በስምከ ።

፲፯ እሊህም ሰብዓ ሁለቱ አርድዕት አቤቱ አጋንንት በስምህ ተገዙልን እያሉ ደስ ብሏቸው ተመለሱ ።

፲፰ ወይቤሎሙ ናሁ ርኢክዎ ለሰይጣን ከመ መብረቅ ወድቀ እምሰማይ ።

፲፰ ሰይጣንን ከሰማይ እንደ ወደቀ መብረቅ አየሁት፤ ሐተታ መብረቅ ከተበተነ በኋላ ሥራ እን ዳይሠራ ሰይጣንም በገዳም በምስቱ አርአስተ ኃጣ ውእ ድል ከነሳሁት በኋላ ሥራ እንዳይሠራ ዓው ቃለሁ ።

፲፱ ወናሁ ወሀብኩክሙ ሥልጣነ ትኪዱ ዲበ ዓቃርብት ወዲበ አራዊተ ምድር ወዲበ ኵሉ ኃይለ ጸላዒ ።

፲፱ በአባብና በጊንጥ በጸላትም ሁሉ ኃይል ላይ ትሔዱ ዘንድ ማለት ሊቃነ አጋንንት አኩያት ፍት ወታት ኃጣውእን ድል ትነሡ ዘንድ እነሆ ሥልጣን ሰጠኋችሁ ።
ወአልቦ ዘይነክየክሙ ።
የሚያገኛችሁ ጉዳት የለም ።

፳ ወባሕቱ በዝስ ኢትትፌሥሑ እስመ አጋ ንንት ይገንዩ ለክሙ ።

፳ ነገር ግን አጋንንት ስለተገዙላችሁ ደስ አይበላችሁ ።
ሐተታ በዚህ ደስ አይበላችሁ ።
በእንተ እለ ይመጽኡ ይትፌወሱ ።
የሚደረግ ተአምራት አለና ፤
እስመ ገቢረ ተአምራት መንከራት ኢይከል ያድ ኅን እምዘነኔ ገሃነም እንዲል ።
ተፌሥሑ ባሕቱ እስመ ተጽሕፉ አስማቲክሙ በሰ ማያት ።
ነገር ግን ስማችሁ በሰማይ ተጽፏልና ማለት በልበ እግዚአብሔር ታውቋልና ፤ ስለዚህ ደስ ይበላችሁ ።

በእንተ ድኅነት ።

፳፩ ወበይእቲ ሰዓት ተፈሥሐ እግዚእ ኢየሱስ በመንፈሱ ቅዱስ ።

፳፩ በዚያን ጊዜም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በመንፈስ ቅዱስ ደስ አለው ።
ወይቤ አአምነከ አባ እግዚአ ሰማይ ወምድር ዘኃ ባዕኮ ለዝንቱ እምጠቢባን ወእምለባውያን ወከሠ ትኮ ለሕፃናት ።
ይህን ከብልሃተኞችና ካስተዋዮች ሰውረህ ለሕፃ ናት የገለጽኸው የሰማይና የምድር ጌታ አባቴ ሆይ አመሰግንሃለሁ ።
እወ አባ እስመ ከማሁ ኮነ ሥምረትከ በቅድሜከ ።
አዎን አባት ሆይ ፈቃድህ በፊትህ እንዲህ ሁኖለችና።

፳፪ ወተመይጠ ኀበ አርዳኢሁ ወይቤሎሙ ኵሉ ተውህበ ሊተ እምኀበ አቡየ።ማቴ፡፲፩፡፳፯።

፳፪ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ተመልሶ ሁሉ ካባቴ ተሰጠኝ አላቸው ።

ወእልቦ ዘየአምሮ ለወልድ ዘእንበለ አብ ፡፡
ወልድን ያለ አብ ማን እንደሆነ የሚያቀው የለም ፡፡
ወእልቦ ዘየአምሮ ለአብ ከመ መኑ ውእቱ አብ ዘእንበለ ወልድ ፡፡
አብንስ ያለወልድ የሚያውቀው ማነው ፡፡
ወለዘፈቀደ ወልድ ይክሥት ሎቱ ፡፡
ወልድ ማን ለወደደው ይገለጥለታል ፡፡

፳፫ ወተመይጠ ካዕበ ኀበ አርዳኢሁ ወይቤሎሙ እንተ ባሕቲቶሙ ብፁዓት አዕይንት እለ ይሬእያ ዘትሬእዩ አንትሙ ፡፡ ማቴ ፡ ፲፫ ፡ ፲፮ ፡፡

፳፫ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ተመልሶ እናንተ የምታዩትን የሚያዩ ዓይኖች የተመሰገኑ ናቸው ፡፡

፳፬ እብለክሙ ከመ ብዙኃን ነቢያት ወነገሥት ፈተዉ ይርአዩ አንትሙ ዘትሬእዩ ወኢርእዩ ፡፡

፳፬ ብዙ ነገሥታትና ነቢያት እናንት የምታዩትን ሊያዩ እንደወደዱ እንዳላዩ ፡፡
ወይሰምዑ ዘትሰምዑ አንትሙ ወኢሰምዑ ፡፡
እናንተ የምትሰሙትንም ሊሰሙ እንደወደዱ እንዳልሰሙ በውነት እነግራችኋለሁ ፡፡

፳፭ ወእምዝ ተንሥአ አሐዱ ጸሐፊ ሀገር ያመክሮ ፡፡ ማቴ ፡ ፳ ፡ ፲፦ ፴፭ ማር ፡ ፲፪ ፡ ፳፰ ፡፡

፳፭ ከዚህ በኋላ አንድ ያገር ጸሐፊ ሊፈትነው ተነሣ ፡፡
ወይቤሎ ኦ ሊቅ ምንተ ገቢርየ እወርስ ሕይወተ ዘለዓለም ፡፡
መምህር ሆይ ምን ሥራ ሠርቼ የዘለዓለም ሕይወት እወርሳለሁ አለው ፡፡

፳፮ ወይቤሎ ውስተ ኦሪትከ ምንተ ጽሑፍ ፡፡
፳፮ በኦሪትህ የተጻፈው ምንድር ነው ፡፡
ወእፎ ታነብብ እንዴትስ ታነባለህ አለው ፡፡

፳፯ ወአውሥአ ወይቤሎ ዘዳ ፡ ፮ ፡ ፭ ፡፡
፳፯ እሱም እንዲህ ብሎ መለሰ ፡፡
አፍቅሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ በኵሉ ልብከ ፡፡
አምላክህ እግዚአብሔርን በፍጹም ልብህ ውደደው ፡፡
ወበኵሉ ነፍስከ ፡፡
በፍጹም ስውነትህ ፡፡
ወበኵሉ ኃይልከ ፡፡
በፍጹም ኃይልህም ፡፡
ወበኵሉ ሕሊናከ ፤
ባሳብህም ሁሉ ፡፡
ወአፍቅር ቢጸከ ከመ ነፍስከ ፡፡
ባልንጀራህን እንደራስህ ውደድ ያለውም ነው አለው

፳፰ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሠናየ ተሠጠውከ
፳፰ ጌታም መልካም መለስህ ፤
ከማሁ ግበር ወተሐዩ ፡፡
እንዲሁ አድርግ ትድንማለህ አለው ፡፡

፳፱ ወፈቀደ ከመ ያጽድቅ ርእሶ ወይመንን ቢጾ ወይቤሎ ለእግዚእ ኢየሱስ መኑ ውእቱ ቢጽየ ፡፡

፳፱ ራሱን ሊያከብር ባልንጀራውንም ሊያዋርድ ወዶ እንደኔ ያለ ማነው አለ ፡፡

በእንተ ተራኅርኆተ ሳምራዊ ወተሠጠዎ እግዚእ ኢየሱስ ፡፡

፴ ወይቤሎ አሐዱ ብእሲ እንዘ ይወርድ እምኢየሩሳሌም ለኢያሪኮ ፡፡
ወፈቀደ ከመ ያጽድቅ ርእሶ ወይመንን ቢጾ ብሎ ነበርና ፡፡

፴ ጌታም መለሰለት አንድ ሰው ከኢየሩሳሌም ወደ ኢያሪኮ ሊወርድ ፡፡
ረከብዎ ፈያት ፡፡
ወንበዴዎች አግኝተውት ፡፡

| | |
|---|---|
| ዘበጥዎ ፤ | ደበደቡት ፡፡ |
| ወፈቀዕዎ ፤ | ገምሰው ፡፡ |
| ወአቍሰልዎ ፤ | አቍስለው ፡፡ |
| ወሰለብዎ ፤ | ልብሱን ገፈው ፡፡ |
| ወገደፍዎ ወሐለፉ ፤ | ጥለውት ሄዱ ፡፡ |
| ወአልጸቀ ይሙት ፤ | ሊሞት ቀረበ ፡፡ |

፴፩ ወተዳደቀ አሐዱ ካህን እንዘ ይወርድ ይእተ ፍኖተ ፡፡

፴፩ በዚያን መንገድ ሲሄድ አንድ ካህን አገኘው ወርእዮ ተዓደወ ወኀለፈ ፡፡
አይቶም አልፎት ሄደ ፡፡

፴፪ ወከማሁ ሌዋዊኒ መጽአ ኀበ ውእቱ መካን ወረከቦ ከመ ቀዳማዊ ፡፡

፴፪ የሌዊ ወገን ሰውም እንዲሁ አገኘው ፡፡
ወርእዮሂ ተዓደወ ወኀለፈ ፡፡
አይቶም ዝም ብሎ ሄደ ፡፡ ወከማሁ ባለው ወከመ ገጽ የሚል አብነት ይገኛል ፡፡ ከመ ቀዳሚ ማለት ነው ፡፡

፴፫ ወረከቦ አሐዱ ሳምራዊ እንዘ የሐውር ይእተ ፍኖተ ፡፡
ሳምራዊም በዚያ መንገድ ሲሄድ አገኘው ፡፡
ወርእዮ ወምሕሮ ፡፡
አይቶም እዘነለት ፡፡

፴፬ ወቀርበ ኀቤሁ ወሦጠ ወይነ ወቅብዓ ውስተ ቍስሊሁ ፡፡

፴፬ ወደሱ ቀርቦ በቍስሉ ወይንና ዘይት አፈሰሰበት ፡፡ ሐተታ ዘይት ያለመልማል ወይን ያደርቃልና ፡፡

ወፀአኖ ዲበ አድጉ ወወሰዶ ኀበ ዓቃቤ ቤተ ነግድ።
በአህያው ላይ አስቀምጦ ወደ መንደረኛው ይዞት
ሄደ ።
ከመ ይፈውሶ ። ያድነው ዘንድ ።
ወአስተሐመመ በግብሩ ።
የሚያድንበትን አሰበ ፤

፴፭ ወበሳኒታ አውፅአ ክልኤተ ዲናረ ወወ
ሀቦ ለዓቃቤ ቤተ ነግድ

፴፭ በነጋውም ሁለት ድሪም አውጥቶ ለመ
ንደረኛው ሰጠው ።
ወይቤሎ ፈውሶ ሊተ በዝንቱ ፤
በዚህ አድንልኝ አለው ።
ወእመቦ ዘአስተዋፃዕከ ሎቱ ዘይበዝኅ እምዝ አፈ
ድየከ አነ እመ ግብአትየ ።
ከዚህም የሚበዛ ስለሱ ያወጣኸው ገንዘብ ቢኖር
በተመልስኩ ጊዜ እከፍልሃለሁ አለው ።

፴፮ መኑ እንከ እምእሉ ፫ቱ ዘይከውኖ ቢጸ
ለዘዘበጥዎ ፈያት ።

፴፯ ወንበዴዎች ለደበደቡት ለዚህ ከሦስቱ
ወዳጅ የሆነው ማነው አለው ።
ወይቤሎ ዘገብረ ምሕረተ ላዕሌሁ ።
ምሕረት ያደረገለት ሳምራዊ ነው አለው ።

፴፯ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑርኬ አንተኒ
ግበር ከማሁ ።

፴፯ ጌታም አንተም ሄደህ እንዲሁ አድርግ
አለው ።
ወተሐዩ ።
ትድን ዘንድ ድኅነት ታገኝ ዘንድ ። አንድም ወተ
ሠጥዎ ብለህ መልስ አዳምን ከልዕልና ወደ ትሕትና
ሲሄድ አግኝተውት አጋንንት አሰተው ልጅነቱን አስ
ወሰደውበት ሄዱ አንድም በአዳም የሁሉን መናገር
ነው ። ወአልጸቀ ይሙት በሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ
በርደተ መቃብር ርደተ ገሃነም ተፈረደበት ። ወተ
ዳደቆ ። መልከ ጼዴቅ በዚህ ዓለም አገኘው በጸ
ለየው ጸሎት ባቀረበው መሥዋዕት አላዳነውም ።
ወከማሁ አሮን በዚህ ዓለም አገኘው አላዳነውም
አንድም አሐዱ ካህን ሙሴ ፣ ሌዋዊ አሮን ።
አንድም አሐዱ ካህን። አሮን ሌዋዊ ከአሮን እስከ
ሐና እስከ ቀያፋ ያሉ ካህናት በጸለዩት ጸሎት
ባቀረቡት መሥዋዕት አለማግለዳቸውን መናገር
ነው ወረከቦ አሐዱ ሳምራዊ ጌታ በዚህ ዓለም አገ
ኘው ሳምራዊ ዐቃቤ ሀገር እንደሆነ ጌታም ዓቃቤ
ልቦና ነውና የሳምራዊ ትውልዱ ከሕዝብ ከአሕዛብ
እንደሆነ የጌታም ትውልዱ ከሕዝብ ከአሕዛብ
ነውና ። ወርእዮ ፣ በዓይነ ምሕረት አየው።ወምሕሮ
አዘነለት ። ወቀርበ ኀቤሁ ፣ ባሕርዩን ባሕርይ አደረ
ገለት በመስቀል ተሰቀለለት።ወሦጠ ወይነ ወቅብዓ ።
ልጅነትን ሥጋውን ደሙን ሰጠው።ወወሰዶ ከጣዖት
ከኃጢአት ፈልሶ የመጣውን ለሚያስተምሩ ለመ
ምህራን ሰጠው ፣ ከመ ይፈውሶ ፣ አስተምረው ያድ
ኑለት ዘንድ ፣ ወፀአኖ በአህያ ተቀመጠለት ተዋ
ረደለት ፣ ወአስተሐመመ የሚያድንበትን አሰበ
ለት ፣ ወበሳኒታ የዕርገት ሳኒታ ጰራቅሊጦስ ነው ፣
የጰራቅሊጦስ ብሉይና ሐዲስ አወጣጥቶ ከጣዖት
ከኃጢአት ፈልሶ የመጣውን ለሚያስተምሩ መም
ህራን ሰጠለት ፣ ወይቤሎ ፈውስ በዚህ መክራችሁ
አስተምራችሁ አድኑልኝ አላቸው ። ወእመቦ
ከዚህም ሌላ ድርሰት ደርሳችሁ ተግሳጽ ጽፋችሁ
ያስተማራችሁት ቢኖር በመጣሁ ጊዜ ዋጋችሁን
እሰጣችኋለሁ ፣ መኑ እንከ እምእሉ ፣ አጋንንት
ልጅነቱን ላስወሰዱበት ለአዳም ከሦስቱ በጐ ሥራ
የሠራለት ማነው አለው ፣ ወይቤ ዘገብረ ምሕረተ
ላዕሌሁ ፣ አንተ ነህ አለው ፣ ወይቤ ሑር አንተኒ
ግበር ከማሁ ፣ እንኪያስ አንተም እኔን አብነት አድ
ርገህ ሥራ ብትሠራ ፣ ወተሐዩ ። ትድናለህ ።

በእንተ ማርያ ወማርታ ።

፴፰ ወእምዝ ሐዊሮሙ ቦኡ አሐተ ሀገረ።
፴፰ ከዚህ በኋላ ሄደው ወደአንድ ሀገር ገቡ።
ወተቀበለቶ አሐቲ ብእሲት ውስተ ቤት እንተ ስማ
ማርታ ፣
ማርታ የምትባል ሴት በቤቷ ተቀበለችው ።

፴፱ ወስመ እኅታ ማርያ ።
፴፱ እኅቷ ማርያ ትባላለች ።
እንተ ነበረት ኀበ እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ከጌታ ዘንድ ስትማር ትውል ነበር ።
ወትሰምዕ ቃሎ ።
ወንጌልን ትሰማ ነበር ።

፵ ወማርታሰ ትሰርሕ በአስተዳልዎ ብዙኃ፤
፵ ማርታ ግን በብዙ ማዘጋጀት ብዙ ትደክም
ነበር ።
ወቆመት ወትቤሎ እግዚእየ ኢያጽሕቀከኑ ግብርየ
ዘተኃድገኒ እኅትየ ባሕቲትየ እንዘ አስተዳሉ ።
ቆማ እኅቴ ብቻየን የምትተወኝ ድካሜ አያሳዝን
ህምን ።
በላኬ ትርድአኒ ።
ትረዳኝ ዘንድ እዘዝልኝ አለችው ።

፵፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ማርታ ማርታ
ለምንት ትሠርሒ ብዙኃ ታስተዳልዊ ።

፵፩ ለዕብራውያን ደጊመ ቃል ልማዳቸው
ነው አብርሃም አብርሃም አልዓዛር አልዓዛር ስም
ዖን ስምዖን እንዲል ማርታ ማርታ ሆይ ታዘጋጂ
ዘንድ ስምን ብዙ ትደክሚያለሽ ።
ወኅዳጥ የአከል ። አንድ እንጀራ ይበቃል ።

ወደ እግዚአብሔር እመልክተሀ ሦስት ዓመት ሦስት ወር ሦስት ቀን ሦስት ሰዓት ዕድሜ አሰጠኝ ።
እስመ በጽሐኒ ማኅፈርየ ። ሞት ተፈርዶብኛልና ቢለው ። ሐተታ ማኅፈር አለው እግዚአብሔርስ ኢገብረ ሞተ አላ ረሚዓን ሰብእ ጸውዖም በቃሎሙ ወአርከ እምሰልዎ እንዲል እምሐቅል እሰ፣ ሞት የባሕርይ እንዳይደለ ለማጠየቅ ።
ወአልብየ ዘአሰብጦ ።
ሞትን የማስቀርበት ሃይማኖት ምግባር የለኝምና ቢለው ።
ወይሠጦ ዝኩ ዓርኩ እምውስጥ ።
ጌታም በመምህረ ንስሐ አድሮ ምሕረት ተከልክ ሏል ቢለው ። ወደቂቅኒ ።
መላእክትም እንዳያማልዱ ምሕረት ተከልክሏል ቢለው ። ንጽሐሙ ለሕፃናት በሥጋሆሙ ወነፍሶሙኒ ዘእንበለ ሕማም እንዲል ፣ በንጽሕና ይመስ ሏቸዋልና ሕፃናት አላቸው ።
እብለከሙ ። ለጊዜው ባያደርግለት ተላጽቆተ ሰኢል ያስደርግለታል ብዮ እነግራችኋለሁ።ሐተታ ሦስትም የተባሉ ፣ ጥምቀት ፣ ሥጋው ደሙ ። ንስሐ ናቸው ። ጥምቀት የአብ ፣ሥጋው ደሙ የወልድ ንስሐም የመንፈስ ቅዱስ ። ንስሐስ ድካም ያለ በት ነው ለመንፈስ ቅዱስ አይስማማውም ብሎ ንስሐ የወልድ ሥጋው ደሙ የመንፈስ ቅዱስ ፣ ኅብስቱ ተለውጦ ሥጋ መለኮት ፣ ወይኑ ተለውጦ ደመ መለኮት የሚሆን በግብረ መንፈስ ቅዱስ ነውና ።

፱ ወእነሂ አብለክሙ ሰአሉ ወይትወሀበክሙ ማቴ ፯፥፯ ማር ፲፩፥፳፬ ዮሐ ፲፮፥፳፫ ያዕ ፩፥፭ ።

፱ እኔም አላችኋለሁ ለምኑ ይሰጣችኋል ።
ጐድጕዱ ወይትርኃወክሙ ።
ደጅ ምቱ ይከፈትላችኋል ።
ኅሡ ወትረክቡ ።
እሹ ታገኙማላችሁ ።

፲ እስመ ኵሉ ዘሰአለ ይነሥእ ።

፲ የለመነ ሁሉ ያገኛል ።
ወዘሂ ኀሠሠ ይረክብ ።
የሻም ያገኛልና ።
ወለዘሂ ጐድጐደ ይትረኃዎ ።
ደጅ ለመታም ይከፈትለታል ።

፲፩ ወእመቦ እምውስቴትክሙ ዘሰአሎ ወልዱ ለአቡሁ ኅብስተ እብንኑ ይሁቦ ። ማቴ ፯፥፱ ።

፲፩ ከእናንተ ወገን ልጁ አባቱን ዳቦ ቢለም ነው ድንጊያ ይሰጠዋልን ።

፲፪ ወእመኒ ዓሣ ሰአሎ አርዌ ምድርኑ ይሁቦ ህየንተ ዓሣ ።

፲፪ ዓሣ ቢለምነው ስለ ዓሣው እባብ ይሰጠዋልን ።
ወእመኒ እንቁላሆ ሰአሎ አቅራብኑ ይሁቦ ህየን ቴሁ ።
እንቁላልስ ቢለምነው ጊንጥ ይሰጠዋልን ።

፲፫ ወሶበ አንትሙ እንዘ እኩያን አንትሙ ተአምሩ ሠናየ ሀብተ ውኂበ ለውሉድክሙ ።

፲፫ እናንተ ሰንኳ ክፋዎች ስትሆኑ ለልጆቻችሁ መልካም ስጦታ መስጠትን የምትወዱ ከሆነ እፎ ፈድፋደ አቡክሙ ዘበሰማያት ይሁብ ሠናየ ሀብተ መንፈስ ቅዱስ ለእለ ይስእልዎ ።
በሰማይ ያለ አባታችሁ ለሚለምኑት የመንፈስ ቅዱስን ሀብት እንዴት አብዝቶ ይሰጣቸው ።

በእንተ ጽሙም ጋኔን ዘአኅዞ ።

፲፬ ወሀሎ ሀየ ያወፅእ ጋኔነ በሐመ ወጽ ሙመ ። ማቴ፥፱፥፴፩ ።

፲፬ ድዳ ደንቆሮ ጋኔንም ያወጣ ነበር ።
ወሶቤሃ ዝኩ ጋኔን ነበበ ወሰምዓ ውእቱ ጽሙም ።
ወበሐም ጋኔኑ በወጣ ጊዜ ድዳ ደንቆሮ የነበረው ተናገረ ።
ወአንከርዎ ሰብእ ።
ሰዎችም አደነቁት ።

፲፭ ወቦ እምውስቴቶሙ እለ ይቤሉ በብዔል ዜቡል በመልአኮሙ ለአጋንንት ያወፅኦሙ ለአ ጋንንት ማቴ፥ ፱፥፴፬ ማር፥ ፫፥፳፪ ።

፲፭ ከሳቸው ወገን በአጋንንት አለቃ በብዔል ዜቡል አጋንንትን ያወጣል ያሉም አሉ ።

፲፯ ወአውሥአ ወይቤ እፎ ይክል ሰይጣን ሰሰይጣን አውፅኦቶ ።

፲፯ ሰይጣን ሰይጣንን ማውጣት እንደምን ይቻለዋል ብሎ መለሰላቸው ።

በእንተ መናፍስት እኩያን ።

ወቦ እለ ያሜክርዎ ። የሚፈትኑትም
ወየኃሥሡ ትእርምተ እምሰማይ ኀቤሁ ።
ከሰማይም ምልክት ያሳያቸው ዘንድ ይሹም ነበር ።

፲፯ ወውእቱ አእመሮሙ ዘይሄልዩ ።
፲፯ እሱ ግን አሳባቸውን ዐወቀባቸው ።
ወይቤሎሙ ኵላ መንግሥት እንተ ትትናፈቅ በበይናቲሃ ትማስን ።
እርስ በርሷ የምትለያይ መንግሥት ሁሉ ትጠፋለች ።
ወቤትኒ ላዕለ ቤት እመ ተናፈቀ ይወድቅ ውእቱ ቤት ።
ቤትም በቤት ላይ ይወድቃል ።

፲፰ ወእመሰ ሰይጣን ተናፈቀ በበይናቲሁ እፎ ይቀውም መንግሥቱ ።

፲፰ ሰይጣንስ እርሱ በርሱ ከተለያየ እንዴት ይጸናል ግዛቱ ።
እስመ ትብሉ በብዔል ዜቡል በመልአኮሙ ለአጋንንት ያወፅእሙ ለአጋንንት ።
በአጋንንት አለቃ በብዔል ዜቡል አጋንንትን ያወጣል ትላላችሁና ።

፲፱ ወእመሰ አነ በብዔል ዜቡል አወፅኦሙ ለአጋንንት ደቂቅክሙ በምንትኑ ያወጽእዎሙ ።

፲፱ እኔማ ሰይጣናትን በብዔል ዜቡል የማወጣ ከሆነ ልጆቻችሁ በምን ያወጧቸዋል ።
ወበእንተ ዝንቱ ይዛለፉክሙ ።
ስለዚህ እርሳቸው ይፈርዱባችኋል ።

፳ ወእመሰ አነ በአፅባዕተ እግዚአብሔር አወፅኦሙ ለአጋንንት ።

፳ እኔ ግን አጋንንትን በእግዚአብሔር ጣቶች ማለት በእግዚአብሔር ሥልጣን የማወጣቸው ከሆነ።
ዮጊኬ በጽሐት እንከሰ ኀቤክሙ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
እንግዲህ ገና የእግዚአብሔር መንግሥት ወደናንተ ደረሰች።ሐተታ ማቴዎስ በመንፈሰ እግዚአብሔር ይላል ሉቃስ በአፅባእተ እግዚአብሔር አለ እንደ ምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም የሁለት ቀን ትምህርት የልሳን መለያየት ። አንድም አጽባእትም መንፈስም ቢል አንድ ነው ሥልጣነ እግዚአብሔር ማለት ነው ታችኛው የአብ መካከለኛው የመንፈስ ቅዱስ ላይኛው የወልድ ምሳሌ ባዕድ ጽፍርን እንደ ተወሐደ ባዕድ ሥጋን ተዋሕዷልና ።

፳፩ ወአምጣነ የዓቅብ ኃያል ዓጸደ ርሱይ በንዋየ ሐቅል ይድኅን ኵሉ ጥሪቱ ።

፳፩ አርበኛ በጋሻ በጦር ተሰልፎ ቤቱን በሚጠብቅበት ጊዜ ገንዘቡ ሁሉ ደህና ይሆናል ።
ወእመሰ ይመጽእ ዘይሄይሎ ይመውኦ ወይሰልቦ ንዋየ ሐቅሉ ዘይትአመን ቦቱ ።

፳፪ ከርሱ የሚበረታ የመጣ እንደሆነ ግን እሸንፎ የሚታመንበትን ጋሻና ጦሩንይ ወስድበታል ።
ወይትካፈል በርበሮ ወምህርካሁ ።
ገንዘቡን ይካፈለዋል ።

፳፫ ዘኢሀሎ ምስሌየ ዕድውየ ውእቱ ።
፳፫ ከኔ ጋራ ያልሆነ እርሱ ባለጋራዬ ነው ።
ወዘኢይትጋባእ ምስሌየ ይዘርወኒ ።
ከኔም ጋራ አንድ የማይሆን እርሱ ይለየኛል ።
፳፬ ወሶበ ይወፅእ ጋኔን እኩይ የዓውድ በድወ ኀበ አልቦ ማይ ።

፳፬ ክፉ ሰይጣን ከሰው በወጣ ጊዜ ወኀ ወደ ሌለበት ምድረ በዳ ይዞራል ።
ወየኃሥሥ ምንባረ ወመካነ ኀበ የአርፍ ።
የሚያርፍበት ቦታ ይሻል ።
ወእምከመ ኢረከበ ይብል እገብእ ውስተ ቤትየ ኀበ ወፃእኩ እምኔሁ ።
ያላቶች እንደሆነ ግን ወደቀደመ ቦታዬ ወደ ወጣሁበት እመለሳለሁ ይላል ።

፳፭ ወመጺአ ይረክብ እንዘ ያስተራክብ ዕዱወ ወሥርግወ ወሥሉጠ ወምሩግ ።
፳፭ በመጣም ጊዜ ተጠርጎ አጊጦ ያገኘዋል።

፳፮ ወእምዝ የሐውር ወያመጽእ ምስሌሁ ሰብዐተ አጋንንተ ካልዓነ እለ የአክዩ እምኔሁ ።

፳፮ ከዚህም በኋላ ከርሱ የሚከፉ ሰባት አጋንንት ያመጣል ።
ወይበውኡ ወየኃድሩ ውስቴቱ ።
ገብተውም ያድሩበታል ።
ወይብእሶ ደኃሪቱ ለውእቱ ብእሲ እምቀዳሚቱ፤
የዚያም ሰው ከፊተኛው የኋለኛው የከፋ ይሆናል ።

ዘከመ ብፁዕ ውእቱ ዘይሰምዕ ቃለ እግዚአብሔር።

፳፯ ወእምዝ እንዘ ይትናገር ከልሐት አሐቲ ብእሲት በማዕከለ ሰብእ ።

፳፯ ከዚህ በኋላ ይህን ሲናገር አንዲት ሴት በሕዝቡ መካከል ጮኸች ።
ወትብሎ ብፅዕት ከርሥ እንተ ጾረተከ ።
አንተን የፀነሰች ማኀፀን የተመሰገነች ናት ።
ወአጥባት እለ ሐፀንከ ።
አንተንም ያጠቡ ጡቶች የተመሰገኑ ናቸው አለችው

፳፰ ወይቤላ ውእቱኒ ብፁዓንሰ እለ ይሰምዑ ቃለ እግዚአብሔር ወየዓቅቡ ።

፳፰ እርሱም የተመሰገኑስ የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው የሚጠብቁ ናቸው አላት ። ሐተታ ብፅዕት ከርሥ ብፁዓት አጥባት ማለቷ እመቤታችንን ማመስገኑዋ ነው ፣ እሱ ብፁዓንስ ማለቱ እመቤታችንን መንቀፉ ነውን ቢሉ እንዳይነቅፋትስ ይእቲ ተዓቢ እምኪሩቤል በንጽሕ ይላታል ብሎ ይህች ሴት በተንኮል መጥታለች ብፁዕ ብለው ብፅዕት ይለኛል ብላ አንች ብፅዕት አይደለሽም ። ብፁዓንስ ወንጌልን ሰምተው የሚጠብቁ ናቸው አላት ።

በእንተ ትእምርተ ዮናስ ።

፳፱ ወእንዘ ጉቡአን ብዙኃን ለብእ ወይትሀ ወኩ አኃዝ ይቤሎሙ ዛቲ ትውልድ እኪት ትእምርተ ተኃሥሥ ። ማቴ፡ ፲፪፡ ፴፱ ።

፴፪ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እለ ታበውኡ ዐሥራተ እደ፡ሁ ለአዛብ ወለጼናታም ወለኵሉ አሕማላት ወትትዔወርዎ ለፍትሐ እግዚአብሔር ወለፍቅረ እግዚአብሔር ።

፵፪ የእግዚአብሔርን ፍቅርና ፍርድ ቸል ብላችሁ የጤናዳምንና የንስላልን የሚለቀመውንም ሁሉ ካሥር አንድ የምታወጡ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ወዮላችሁ ።
ወዘንተሰ ርቱዕ ትግበሩ ።
ይህንም ልታደርጉ ይገባል ።
ወዝከተሰ ኢትኅድጉ ።
ያንም አትተው ።

፵፫ አሌለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን መደ ልዋን ። ማቴ. ፳፫ ፤ ፮ ማር ፤ ፲፪፣ ፴፱ ሉቃ . ፳ ፵፮ ።

፵፫ ግብዞች ጸሐፍት ፈሪሳውያን ወዮላችሁ ፤
እስመ ታፈቅሩ ነቢረ ፍጽም በውስተ አዕዋዳት ።
በሸንጎ በላይ መቀመጥ ትወዳላችሁና ።
ወተአምኆ በውስተ ምሥያጥ ወርእሰ ምርፋቃት በውስተ ምሳሐት።
በምሳ በላይ መቀመጥን በገበያ እጅ ሊነሷችሁ ።

፵፬ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ፈሪሳውያን መደ ልዋን ።

፵፬ ግብዞች ጸሐፍት ፈሪሳውያን ወዮላችሁ።
እስመ አንትሙ ከመ መቃብር ዘኢይትዓወቅ ዘያንሶሱ ሰብእ ላዕሌሁ ወኢያአምሮ ።
የሚመላለስበት ሰው እንዲያውቀው እንደተሰወረ መቃብር ናችው ።

፵፭ ወአውሥአ አሐዱ እምጸሐፍተ ሀገር ።
፵፭ ካገር ጸሐፎችም አንዱ መለሰ ።
ወይቤሎ ሊቅ ዘንተ እንዘ ትብል ከያነ ትጼዕል ።
መምህር ሆይ እንዲህ ማለትህ እኛን መንቀፍ ነው አለው ።

፵፮ ወይቤሎ ለከሙሂ ወለጸሐፍተ ሀገር አሌ ለክሙ ። ማቴ ፳፫፣፬ ።

፵፮ ለናንተም ለጸፎችም ወዮላችሁ አለው ።
እስመ ታጸውርዎ ለሰብእ ጾረ ክቡደ ።
ሰውን ጽኑ ሸክም ታሸከሙታላችሁና ።
ወለሊክሙሰ ኢትለክፍዎ ወኢትገሥሥዎ በአሐቲ አፅባዕትክሙ ጥቀ ለውእቱ ጾር ።
እናንተ ግን ያን ሸክም ባንድ ጣታችሁ ስንኳ አትነኩትም ።

፵፯ አሌ ለክሙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እስመ ተሐንጹ መቃብሪሆሙ ለነቢያት እለ አበዊክሙ ቀተልዎሙ ።

፵፯ አባቶቻችሁ የገደሏቸውን የነቢያት መቃብር ታንጻላችሁና ወዮላችሁ ።

፵፰ አደመክሙኑ ምግባሮሙ ለአበዊክሙ ፤
፵፰ ያባቶቻችሁ ሥራ ደስ ይላችኋልን ።
ወስሊክሙ ሰማዕቶሙ ።
እናንተም ምስክሮች ናችሁ ።
እስመ ዘአሙንቱ ቀተሉ ወአንትሙ ተሐንጹ መቃብሪሆሙ ።
እርሳቸው የገደሏቸውን እናንተ መቃብራቸውን ትሠራላችሁና ።

፵፱ ወበእንተ ዝንቱ ትቤ ጥበቢሁ ለእግዚአብሔር ናሁ እነ እፌኑ ኀቤሆሙ ነቢያተ ወሐርያተ ።

፵፱ ስለዚህ የእግዚአብሔር ጥበብ ወልድ ነቢያትን ሐዋርያትን ወደርሳቸው እልካለሁ አለች ።
ወይቀትሉ እምኔሆሙ ከርሳቸውም ይገለላሉ ።
ወይሰድዱ ።
ካገርም አስወጥተው ይሰዷቸዋል አለች ።

፶ ከመ ይትበቀሎሙ በእንተ ደመ ኵሉ ነቢያት ዘተከዕወ እምፍጥረተ ዓለም እስከ ዛቲ ትውልድ

፶ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ እስከዚች ትውልድ ድረስ በፈሰሰ በነቢያት ደም ሁሉ ይበቀላቸው ዘንድ ።

፶፩ እምደመ አቤል ጻድቅ እስከ ደመ ዘካርያስ ዘቀተልዎ በማእከለ ቤተ መቅደስ ወምሥዋዕ ለእግዚአብሔር ።

፶፩ ከአቤል ደም ጀምሮ ከቤተ መቅደስና በመሠዊያው መካከል እስከ ገደሉት እስከ ዘካርያስ ደም ድረስ ።
እወ እብለክሙ ይትኃሠሥዋ ወይትቤቀልዋ ለዛቲ ትውልድ ።
ከዚች ትውልድ እንዲፈላለጉ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፶፪ አሌ ለክሙ ጸሐፍተ ሀገር ወፈሪሳውያን ።
፶፪ ያገር ጸሐፊዎችና ፈሪሳውያን ወዮላችሁ።
እስመ ነሣእክሙ መራኁተ ጽድቅ ወአእምሮ ወተኃብኡ ።
የውቀትና የውነት መክፈቻ ወስዳችሁ ትሰውራላችሁና ማለት የተነገረውን ትንቢትና የተቈጠረውን ሱባኤ ዐውቃችሁ ሰውራችኋልና ።
ለሊክሙኒ ኢትበውኡ ።
እናንተም አትገቡ ።
ወለእለሂ ይበውኡ ትከልእዎሙ በዊአ ።
የሚገቡትንም እንዳይገቡ ትከለክሏቸዋላችሁ ።

፶፫ ወእንዘ ይነግሮሙ ዘንተ በቅድመ ኵሉ ሕዝብ አኃዙ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ያመንዝዝዎ በእከይ ።

፶፫ በሕዝቡ ሁሉ ፊት ይህን ሲነግራቸው ጸሐ
ፍት ፈሪሳውያን አጽንተው ይጣሉት ጀመር ።
ወይትቄየምዎ ።
ቂም ያዙበት ።

፶፬ ወይንዕውዎ ።
፶፬ በነገር አደኑት ።
ወያስሕትዎ በቃለ አፉሁ ።
እናግረን እናስተዋለን አሉ ።

በእንተ ብኑእ ዘፈሪሳውያን

ምዕራፍ ፲፪ ።

፩ ወተጋብኡ ኅቤሁ አእላፍ ሰብእ ማቴ፡፲፯፡፯
ማር፡ ፰፡ ፲፭ ።

፩ ብዙ ሰዎች ወደሱ ተሰበሰቡ ።
እስከ ይትካየዱ በበይናቲሆሙ ።
እስኪጠቃጠቁ ማለት አንዱ አንዱን እስኪ ጠቀ
ጥቀው ድረስ ።
ወአኃዘ ይበሎሙ ለአርዳኢሁ ቅድሙ ወተዓ
ቀቡ እምነ ብሑእሙ ለፈሪሳውያን ።
ለደቀ መዛሙርቱ አስቀድሞ ከፈሪሳውያን እርሾ
ተጠበቁ ይላቸው ጀመረ ።
ዘውእቱ አድልዎ ።
እርሱም ግብዝነት ።

፪ እስመ አልቦ ክዱን ዘኢይትከሠት ።
፪ የማይገለጥ የተሸሸገ የለምና ።
ወአልቦ ኅቡእ ዘኢያስተርኢ ።
የማይታይ የተሰወረም የለም ።

፫ ወዘተናገሩ በጽልመት ይትናገርዎ በብርሃን
ወይሰማዕ ።

፫ በጨለማ የተናገሩትን በብርሃን ይናገሩታል
ይሰማል ።
ወዘኒ አልኆሰሱ በእዝን ይሰብክዎ በአጽራሕ ወበአ
ንሕስት ።
በጆሮ የነገርዋቸውን በሰገነት ያስተምሩታል ።

፬ እብለክሙ ለክሙ ለአእርክትየ ኢትፍ
ርሕዎሙ ለእለ ይቀትሉክሙ ሥጋክሙ ወነፍ
ስትክሙ

፬ ለናንተ ለወዳጆቼ ሰውነታችሁን የሚገ
ሏችሁን አትፍሩ እላችኋለሁ ።
ወእምዝ አልቦ ፈድፋደ ዘይክሉ ገቢረ ።
ከዚህ በኋላ ከዚህ የበለጠ የሚበልጥ የሚሠሩት
የለምና ።

፭ ወባሕቱ አርእየክሙ ዘትፈርሁ ።
፭ የምትፈሩትንስ አሳያችኋለሁ ።

ፍርህዎሰ ለዘእምድኅረ ቀተለ ብውህ ሎቱ ከመ
ይደይ ነፍሰኒ ወሥጋኒ ውስተ ገሃነም ።
መፍራትስ ከገደለ በኋላ ነፍስንና ሥጋን
ወደ ገሃነም ያገባ ዘንድ ሥልጣን ያለውን እርሱን
ፍሩት እንጂ ።
እወ እብለክሙ ኪያሁ ፍርሁ ።
እሱን ፍሩት ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፮ አኮኑ ኃምስ አዕዋፍ ይሰየጣ በክልኤ
ጸሪቀ አሶርዮን ።

፮ አምስቱ ዎፎች በሁለት ናስ ይሸጡ የለምን።
ወአሐቲ እምኔሆን ኢትትረሳእ በቅድመ እግዚ
አብሔር ።
ከርሳቸው አንዲቱ በእግዚአብሔር ፊት አትረሳም።
ሐተታ ማቴዎስ ሁለት ይላል ሉቃስ አምስት
አለ አይጣላም ቢሉ አይጣላም ማቴዎስ የውዱን
ሉቃስ የረኪሱን ተናገሩ ። ሲወደድ አንድ ሳንድ
ሲረክስ ባንድ ሁለት ባንድ ሦስት ይገዛልና ።
አምስቱ አዕዋፍ ፡ ነቢያት ካህናት ደቂቀ እስራኤል
ነገሥት ጻድቃን ሊቃውንት እለ ፈጸሙ ሕግ ናቸው።

፯ ወለክሙኒ ሥእርተ ርእስክሙኒ ኍሉ
ኍሉቅ ውእቱ ።

፯ የእናንተስ የራስ ጸጉራችሁ ስንኳ የተ
ቈጠረ ነው ።
ኢትፍርሁ እንከ ።
እንግዲህ አትፍሩ ።
እስመ እምብዙኅ አዕዋፍ ትኄይሱ አንትሙ ።
ከብዙ ዎፎች እናንተ ትሻላላችሁና ።

፰ እብለክሙ ኵሉ ዘየአምን ብየ በቅድመ
ዕጓለ እመሕያው አነኒ አአምኖ በቅድመ መላእክተ
እግዚአብሔር ። ማቴ ፫ ፡ ፴፪ ማር ፰ ፡ ፴፰ ።

፰ በሰው ፊት ያመነብኝን ሁሉ በእግዚአብሔር
መላእክቶች ፊት አምነዋለሁ ።

፱ ወለዘሰ ክህደኒ በቅድመ ሰብእ አነኒ እክ
ህዶ በቅድመ መላእክተ እግዚአብሔር ፪ ጢሞ ·
፪፡ ፲፪ ።

፱ በሰው ፊት የካደኝን እኔም በእግዚአብሔር
መላእክቶች ፊት እክደዋለሁ ።

፲ ወኵሉ ዘነበበ ቃለ ጽርፈት ላዕለ ወልደ
ዕጓለ እመሕያው ይትኃደግ ሎቱ ። ማቴ ፲፪፡፴፩፡
ማር ፫ ፡ ፳፰ ።

፲ በሰው ልጅ ላይ የስድብ ነገር የሚናገር
ሁሉ ኃጢአቱ ይሰረይለታል።
ወዘሰ ነበበ ቃለ ጽርፈት ላዕለ መንፈስ ቅዱስ
ኢይትኃደግ ሎቱ

በመንፈስ ቅዱስ ላይ የስድብ ነገር የሚናገር ግን ኃጢአቱ አይሰረይለትም ።
ኢበዝ ዓለም ።
በዚህም ዓለም ።
ወኢበዘይመጽእ ዓለም ።
በሚመጣውም ዓለም ሁኖ ።

፲፩ ወሶበ ይወስዱክሙ አዕዋዳተ ።
፲፩ ወደዐደባባይ በወሰዷችሁም ጊዜ ።
ውኅበሂ መላእክት ።
ወዳለቆችም ።
ወነገሥት ወመኳንንት ።
ወደ መኳንንትና ወደ ነገሥታት በወሰዷችሁ ጊዜ።
ኢትሐልዩ ዘከመ ትብሉ ወዘከመ ትትናገሩ ።
የምትናገሩትን የምትመልሱትን አታስቡ ።

፲፪ እስመ መንፈስ አቡክሙ ውእቱ ይትናገር ላዕሌክሙ ሶቤሃ ።

፲፪ ያን ጊዜ መንፈስ ቅዱስ በናንተ አድሮ ይናገራል ።

በእንተ ትዝኅርት ወበእንተ እኩይ ባዕል ።

፲፫ ወይቤሎ አሐዱ እምሕዝብ ሊቅ በሎ ለእኁየ ይከፍለኒ ርስትየ ።

፲፫ ከሕዝቡ አንዱ መምህር ሆይ ርስቴን እን ዲያካፍለኝ ወንድሜን እዘዝልኝ አለው ።

፲፬ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንተ ብእሲ መኑ ሤመኒ ከፋሌ ወመኰንነ ላዕሌክሙ ።

፲፬ አንተ ሰው በናንተ ላይ ገዢ ዳኛ አድርጎ ማን ሾመኝ አለው ። ሐተታ አእምር ከመ ልዑል ይኴንን መንግሥተ ደቂቀ ዕጓለ እመሕያው ወለዘ ፈቀደ ይሁብ ይል የለም ቢሉ አልመጣሁ ብትም ሲል እንዲህ አለ ። አንድም ይህ ሰው በተ ንኮል ተነሥቷል እንዲህ ያልኩት እንደሆነ እሱማ እኔን ተከትሎ ይሄዳል ገንዘቡ ላንተ ይሁን ይለኛል ብሎ በተንኮል መጥቷልና የሕሊናውን ዐውቆበት እንዲህ አለ ።

፲፭ ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ዑቁ ወተዓቀቡ እምነ ኵሉ ትዕግልት ።

፲፭ ይህ ሰው እንዲህ ማለቱ ገንዘብ ወዶ ወን ድሙን ጠልቶ እንጂ ነው ከፍቅረ ንዋይ ተከልከሉ አላቸው ።
እስመ አኮ በአብዝኖ ንዋይ ዘየሐዩ ሰብእ ።
ሰው የሚድን በገንዘብ ብዛት አይደለምና ።

፲፮ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ አሐዱ ብእሲ ባዕል ዘሠምረ ሎቱ ተግባሩ ።

፲፮ ቢያሳርስ ቢያስነግድ የበጀለት ወደለዎ ብሔር ።
አገር የተቀበለው አንድ ባለጠጋ ሰው ነበር ብሎ መስሎ ነገራቸው ።
ወሀለየ በልቡ በልቡ አሰበ

፲፯ ምንተ እሬሲ ዘአልብየ ኀበ እዘግብ እክልየ ወበረከትየ ።

፲፯ አዲሱን እህሌን የከረመውን የምሰበስ ብበት ጎታ የለኝ ምን አደርጋለሁ አለ ።

፲፰ ወይቤ ከመዝ እገብር ።
፲፰ እንዲህ አደርጋለሁ አለ ።
እነሥት ዘትካት መዛግብትየ ።
የቀደመውን ጎተራዬን አፍርሼ ።
ወአሐንጽ ካልዓ ዘየዓቢ ።
ሌላ የበለጠ እሠራለሁ ።
ወእዘግብ ህየ እክልየ ወበረከትየ ።
የከረመውንም የዘንድሮውንም እሰበስባለሁ

፲፱ ወእብላ ለነፍስየ እ ነፍስየ ብኪ ብዙኅ በረከት ዘዘገብኩ ለኪ ዘየዓክለኪ ለብዙኅ ዓመታት።
ሲራ ፲፩ ፤ ፲፱ ።

፲፱ ሰውነቴን ለብዙ ዘመን የሚበቃሽ የሰበ ሰብኩልሽ ብዙ ገንዘብ አለሽ ።
አዕርፊ እንከ ብልዒ ወስትዪ ወተፈሥሒ ።
እንግዲህ ወዲህ በልተሽ ጠጥተሽ ደስ ይበልሽ እላታለሁ ብሎ አሰበ ።

፳ ወይቤሎ እግዚአብሔር እ አብድ በዛቲ ሌሊት ይነሥእዋ ለነፍስከ እምኔከ ።

፳ እግዚአብሔርም አለው እንተ ሰነፍ በዚች ሌሊት ነፍስህን ከሥጋህ ይለዩዋታል ካንት ሊወ ስዷት ።
ለመኑ እንከ ይከውን ዝንቱ ዘአስተዳለውከ ።
ይህ ያሰናዳኸው ለማን ይሆናል አለው ።

፳፩ ከማሁኬ ዘይዘግብ ሎቱ መዝገበ ዘኢኮነ እምእግዚአብሔር ብዕሉ ።

፳፩ በእግዚአብሔር ፈቃድ ያልሆነ ገንዘብ እሰበስባለሁ የሚል ሰው ሁሉ እንደዚህ ሰው ነው አንድም ዘኢኮነ ብዕሉ እምእግዚአብሔር ይላል ፣ ብዕሉ በእግዚአብሔር ፈቃድ ያይደለ ሰው ሁሉ እንደዚህ ሰው ነው ።
ሐተታ ፤ በእግዚአብሔር ፈቃድ ያይደለ ምን አለ ቢሉ ሰጥቶለት በልቶለት የበረከተ በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው ። ሳይበላለት ሳይጠጣለት ሳይለብስለት ጦሙን እየዋለ ጥሬ እየበላ ለሰው ሳይሰጥለት የበ ረከተ እንደሆነ ግን በእግዚአብሔር ፈቃድ አይ ባልም በምሳው ከበረ ይባላል እንጂ ። አንድም

ወመሰለ ሎሙ ብሰሀ መልስ ፡ ልጅነት የተሰጠው ገነት የተቀበለችው አዳም ነበር ።

ወነሰየ ፡ የባሕርይ አምላክነት የለኝ ምን አደርጋለሁ ምን ለአድርግ አለ ። ወይቤ ከመዝ እገብር ። ይህን የጸጋ አምላክነትን ትቼ የባሕርይ አምላክነትን ገንዘብ አደርጋለሁ ። ወእብላ ። ሰውነቴን ገንዘብ ያደረኩልሽ የባሕርይ አምላክነት አለልሽ ደስ ይበልሽ እላታለሁ አለ ።

ወይቤሎ እግዚአብሔር አንተ ሰነፍ ሰው በዚች ሌሊት ነፍስህን ከሥጋህ ይለዩዋታል ገንዘብ ያደረግኸው የባሕርይ አምላክነት ለማን ይሆናል አለው። ወአመ በላዕክሙ እምውእቱ ዕፀ ሞተ ትመውቱ ያለው ነገር ሊፈጸም ሽህ ዘመን ሊመላው ሰባ ዘመን ሲቀረው ሙቷልና ፡ ወእሕጸረ ሰብዓ ከራማተ እንዲል መላ ዘመኑን ዘጠኝ መቶ ሠላሳ ነው ፡ በእግዚአብሔር ዘንድ እንዱ ቀን አልተፈፈጸመም ። ከማሁኬ በእግዚአብሔር ፈቃድ ያይደለ ከብርን አከብራለሁ የሚል ሰው ሁሉ እንደ አዳም ነው ።

ዘኢኮነ ብዕሉ ከብሩ በእግዚአብሔር ፈቃድ ያይደለ ሰው ሁሉ እንደ አዳም ነው ።
ወሶበ ተናገረ ዘንተ ከልሐ ወይቤ ዘቦ እዕዛን ሰማዕያን ለይስማዕ ።
ይህን በተናገረ ጊዜ ዦሮ ያለው ይስማ አለ ።

ዘከመ ኢይደልዎ ለክርስቲያን ተሀዕቦት በከንቱ ።

፳፪ ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ በእንተ ዝንቱ እብለክሙ ኢትሃልዩ ለሥጋክሙ ዘትለብሱ ወለ ነስፍክሙ ዘትሰትዩ ። መዝ ፡ ፶፬ ፡ ፳፫ ማቴ ፡ ፮ ፡ ፳፭ ፩ ፡ ጴጥ ፡ ፭ ፡ ፯ ።

፳፪ ለደቀ መዛሙርቱ ስለዚህ ለሥጋችሁ የምትለብሱት ለነፍሳችሁ የምትበሉትን አታስቡ እላችኋለሁ አላቸው ።

፳፫ እስመ ነፍስ ተዓፅብ እምሲሲት ።

፳፫ ከመብል ነፍስ ትቸገራለችና ፤
ወሥጋ የዓፅብ እምዓራዝ ።
ሥጋም ከልብስ ይቸገራልና ።

፳፬ ርእዩ ዕጕለ ቋዓት ዘኢይዘርዑ ወኢየዓርሩ ወአልቦሙ መዛግብት ።

፳፬ የማይዘሩ የማያጭዱ ማከማቻ የሌላቸው የቁሮች ጫጩቶችን ተመልከቱ ።
ወኢውኅሮያት ።
ጎተራም የሌላቸውን ።
ወእግዚአብሔር ይሴስዮሙ ።
እግዚአብሔር ግን ይመግባቸዋል ። ሐተታ ማቴዎስ አዕዋፈ ሰማይ ይላል ሉቃስ ዕጕለ ቋዓት አለ እን ደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም የሁለት ቀን ትምርህት የልሳን መለያየት ነው ። አንድም አዕዋፍ የወል ስማቸው ። ቋዓት የጕልማ ስማቸው ነው ። ማቴዎስ የወል ስማቸውን ሉቃስ የጉልማ ስማቸውን ተናገረ ። ዕጕል ማለቱ ግን በሚጸናባቸው ሲናገር ሲወለዱ ፍህም መስለው ይወለዳሉ እናት አባታቸው ደንግጠው ጥለዋቸው ይሄዳሉ ። ከአካላቸው ርጥበት አይታጣምና ተሐዋስያን ርጥበቱን ሲሹ ይቀርባሉ፡ እስከ አርባ ቀን ድረስ በትንፋሻቸው እየሳቡ ሲመገቡ ይሰነብታሉ ። ከአርባ ቀን በኋላ ጠጉር ያበቅላሉ በመልክ ይመስሏቸዋል ተመልሰው ይረዷቸዋልና በጸናው ተናገረ ።
እፎ እንከ ፈድፈደ ትኄይሱ አንትሙ እምአዕዋፍ።
እናንተማ ከወፎች እንደምን ትበልጡ ።

፳፭ መኑ እምኔክሙ በሐልዮ ዘይክል ወስከ አሐደ እመተ በዲበ ቆሙ ።

፳፭ ከናንተ ወገን አስቦ በቁመቱ ላይ አንድ ክንድ ሙሉ ቁመት ማከል የሚቻለው ማነው ፡

፳፮ ወሶበ ኢትክሉ ዘንተ ዘይቀልል ለምንት ትሔልዩ ዘየአፅብ ።

፳፮ ይህን ትንሹን ማድረግ የማይቻላችሁ ከሆነ ለምን በሌላው ታስባላችሁ ።

፳፯ ናሁ ጽጌያተ ገዳም ርእዩ ዘከመ ይልሕቁ ኢይጸምዉ ወኢይፈትሉ ።

፳፯ ሳይደክሙ ሳይፈትሉ እንዴት እንዲያድጉ ጽጌያትን እዩ ።
እብለክሙ ከመ ሰሎሞን ጥቀ ኢለብሰ በኵሉ መዋዕለ ከብሩ ከመ አሐዱ እምኔሆሙ ።
ሰሎሞን ስንኳ ከብሮበት ባለ ዘመን ሁሉ ካበቦች እንዳንዱ አሰበሰም ብየ እነግራችኋለሁ ።

፳፰ ወለእመ ከነ ሥርወ ጽጌ ዘዮም ሀሎ ወጌሰመ ይትወደይ ውስተ እሳት ዘከማሁ ይሬሲ እግዚአብሔር ።

፳፰ ነገ በእሳት የሚጣለውን ዛሬ በልምላሜ ያለውን ቅጠል እግዚአብሔር እንዲህ የሚያደርገው ከሆነ ።

፳፱ እፎ እንከ ፈድፋደ ለክሙ ሕጹጻነ ሃይማኖት ።

፳፱ እናንተ ሃይማኖት ያነሣችሁ ለእናንተ እንደ ምን ያደርግላችሁ ።
አንትሙሂ ኢትኅሥሡ ዘትበልዑ ወዘትሰትዩ ።
እናንተም የምትበሉትን የምትጠጡትን በሚያስጨንቅ አሳብ አትሹ ።
ወኢትትኄለሉ ።
ክንዱ ወዳንዱ አትበሉ ።

መልደ ዕጓለ እመሕያው፡ ክርስቶስ ባልጠረጠራችሁት ጊዜ ይመጣልና ።

፵፩ ወይቤሎ ጴጥሮስ እግዚኦ ለነ ትሜስል ዘንተ ምሳሌ ።

፵፩ ጴጥሮስም አቤቱ ይህን የምትመስል ለኛ ነውን ።

ወሚመ ለኵሉ ።

ወይስ ለሁሉ ነው አለው ።

፵፪ ወይቤሎ እግዚእ ።

፵፪ ጌታም መለሰ ።

መኑ እንጋ ውእቱ መጋቢ ኄር ወምእመን መጠቢብ ዘይሰይሞ እግዚኡ ላዕለ ኵሉ ቤቱ ።

ጌታ በባሮቹ ላይ የሚሾመው የታመነ ብልህ አስተዋይ ሹም ማነው ።

ከመ የሀቦሙ ሲሳዮሙ በበጊዜሁ ።

ምግባቸውን በየጊዜው ይሰጣቸው ዘንድ ።

፵፫ ብፁዕ ውእቱ ገብር ዘመጺኦ እግዚኡ ይረክቦ እንዘ ከመዝ ይገብር ።

፵፫ ጌታው በመጣ ጊዜ እንዲህ ሲያደርግ የሚያገኘው የተመሰገነ ነው ።

፵፬ አማን እብለክሙ ከመ ላዕለ ኵሉ ንዋዩ ያሜግቦ ።

፵፬ በከብቱ ሁሉ ላይ ይሾመዋል ብዩ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፵፭ ወእመሰ ይቤ ውእቱ ገብር እኩይ በልቡ ይጐነዲ አቲወ እግዚእየ ።

፵፭ ያ ክፉ ባርያ ግን በልቡ ጌታዬ የሚመለስበት ገና ነው ቢል ።

ወይእኅዝ ይዝብጥ ወያመንዝዝ ደቀ ወአዋልደ ዘቤተ እግዚኡ ይበልዕ ወይሰቲ ምስለ ሰካርያን ወይስክር ከሰካሮች ጋራ እየበላ እየጠጣ እየሰከረ የጌታውን ወንዶች ባሮች ሴቶች ባሮች ሊመታ ይጀምራል ።

፵፮ ወይመጽእ እግዚኡ ለውእቱ ገብር በዕለት ኢይሔውዞ ወበጊዜ ኢያእመረ ።

፵፮ የዚያ ያባርያ ጌታው ባላወቀው ሰዓት ባልጠረጠረው ዕለት መጥቶ ።

ወይመትሮ እማዕከሉ ።

ይለየዋል ይሸረዋል ።

ወያገብእ ወይሬሲ መክፈልቶ ምስለ አለ ኢየአምኑ ፋንታውንም ከማያምኑ ጋራ ያደርግበታል ።

፵፯ ወለአገብርሰ ዘየአምሮ ፈቃደ እግዚኡ ወኢይገብሮ ።

ጌታውን የሚያውቀውን ፈቃዱን የማያደርግ ግን

ወኢያስተዳሉ ዘከመ ይፈቅድ ።

እንደ ፈቃዱም የማያደርግ ባርያ ግን ብዙን መቅሠፍቱ ።

ፍዳው ብዙ ነው ።

፵፰ ወዘሰ ኢየአምር ለእመ አገብረ ኀዳጥ መቅሠፍቱ ።

፵፰ የጌታውን ፈቃድ የማያውቅ ግን ባይሠራ ፅዳው ጥቂት ነው ።

እስመ ለኵሉ ዘብዙኀ ወሀብዎ ብዙኀ ይትኀሠሥዎ ።

ብዙ ከሰጡት ሁሉ ብዙ ይሹበታልና ።

ወለዘሂ ኀዳጠ አማኀፀንዎ ኀዳጠ ይትኀሠሥዎ ።

ጥቂት ያስጠበቁትንም ጥቂት ይመረምሩታል ።

፵፱ እሳተ አምጻእኩ ላብሔር ።

፵፱ በሀገር እሳትን አመጣሁ ማለት ለሰው ሁሉ ሃይማኖትን አስተምራለሁ ።

ወምንተ እፈቅድ ዘእንበለ እንድዶታ ።

እሷን ከማንደድ በቀር ሌላ ምን እሻለሁ ሃይማኖት ልትነገር እሻለሁ እንጂ ሌላ ምን እሻለሁ ።

፶ ወባሕቱ ብየ ጥምቀት ዘእጠመቅ ።

፶ ነገር ግን የምጠመቃት ጥምቀት አለችኝ ማለት የምሞታት ሞት አለችኝ ።

ወጥቀ እትኤገሥ እስከ እፈጽማ ።

እስከሞት ድረስ ሃይማኖትን ከመግለጥ እከለከላለሁ፡ ሐተታ ። ጌታ ካልሞተ ካሣ አይፈጸምም ካሣም ካልተፈጸመ ልጅነት አይሰጥም ልጅነትም ካልተሰጠ ሃይማኖት አይገለጥምና ምነው ሃይማኖት አይቀድምም ልጅነት አይከተልም ቢሉ ወአልቦ ዘይክል ብሂለ እግዚእ ኢየሱስ ዘእንበለ ዘመንፈስ ቅዱስ ካዕበሁ እንዲል መጽናናቱን መተላቱን መገለጹን ሲያይ እንዲህ አለ እንጂ እውነት ነው ሃይማኖት ይቀድማል ልጅነት ይከተላል ። አንድም እሳተ አምጻእኩ ብለህ መልስ ለሰው ልጅነትን አመጣሁ ። ወምንተ እፈቅድ ልጅነት ልትሰጥ እወዳለሁ እንጂ ሌላ ምን እሻለሁ ወባሕቱ ነገር ግን የምሞተው ሞት አለኝ ወጥቀ እትኤገሥ እስከ ሞት ድረስ ልጅነትን ከመስጠት እከለከላለሁ አሁን የተመቸ ጌታ ካልሞተ ካሣ አይፈጸምም ካሣም ካልተፈጸመ ልጅነት አይሰጥምና ።

፶፩ ወይቤሎሙ ለሕዝብ ይመስለክሙኑ ሰላመ ዘአምጻእኩ ለምድር ።

፶፩ ለሕዝቡ ለምድር በዓለም ያመጣሁ ይመስላችኋልን አላቸው ።

፶፪ አልቦ እብለክሙ ።

፶፪ አይደለም እላችኋለሁ

ዘእንበለ መጥባሕት ወፍልጠት መለያየትን ሰይፍን ነው እንጂ ለእምይእዜሰ ለእመ ሀለዉ ውስተ ፩ ቤት ይትፈለጡ ሐመስቱ እምኔሆሙ ።

ከዛሬ ጀምሮ አምስት ሰዎች ባንድ ቤት ቢኖሩ ሦስቱ ከሁለቱ ይለያሉ ።
ወይትፈለጡ ክልኤቱ እምሠለስቱ ።
ሁለቱም ከሦስቱ ይለያሉ ።
ወይትፈለጥ አሐዱ እምክልኦሙ ።
አንዱም ካንዱ ይለያል ።

፶፫ ወይትፈለጥ አብ እምወልዱ ።
፶፫ አባት ከልጁ ይለያል ።
ወወልድኒ እምአቡሁ
ልጅም ካባቱ ይለያል ።
ወትትፈለጥ እም እምወለታ ።
እናትም ከልጅዋ ትለያለች ።
ወወለትኒ እምእማ ።
ሴት ልጅም ከናትዋ ።
ወሐማትኒ እመርዓታ ።
አማትም ከምራቷ ።
ወመርዓትኒ እምሐማታ ።
ምራትም ካማቷ ። ሐተታ ኃምስቱ የተባሉ ሐሳዌ ኤልያስ ሐሳዌ ኤልሳዕ ሐሳዌ አብድዩ ሄኖክ ኤልያስ ናቸው ሦስቱ ከሁለቱ ይለያያሉ አለ በክህደት ሁለቱ ከሦስት ይለያያሉ አለ በሞት አንድም ኃምስቱ የተባሉ አራቱ ባሕርያት ሥጋ አምስተኛ ባሕርየ ነፍስ ናቸው ሦስቱ ከሁለቱ ይለያሉ አለ ነፍስ ስትለይ ነፋስ እሳት ይለያያሉ ሁለቱ ከሦስቱ አለ መሬት ውሃ ... ይለያያሉ ... ከመሬት ... ይቀራሉና ። አንድም ኃምስቱ የተባሉ ኃጢአት ሰውነት ሰይጣን ነፍስ መንፈስ ቅዱስ ናቸው ። ሦስቱ ከሁለቱ ይለያሉ አለ ። ኃጢአት ሰውነት ሰይጣን ናቸው ሁለቱ ከሦስት አለ ነፍስ መንፈስ ቅዱስ ሁለቱም ይለያያሉ ማለት ጠላት ገል ጠጠር ጅሮሳል ባለቤት የነቃበት ውሻ የሙኸበት እንደ ሆነ ይመለሳል ። ባለቤት ያልነቃበት ውሻ ያልሙኸበት እንደሆነ ገብቶ ባለቤቱን ገድሎ ቤቱን ዘርፎ ይሄዳል ። ሰይጣንም በነፍስ ጥቂት ጽኑነት ያገኘበት እንደሆነ ጥልቅ ብሎ ገብቶ ከሕይወቷ ከመንፈስ ቅዱስ ይለያታልና ወለእመ ረከበ ንቡረ መብእ ውእቱኒ ያርጎበ ለመካን እንዲል ።

፶፬ ወእምዝ ይቤሎሙ ለሕዝብ ሶበ ትሬእዩ ደመና ዘይሠርቅ መንገለ ዓረብ ዝናም ለመጺእ ዘመዝ ይከውን ትብሉ ማቴ ፲፮ ፪ ።

፶፬ ሕዝቡንም ለመዝነም በምዕራብ በኩል ደመና ያያችሁ እንደሆነ እንዲህ ይሆናል ትላላችሁ አላቸው ።

፶፭ ወሶበ ይነፍሕ ነፋስ ዓዜብ ሐሩር ለመጺእ ከመዝ ይከውን ትብሉ ።

፶፭ ትኩሳት ሊመጣ የዓዜብ ነፋስ የነፈሰ እንደሆነ እንዲህ ይሆናል ትላላችሁ ።

፶፮ እ መድልዋን ለገጸ ሰማይ ወምድር ተአምሩ ፈክሮቶ ።

፶፮ እናንተ ግብዞች የሰማይና የምድርን ፊት መመርመር እናውቃለን ትላላችሁ ።
ወእፎ ኢተአምሩ አመክሮቶ ለዝንቱ መዋዕል ።
ይህን ወራት እንደምን አታውቁ ።

፶፯ ወለምንትኑ ኢትፈትሑ ጽድቀ ለሊክሙ ወዘይደሉ ላዕለ ነፍሳቲክሙ ።

፶፯ እናንተ ራሳችሁ ምነው እውነት አትፈርዱ ።

በእንተ ዕርቅ ።

፶፰ ሶበ ተሐውር ምስለ ዕድውከ ኀበ መልአክ ተዓረቅ በፍኖት ። ማቴ ፭ ፳፭ ።

፶፰ ከባለጋራህ ጋራ ወደዳኛ በምትሔድበት ጊዜም ከባለጋራህ ጋራ በመንገድ ታረቅ ።
ወሰልጥ ዘትፈድዮ ።
የምትከፍለውንም ጨርሰህ ስጥ ።
ከመ ኢይትባጽሐከ ኀበ መኰንን ።
ወደ ዳኛ እንዳያደርስህ ።
ወመኰንን ይሜጥወከ ለወዓሊሁ ።
ዳኛውም ለሎሌው ይሰጥሃል ።
ወወዓሊሁ ይሞቅሐከ ።
ብላቴናውም ያስርሃል ።

፶፱ እብለከ ከመ ኢትወፅእ እምህየ እስከ ሶበ ትሜልጥ ደኃሬተ ገመስ ዘላዕሌከ ።

፶፱ የኋለኛውንም ድጥኝ እስክትሰጥ ድረስ ከዚያ አትወጣም ብዬ እነግርሃለሁ ።

ዘከመ ይደልዎ ለክርስቲያን ገቢረ ንስሐ በሠርህ ።

ምዕራፍ ፲፫ ።

፩ ወአሚሃ መጽኡ ሰብእ ኀቤሁ ወዜነውዎ በእንተ ገሊላውያን እለ ደመረ ጲላጦስ ደሞሙ ምስለ መሥዋዕቶሙ ።

፩ ደማቸውን ከመሥዋዕታቸው ጋራ የቀላቀለው የገሊላውያንን ነገር ነገሩት አንድም ሰብእ መጥተው የነገሩት ሰዎች አሉ ሐተታ ለገቢረ በዓል አልመጡም ነበርና ለበዓል ስለምን አልመጡም ብሎ በሀገራቸው መሥዋዕት ሠውተው በዓል አድርገው ሳሉ ገሥግሦ ደርሶ ፈጅቷቸዋል ። ይህም እንዳይሆን ጲላጦስ ሮማዊ ነው እንጂ አይሁዳዊ ነውን ለሕግ ይቀናልን ብሎ ግብር አስቀርተው ነበርና በሀገራቸው መሥዋዕት ሠውተው በዓል አድርገው ሳሉ ገሥግሦ ሄዶ ፈጅቷቸዋል ይህን መጥተው ነገ

ሩት መልካም አደረገ ቢል የእግዚአብሔር ወገን ነኝ ይላል የሰው ጥፋት እያሳዝነው ለማለት መልካም አሳደረገም ቢል ከጲላጦስ ጋራ ለማጣላት ነው።

፪ ወተሠጥዎሙ እግዚእ ኢየሱስ ።

፪ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎሙ ይመስለክሙኑ ከመ እሙንቱ ገሊላውያን ኃጥአን እምዙሉ ሰብእ ገሊላ ።
በገሊላ ካለው ሰው ሁሉ ተለይተው እሊህ ገሊላውያን ኃጥአን ይመስሏችኋልን ።
እስመ ዛቲ ሕማም ረከቦሙ ።
ይህች ሞት ተፈርዳባቸዋለችና ።

፫ አልቦ ። አይደለም ።

እብለክሙ እመሰ ኢነሣሕክሙ አንትሙኒ ከማሆሙ ትትኃጐሉ ዙልክሙ ።
እናንተም ንስሐ ካልገባችሁ ሁላችሁም እንደነሱ ትጠፋላችሁ ብዬ እነግራችኋለሁ ።

፬ ወሚመ ይመስለክሙኑ እሉ ዐሠርቱ ወስመንቱ እለ ወድቀ ዲቤሆሙ ማኅፈድ በሰሊሆም ወቀተሎሙ ይመስለክሙኑ ከመ እሙንቱ ኃጥአን እምዙሉ ሰብእ ኢየሩሳሌም ።

፬ በሰሊሆም ግምብ ፈርሶ የገደላቸው እኒህ ዐሥራ ስምንት ሰዎች በኢየሩሳሌም ካሉ ሰዎች ሁሉ ተለይተው ኃጥአን ይመስሏችኋልን ።

፭ አልቦ ። አይደለም ።
እብለክሙ እመሰ ኢነሣሕክሙ ከማሆሙ ትትኃጐሉ አንትሙሂ ዙልክሙ ።
ካልተመለሳችሁ ሁላችሁም እንደነሣቸው ትጠፋላችሁ ብዬ እነግራችኋለሁ መከሩ አንድ ጊዜ ይከተታልን ፊት የደረሰው ፊት ኋላ የደረሰው ኋላ ይከተት የለምን ሞትም እንደዚህ ነው። ሐተታ ይህ ግምብ ፈርሶ ሰው ያጠፋል ተብሎ ሲነገር ነበር በዝናም ጊዜ ተሰብስበው ከዚያ ገብተው ተቀምጠው ሳሉ ተጭኖ ፈጅቷቸዋል የሐንስ መደብር ግን በቅትለተ ሕፃናት ጊዜ የሄሮድስ ሠራዊት ተሰብስበው ገብተው እኔ ዐሥር ፈጀሁ እኔ ዐሥራ አምስት ፈጀሁ እኔ ሀያ ፈጀሁ ። የሆንኩት የለም ሲባባሉ ይህ ግምብ ፈርሶ ተጭኖ ፈጅቷቸዋል ብሏል ።

በእንተ በለስ ዘአልባቲ ፍሬ ።

፮ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ አሐዱ ብእሲ ቦቱ በለስ ውስተ ዓጸደ ወይኑ እምርት ፣ ጸሎት መላሱ መጻለይ እንዲገባ ፊጥኖ መተው እንዳይገባ ለጊዜው ቢያደርገው ያልወደደውን ተሳጽቆታ ሲሊል እንዲያስደርግለት ምሳሌ መስሎ ያመጣል ።

፮ ላንድ ሰው ፀታዉቀች በወይኑ በታ በለስ ነበረችው። ሐተታ አንዱ ወሎ የበለስ አንድ ወይኑ

የወይን ይህስ የሆነ እንደሆነ ሥሩ እየተዛመተ እያፈራም ብሎ ቀድሞ የወይን ነበር ኋላ የበለስሁትዋል፤ ወሐረ ኀቤሃ ይንሣእ ፍሬሃ ።
ፍሬ ባገኝባት ብሎ ወደሷ ሄደ ።

፯ ወኢረከበ

፯ አላገኘም

ወሶበ ኢረከበ ይቤሎ ለዓቃቤ ወይን ናሁ ሣልስየ ክረምት እንዘ እመጽእ እንሣዕ ፍሬሃ ለዛቲ በለስ ። ባያገኝባት ለጠባቂው እንዲህ አለው ። በዚህች በለስ ፍሬ ባገኝባት ብዬ ስመላለስ እነሆ ሦስት ዓመቴ ነው ።
ወኢረከብኩ ። አላገኘሁም ።
ግዝማ እንከሰ ከመ ኢታፅርዕ ምድረነ ።
እንግዲህስ ወዲህ ምድራችንን እንዳታበዝን ቁረጣት አለው ።

፰ ወአውሥአ ዓቃቤ ወይን ፤

፰ ወይን ጠባቂውም መለሰ ፤
ወይቤሎ ኅድጋ እግዚኦ ሐሪፈኒ ።
አቤቱ የዘንድሮን ተዋት ።
እስከ እከሪ መሬተ ዐእወዲ ወእክዑ ድኩአ ታሕቴን በሥሯ ዐፈር እስታስታቅፋት ፍግ እስካፈስባት ድረስ።
ለእመቦ ከመ ትፈሪ ለዘይመጽእ ።
ምናልባት ለሚመጣው ዘመን ታፈራ እንደሆነ ።

፱ ወእመ አኮስ ንገዝማ እመሐየነ ።

፱ ያለዚያ ግን ብንፍር እንቆርጣታለን አለው ። በሰው ሞት ያጠራጥረዋልና አንድም እሑጹ ብእሲ ቦቱ በለስ ብለህ መልስ ብእሲ ጌታ በለስ ቤተ እስራኤል ናቸው በለስ ዘይቤ ቤተ እስራኤል እሙንቱ እንዲል ሕግ በሚጠብቁባት በኢየሩሳሌም ለጌታ ቤተ እስራኤል እሉት ወሐረ ኀቤሃ በመምህራኑ ብሊት አድሮ ሃይማኖት ምግባር ባገኝባቸው ብሎ ሄደ ወኢረከበ ። ሃይማኖት ምግባር አላገኘባቸውም ወሶበ ኢረከበ ባያገኝባቸው ይቤሎ ለመጋቢሁ ። መጋቤ ብሉይ ቅዱስ ሚካኤልን ሃይማኖት ምግባር ባገኝባቸው ብዬ ስመላለስ ሦስት ዓመቴ ነው ማለት ዘመነ መሳፍንት ዘመነ ነገሥት ዘመነ ካህናት ። ወኢረከብኩ አላገኘሁባቸውም ። ግዝማ እንከሰ ። አጥፋቸው ። ከመ ኢታጽርዕ ምድረነ እብነት ሁነው ሌላውን እንዳያስገድዱ አለው ። ወአውሥአ ወይቤሎ አቤቱ የዘንድሮን ይቅር በላቸው እስከ እከሪ መሬተ ተራድቼ ሥራ እስኪሠሩቸው ድረስ ። ለእመቦ ከመ ትፈሪ ለዓም። ምናልባት ለሚመጣው ዘመን ሃይማኖት ቢይዙ ምግባር ቢሠሩ ወእመ አኮስ ። ያለዚያ ግን እናጠፋቸቀለን ። እመ ሐዮን መቼም መቸ ነቀሮዎች ነገና አንድም መልስ በለስ ቤተ እስራኤል ናቸው እይ

ፅዋጥም ከብ ቢሉ በልጁ ሁሉ ሁኖ ወልድ ቢሉ ሰው ሁኖ ሃይማኖት ምግባር አገኝባቸዋለሁ ብሎ ወደ እስራኤል ሄደ ። ወኢረከበ አላገኘባቸውም ወሰበ ኢረከበ ባያገኝባቸውም ይቤሎ ለመጋቢሁ ። መጋቤ ሐዲስ ቅዱስ ገብርኤልን ምግባር ሃይማኖት ባገኝባቸው ብዬ ስመላለስ ዛሬ ሦስት ዓመቴ ነው እሁን የተመቸ ጌታ ያስተማረ ሦስት ዓመት ነውና ወኢረከብኩ ሃይማኖት ምግባር አላገኘሁባቸውም ። ግዝማ እንከስ ከመ ኢታጽርዕ ምድረነ ። አብ ነት ሆነው ሌላውን እንዳያስጐዱ አጥፋቸው አለው ። ከዚህ በታች አይለወጥም አንድም መልስ ብእሲ አይለወጥም ጌታ ነው ። ሕግ በሚጠብቁበት ፀእያናዳሉም ለጌታ ምእመናን አሉት ። ወሐረ ነቢሃ በመምህራን ሐዲስ አድሮ ሃይማኖት ምግባር አገኝባቸዋለሁ ብሎ ሄደ ።
አላገኘባቸውም ወሰበ ኢረከበ
ሃይማኖት ምግባር ባያገኝባቸው መልአከ ዑቃቢውን መምህረ ንስሐውን ሃይማኖት ምግባር ባገኝባቸው ብየ ስመላለስ ሦስተኛ ዓመቴ ነው ማለት ሕፃንነት ውርዝውና ዕርግና። ወኢረከብኩ፡አላገኘሁባቸውም። ግዝማ ። መልአከ ዑቃቢውን አጥፋቸው አብነት ሁነው ሌላውን እንዳያስጎዱ አለው ።
መምህረ ንስሐውን አውግዛቸው አለው ። መልአከ ዑቃቢው የዘንድሮን ተዋቸው ተፈድሼ ሥራ እስኪሠሩቸው ድረስ ። ለእመበ ፡ ምናልባት [illegible] ወእመ አኮሰ ንገሥግ ፡ ያለዚያ ግን እናጠፋቸዋለን ። እመ ሐዮነ ። መችም መች ነዋሪዎች ነንና መምህረ ንስሐው የዘንድሮን ተዋቸው መከሬ አስተምሬ ሃይማኖት እስካስይዛቸው ምግባር እስካሠራቸው ድረስ ምናልባት ለሚመጣው ዘመን ሃይማኖት ቢይዙ ምግባር ቢሠሩ ያለዚያ ግን አውግዠን እን ለያቸዋለን እመ ሐዮነ ባንሞት በሰው ሞት ያጠራጥራል ።

በአንተ ብእሲት ዘድኅነት በዕለተ ሰንበት ።

፲ ወእንዘ ይሜህሮሙ በሰንበት በ፩ ምኵራብ ።
፲ ቀዳሚ ባንድ ምኵራብ ሲአስተምራቸው ።

፲፩ ወሀለወት አሐቲ ብእሲት እንተ አድወያ ጋኔን ፲ ወ፰ ዓመተ ፤

፲፩ በይማን ዐሥራ ስምንት ዓመት እንድት ታመም ያደረጋት ሴት ነበረች ።
ወጐሕቊት ኅባጣም ነበረች ። እንድም ወጐሕቊት እንተ አድወያ ጋኔን ወእንተ ጐሕቊት በል ።
ወኢትክል ቀዊመ ግሙራ ።
ቀንቶ መሄድ አይቻላትም ነበር ።

፲፪ ወርእያ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፪ ጌታም አየት ።

ወጸውዓ ወይቤላ እ ብእሲቶ ተፈታሕኪ እም ደዌኪ ።
ጠርቶ እንቺ ሴት ከደዌሽ ተለይተሻል አላት ።
ሐተታ ተፈታሕኪ ማለቱ ግን እንደተቋጠረ እቅ ማጸ አድርጓት ነበርና ።

፲፫ ወአንበረ እዴሁ ላዕሌሃ ።
፲፫ እጁን በላይዋ ጫነባት ።
ወረትዓት ሶቤሃ ። ፈጥና ቀናች ።
ወእዕኰተቶ ለእግዚአብሔር ።
እግዚአብሔርንም አመሰገነች ።
ከደዌዬ የፈወስኸኝ ከዚህ ያደረስከኝ ብላ ።

፲፬ ወአውሥአ መጋቤ ምኵራብ እንዘ ይት መዓዕ ።

፲፬ የምኵራቡ ሹም ተበሳጭቶ ተናገረ ።
እስመ በሰንበት ፈወሰ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም ቀዳሚ ፈውሷልና ።
ወይቤሎሙ ለሕዝብ እኮኑ ሰዱስ መዋዕል ዘት ትገበሩ ግብረክሙ ቦቶን ።
ሥራችሁን የምትሠሩባቸው ስድስት ዕለታት ያሉ ላቸሁ አይደለምን ።
ውእቶ አሚረ ንዑኬ ተፈወሱ በውእቶን ዕለታት።
ያን ጊዜ መጥታችሁ ተፈወሱ ።
ወአኮ በዕለተ ሰንበት ።
በሰንበት ግን ልትፈወሱ አይገባም አላቸው ።
ሐተታ እንዲህ ያልኋቸው እንደሆነ ለሥራቸው ሲሳሱ ይቀራሉ ፡ ተአምራት አይደረግም ሰው አይሳብም እሪት እትጠፋም ወንጌል እትሰፋም ብሎ ነው ።

፲፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፭ ጌታችን ኢየሱስም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ።
እንዲህም አላቸው ።
እ መደልዋን ፡
እናንተ ግብዞች ።
እንትሙሰ ኢትፈትሑኑ እድገክሙ ወላህመክሙ እምኑ ምቅማህ ወኢትወስድዎኑ ታስትይዎ ማየ በዕለተ ሰንበት ።

እናንተስ አህያችሁን በሬያችሁን በሰንበት ገለባ ከሚበላበት ፈትታችሁ ውኃ ልታጠጡት ትወስ ዱት የለምን ፡

፲፮ ወዛቲ ወለተ አብርሃም እንተ አሰራ ሰይጣን ፲ተ ወ፰ተ ዓመተ አኮኑ ርቱዕ ትትፈታሕ እምኑ ማእሰራ ይእቲኒ በዕለተ ሰንበት ፡

፲፮ ያንማ እንዲታ በውኃ ጥም ይሙቱን ትሉኝ እንደሆነ ፡ ሰይጣን ዐሥራ ስምንት ዓመት እንድ

ትታመም ያደረጋት ይህችስ የአብርሃም ልጅ ከደዌ ማሰሪዋ ልትፈታ አይገባምን አላቸው ፤

፲፯ ወሶበ ተናገረ ዘንተ ተኃፍሩ ኵሎሙ እለ ቆሙ ላዕሌሁ ፤

፲፯ ይህን በተናገረ ጊዜ በጠላትነት የቆሙበት ሁሉ ምላሽ አጡ ፡፡
ወተፈሥሑ ኵሉ ሕዝብ በእንተ ኵሉ መንክር ሠናይ ዘይትገበር እምኔሁ ላዕሌሁ ፡፡
በሱ ሥልጣን ስለ ሚደረገው ተአምራት ሕዝቡ ሁሉ ደስ ብሏቸው አደነቁ ፡፡

በእንተ ኅጠተ ሰናፔ ወበእንተ ዘርዕ ወብኁእ

፲፰ ወይእቲ ዕለተ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ምንተ ትመስል መንግሥተ ሰማያት ፡፡

፲፰ ይህ ሰው እንዲህ ማለቱ እንዴህ ያልኋቸው እንደሆነ ስለሥራቸው ሲሳሱ ይቀራሉ ተአምራት አይደረግም ሰው አይሳብም እሬት አትጠፋም ወንጌል አትስፋም ብሎ እንጂ ነው ፡፡
ወንጌልማ ትጠፋ ዘንድ ምን ትመስላለች ፡፡
ወበምንት እስተማስላ ፡፡
በምንስ እመስላታለሁ ፡፡

፲፱ ትመስል ኅጠተ ሰናፔ እንተ ነሥአ ብእሲ ወዘርዓ ውስተ ገራህቱ ፡፡

፲፱ ሰው በርሻው ውስጥ የዘራትን ሰናፍጭ ትመስላለች ፡፡
ወልሕቀት ፡፡ አደገች ፡፡
ወኮነት ዕፀ ዓቢየ ፡፡ ታላቅ ዛፍ ሆነች ፡፡
ወአጽለሉ አዕዋፈ ሰማይ ውስተ አዕጹቂሃ ፡፡
ወፎችም መጥተው ተቀመጡባት ፡፡

፳ ወካዕበ ይቤ በምንት አስተማስላ ለመንግሥተ እግዚአብሔር

፳ ዳግመኛ የእግዚአብሔርን መንግሥት በምን እመስላታለሁ ፡፡

፳፩ ትመስል ብሑአ ዘነሥአት ብእሲት ፡፡
፳፩ ሴት የወሰደችውን እርሾ ፡፡
ወኀብአቶ ውስተ ሠለስቱ መሥፈርተ ሐሪጽ ፡፡
ሦስት መስፈሪያ ዱቄት የለወሰችውን ፡፡
ወእስከ አብኀአ ኵሎ ፡፡
ሁሉን መጣጣ ያደረገ እርሾን ትመስላለች ፡፡

በእንተ ትልቁ ኅሩያን ፡፡

፳፪ ወኮነ የሐውር አህጉረ ወአዕጻዳተ ወያንሶሱ በኢየሩሳሌም ወይሜህር ፡፡

፳፪ በየሀገሩና በየአውራጃው በኢየሩሳሌምም እየተመላለሰ ያስተምር ነበር ፡፡

፳፫ ወይቤሎ አሐዱ ብእሲ እግዚኦ ውሑዳ ኑኑ እለ ይድኀኑ ፡፡

፳፬ ኅሎት ፀናፔ ቤልበት ከነሱ አንዱ መንግሥቱ በማያልቅ የሚገቡ ጻድቃን ጥቂቶቹ ናቸው አለው፤
፳፬ ወይቤሎሙ ተጋየሉ ትባኡ እንተ ጸባብ አንቀጽ ፡፡

፳፭ በጠባቡ ደጅ ለመግባት ድል ንሱ አላቸው ፡፡ አንድም ሕግን ለመጠበቅ ተበረቱ ፡፡ እብለክሙ ብዙኃን እለ የኃሥሡ ይባኡ ፡፡
ሊገቡ የሚወዱ ብዙ ናቸው ወኢይክሉ አይቻላቸውም ብየ እነግራችኋለሁ ፡፡

፳፭ እስመ ይትነሣእ በዓለ ቤት ወየአጹ ኖኅቶ ማቴ ፳፭ ፣ ፲፩ ፡፡

፳፭ ባለቤት ተነሥቶ ደጁን ይዘጋልና ማለት እምጻኤ ዓለማት ጌታ ምሕረት ይከለከላልና ፡፡
ወይእቲ ጊዜ ትቀውሙ አፍአ ወትጐድጕዱ ፡፡
ያን ጊዜም ከውጪ ቆማችሁ ደጅ ትመታላችሁ ፡፡
እንዘ ትብሉ እግዚኦ እግዚኦ አርኅወነ ፡፡
አቤቱ አቤቱ ክፈትልን እያላችሁ ፡፡
ወያወሥአ ወይብለክሙ ኢያእምረክሙ እምአይቴ አንትሙ ፡፡
ከወዴትም እንደ ሆናችሁ አላውቃችሁም ብሎ ይመልስላችኋል ፡፡

፳፮ ወእምዝ ትእኀዙ ትብልዎ በላዕነኒ ወሰተይነ በቅድሜከ ፡፡

፳፮ ከዚህ በኋላ በፊትህ በላን ጠጣን አል ነበረምን ፡፡
ወመሀርከ በመራህብቲነ ፡፡
ባደባባያችንስ ስታስተምር አልነበረምን ትሉ ትጀምራላችሁ ፡፡

፳፯ ወይብለክሙ ኢያእምረክሙ ፡፡ ማቴ ፯ ፳፫ መዝ ፮ ፰ ፡፡

፳፯ ዐላውቃችሁም ይላችኋል ፡፡
ረኃቁ እምኔየ ገበርተ ዓመፃ ፡፡
ግፍ የምታደርጉ ሁሉ ከኔ ራቁ

፳፰ ወሐቱ ውስተ ብካይ ወሐቅየ ስነን ፡፡
፳፰ ሐዱ ልቅሶ ጥርስ ማፋጨትም ወዳለበት ወእመ ርኢክሙ ለአብርሃም ወለይስሐቅ ወለያዕቆብ ወለኵሎሙ ነቢያት እንዘ ይረፍቁ በመንግሥተ እግዚአብሔር ፡፡

አብርሃምን ይስሐቅን ያዕቆብንም ነቢያትንም ሁሉ በመንግሥተ ሰማይ ባያችኋቸው ጊዜ ፡፡
ለክሙስ ያወፅኡክሙ አፍአ ፡፡
እናንተን ግን ከመንግሥተ ሰማይ ውጭ ያወጧችኋል ፡፡

፳፱ ወይመጽኡ እምጽባሕ ወእምዕራብ ወእም ሰሜን ወእምደቡብ ።

፳፱ ከምሥራቅ ከምዕራብ ከሰሜን ከደቡብ መጥተው ።

ወይትፌሥሑ በመንግሥተ እግዚአብሔር ። በእግዚአብሔር መንግሥትም ተድላ ያደርጋሉ ።

፴ ወይከውኑ ቀደምት ደኃርተ ።
ማቴ. ፲፱ ፥ ፴ ማር. ፲ ፥ ፶ ።

፴ ፊተኞች ኋለኞች ይሆናሉ ።

ወደኃርት ቀደምተ ።
ኋለኞችም ፊተኞችን ይሆናሉ

በእንተ ጽልዕ ዘሄሮድስ ።

፴፩ ወበይእቲ ዕለት መጽኡ ሰብእ እምፈሪሳውያን ።

፴፩ በዚያች ቀንም ከፈሪሳውያን ወገን መጥተው።

፴፪ ወይቤልዎ ፃዕ ወሑር እምዝየ እስመ ሄሮድስ የኀሥሥ ወይፈቅድ ይቅትልከ ።

፴፪ ሄሮድስ ሊገድልህ ይሻልና ከዚህ ሂድ አሉት። ሐተታ ለሱ አገልጋዮቹ ያልሆኑ ... [illegible] እንደሆነ ተአምራት ያደረገ ... [illegible] ትመስላት ወንጌል ትሰፋለች ... እንጂ ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሑሩ በልዎ ለዛቲ ቀንጽል ።
ያችን ቀበሮ ሄዳችሁ እንዲህ በሏት ።
ናሁ አወፅእ አጋንንተ ።
እነሆ አጋንንትን አወጣለሁ ።
ወእሁብ ሕይወተ ።
ድውይንም እፈውሳለሁ ።
ዮም ።
የነገሩት በመጀመሪያ ዓመት ነው ያሉ እንደሆነ ።
ዮም በመጀመሪያው ዓመት ።
ወጌሠመ ።
በሁለተኛው ዓመት ።
ወበሣልስት ዕለት እፌጽም ።
በሦስተኛውም ዓመት እፈጽማለሁ ማለት አሞታለሁ ። እንደዋ በሁለተኛው ዓመት ነው ያሉ እንደ ሆነ ዮም በሁለተኛው ዓመት ጌሠም በሦስተኛው ዓመት ድውይ እፈውሳለሁ ጋኔን አወጣለሁ ። ወሣልስት በሦስተኛው ወር እሞታለሁ ።

፴፫ ወባሕቱ ዮምሰ ወጌሠመ ሀለወኒ ።

፴፫ ነገር ግን ዛሬና ነገ እኖራለሁ ።
ወበሣልስት እሐውር ።
በሦስተኛውም ዓመት እሞታለሁ ።

እስመ ኢይደልዎ ለነቢይ መዊት በአፍአ ዘእንበለ በኢየሩሳሌም ።

ለነቢይ ለክርስቶስ በኢየሩሳሌም እንጂ ከኢየሩሳሌም ውጭ ተሰቅሎ መሞት አይገባውምና ። ሐተታ በኢየሩሳሌም መሰቀሉ ስለ ምን ነው ቢሉ ወንበረ መድኃኒት በማእከለ ምድር ያለው ትንቢት ሊፈጸም አንድም ርእሰ አዳም ከዚያ አለና እሱን ከማዳን እንደ መጣ ለማጠየቅ አንድም አዳምን ያሳተ ርእሰ አርዌ ከዚያ ወድቆ ነበርና ያን ለማጥፋት እንደመጣ ለማጠየቅ ።

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ ተኃድጎታ ለኢየሩሳሌም ።

፴፬ ወይቤ ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም እንተ ትቀትሎሙ ለነቢያት ። ማቴ. ፳፫ ፥ ፴፯ ።

፴፬ ኢየሩሳሌም ኢየሩሳሌም ሆይ አንች ነቢያትን ገዳይ ።
ወትዌግሮሙ ለሐዋርያቲሃ እለ ተፈነዉ ሀቤሃ ።
ወዳንች የተላኩትንም ሐዋርያት የምትወግሪ ።
ሚመጠነ ፈቀድኩ እስተጋብኦሙ ለደቂቅኪ ከመ እንተ ታስተጋብእ ዶርሆ ዕጕሊሃ ታሕተ ክንፊሃ ።
ዶሮ ልጆችዋን በክንፏ እንድትሰበስብ ልጆችሽን እሰበስብ ዘንድ ምን ያህል ወደድኩ ።
ወኢፈቀድክሙ ። እምቢ አላችሁ ።

፴፭ ወናሁ ይትኃደግ ለክሙ ቤትክሙ በድው ።

፴፭ እነሆ ቤታችሁ ፈርሶ ይቀርላችኋል ። እብለክሙ ከመ ኢትሬእዩኒ እምይእዜ እስከ ሶበ ትብሉ ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር ። በእግዚአብሔር ስም የሚመጣ የተባረከ ነው እስከ ትሉ ከእንግዲህ ወዲህ አታዩኝም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

ምዕራፍ ፲፬ ።

ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ ለቅብው በእለተ ሰንበት።

፩ ወእምዝ ሶበ ሖረ ቦአ ቤተ አሐዱ ብእሲ እምን መልእክቶሙ ለፈሪሳውያን በሰንበት ከመ ይብላዕ እክለ ።

፩ ከዚህ በኋላ በሄደ ጊዜ እህል ይበላ ዘንድ ከፈሪሳውያን አለቆች ወዳንዱ ቤት በሰንበት ገባ ።
ወእሙንቱሰ ይትዓቀብዎ ።
እነሱም ይጠባበቁት ነበር ።

፪ ወሀሎ እሐዱ ብእሲ ቅብው ቅድሜሁ ።
፪ ሆዱ የተነፋ ሰው በፊቱ ነበር ።
ቅድሜሁ ሀሎ ሀሎ ቅድሜሁ ብለህ ግጠም ።

፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፫ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎሙ ለጸሐፍት ወለፈሪሳውያን ይከውን በሰንበት ፈውሶ ወሚመ ኢይከውንሁ ።
በሰንበት ድውይ መፈወስ ይገባልን ወይም አይገባም ብሎ የሕግ አዋቂዎችንና ፈሪሳውያንን ጠየቃቸው ።

፬ ወአርመሙ ዝም አሉ ።
ወአኀዞ ወፈወሶ ወፈነዎ ።
ወይዞ ፈውሶ ሰደደው ።

፭ ወእምዝ ይቤሎሙ አመቦ እምኔክሙ ዘወድቀ ላህሙ አው አድጉ ውስተ ዐዘቅት ።

፭ ከእናንተ በሬው ወይም አህያው ከጉድጓድ ቢወድቅበት ።
አኮኑ በጊዜሁ ያንሥኦ ወያወፅኦ በዕለተ ሰንበት ።
በሰንበት ያን ጊዜውን ያነሣው የለም አላቸው ።

፮ ወስእኑ አውሥኦቶ በእንተ ዝንቱ ነገር ።
፮ ስለዚህ ነገር መመለስ ተሳናቸው ።
ዘከመ መሀረ ኢየሱስ ትሕትና ወፍቅረ ለእለ ይረፍቁ ።

፯ ወመሰሎ ሎሙ ወይቤሎሙ ለእለ ሀለዉ ውስተ ምሳሕ ።

፯ በምሳ ላሉ ምሳሌውን መስሎ ነገራቸው ።
ወመሀሮሙ ሶበ ርእዮሙ እንዘ ይትባደሩ ውስተ ርእሰ ምርፋቅ ።
በላይ ለመቀመጥ ሲቀዳደሙ ባያቸው ጊዜ ምን ጣፍ መጪጊያ ካለበት ጽዋ ከሚጀመርበት እንጀራ ከበዛበት ወጥ ከተደራረበበት ሲቀዳደሙ ባያቸው ጊዜ ።

፰ ወይቤሎ ።
፰ እንዲህም አላቸው ።
እመቦ ዘጸውዓከ ውስተ ምሳሕ ኢትርፍቅ ውስተ ርእሰ ምርፋቅ ከቡር ።
ለምሳ የጠራህ ሰው ቢኖር ከራስጌ አትቀመጥ ።
የጊ ይመጽእ ዘይከብረከ ።
ወይም ካንተ የበለጠ ይመጣ ይሆናል ።

፱ እስመ መጺእ ድኅረ ይብለከ ዝኩ ዘጸውዓከ ኀድግ ሎቱ ዘንተ ገጸ ።

፱ ያ የጠራህ ኋላ መጥቶ ይህን ሥፍራ ለእገሌ ተውለት ይልሃልና ።
ወትትኀፈር ውእተ ጊዜ ወትወርድ ውስተ ምርፋቅ ዘደቂቀ ።
ያን ጊዜም አፍረህ ከታችኛው መቀመጫ ትወርዳለህ ።

፲ ዘእመሰ ዘጸውዓከ ። ምሳ ፳፩ ፳፪ ።
፲ የጠራህ ሰው ቢኖር ።
ሑር ርፍቅ ውስተ ታሕታይ ምርፋቅ ።
ከታች መቀመጫ ተቀመጥ ።
ከመ ሶበ መጽአ ዘጸውዓከ ይበልከ አርኀየ ዕርግ ውስተ ዘይትሌዓል ምርፋቅ ።
የጠራህ ሰው በመጣ ጊዜ ወዳጅ ከዚህ ወደላይ ወጥተህ ተቀመጥ ይልህ ዘንድ ።
ወውእቱ ጊዜ ይከውነከ ክብረ በቅድመ ኵሎሙ እለ ይረፍቁ ወይመስሑ ምስሌከ ።
ያን ጊዜም ካንተ ጋራ ተቀምጠው የሚበሉት ሁሉ ያከብሩሃል ።

፲፩ እስመ ኵሉ ዘአዕበየ ርእሶ የኀሥር ። ማቴ. ፳፫ ፲፪ ሉቃ. ፲፰ ፲፬ ።

፲፩ ራሱን ያከበረ ሁሉ ይዋረዳልና
ወዘአትሐተ ርእሶ ይከብር ።
ራሱንም ያዋረደ ይከብራልና ።
ወይቤሎ ለዘጸውዖ ።
ለጠራውም ሰው እንዲህ አለው ።

፲፪ ሶበ ትገብር በዓለ ወምሳሐ አው ድራረ ። ምሳ ፲፫ ፱ ።

፲፪ በዓልም በምታከብርበት ምሳም በምታቀርብበት ዝክርም በምትዘክርበት ጊዜ ።
ኢትጸውዕ ፍ. አእርክቲከ ወአኀዊከ ።
ወንድሞችህንና ወዳጆችህን አትጥራ ።
ዘአዝማዲከ ወጐረቤከ ወማኅፈረከ ።
ዘመዶችህንና ጐረቤቶችህን ።
ወቢጸከ አብዕልተ ።
ባለጠጎችን ።
ከመ ይጼውዑከ እሙንቱሂ ።
እርሳቸውም ይጠሩህ ዘንድ ።
ወይከውነከ ፍዳ በነቢሆሙ ።
ብድራት ይሆንብሃልና ።

፲፫ አላ አንተሰ ሶበ ትገብር በዓለ ወምሳሐ ጦቢ ፬ ፯ ።

፲፫ ዝክር በምትዘክርበት ምሳ በምታቀርብበት ጊዜ ።
ጸውዕ ነዳያነ ወምስኪናነ ።
የተቸገሩትንና ድሆችን ጥራ
ወዕውራነ ። ዕውራንን ።
ወስቡራነ ። አንካሶችንም ።

፲፬ ወብፁዕ አንተ ።
፲፬ እንዲህ ያደረግህ እንደሆነ የተመሰገንክ ነህ
እስመ አልቦሙ ዘይፈድዩከ ።
የሚከፍሉህ የለቸውምና ።
ባሕቱ ትትዓሠይ አመ ይትነሥኡ ጻድቃን ።
ጻድቃን በሚነሡበት ቀን ዋጋህን ታገኛለህ እንጂ ።

፲፬ ወሰሚዖ ዘንተ አሐዱ እምእለ ይረፍቁ ። ይቤሎሙ ብፁዕ ውእቱ ዘይበልዕ እክለ በመንግሥተ ሰማያት ።

፲፭ ከተቀመጡት አንዱ ይህን ሰምቶ በመንግሥት ሰማይ እህል የሚበላ ሰው የከበረ ነው አለ ። የእንብላው መጣፍ የጅብ መጣፍ እንዲሉ ። በዚህ ዓለም እህል ትምህርትን የሚመገብ ሰው በመንግሥት ሰማይ ንዑድ ክቡር ነው ። አንድም ወመሰለ ሎሙ ብለህ መልስ ። በትምህርት ሳሉ ምሳሌ መስሎ ነገራቸው ለማስተማር ሲቀዳደሙ ባያቸው ጊዜ ። ወይቤሎሙ በትምህርት የጠራህ ሰው ቢኖር አስተምራለሁ አትበል ዮጊ ይመጽእ ወይም የተማረ ካንተ የበለጠ ይሆናል እስመ መጺእ ፡ የጠራህ ሰው መጥቶ ማስተማሩን ለእገሌ ተውለት ይልሃልና ፡ ወትትኃፈር ያን ጊዜ እፍረህ ወደትምህርት ትመለሳለህ ። ወእመሰ ቦ ወደመምርት የጠራህ ሰው ቢኖር ወሖርከ ፡ አንተም ብትሄድ ፡ ርፍቅ ውስተ ታሕታይ ምርፋቅ እማራለሁ በል ፡ ከመ ሶበ መጽአ የጠራህ ሰው ወዳጄ መማሩ ይበቃሃል አስተምር ይልህ ዘንድ ወውእቱ ጊዜ ይከውነከ ክብረ ያን ጊዜ በሁሉ ዘንድ ክብር ይሆንልሃል ። እስመ ኵሉ ራሱን ያከበረ ይዋረዳልና አስተምራለሁ አትበል ወዘአትሐተ ርእሶ ራሱን ያዋረደ ይከብራልና እማራለሁ በል ። ወይቤሎ ለዘጸውዖ ። በምታስተምርበት ጊዜ የተማሩትን አስተምራለሁ አትበል ።

ከመ ይጸውዑከ ። ያስተምሩህ ዘንድ ። ወይከውነከ ፍዳ ። ብድራት ይሆንብሃልና እላ ሶበ ትገብር ። በምታስተምርበት ጊዜ ያልተማሩትን አስተምር እንጂ ወብፁዕ ። እንዲህ ያደረግህ እንደሆን የተመሰገንክ ነህ።እስመ አልቦሙ ፡ የሚያስተምሩህ የላቸውምና ። ወባሕቱ ጻድቃንዋጋቸውን በሚያገኙበት ጊዜዋጋህን ታገኛለህ እንጂ ነገር ግን ዋጋህን ታገኛለህ አንድም ወመሰለ ሎሙ ብለህ መልስ በምናኔ ላሉ ምሳሌ መስሎ ነገራቸው ፡ ሶበ ርእዮሙ ፡ ለተባሕትዎ ሲቀዳደሙ ባያቸው ጊዜ ይቤሎሙ ፡ ወደምናኔ የጠራህ ሰው ቢኖር ተባሕትዎ እይዛለሁ እዘጋለሁ አትበል ፡ ዮጊ ወይም ካንተ የበለጠ የረዳ ይኖራል ፡ እስመ መጺእ ። ወደምናኔ የጠራህ መጥቶ ተባሕትዎውን ለእገሌ ተውለት ይልሃልና ፡ ወውእተ ጊዜ፡ ያን ጊዜ እፍረህ ልርዳ ትላለህና ፡ ወደመርዳት ትመለሳለህ ፡ ወያወፅእዎ ዘበአሕሥሮት እንዲል ፡ ሳይረዳ የዘጋውን ያስወጡታል ፡ ወእመሰቦ የጠራህ ሰው ቢኖር ። ወሖርከ ፡ አንተም ብትሄድ ። ርፍቅ እረዳለሁ በል ። ከመ ሶበ መጽአ ። ወደምናኔ የጠራህ ሰው ርዳታው ይበቃሃል ተባሕትዎ ያዝ ይልህ ዘንድ ወውእተ ጊዜ ያን ጊዜ በሁሉ ዘንድ ክብር ይሆንሃል ። እስመ ኵሉ ዘአዕበየ ። አይለወጥም ወይቤሎ ። በምትመነንበት ጊዜ የተማሩትን ይገፍ እመነናለሁ አትበል ከመ እሙንቱሂ ግርማ ሌሊቱ ድምፀ አራዊቱ ዕፀ ገዳሙ እንደምን ይቻላል እያሉ ይከራከሩሃልና ፡ እላ ሶበ ትገብር ። ወደምናኔ በምትጠራበት ጊዜ ያልተማሩትን ይዘህ መንን እንጂ ። ይኄይስ ብእሲ ዘጠበ በለቢሰ ምግባራት እምነ ብእሲ በዓለ ኃሠሣ ወንጽር እንዲል ። ወብፁዕ አንተ እንዲህ የሆን እንደሆን ንዑድ ክቡር ነህ ። እስመ አልቦሙ ያሰብከውን አይከራከሩህምና አያስቀሩብህምና ወሰሚዖ አይለወጥም ።

በእንተ ምሳሌ ዘዕሡራን ።

፲፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አሐዱአ ብእሲ ገብረ ምሳሐ ዓቢየ ። ማቴ · ፳፪ ፡ ፪ ራእ · ፲፱ ፡ ፱ ።

፲፮ አንድ ሰው ታላቅ ምሳ አደረገ ።
ወዓሠርሙ ለብዙኃን ።
ብዙ ሰዎችንም ጠራ ።

፲፯ ወሶበ በጽሐ ዓሡር ፈነወ ገብሮ ይጸውዖሙ ለእለ ተአሥሩ ።

፲፯ የታደሙበት ቀን በደረሰ ጊዜ የታደሙትን ይጠራ ዘንድ ባሪያውን ላከ ።
ወሖረ ገብሩ ወይቤሎሙ ለእለ ዓሠርዎሙ ንዑአ
እስመ ናሁ ወዳእነ አስተዳለውነ ምሳሐ ።
ሂዶ ምሳውን አዘጋጅተን ፈጽመናልና ኑ አላቸው ።
ወዓበይዎ ኵሎሙ ጽቡረ ።
ሁሉም ባንድ ቃል እንቢ አሉ ።

፲፰ ወይቤሎ ቀዳማዊ ገራኅተ ተሣየጥኩ ።
፲፰ የፊተኛው ምድር ገዝቻለሁ ።
ወእጽሕቅ እሑር እርኣያ ።
ልመራት እወዳለሁ ።
ወበሎ ረሲ ሊተ ከመ ዘኢእበይኩ ።
ስለዚህ መምጣት አይቻለኝምና ከመጣሁ ቍጠር
ልኝ በለው አለው ፡

፲፱ ወይቤሎ ካልኡ ኃምስተ ጽምደ አልህምት ተሣየጥኩ ።

፲፱ ሌላውም አምስት ጥምድ በሮች ገዝቻለሁ ። ክልኤተ ጽምደ አኃ ይላል ሁለት ወይፈን ገዝቻለሁ ።
ወእሐውር እርእዮሙ ወእፍትኖሙ ።
ልፈትናቸውም እሔዳለሁ ፡
ወበሎ ረሲ ሊተ ከመ ዘመጻእኩ ወኢዓበይኩ ።
ከመጣሁ ቈጠርልኝ በለው አለው ።

፳ ወማልሱኒ ይቤሎ ብእሲተ አውሰብኩ ።

፳ ሦስተኛውም ሚስት አግብቻለሁ ።
ወበእንተዝ ኢይክል መጺአ ወረሲ ሊተ ከመ ዘኢ
ዓበይኩከ ስለዚህም መምጣት አይቻለኝም ከመጣሁ
ቍጠርልኝ በለው አለው ። ሐተታ ገራህተ ተሣየጥኩ፥
ማለታቸው ሰማያዊ ልደቱን ቢነግሯቸው እኛስ ምድ
ራዊ ልደቱን እናውቃለን እንጂ ሰማያዊ ልደቱን
አናውቅም ማለታቸውን መናገር ነው ፤ ኃምስተ
ጽምደ አልህምት ማለታቸው በኀቱም ድንግል ተፀ
ንሶ በኀቱም ደንግልና መወለዱን ቢነግራቸው እኛስ
እምስቱ ሕዋሳቶች ካምስቱ ሕዋሳቶቹ አንድ ሁኖ
የሚወለዱትን ልደት ነው እንጂ በኀቱም ድንግልና
ተፀንሶ መወለዱን አናወቅም ማለታቸውን መና
ገር ነው ፤ ጽምደ አኃ ማለታቸው አምስቱን አዕማደ
ምሥጢር ቢነግሯቸው በሁለቱ ጽላት የተጻፉትን
ሕገጋት እንጂ እምስቱን አዕማደ ምሥጢር እናው
ቅም ማለታቸውን መናገር ነው ። ብእሲተ አውስ
ብኩ ማለታቸው እንበለ ዘር መወለዱን ቢነግራ
ቸው እኛስ በዘር በሩካቤ የሚወለደውን እናውቃ
ለን እንጂ እንበለ ዘር የሚወለደውን ልደት እናው
ቅም ማለታቸውን መናገር ነው ።

፳፩ ወገብአ ዝኩ ገብሩ ወነገሮ ከመዝ ለእግዚ እ።
፳፩ ባሪያውም ተመልሶ ይህን ለጌታው ነገረው።
ወእምዝ ተምዓ በዓለ ቤት ይእተ ጊዜ ።
ያን ጊዜም ባለቤቱ ተቆጣ ።
ወይቤሎ ለገብሩ ሑር ወፃእ ፍጡነ ውስተ መራህብት
ወውስተ አስኳተ ሀገር ።
ባሪያዉንም አለው ፈጥነህ ወደዐደባባይ ሂድ ።
ጸውዕ ወእምጽእ ሊተ ዝየ ነዳያነ ወፅሑሳነ ።
የተቸገሩትንና ድሆችን ።
ወዕውራነ ። የታወሩትን ።
ወስቡራነ እንካሶችን አምጣልኝ አለው ።

፳፪ ወይቤሎ ገብሩ ገበርኩ እግዚእ በከመ
አዘዝከኒ ።

፳፪ ከዚህ በኋላ ባሪያው አቤቱ እንዳዘዝከኝ
አደረግሁ አለው ።
ወዓዲ ቦ መካን ።
ደግሞም ስፍራ አለ አለው ። ሐተታ የሚገባ በትቶ
ከተገኘ እስመከልከለን መናገር ነው

፳፫ ወይቤሎ እግዚኡ ለገብሩ ሑር ፍጡነ
ውስተ ፍናው ወውስተ ጥቅመ ሀገር ወበግብር እብእ
ሰብእ ።

፳፫ ጌታውም ባሪያውን ወደቅጥሩና ወደ ሙን
ገድ ውጣና የግድ አስገባ ።
ከመ ይምላእ ቤትየ ።
ቤቴ ይመላ ዘንድ አለው ።

፳፬ እብለክሙ ከመ አሐዱሂ እም እለ ተዓሥሩ
እለ ጸዋዕኩ ኢይጥዕምዋ ለበዓልየ ።

፳፬ ከነዚህ ከተጠሩት ሰዎች አንዱ ስንኳ
እንጀራዬን አይቀምሳትም ብየ እነግራችኋለሁ ።
እልቦ ዘይጥዕም ለበዓልየ አሐዱሂ ኢይጥዕም ለበ
ዓልየ ይላል ። እንደዚህም ሁሉ ትንቢት ከተነገረ
ላቸው ተስፋ መስቀልን ካናገርንላቸው አንድ ስንኳ
እንዳይገባ በውነት እነግራችኋለሁ ።
እስመ ብዙኃን እሉራን ወኅዳጣን ኅሩያን ።
የታደሙ ብዙ ናቸውና ። የተመረጡ ጥቂት ናቸውና ።

ዘከመ ይደሉ ተሊዎተ ኢየሱስ

፳፭ ወእምዝ እንዘ የሐውሩ ምስሌሁ ብዙ
ኃን ሰብእ ተመይጠ ወይቤሎሙ ።

፳፭ ከዚህ በኋላ ብዙ ሰዎች ከርሱ ጋራ ሲሄዱ
ተመልሶ እንዲህ አላቸው ።

፳፮ ዘይመጽእ ኀቤየ ። ማቴ. ፲ ፥ ፴፯ ።

፳፮ ወደኔ የሚመጣ ።
ወዘይፈቅድ ይትልወኒ ።
ሊከተለኝም የሚወድ
ወዘኢጸልአ አባሁ ወእሞ ።
እናት አባቱን ያልጠላ ።
ወብእሲቶ ፤ ሚስቱን ።
ቤቶ ። ቤቱን
ወውሉዶ ። ልጆቹን
ወአኃዊሁ ። ወንድሞቹን
ወአኃቲሁ ። እኅቶቹንም የማይጠላ
ወዓዲ ነፍሶሂ እንቲአሁ ።
ደግሞም ነፍሱን የማይጠላ ።
ኢይክል ከዊነ ረድዕየ ።
የኔ ደቀ መዝሙር መሆን አይቻለውም ።

፳፯ ዘኢይጾውር መስቀለ ሞቱ ወኢይመጽእ
ይትልወኒ ኢይክል ከዊነ ረድዕየ ። ማቴ. ፲ ፴፰
ማር. ፰፥ ፴፬ ።

፳፯ መስቀሉን ተሸክሞ የማይከተለኝም የኔ
ደቀ መዝሙር መሆን አይቻለውም ።

፳፰ ወእመቦ አሐዱ እምኔክሙ ዘይፈቅድ ይሕ
ንጽ ማኅፈደ ።

፳፰ ከናንተ ወገን ግምብ ሊሠራ የሚወድ
ሰው ቢኖር
አኮኑ ያቀድም ይንበር ወየሐስብ ፃዕፃዖ ።
አስቀድሞ ተቀምጦ የሚበቃውን ያስብ የለምን ።
እመ የአክሎ ከመ ይሣርር መሠረተ ።
ይበቃው እንደሆነ መሠረት ይጀምር ዘንድ ።

፳፱ ከመ ኢይበሉ ... 

፳፱ ከመ ግሬሮ መሠረተ እመ ሰእነ ፈጽሞ ኵሎሙ እለ ርእይዎ ይእኀዙ ይሣለቁ ላዕሌሁ እንዘ ይብሉ ዝንቱ ብእሲ አኃዘ ይኅንጽ ወስዕነ ፈጽሞ ፡፡

፳፱ መሠረት ጀምሮ መፈጸም የተሳነው እን ደሆነ ያዩት ሰዎች ሁሉ ይህ ሰው ቤቱን ሊሠራ ጀምሮ ነበር መፈጸም ተሳነው ብለው እንዲዘብቱበት እንድም እመቦ ብለህ መልስ ከናንተ ወገን የምናኔ ሥራ ሊሠራ የሚወድ ሰው ቢኖር ይቻለውም አይ ቻለውም እንደሆነ በዓለም ሳለ ያወጣ ያወርድ የለምን ፡፡ ከመ ግሬሮ ከጀመረ በኋላ መፈጸም ቢላ ነው ያዩት ሰዎች ያዩት አጋንንት ይህ ሰው የምናኔ ሥራ ሊሠራ ጀምሮ ነበር መፈጸም ተሳነው ብለው እንዲዘብቱበት ፡፡

፴፩ ወእመኒ ንጉሥ ፈቀደ ይሑር ይጽብዖ ለካልዕ ንጉሥ ፡፡

፴፩ ንጉሥ ንጉሥን ሊወጋው ቢወድ ፡፡
አኮኑ ይቀድም ወይነብር ወይመክር ለእመ ይክል በእልፍ ጸቢአቶ ለዘይመጽእ ኀቤሁ ምስለ ክልኤ እልፍ፡ ሁለት እልፍ አስከትሎ የሚመጣበትን ንጉሥ እልፍ ሠራዊት ይዞ ድል ይነሣው እንደ ሆነ አስቀድሞ ተቀምጦ አውጥቶ አውርዶ ይመክር የለምን ፡፡

፴፪ ወእመ አኮሰ እንዘ ርኁቅ ውእቱ ይፌኑ ተናብልተ ፡፡

፴፪ ያለዚያ ግን በሩቅ ሳለ ልገብር ብሎ እማ ላጅ ይልክ የለምን ፡፡ ወይዜንውዎ ሰላመ ፡፡
ልገብር እለ ብለው ይነግሩት የለምን ፡፡ እንድም ባሕታዊ ሰይጣንን ድል ሊነሣው ቢወድ አስቀ ድሞ በዓለም ሳለ ያወጣ ያወርድ የለምን ለእመ ይክል ፍትወታት እኩያት ኃጣውእን የሚያመጣበት ሰይ ጣንን በጥቂት ትሩፋት ድል መንሣት ይቻለውም እን ደሆነ ወእመ አኮሰ ያለዚያ ግን በበላዩ ወዳሉ ባሕ ታውያን አትርሱኝ አዘኑልኝ ብሎ ይልክ የለምን ፡፡

፴፫ ወከማሁ ኵሉ ሰብእ ዘእምኔከሙ ዘኢ.ወ ዕአ እምኵሉ ወዘኢይትናከር ኵሎ ዘዚአሁ ንዋየ ኢይክል ከዊነ ረድዕየ ፡፡ ማቴ. ፲ ፲፫ ማር. ፱ ፡ ፵ ፡፡
፴፫ እንደዚህም ሁሉ ከናንተ ወገን ከቤቱን ሁሉ ያልተወ ከገንዘቡ ሁሉ ያልተለየ የኔ ደቀ መዝሙር መሆን አይቻለውም ፡፡

፴፬ ሠናይ ውእቱ ጼው ፡፡
፴፬ ጨው መልካም ነው ፡፡
ወእመሰ ጼው ለስሐ በምንት እንከ ይቄስምዎ ፡፡
ጨው ቢያልጥ ግን በምን ያጣፍጡታል ፡፡
፴፭ አኮኑ ይገድፍዎ አፍአ ውስተ መሬት፡፡
፴፭ ከዳሪ ይጥሉታል እንጂ ፡፡
፴፮ ዘቦ እዝን ሰሚዓ ለይስማዕ ፡፡

፴፮ ጆሮ ያለው ይስማ እንድም ሠናይ ውእቱ ጼው ብለህ መልስ ምናኔ መልካም ነው ምናኔ ከሌለ የተባሕትዎውን ሥራ በምን ይሠሩታል ዘቦ እዝን ጼው የተባለ በቄሙ ጨው እንዳይደለ ምናኔ እንደ ሆነ እዝነ ልቡና ያለው ያስተውል ፡፡

በእንተ ተገድፎተ በግዕ ፡፡

ምዕራፍ ፲፭ ፡፡

፩ ወቀርቡ ኀቤሁ መጸብሐን ወኃጥአን ይስ ዕምዎ ፡፡

፩ ቀራጮች ኃጥአንም ከርሱ ሊሰሙ ወደርሱ ቀረቡ ፡፡

፪ ወአንጐርጐሩ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን እንዘ ይብሉ ዝንቱሰ ኃጥአነ ይትዌከፍ ፡፡

፪ ፈሪሳውያንና ጸፎችም አንጐራጐሩ እንዲህ ሲሉ ይህስ ኃጢአተኞችን ይቀበላል ፡፡
ወይበልዕ ምስሌሆሙ ፡፡
ከርሳቸውም ጋራ ይበላል ፡፡

፫ ወመሰለ ሎሙ ዘንተ ምሳሌ ወከመዝ ይቤሎ፡፡
፫ እንዲህ ያለ ምሳሌ መስሎ መስሎ ነገራቸው
፬ እመቦ ብእሲ እምኔከሙ ዘቦ ምእት አባግዕ
፬ ከናንተ ወገን መቶ አባግዕ ያሉት ቢኖር ፡፡
ወለእመ ተገድፈ አሐዱ እምኔሆሙ ፡፡
ከመቶው አንዱ ቢጠፋበት ፡፡
አኮኑ የኀድግ ተስዓ ወተስዓተ ውስተ ገዳም ወየ ሐውር ይኅሥሥ ኀበ እንተ ተገድፈ ፡፡
ዘጠና ዘጠኙን ከበረሀ ትቶ ወደጠፋበት ሊሻ ይሄድ የለምን ፡፡
እስከ ይረከቦ ፡፡
እስኪያገኘው ድረስ ፡፡

፭ ወእምከመ ረከቦ ይጸውሮ ዲበ መትከፍቱ እንዘ ይትፌሣሕ ፡፡

፭ ባገኘውም ጊዜ ደስ ብሎት በትከሻው ይሸ ከመው የለምን ፡፡

፮ ወአቲዎ ቤቶ ይጼውዕ አእርክቲሁ ወጎሮ ፡፡
፮ ከቤቱም በገባ ጊዜ ጐረቤቶቹንና ወዳጆቹን ጠርቶ ፡
ወይቤሎሙ ተፈሥሑ ሊተ ፡
ደስ ይበላችሁ ይላቸዋል ፤
እስመ ረከብኩ በግዕየ ዘተገድፈኒ ፡፡
የጠፋብኝን በጌን አግኝቼዋለሁና ፡፡

፯ እብለክሙ ከመ ከመዝ ይከውን ዓቢይ ትፍ ሥሕት በሰማያት በበይነ ፩ዱ ኃጥእ ዘይኔሥሕ ፈድ

ፋዶ እምተስዓ ወተስዐቱ ጻድቃን እለ ኢይፈቅዱ ይነስሑ ።

፯ ንስሐን ከማይሹ ከዘጠና ዘጠኙ ጻድቃን ይልቅ ንስሐ በሚገባ ባንድ ኃጥእ እንደዚህ ያለ ደስታ በሰማይ ይደረጋል ብየ እነግራችኋለሁ ።

በእንተ ተረክቦተ ገመስ ።

፰ ወእመኒ ብእሲት ዘባቲ ዓሥሩ ጠፉልሐ አግሙስ ።

፰ እንደዚሁም ሁሉ ዐሥር ምዝምዝ የወርቅ ቀለበት ያላት ሴት ብትኖር ።
ወለእመ ትገድፈታ አሐቲ እምኔሆን ።
ካሥሩ አንዲቱ ብትጠፋባት ።
አኮኑ ታሐቱ ማሕቶተ ወትፌነቅል ኵሎ ንዋያ ዘውስተ ቤታ ወትኮስትር ወትኀሥሥ እስተሐሚማ ።
መብራት አብርታ ቤቷን ጠርጋ ዕቃዋን አውጥታ ፡ ትሻታ ትፈልገው የለምን ።
እስከ ትረክበ ።
እስከታገኘው ድረስ ።

፱ ወእምከመ ረከበት ትጼውዕ አእርክቲሃ ወአግዋሪሃ ።

፱ ያገኘችው እንደሆነ ጐረቤቶቿን ወዳጆቿን ጠርታ ።
ወትቤሎሙ ተፈሥሑ ሊተ ።
ከኔ ጋራ ደስ ይበላችሁ ።
እስመ ረከብኩ ገመስየ እንተ ተገድፈተኒ ።
የጠፋብኝን ቀለበቴን አግኝቻታለሁና የምትላቸው አይደለምን ።

፲ እብለክሙ ከመ ከማሁ ይከውን ፍሥሐ በሰማያት በቅድመ መላእክተ እግዚአብሔር በእንተ ኢሐዱ ኃጥእ ዘይኔስሕ ።

፲ ንስሐ ሰለሚገባ ሰለ ፩ድ ኃጥእ በእግዚአብሔር መላእክት ዘንድ እንዲህ ያለ ደስታ ይደረጋል ብየ እነግራችኋለሁ ። ሐተታ ማቴዎስ መቶ አለ ። ሉቃስ ዐሥር አለ እንደምን ነው ቢሉ መቶው የኃጥ አለቃ ዐሥር ደምሳሽ አለቃ አላቸው ከመቶው የኃጥ አለቃ አንዱ ዲያብሎስ ወርዷልና ። ማቴዎስ መቶ አለ ካሥሩ ደምሳሽ አለቃ አንዱ ዲያብሎስ ወርዷልና ሉቃስ እንዲህ አለ አንድም በከተማ ዐሥር በነገድ መቶ ናቸውና ካሥሩ ከተማ አንዱ ዲያብሎስ ወርዷልና ሉቃስ ዐሥር አለ ከመቶው ነገድ አንዱ ዲያብሎስ ወርዷልና መቶ አለ ።

በእንተ ተኀጕሎቱ ወተመይጦቱ ለወልድ ።

፲፩ ወይቤሎሙ ካዕበ እግዚእ ኢየሱስ አሐዱ ብእሲ ቦቱ ክልኤቱ ደቂቅ ።

፲፩ ላንድ ሰው ሁለት ልጆች ነበሩት

፲፪ ወይቤሎ ዘይንእስ ወልዱ ለአቡሁ አባ ሀበኒ መክፈልተ ርስትየ ዘይረከበኒ እምንዋይከ

፲፪ ታናሹ ልጁ አባቱን አባቴ
ከገንዘብህ የሚደርሰኝን ክፍለህ ስጠኝ አለው ።
ወከፈሎ መክፈልቶ እምንዋዩ
ገንዘቡንም ከፍሎ ሰጠው ።

፲፫ ወእምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል አስተጋብአ ኵሎ ንዋዮ ዝኩ ወልዱ ዘይንእስ ሖረ ወነገደ ርኁቀ ብሔረ ።

፲፫ ታናሽ ልጁ ከጥቂት ቀን በኋላ ገንዘቡን ሁሉ ሰብስቦ ወደሩቅ አገር ሄደ ።
ወበህየ ዘረወ ወአማሰነ ኵሎ ንዋዮ እንዘ የሐዩ በምርዓት በዚያም አገር በድርዓት እየኖረ ገንዘቡን ሁሉ አበላሸ ።

፲፬ ወእኅሊቆ ኵሎ ንዋዮ መጽአ ረኃብ ዓቢይ ውስተ ውእቱ ብሔር ።

፲፬ በድርዓት እየኖረ ገንዘቡን ሁሉ ከጨረሰ በኋላ በዚያ አገር ጽኑ ረኃብ ሆነ ።
ወተፀነሰ ፡ ተቸገረ ።

፲፭ ወሖረ ወተፀምደ ኀበ አሐዱ እምሰብእ ውእቱ ብሔር ።

፲፭ ሄዶም በዚያ አገር ካሉ ሰዎች ላንዱ ተገዢ ሆነ ።
ወፈነዎ ውስተ ዓጸደ ወፍሩ ይርአይ አኅርወ ።
እርያ ይጠብቅ ዘንድ እርሱ ወደሚሠማራበት እስማራው ።

፲፮ ወፈተወ ይጽገብ እምሐመረ ጽራዕ ዘይሴስዩ አኅርው ።

፲፮ እሪያዎች የሚመገቡትን ተረን ቃሞ ሊመገብ ወደደ ።
ወአልቦ ዘይሁቦ
ያኑ ቅሉ የሚሰጠው የለም አለ እሪያዎች እየተቀደሙ እየበሉበት አንድም በቃህ የሚለው አጣ ።
አንድም እህል የሚሰጠው አላገኘም ።

፲፯ ወሐለየ በልቡ ወይቤ ሚመጠን አግብርቲሁ ለአቡየ እለ ያተርፍዎ ለእክል ።

፲፯ በልቡ አስቦ በቃሉ እንዲህ አለ ባባቴ ቤት እህል ተርፏቸው የሚኖሩ ያባቴ ቤተሰዎች ምን ያህላሉ ።
ወአንሰ እመውት በረኃብ በዝየ ።
እኔ ግን እህል አጥቼ በባዕድ አገር በረኃብ እሞታለሁ ።

፲፰ አትንሣእ ወእሐውር ኀበ አቡየ ።
፲፰ ተነሥቼ ወደ አባቴ እሄዳለሁ
ወእብሎ አባ አበስኩ በሰማይኒ ወበቅድሜከኒ ።
አባቴ አንተንም ፈጣሪዬንም በደልኩ ።

፲፱ ወኢይደልወኒ እንከ እሰመይ ወልደከ ።
፲፱ እንግዲህ ወዲህ ልጅህ ልባል አይገባኝም
አላ ረስየኒ ከመ አሐዱ እምአግብርቲከ ።
ከባሮችህ እንዳንዱ ቊጠረኝ እንጂ እለዋለሁ ብሎ።

፳ ወተንሥአ ወሖረ ኀበ አቡሁ ።
፳ ተነሥቶም ወይአባቱ ሄደ ።
ወርእዮ አቡሁ እምርኁቅ ምሕሮ ።
እባቱም በሩቅ አይቶ አዘነለት ።
ወሮጸ ወሐቀፎ ከማዶ ወሰዓሞ ።
ፈጥኖ አንገቱን አቅፎ ሳመው

፳፩ ወይቤሎ ወልዱ ለአቡሁ አባ አበስኩ በሰማይኒ ወበቅድሜከኒ ።

፳፩ ልጁም አለ አባቴ አንተንም ፈጣሪዬንም በደልኩ ።
ወኢይደልወኒ እንከ እሰመይ ወልደከ ።
ከእንግዲህ ወዲህ ልጅህ ልባል አይገባኝም ።
አላ ረስየኒ ከመ አሐዱ እምአግብርቲከ ።
ከባሮችህ እንዳንዱ ቊጠረኝ እንጂ አለው ።

፳፪ ወይቤሎሙ አቡሁ ለአግብርቲሁ አምጽኡ ፍጡነ አልባሰ ቅድወ ወአልብስዎ ።

፳፪ አባቱ ባሮቹን እለ ያማረውን ግምጃ ቶሎ ጥታችሁ ፈጥናችሁ አልብሱት ።
ወደዩ ሕልቀተ ውስተ አፃብዒሁ ወአሣዕነ ውስተ እገሪሁ ።
ቀለበት ከጣቱ ጫማ ከእግሩ አግቡለት አላቸው ።

፳፫ ወአምጽኡ ላሕመ መግዝዓ ወጥብሑ ።
፳፫ ማለፊያ ፍሪዳ አምጥታችሁ እረዱ ።
ንብላዕ ወንትፈሣሕ ምስሌሁ ።
በልተን ከሱ ጋራ ደስ ይበለን

፳፬ እስመ ዝንቱ ወልድየ ሞተሂ ወሐይወ ።
፳፬ ይህ ልጄ ሞተ ካልሁት በኋላ ደኑዋልና ።
ተኃጕለሂ ወተረክበ ።
ጠፋ ካልሁት በኋላ ተገኝቷልና ።
ወአኃዙ ይትፈሥሑ ።
ተድላ ደስታ ያደርጉ ጀመሩ ።

፳፭ ወወልዱሰ ዘይልሕቅ ሀሎ ውስተ ሐቅል ።
፳፭ ታላቁ ልጁ ግን ከበረሀ ነበር ።
ወሶበ በጽሐ ወቀርበ ኀበ ጸንፈ ሀገር ።
ተመልሶ ከከተማ ሊገባ በቀረበ ጊዜ ።
ሰምዓ ዕንዚራ ወማኅሌተ ።
የዘፈን የጫወታ ድምፅ ሰማ ።

፳፮ ወጸውዓ አሐደ እምአግብርተ አቡሁ ወይቤሎ ምንትኑ ዝ ዘእሰምዕ ።

፳፮ ካባቱ ባሮች አንዱን ጠርቶ ይህ የምሰማው ምንድርነው አለው ።

፳፯ ወይቤሎ እስመ አተወ እኁከ ወጠብሐ አቡከ ላህመ መግዝዓ ።

፳፯ ወንድምህ መጥቷልና አባትህ ሚልዓች አርዶለታል ።
እስመ ረከቦ ሕያዎ ።
ሞቶ ካለው በኋላ ደኑዋል ጠፋ ካለው በኋላ ተገኝቷልና አለው ።
፳፰ ወተምዓ ወአብየ በዊአ ።
፳፰ ተቆጥቶ አልገባም አለ ።
ወወፅአ አቡሁ ወአስተብቍዖ ።
አባቱም ወጥቶ ማለደው ።

፳፱ ወአውሥአ ወይቤሎ ናሁ መጠነ ዝ ዓመታተ ተቀነይኩ ለከ ።

፳፱ እነሆ ይህን ያህል ዘመን ተገዛሁልህ ።
ወኢኃለፍኩ ወኢተዓደውኩ እምትእዛዝከ ግሙራ ።
ከቶ ከትእዛዝህ አልወጣሁም ትእዛዝህን አላፈረስኩም
ወሊተሰ ኢወሀብከኒ መሐስአ ጠሊ ጥቀ በዘእትፈሣሕ ቦቱ ምስለ አዕርክትየ ወአብያጽየ ።
ለኔ ግን ከባልንጀሮቼ ከወዳጆቼ ጋራ ደስ በሚለኝ ገንዘብ ደስ ይለኝ ዘንድ የፍየል ጠቦት ስንኳ አልሰጠኸኝም ።

፴ ወእቲዎሰ ዝንቱ ወልድከ ዘአኅለቀ ኵሎ ንዋየከ ምስለ ዘማት ጠባሕከ ሎቱ ላህመ መግዝዓ ።

፴ በድርአት እየኖረ ገንዘብህን ያበላሸ ይህ ልጅህ በተመለሰ ጊዜ ግን ሚልዓች አረድክለት ።

፴፩ ወይቤሎ አቡሁ ወልድየ አንተሰ ዘልፈ ሀሎከ ምስሌየ ።

፴፩ እባቱም አለው ልጄ አንተስ ዘወትር ከኔ ጋራ ትኖራለህ ።
ወኵሉ ዘዚአየ ዚአከ ውእቱ ።
የእኔም ገንዘብ ሁሉ ገንዘብህ ነው ።

፴፪ ወባሕቱ ርቱዕሰ ንትፈሣሕ ።
፴፪ አገባብስ በዚህ ደስ ሊለን ይገባል ።
እስመ ዝንቱ እኁከ ሞተሂ ወሐይወ ተኃጕለሂ ወተረክበ ።

ይህ ልጄ ከሞተ በኋላ ድንዋል ከጠፋም በኋላ ተገኝቷልና አንድም አሐዱ ብእሲ አያልክ መልስ ። ብእሲ የተባለ ጌታ ነው እንደ ታላቅ ልጅ ጸሐፍት ፈሪሳውያን እንደ ታናሽ ልጅ ኃጥአን መጸብሐን ናቸው ። እባ ሀበኒ መክፈልተ ርስትየ ።

ለሁሉም እንዲያሻቸው ዐውቆ ሕግ መሥራቱን
መናገር ነው ።

ወእምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል ። ኃጥአን መጸብ
ሐን ሕጉን ተቀብለው ጥቂት ቀን ከኖሩ በኋላ ወደ
አሕዛብ ሀገር ሄዱ ። ወበህየ ዘረወ በአምልኮተ ጣዖት
በገቢረ ኃጢአት እየኖሩ ሕጉን አፈረሱ ። ወአኅሊቆ
ሕጉን ካፈረሱ በኋላ ። መጽአ ረኃብ ዓቢይ የሚያ
ስተምራቸው አጡ ። ወተፀነሱ ከትምህርት ተቸገሩ
ወሖረ ወተጸምደ በዚያ ሀገር ካሉ ሰዎች ለአንዱ
ተገዢ ሆኑ ። ወፈነዎ ውስተ ዓጸደ ወፍሩ ይርአይ
አኅርወ ። አሕዛብን ይመስሉ ዘንድ ወደሚሠሩት
ኃጢአት ወደሚያመልኩት ጣዖት አሠማሯቸው ።
ወፈነወ ይጸገብ የሚሠሩትን ኃጢአት ሊሠሩ የሚ
ያመልኩትን ጣዖትሊያመልኩ ወደዱ ሠሩ አመለኩ።
ወአልቦ የሚያስተምራቸው አጡ ። በልቡናቸው
አሰበው እንዲህ አሉ ባባታችን ቤት በቤተ መቅ
ደስ እህል ትምህርት ተርፏቸው የሚኖሩ ምእመ
ናን ምን ያህላሉ ። ወአንሰ አመውት ። እኛ ግን
በአሕዛብ አገር የሚያስተምረን አጥተን በነፍስ
እንሞታለን ። እትነሣእ ወእሐውር ። ንስሐ ገብ
ተን ወደ አባታችን ወደ እግዚአብሔር ተመልሰን
ወእብሎ መለኮትህን ትስብእትህን በደልን ወኢይደ
ልወኒ ከእንግዲህወዲህ ወልድየ ዘበኵርየ ከተባሉ ከእ
ስራኤል ልንቈጠር አይገባንም ። አላ ከመ አሐዱ
ከተንሣሕያን አሕዛብ እንዳንዱ ቍጠረን እንጂ
እንለዋለን ብለው ሄዱ ። ወርእዮ አቡሁ ኣላበጀ
ንም ማለታቸውን አውቆ አዘነላቸው ወሮጸ ፈጥኖ
በረድኤት ተቀበላቸው ።

ወሰዓሞ በፍቅር ወደዳቸው ወይቤሎ ወልዱ
መለኮትህን ትስብእትህን በደልን ወኢይደልወኒ ።
ከእንግዲህ ወዲህ ወልድየ ዘበኵርየ ከተባሉ ከእስ
ራኤል ልንቈጠር አይገባንም ። አላ ረስየኒ ከተንሣ
ሕያን አሕዛብ እንዳንዱ ቍጠረን እንጂ አሉት
ወይቤሎ አቡሁ ። ጌታ ሐዋርያትን አልባስ ቅድወ
ልጅነት እንዲሰጣቸው ወደዩ ኅልቀተ ሃይማኖትን
እንዲይዙ ወአሣዕነ ምግባር እንዲሠሩ አድርጓቸው
አላቸው ።

ወአምጽኡ ላህመ ታምራት አድርጉላቸው እስመ
ዝኩ ወልድየ ኃጥአን መጸብሐን ከሞቱ በኋላ ድነ
ዋል ከጠፉ በኋላ ተገኝተዋልና ። ወአኃዙ ይትፌ
ሥሑ በትምህርት ተድላ ደስታ ያደርጉ ጀመር ወወ
ልዱስ ፈሪሳውያን ግን እሪትን እንጠብቃለን ይሉ
ነበር ወአቲዎ ። በወንጌል እናምናለን ብለው ባሉ
ጊዜ ሰምዓ እንዚራ ለኃጥአን መጸብሐን የተደረ
ገውን ታምራት ሰሙ ወጸውዓ አሐደ ፡ አንዱ
እንዱን ጠርቶ ይህ የምሰማው ምንድርነው አለው ።
ወይቤሎ እስመ አተወ ። ኃጥአን መጸብሐን በወ
ንጌል ሰላሙ ። ወጠብሐ ። ደኃጉን ጠቃቅንን ተአ
ምራት አድርጎላቸዋል ። እስመ አተወ ከሞቱ በኋላ
ድነዋል ። ከጠፉ በኋላ ተገኝተዋልና አለው ።

ወተምዓ ወአበየ ዝሰ ኃጥአኑ ይትዌከፍ ኅበ
ብእሲ ኃጥእ ቦአ ያለማለታቸውን መናገር ነው ።
ወመጽአ አቡሁ ወአኮ ጥዑያን ማለቱን መናገር
ነው ። ናሁ መጠነዝ ይህን ያህል ዓመት ባሥሩ
ቃላት ጸንተን ተገዛንልህ ወኢኃለፍኩ ዓሠርቱ ቃላ
ትን አላፈረስንም ። ወሊተሰ ለኛ ግን ከባልንጀር
ቻችን ጋራ ደስ በሚለን ገንዘብ ጥቂት ስንኳ ተአ
ምራት አላደረግህልንም ወአቲዎሰ በአምልኮተ
ጣዖት በገቢረ ኃጢአት እየኖሩ ሕግን ያፈረሱ ኃጥ
አን መጸብሐን በተመለሱ ጊዜ ግን ደኃጉን ጠቃ
ቅንን ተአምራት አደረግህላቸው ።

ወልድየ አንተሰ ሀሎከ ምስሌየ ወኵሉ ዚአየ
ኢመጻእኩ እጸውዕ ጻድቃነ ማለቱን መናገር ነው
ወባሕቱ ርቱዕሰ ሕሙማን ይፈቅድዎ ለዓቃቤ ስራይ
አላ ኃጥአን ለንስሐ ማለቱን መናገር ነው ። አን
ድም አሐዱ ብእሲ ብለህ መልስ ከልኤቱ ደቂቅ
የተባሉ እንደ ታላቅ ልጅ ባሕታውያን እንደ ታናሽ
ልጅ ሰብአ ዓለም ናቸው ወይቤሎ ዘይንእስ ለሁሉም
ሕግ እንዲያሻቸው አውቆ ሕግ መሥራቱን መና
ገር ነው ወእምድኅረ ኅዳጥ ። ሰብአ ዓለም ሕጉን
ተቀብለው ጥቂት ቀን ከኖሩ በኋላ ወደ አሕዛብ
አገር ሄዱ ። ወበህየ ዘረወ በኃጢአት እየኖሩ ሕጉን
አፈረሱ ወአኅሊቆ ብለህ ወኢይደልወኒ እስካለው
ጣዖትን ብቻ እየተውከ አውርድ ወኢይደልወኒ።
ከእንግዲህወዲህ በወልድ ውሉድ በክርስቶስ ክርስ
ቲያን ከተባሉት ልንቈጠር አይገባንም አላ ረስየኒ
ከተነሳሕያን አሕዛብ ቍጠረን እንጂ እንሊዋለን
ብለው ሄዱ ።

ወርእዮ አቡሁ እንዳለፈው ወአምጽኡ አል
ባስ ቅድወ ልጅነት እንዲመለሰላቸው ወደዩ ኅል
ቀተ ሃይማኖትን እንዲረዱ ምግባር እንዲሠሩ
አድርጉላቸው ወአምጽኡ ላህመ ሥጋ
ውን ደሙን ስጧቸው ንብላዕ በልተን ደስ ይበ
ለን እስመ ዝንቱ ወልድየ ሰብአ ዓለም ከጠፉ
በኋላ ተገኝተዋል ከሞቱ በኋላ ድነዋልና ወአኃዙ
በነፍስ ተድላ ደስታ ያደርጉ ጀመር ወወልዱሰ
ዘይልሕቅ ባሕታውያን ግን በበረሀ ነበሩ ወአቲዎ
ወደዓለም በመረመሩ ጊዜ ሰምዓ ዕንዚራ ለሰብአ
ዓለም የተደረገውን ሰሙ ወጸውዓ ወይቤሎ አንዱ
አንዱን ጠርቶ ይህ የምንሰማው ምንድርነው ብሎ
ጠየቀው ። ወይቤሎ እስመ አተወ ሰብአ ዓለም
ከጠፉ በኋላ ተገኝተዋል ከሞቱ በኋላ ድነዋል ።

ወጠብሐ ሎቱ ሥጋውን ደሙን ስጥቷቸዋልና እስመ ረከበ ከጠፉ በኋላ ተገኝተዋል ከሞቱ በኋላ ድነዋልና ። ወተሞዓ ቁጣ የለም አደነቁ ። ወአበየ በዊአ በዚያው ጸኑ ወመጽአ አቡሁ ጌታቸው በዚያው አጸናቸው ወአውሥአ ወይቤሎ ይህን ያህል ዘመን በተባሕትዎ ጸንተን ተገዛንልህ ወኢኃለፍኩ ዐሠርቱ ቃላትን አላፈረስንም ወሊተስ ለኛ ግን ጥቂት ስንኳ ተአምራት አላደረግህልንም ወኢቲዎ በኃጢአት እየኖሩ ሕግህን ያፈረሱ ሰብአ ዓለም በተመለሱ ጊዜ ግን ሥጋህን ደምህን ሰጠሀቸው አሉት ። ወይቤሎ አቡሁ በናንተስ አድሬባችሁ እኖራለሁ ወኵሉ ዚአየ ተአምራቱንም እናንተው ታደርጉታላችሁ እገባብስ በሰብአ ዓለም ደስ ሊለን ይገባል ።

እስመ ዝንቱ ሰብአ ዓለም ከጠፉ በኋላ ተገኝተዋል ከሞቱ በኋላ ድነዋልና እንድም አሐዱ ብኺ ሲ ብለህ መልስ ክልኤቱ ደቂቅ የተባሉ መላእክትና ደቂቀ አዳም ናቸው እንደ ታላቅ ልጅ መላእክት እንደ ታናሽ ልጅ ደቂቀ አዳም ናቸው ። አስተሐምሞተ አኃው ዓቢያን ከመ ዘለንኡሳን እንዲል ወይቤሎ ወልዱ ለሁሉም እንዲያሻቸው አውቆ ሕግ መሥራቱን መናገር ነው ትርጓሜው አይለወጥም

## ምዕራፍ ፲፮ ።

### በእንተ መጋቢ ዘኢይትአመን ።

፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ ፩ዱ ብእሲ ባዕል ቦቱ መጋቢ ወከመዝ ኮነ መጋቢሁ ዘያማስን ንዋዮ ።

፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለደቀ መዛሙርቱ እንዲህ አላቸው ላንድ ባለጸጋ ገንዘቡን የሚያበላሽ አንድ ሹም ነበረው ።
ወአስተዋደይዎ ኀቤሁ ከመ ይዘሩ ኵሎ ንዋዮ ።
ገንዘብህን ሁሉ ያበላሻል ብለው ከሰሱት ።

፪ ወጸውዖ እግዚኡ ወይቤሎ ምንትኑዝ ዘእሰምዕ በእንቲአከ ፤

፪ ጌታው ጠርቶ ይህ የምሰማብህ ነገር ምንድር ነው አለው ።
አግብእ እንከሰ ሐሳበ ምግብናከ ።
እንግዲህስ ወዲህ ሹመትህን አበርከተኝ ።
እስመ ኢትክውነኒ እንከ መጋቤ ሊተ ።
ከእንግዲህ ወዲህ ሹም አትሆነኝምና አለው ።

፫ ወሐለየ ውእቱ መጋቢ ።
፫ ያም ሹም አሰበ ።
ወይቤ ምንተ እሬሲ ።
ምን ላድርግ አለ ።
ናሁ ይሥዕረኒ እግዚእየ እምግብናየ ።
እነሆ ጌታዬ ከሹመቴ ይሽረኛል ።
ሐሪሰኒ ኢይክል ።
እርሻ አልችል ።
ወሰኢለኒ አኃፍር ።
እንዳለምንም አፍራለሁ ።

፬ አአምር እንከሰ ዘእገብር ።
፬ እንግዲህስ ወዲህ የማደርገውን አውቃለሁ
እምከመ ሠዓረኒ እግዚእየ እምግብናየ ።
ጌታዬ ከሹመቴ የሻረኝ እንደሆነ ።
ከመ ይትወከፉኒ ውስተ አብያቲሆሙ ።
በቤታቸው ይቀበሉኝ ዘንድ ብሎ ።

፭ ወጸውዖሙ ለእለ ይፈድይዎ ዕዳ ለእግዚኡ።
፭ የጌታውን ባለዕዳዎች ጠርቶ
ወይቤሎ ለቀዳማዊ ሚመጠነ ዕዳ ትፈድዮ ለእግዚእየ።
አንዱን አንተ ለጌታዬ ምን ያህል ትከፍለዋለህ አለው።
ወይቤሎ ፻ተ በመሥፈርተ ባዶስ ቅብዓ ።
መቶ ማድጋ ዘይት ነው አለው እንድም ዘትፈድዮ የምትከፍለው ምን ያህል ነው አለው መቶ ማድጋ ዘይት አለብኝ አለው ።
ወይቤሎ ናሁኬ መጽሐፍከ ።
እነሆ ደብዳቤህ ።
ንበር ወጸሐፍ ፍጡነ ሃምሳ ላዕሌከ ።
ሃምሳ ነው ብለህ ፈጥነህ ጻፍ ሃምሳው ይቅርልህ አለው ።

፮ ወይቤሎ ለካልኡ አንተስ ሚመጠነ ዕዳ ትፈድዮ ለእግዚእየ ።

፮ ሌላውንም አንተስ ለጌታዬ ምን ያህል ትከፍለዋለህ ። ዘትፈድዮ የምትከፍለው ምን ያህል ነው አለው ።
ወይቤሎ ምእተ በመሥፈርተ ቆሮስ ሥርናየ ።
መቶ ቆሮስ ሥንዴ አለብኝ አለው ሐተታ አንዱ ቆሮስ ያሥራ ሁለት በቅሎ ጭነት የሚያነሣ ዐሥራ ሁለት ጫን ነው ።

፯ ወይቤሎ ናሁኬ መጽሐፍከ ።
፯ እነሆ ደብዳቤህ ።
ንበር ወጸሐፍ ፍጡነ ሰማንያ ላዕሌከ ።
ሰማንያ ነው ብለህ ፈጥነህ ጻፍ ሃያው ይቅርልህ አለው ።

፰ ወንዕዶ እግዚአብሔር ለመጋቤ ዓመፃ ።
፰ እግዚአብሔርም ይህን የግፍ ሹም አመሰገነው።
እስመ ከመ ጠቢብ ገብረ ያዋቂ ሥራ ሠርቷልና ።
እስመ ውሉደ ዝዓለም ይጠበቡ እምውሉደ ብርሃን በዓለሞሙ ።
ከብርሃን ልጆች ከጻድቃን ይልቅ የዚህ ዓለም ልጆች በዓለማቸው የሚራቀቁ ስለሆኑ ሐተታ እኒያ ይህን ዓለም በወዲያው ዓለም ለውጠው ይገባሉ እኒህ

ግን በወዲሁም ሰጥተው መጽውተው በወዲያውም ደስ ይላቸዋልና አንድም አሐዱ ብእሲ እያልክ መልሰ ባዕል የተባለ ጌታ ነው ፨ ለጌታ ባለጺጋ ሹም አለው ጌታ ሰውን ባለጺጋ ማድረጉ በድኆች ላይ መሾሙ ነውና ፨ ወእስተዋደይዎ ካዝማሪ ከዘዋሪ ጋራ እየበላ አይሰጥም አይመጸውትም ብለው ነዳያን ከሰሱት ወጸውዖ ወይቤሎ ፤ ጌታም በደዌ ጠርቶ ይህ የምሰማብህ ምንድነው አግብእ እንከ ሐሳበ ምግብናከ ፨ ሹመትህን አበርክተኝ ፨ እስመ ኢትክውነኒ እንግዲህ ሹም አትሆነኝምና አለው ፨ ወሐለየ እንግዱህ ምን ሳድርግ ፥ ናሁ ይሥዕረኒ ፤ እነሆ ጌታዬ ነፍሴን ከሥጋዬ ይለያታል ሐሪሰሂ ገሃነም ከገቡ በኋላ ሃይማኖት ይዞ ምግባር ሠርቶ ክብር ማግኘት መንግሥተ ሰማያት መግባት አይቻልም ፨

አእምር እንግዲህስ ወዲህ የምሠራውን አውቃለሁ ፨እምከመ ሠዐረኒ ጌታዬ ነፍሴን ከሥጋዬ የለያት እንደሆነ ከመ ይትወከፉኒ ነዳያን በቤታቸው በመንግሥተ ሰማይ ይቀበሉኝ ዘንድ በርሳቸው ምክንያት የምትወረስ ስለሆነች አብያቲሆሙ አለ ፨ ዕድው ድኩማን የሐንጻ አብያተ እንዲል ፨ ወጸውዖሙ ኃጢአት ሠርተው ፍዳ የሚቀበሉትን ጠርቶ ወይቤሎ ለቀዳማዊ አንዱን ምን ቸግሮሃል አለሁ ምግብ አለኝ ልብስ የለኝም ልብስ አለኝ ምግብ የለኝም አለው ፨ ወይቤሎ ናሁኬ የቸገረህን ውሰድ አለው ፨ ወይቤሎ ለካልዐሂ ሌላውንም አንተስ ምን ቸግሮሃል የቸገረህ ምንድርነው አለው ልብስ ምግብ አለኝ ከልብስ ከምግብ ቀሚስ ሰናፌል ቸግሮኛል አለው ፨ ወይቤሎ ናሁኬ የቸገረህን ውሰድ አለው ፨ ወንዕዶ እግዚአብሔር በኃላፊ ክብት የተሾመ ባለጸጋን እግዚአብሔር አመሰገነው እስመ ከመ ጠቢብ ገብረ ያዋቂ ሥራ ሠርቷልና ፨ እስመ ውሉደ ዝዓለም ይጠበቡ እምውሉደ ብርሃን በዓለሞሙ ከውሉደ ብርሃን ከጻድቃን ይልቅ ሰብአ ዓለም በዓለማቸው የሚራቀቁ ስለ ሆነ ፨ ሐተታ ጻድቃን በዚህ ዓለም የወዲያኛውን ዓለም ሰውጠው ይገባሉ እሊህ ግን ይህ ሳይቀርባቸው መጥተው ዐሥራት በኵራት አውጥተው ያን ዓለም ይወርሱታልና ታሪክ እንደ ፩ድ ንጉሥ ያንድ አገር ሰዎች ዓመት አንግሠው ከደሴት ያግዙታል በረኃብ በጽም ይሞታል አንድ ንጉሥ ግን ይህን ያውቃልና ከነገሠባት ቀን ጀምሮ ገንዘብ እየሰደደ ሲያከማች ኖረ እንደ ልማዳቸው አጋዙት ያኖረውን እየተመገበ በተድላ የሚኖር ሆኑዋል እንደ ዚህም ሁሉ በዚህ ዓለም ቢሰጡ ቢመጸውቱ በወዲያኛው ክብር ይገኛል ፨ አንድም አሐዱ ብእሲ ብለህ መልስ ብእሲ አይለወጥም ለጌታ ሹም አለው መምህረ ንስሐ ነው አያስተምርም ንስሐን ሥጋውን ደሙን አይሰጥም ብለው ምእመናን ከሰሱት ወጸውዖ ጌታ በደዌ ጸራው ከዚህ በላይ አይለወጥም ወጸውዖሙ ፨ ኃጢአት ሠርተው ንስሐ የሚቀበሉትን ጸራቸው ወይቤሎ ለቀዳማዊ አንተ ምን ኃጢአት ሠርተሃል የሠራኸው ኃጢአት ምንድነው አለው ፨ ወይቤሎ ምእተ በመሥፈርተ ባዶስ ፥ ፍጹም ኃጢአት ሠርቻለሁ አለው ወይቤሎ ጸሐፍ ላዕሌከ ሃምሳ እኩሉን ጹም እኩሉን እኔ እጾምልሃለሁ አለው ፨ ወይቤሎ ለካልዑ አንተስ ምን ኃጢአት ሠርተሃል አለው ወይቤሎ ምእተ ፨ ፍጹም ኃጢአት ሠርቻለሁ የሠራሁት ኃጢአት ፍጹም ነው አለው ፨ ሦስቱን እጅ አንተ ጹም ቢሶውን እኔ እጾማለሁ አለው ፤ ተመየጥ አንተ ወእነ እትዌከፍ ሞተ ህየንቴከ በከመ ተወክፈ ክርስቶስ ህየንቴየ ወህየንተ ኵሎሙ እንዲል ወንዕዶ እግዚአብሔር በዓመፃ የሚፈርድ መምህረ ንስሐን እግዚአብሔር አመሰገነው እስመ ጠቢብ ፨ ዐዋቂ እንደ መሆኑ ያዋቂ ሥራ ሠርቷልና እስመ ውሉደ ዝዓለም ፨ ከውሉደ ብርሃን ከጻድቃን ይልቅ ሰብአ ዓለም በዓለማቸው የሚራቀቁ ስለ ሆኑ ፨ ሐተታ ጻድቃን ራሳቸውን ጠብቀው ብቻቸውን ነው መንግሥተ ሰማይ የሚገቡ መምህራን ግን ብዙ አስተምረው አሳምነው አጥምቀው ወደኃጢአት ወደክህደት የሄደውን በንስሐ መልሰው ብዙ ሁነው ነውና ፨

፱ ወእነሂ እብለክሙ ግበሩ ለክሙ አዕርክተ እምንዋየ ዓመፃ ፨

፱ በኃላፊ ከብት ወዳጅ ግዙበት አላችኋለሁ ከመ አመ የሐልቅ ንዋይክሙ ይትወከፉክሙ እሙንቱሂ ውስተ አብያቲሆሙ ዘለዓለም ፨ ዘለዓለም ገንዘባችሁን ሰጥታችሁ በጨረሳችሁ ጊዜ እርሳቸውም በቤታቸው በመንግሥተ ሰማይ ይቀበሏችሁ ዘንድ ታሪክ እንዳንድ ባለጸጋ ፥ ከብሮ የነበረ ተዋርዶ አግኝቶ የነበረ አጥቶ ሳለ ንጉሥ አጸራው ፥ ከብሬ የነበረ ተዋርጄ አግኝቼ የነበረ አጥቼ ልብስ ስንቅ የምሰጥው ገጸ በረከት የለኝ ምን አደርጋለሁ አለ ፨ ከራሱ አብልጦ የሚወደው እንደ ራሱ አድርጎ የሚወደው ንቆ አጥቅቶ የሚወደው ወዳጆች ነበሩት ከራሱ አብልጦ ከሚወደው ወዳጁ ዘንድ ሂዶ አንድ ግርባብ ሰጥቶ ሰደደው እንደራሱ አድርጎ ከሚወደው ቢሄድ አልቅሶ ሸኝቶ ሰደደው ንቆ አጥቅቶ ከሚወደው ወዳጁ ዘንድ ሂዶ ምንስ ንቄ አጥቅቼ ብወደው ወዳጄ አይደለምን አንድ ነገር ቢሰጠኝ ብሎ ነገረው እርሱም አለው ሁሉ ከኔ አለልህ ልብስ ብትል ስንቅ ገጸ በረከት ብትል ውሰድ እንዲህም አድርጌ እኔ አልቀርም ከንጉሡ ባለሟል ነኝ ባለሟሎቹም ወዳጆቼ ናቸው ሂጂ ነገርህን አቀናልሃለሁ ብሎ ሂዶ ነገሩን አቅንቶለታል፨ ባለጸጋ የተባለ ሰው ሁሉ ነው ንጉሥ የጌታ ምሳሌ እንደማስጠራቱ ጌታ ሰውን በሞት መጥራቱን መናገር ነው ፨ ከራሱ

እብልጦ የሚወደው ወዳጅ የተባለ ገንዘብ ነው ። እርሱ ከጦርነት ሲሄድ ገንዘቡን ከገዳም አግብቶት ይሄዳልና ። ግርባብ እንደሰጠው የከፈን ያህል ይዞ ይሄዳልና እንደራሱ አድርጎ የሚወደው ወዳጅ የተባለ ሚስትና ልጅ ናቸው ። እልቅሶ ሸኝቶ እንደሰደደው አልቅሰው ወደመቃብር ሸኝተውት ይመለሳሉና ። ንቆ አጥቅቶ የሚወደው ወዳጅ የተባለ ምጽዋት ነው የሚያወርሰው ክብር አልታየምና ፡ የሚሻውን ሁሉ እንደሰጠው በምጽዋት ዋጋ መገኘቱን መና ገር ነው ። ለባለሟሎቹ እንደነገረለት ምጽዋት በጻድቃን በሰማዕታት በመላእክት ስም ይደረጋ ልና ለንጉሡ እንደነገረለት ፍጻሜው በጌታ ነውና

፲ ወዘሰ በወኅድ ምእመን በብዙኅኒ ምእ መን ውእቱ ።

፲ በጥቂቱ የታመነ በብዙ የታመነ ይሆናልና። ወዘሰ በኅዳጥ ዓማፂ በብዙኅኒ ዓማፂ ውእቱ ።

በጥቂቱ ግን ያልታመነ በብዙውም ያልታመነ ነው ።

፲፩ ወሶበ በንዋየ ዓመፃ ሃይማኖት አልብ ከሙ በንዋየ ጽድቅ መኑ የአምነክሙ ።

፲፩ በሐሰት ክብት ካልታመናችሁ በውነተኛው ክብት ማን ያምናችኋል ማለት በሚያልፈው ገን ዘብ ካልታመናችሁ የማያልፈውን ማን ይሰጣች ኋል መንግሥተ ሰማያት ጽድቀ ዘልፈ የሆነ ብሏል ።

፲፪ ወእመሰ በነዋየ ባዕድ ሃይማኖት አልብክሙ ዘእሁ መኑ ይሁበክሙ ።

፲፪ በሌላው ክብት ካልታመናችሁ ገንዘቡን እምና ማን ይሰጣችኋል ። ሐተታ እሱ ከሞተ በኋላ ልጅ ሚስት ቢበሉት ቢጠጡት ቢለብሱት ባዕድ ነውና እንድም ካልሰጠለት ለዘራፊ ለገፋፊ ይሰጥበታልና ለዝንቱስ ዘይወስድዎ ሰረቅት ወፈ ያት እንዲል ።

፲፫ አልቦ ገብር ዘይክል ተቀንዮ ለ፪ቱ እጋ ዕዝት ማቴ ፮ ፡ ፳፬ ።

፲፫ ለሁለት ጌታ መገዛት የሚቻለው ባሪያ የለም ።

ወእመ እኮ ፩ደ ያፈቅር ወካልዖ ይጸልዕ ።

ይህ ቢሆን ግን አንዱን ይወዳል አንዱንም ይጠላል። ወእመ እኮ ለአሐዱ ይትኤዘዝ ወለካልዑ የዓቢ ። ይህም ባይሆን ላንዱ ይታዘዛል ለሁለተኛውም አይ ታዘዝም ኢትክሉኬ ለእግዚአብሔር ተቀንዮ እንዘ ንዋየ ታፈቅሩ ገንዘብ ስትወዱ ከተገኛችሁ ገንዘብ ከወደዳችሁ ለእግዚአብሔር መገዛት አይቻላችሁም።

በእንተ ተመድልዎት ዘፈሪሳውያን ።

፲፬ ወሰሚዖሙ ዘንተ ኵሎሙ ፈሪሳውያን ተቃ ጸብዎ ።

፲፬ ፈሪሳውያን ይህን ሰምተው ተጠቃቀሱበት።

እስመ መፍቀርያነ ንዋይ እሙንቱ ።

ገንዘብ ወዳዶች ናቸውና ዛሬስ ክብት አትገዙ የሚለን መጣ ብለው ።

፲፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አንትሙሰ ትጼደቁ ለዓይነ ሰብእ ።

፲፭ እናንተስ በሰው ዘንድ ደጋግ መስላችሁ ትታያላችሁ ።

ወእግዚአብሔር የአምር ልበክሙ ።

እግዚአብሔር ግን የልባችሁን ክፋት ያውቅባችኋል። እስመ ዘበኀበ ሰብእ ዓቢይ በኀበ እግዚአብሔር ትሑት ውእቱ ።

በሰው ዘንድ የከበረው በእግዚአብሔር ዘንድ የተ ዋረደ ነውና ፡ ታሪክ አንድ ንጉሥ ሁለት ልጆች ነበሩት በሚሞትበት ጊዜ ታናሹን እንግሡ ብሎ ሞተ አድልቶ አይደለም ብልህ ነው ሰው ማሳደር ያውቃል ብሎ ነው እንጂ ከዕለታት ባንድ ቀን በፈረስ በሠረገላ ሁኖ ሲሄድ ታላቅ ወንድሙ ተከ ትሎት ሄደ ከመንገድ ቁረንጮ የለበሰ ባሕታዊ አገኘ ከፈረስ ከሠረገላ ወርዶ ከእግሩ ወድቆ እቡን ዘበሰማያት ተቀበለው ።

ታያላችሁን ይህ መንግሥት አዋራጅ ከፈረስ ከሰ ረገላ ወርዶ ከቁረንጮ ሲወድቅ አለው ። ሰምቶ ዝም ብሎ ሄደ ከተግባሩ ደርሶ ሲመለስ ከደጁ ነጋሪት ምቱ እሳት አንድዱ አለ በሀገራቸው ትእምርተ ጸብእ ነው እሳት እነደዱ ነጋሪት መቱ ፡ ምን አደረ ግሁ ምን አልኩና ተጣላኸኝ አለው ምነው እንዲህ አላልከኝም አሰው ። ቢከፋኝ እኔ መንግሥት የተ ዋረደ መሰሎኝ ነው እንጂ አለ ፡ ከዚህ በኋላ ባረጀ ሳጥን ዝግም ወርቅ መልቶ በባሕር ቍልፍ ቆልፎ የባሕር ዓረብ በተሸፈነ ባዲስ ሣጥን ጠጠር ገል መልቶ በባሕር ቍልፍ ቆልፎ ሁለቱንም አቅርቦ አስጠራው በል ከዚህ የመረጥኸውን ውሰድ አለው ፡ በባሕር ዓረብ የተሸፈነውን ይዞ ሄደ መልሰህ አምጣ አለው እስኪ ከፍተህ እየው አለው ከፍቶ ቢያ የው ጠጠር ገል አገኘ ንቀህ የተውኸውን ከፍተህ እየው አለው ከፍቶ ቢያየው ዝግም ወርቅ አገኘ ያ የኛ ምሳሌ ነው በእፍአ አጊጦ እንዳየኸው እኛም በሰው ዘንድ የከበርን ነን በውስጡ እንዲህ ያለ እንዳገኘህበት እኛም በእግዚአብሔር ዘንድ የተናቅን የተዋረድን ነን ። ይህ የናቅኸው የባሕታዊ ምሳሌ ነው አንተ እንደ ናቅኸው እሱም በሰው ዘንድ የተ ናቀ ነው ። በውስጡ ዝግም ወርቅ እንዳገኘህበት በእግዚአብሔር ዘንድ የከበረ የተወደደ ነው ። እንዲበልጠኝ አውቄ ነው እንጂ እንዲያው አደ ርጌዋለሁ መሰሎሃል ብሎ ወርቁን አስይዞ ሰዶታል ።

፲፮ ኦሪትኒ ወነቢያትኒ እስከ ዮሐንስ ሰበኩ እምትካት በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ማቴ. ፲፩ ፣ ፲፪ ፨

፲፮ ኦሪትም ነቢያትም ከጥንት ጀምረው የእግዚአብሔርን መንግሥት ነገር አስተማሩ ፨
ወኵሉ ይትገፋዕ በእንቲአሃ ፨
ሰው ሁሉ ስለርሷ ይገፋል ፨

፲፯ ወባሕቱ ይቀልል ሰማይ ወምድር ይኅልፍ እምትደቅ አሐቲ ቃል እምኦሪት ወእምነቢያት ፨ ማቴ . ፭ ፣ ፲፰ ፨

፲፯ ነገር ግን ከኦሪት ከነቢያት አንዲት ቃል ከምትወድቅ ሰማይና ምድር ቢያልፍ ይቀላል ፨

፲፰ ወኵሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ወያወስብ ካልዕተ ዘመወ ፨ ማቴ. ፭ ፴፫ ፨ ማር ፲፣፳፩ ፨ ፩ ቆሮንቶስ ፯ ፣ ፲ ፨

፲፰ ሚስቱን ፈትቶ ሌላይቱን የሚያገባ ሁሉ አመነዘረ ፨
ወዘኒ ያወስብ ኅድግተ ዘማዊ ውእቱ ፨
የተፈታችውንም ያገባ ሴሰኛ ነው ፨
ወእንተኒ ደኃራ ምታ ለእመ ቀርበት ካልዓ ዘመወት ባሏ የሞተባትም ሌላ ወንድ ብታገባ አመነዘረች ፨

በእንተ ባዕል ፨

፲፱ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ባዕል ወይለብስ ሜላተ ወለየ ወልብሰ ቢሶስ ፨
ሐተታ ስለ ሦስት ነገር ያመጣዋል ፨ ጽድቅ ቢሠሩ ዋጋ ኃጢአት ቢሠሩ ፍዳ እንዳይቀር ፨ ጻድቃን በፈቃዳቸው ኃጥአን ወዳሉበት ኃጥአንም በፈቃዳቸው ጻድቃን ወዳሉበት መሄድ መምጣት እንዳይቻላቸው ፨

፲፱ ለመንገር ፨ ቀይ ሐር ነጭ ሐር ቀጭን ልብስ የሚለብስ ማለት ልልበስ ያለውን የማያጣ ፨
ወይትፌሣሕ ወይትፈጋዕ ኵሎ አሚረ ፨
ዕለት ዕለት ተድላ የሚያደርግ ነዌ የሚባል አንድ ባለጠጋ ነበር ፨ ሐተታ ስሙን የሚጽፍም የማይጽፍም ይገኛል ፨ ያልጻፈም እንደሆነ የተመቸ ከታወቀ ብሎ የጻፈ እንደሆነ አገረረበት ፍጡር ከሆነ ምንም ኃጥእ ቢሆን ከዲያብሎስ በቀር ፈጽሞ ጸናና የለምና ጥቂት ቅንነት ነበረችውና የዚህን ዋጋ በዚህ ዓለም ብዕለ ሥጋን ተቀብሏል ከጥቂር ላም አንድ ነጭ ጠጕር እንዳይጠፋ ፨

፳ ወሀሎ ፩ ነዳይ ዘስሙ አልዓዛር ግዱፍ ውስተ ዴዴሁ ለባዕል ፨

፳ ከነዌ ደጅ ወድቆ የሚኖር ፨
እንዘ ይደዊ በሕማመ ቁስል ቁስለ ሥጋ የታመመ አልዓዛር የሚባል አንድ ሰው ነበር ፨

፳፩ ወይፈቱ ይጽጋብ እምፍርፋራት ዘይወድቅ እማዕዱ ለባዕል ፨

፳፩ ከነዌ ማዕድ የወደቀውን ፍርፋሪ ይመገብ ዘንድ የሚወድ ፍጡር ከሆነ ከመቤታችን በቀር ፈጽሞ ደግ የለምና ጥቂት ጽንንት ነበረችውና የዚያን ፍዳ በዚህ ዓለም ንዴተ ሥጋውን ተቀብሏል ፨

ወከለባትኒ ይመጽኡ ወይልህሱ ቁስሊሁ ፨
ውሾቹም እየመጡ ቁስሉን ይልሱ ነበር ፨ ሐተታ የውሻው መላስ ልዝብ ነውና ደስ እያለው አይከለክላቸውም ነበር ፨

፳፪ ወእምዝ ሞተ ዝኩ ነዳይ ፨
፳፪ ከዚህ በኋላ አልዓዛር ሞተ ፨
ወወሰድዎ መላእክት ውስተ ሕፅነ አብርሃም ፨
መላእክት ወደ አብርሃም ጭን በአብርሃም ኪዳን ወደምትወረስ ወደገነት ወሰዱት ፨
ወሞተ ባዕልኒ ፨ ነዌም ሞተ ፨
ወተቀብረ ፨
ተቀበረ ፨ ሐተታ አልዓዛርን ሞተ ብሎ ተቀበረ አላለውም በርደተ መቃብር ርደተ ገሃነም እንደሌለበት ለማጠየቅ ፨ ነዌን ግን ሞተ ብሎ ተቀበረ አለው በርደተ መቃብር ርደተ ገሃነም እንዳለበት ለማጠየቅ ፨

፳፫ ወበሲኦልኒ አንሥአ አዕይንቲሁ እንዘ ሀሎ ውስተ ኵነኔ ወደያን ወርአዮ ለአብርሃም ርኁቀ ፨
፳፫ በፍዳ ተይዞ በሲኦል ዓይኑን አራምዶ አብርሃምን በሩቅ አየው ፨
ወአልዓዛርሃ ይረፍቅ ውስተ ሕፅኑ ፨
አልዓዛርም ባጠገቡ ተቀምጦ ነበር ፨

፳፬ ወጸውዖ ወይቤሎ አአባ አብርሃም ተሣሃለኒ ፨

፳፬ አብርሃም አባቴ ሆይ እዘንልኝ ፨
ወፈንዎ ለአልዓዛር ከመ ይጥማዕ ጽንፈ አፅባዕቱ ማየ ወያቍርረኒ ልሳንየ ፨
ጣቱን ከውኃ ነክሮ አንደበቴን ያቀዘቅዝልኝ ዘንድ አልዓዛርን ወደኔ ላክልኝ ፨
እስመ ሐመምኩ ፈድፋደ በዛቲ እሳት ፨
በዚህች እሳት ፈጽሜ ተቃጥያለሁና አለው ፨

፳፭ ወይቤሎ አብርሃም ተዘከር ኦ ወልድየ ዘከመ ተፈጋዕከ ወተፈሣሕከ በሕይወትከ ፨

፳፭ አብርሃምም ልጄ ሆይ በሕይወተ ሥጋ ሳለህ ተድላ ታደርግ እንደነበር ፤
ወአልዓዛርስ ከማሁ ከመ በተጽናስ ፨

አልዓዛርም በችጋር እንደ ነበረ ዕወቅ አስብ አለው።
ወይእዜሰ ከማሁ ከመ ውእቱ ይትፌሣሕ በዝየ ።
ዛሬ ግን አንተ ተድላ ሥጋ ታደርግ እንደነበረ እር
ሱም ተድላ ነፍስ ያደርጋል ።
ወአንተስ ተሐምም ።
እርሱም በንዴተ ሥጋ ይኖር እንደነበር አንተ
በንዴተ ነፍስ ትኖራለህ ።

፳፮ ወምስለ ዝንቱ ኵሉ ጸድፍ ዐቢይ ይከ
ልዓነ ማዕከሌነ ወማዕከሌክሙ ።

፳፮ ከዚህም ሁሉ ጋራ ታላቅ ገደል በእኛና
በአንተ መካከል ይበለክበናል ማለት ጽኑ ፍትሐ
እግዚአብሔር አለ ። ከመ እለሂ ይፈቅዱ ይኅልፉ
እምለፌ ኢይክሀሉ መጺአ ኀቤክሙ ።
ከኛ ወደናንተ ማለፍ የሚወዱ መምጣት እንዳይ
ቻላቸው ።
ወእለሂ መንገሌክሙ ኢይዕድው ኀቤነ ።
ከናንተም ያሉ ወደኛ እንዳያልፉ ። ኢንሬዕዮሙ
ንሕነ ወእሙንቱ ኢይሬዕዩነ እስመ ጽልመት ሀሎ
ማዕከሌነ ወኢየኃድገነ ንትርአይ በበይናቲነ ወይ
መስለነ ከመ ሀሎነ ባሕቲትነ እንዘ ብዙኃ ጉባኤ
ምስሌነ እንዲል ።

፳፯ ወይቤሎ እስእለከ እአባ አብርሃም ትፌ
ንዎ ለአልዓዛር ቤተ አቡየ ።

፳፯ አብርሃም አባቴ ሆይ አልዓዛርን ወደ
አባቴ ቤት ትልከው ዘንድ እለምንሃለሁ አለው።

፳፰ እስመ ሀለዉ ኃምስቱ አኃውየ ።
፳፰ አምስት ወንድሞች አሉኝና ።
ይንግሮሙ ወይሰምዑ ከመ ኢይምጽኡ እሙንቱሂ
ውስተ ዛቲ ብሔረ ሕማም ፤
ነገሯቸው ሰምተው ደግሞ ወደዚህች ስቃይ ሥፍራ
እንዳይመጡ ፤

፳፱ ወይቤሎ አብርሃም ቦሙ ሙሴ ወነቢ
ያት ኪያሆሙ ለይሰምዑ ።

፳፱ ሙሴ ነቢያትም አሏቸው እርሳቸውን
ይስሙ ማለት አሪት ነቢያት አሉላቸው በርሳቸው
ጸንተው ይኑሩ ። ወሙሴሰ ሕግ ውእቱ እንዲል ፤

፴ ወይቤሎ አልቦ አባ አብርሃም ፤
፴ እርሱም አባቴ አብርሃም ሆይ አይደለም።
አሐዱ እምነ ምውታን ለእመ ኢሖረ ኀቤሆሙ
ወለእመ ኢነገሮሙ ኢየአምኑ ወኢይኔስሑ ።
ከሙታን አንዱ ወደርሳቸው ካልሄደ ካልነገራቸው
አያምኑም አይመለሱም አለው ።

፴፩ ወይቤሎ አብርሃም ለእመሰኬ ሙሴሃ ወነ
ቢያተ ኪያሆሙ ኢይሰምዑ ።

፴፩ አብርሃምም ሙሴን ነቢያትን ካልተቀበሉ፤
እመሂ ቦ ዘተንሥአ እምውታን ኢይሰምዕዎ ወኢ
የአምንዎ ።
ከሙታን ተለይቶ የተነሣም ቢኖር አያምኑም ሕገ
ጋትን ካልተቀበሉ ከደጃቸው ወድቆ ይኖር የነበረ
አልዓዛርንም አይቀበሉትም አለው ። ሐተታ ፣
ነዌ በብሉይ ነው ቢሉ የተመቸ ምንም ጻድቃንን
እደ እግዚአብሔር ቢጠብቃቸው ቦታ ያገናኛቸዋ
ልና በሐዲስ ነው ቢሉ ነገሩ የሚያስኝ ስለ ሆነ አል
ዓዛር የእስራኤል ነዌ የፈርያን አምስቱ አኃው የኃ
ምስ አብዳት ምሳሌ ።

---

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ ላዕለ ዕቅፍት ።

ምዕራፍ ፲፯ ።

፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ
ግብር ይመጽእ መንሱት ። ማቴ፡፲፰፡፯ ማር፡፱፡፵፪።

፩ ለደቀ መዛሙርቱ አላቸው መከራ ግድ
ይመጣል ።
ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለዘያመጽአ ለመንሱት እም
ኀቤሁ ።
ነገር ግን መከራን ከራሱ ለሚያመጣት ሰው ወዮ
ለት ።

፪ እምኃየሶ ይእስሩ ዐከሣዱ ማኅረፀ እድግ
ወያስጥምዎ ውስተ ቀላየ ባሕር እምየስሕቶ ለአ
ሐዱ እምእሉ ንኡሳን ።

፪ ከነሀ ከታናናሾቹ አንዱን ከሚያስት የወፍጮ
ደንጊያ ባንገቱ አስረው ከጥልቅ ባሕር ቢያሠጥ
ሙት ይሻለው ነበር አላቸው ።

፫ ዑቁ ርእሰክሙ ። ሌዋ ፲፱፡፲፯ ሲራ ፲፱፡፲፫
ማቴ ፲፰፡፲፭ ።

፫ ለራሳችሁ ተጠበቁ ።
ለእመ አበሰ ለከ እኁከ ገሥጾ ለባሕቲቱ ።
ወንድምህ ቢበድልህ ለብቻው ተቆጣው ።
ወለእመኒ ነስሐ ኅድግ ሎቱ ።
ቢመለስም ይቅር በለው ።

፬ ወለእመኒ ስብአ ለለዕለቱ አበሰ ወስብዓ
ለለዕለቱ ተጋነየ ኅድግ ሎቱ ።

፬ በቀንም ሰባት ጊዜ ቢበድል ሰባት ጊዜም
ቢመለስ ይቅር በለው ። ሐተታ ማቴዎስ ሚመጠነ
እመ አበሰ ሊተ እኁየ እኅድግ ሎቱ አለው ይላል ።
ሉቃስ እመኒ ስብዓ ለለዕለቱ አበሰ ወስብዓ ለለ
ዕለቱ ተጋነየ ኅድግ ሎቱ አለው አለ እንደ ምን
ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም እንደ ማቴዎስ ሚመ
ጠነ እመ አበሰ እኁየ እኅድግ ሎቱ ቢለው

እመኒ ሰብዓ ለለዕለቱ አበሰ ወሰብዓ ለለዕለቱ
ተጋንየ ኀድግ ሎቱ ብሎታል ከዚህ] በኋላ እስከ
ሰብአት ይላል አይብለከ እስከ ስብዕ አላ እስከ ፸
በበሰብዕ ብሎታል አንድም ሚመጠነ እመ
አበሰ እኁየ እኅድግ ሎቱ እስከ ሰብዕኑ ቢለው
አይብለከ እስከነ ሰብዕ አላ እስከ ፸ በበሰብዕ ብሎ
ከዚህም ለእመ አበሰ ለከ እኁከ ሰብዓ ጊዜያተ
ወሰብዓ ለለዕለቱ ትጋንየ ኀድግ ሎቱ ይላል ።

በእንተ ኀይል ዘሃይማኖት ወዘከመ ይደሉ
ፈጽሞቱ ለግብር ።

፭ ወይቤልዎ ሐዋርያት ለእግዚእነ ወሰከነ ሃይ
ማኖተ ።

፭ ሐዋርያትም ጌታን ሃይማኖት ጨምርልን
አሉት ሃይማኖት የሚጨምር መስሏቸው ። አን
ድም ይጨመራል የወጣኒው ከማዕከላዊ ፡ የማዕ
ከላዊ ከፍጹም ሲደርስ ይጨመራልና ። አንድም
ተአምራት አድርግልን አሉት ሰው የሚያምንበት
ስለሆነ ሃይማኖት አለው ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እመ ብከሙ
ሃይማኖት መጠነ ኅጠተ ሰናፔ ወትብልዋ ለዛቲ
ሰግላ ተመልሒ እምሥርውኪ ወተተከሊ ውስተ
ባሕርት ትዔዘዝ ለከሙ ።

፮ ጌታም አለ ሃይማኖትስ ቢኖራችሁ የሰና
ፍጭ ቅንጣት የምታህል ይህችን ሾላ ተነቅለሽ
ከባሕር ተተከይ ብትሏት ትታዘዝላችኋለች ።

፯ መኑ እምኔክሙ ዘቦ ገብር ሐረሳዊ ።
፯ ከናንተ ወገን ገበሬ ባርያ ያለው ።
ወእመኒ ኖላዊ ።
ጠባቂም ቢሆን ያለው ማነው
አቲዎ እምወፍሩ ።
ከተሰማራበት በተመለሰ ጊዜ ።
ይቤሎኑ እግዚኡ ዕርግ ነዓ ወርፍቅ ዝየ ።
ከኔ ጋር ተቀምጠህ ብላ ጠጣ ይለዋልን ።

፰ አኮኑ ይብሎ አስተዳሉ ሊተ ዘእዴሬር ።
፰ የምበላውን አዘጋጅልኝ ፡
ወቅንት ወመጥወኒ እስከ እበልዕ ወእሰቲ ።
ታጥቀህ የምበላውን የምጠጣውን አሳልፍልኝ ።
ወእምዝ ብላዕ ወሰተይ አንተኒ ።
ከዚህ በኋላ አንተም ብላ ጠጣ ይለው የለምን ።

፱ ቦኑ እንጋ ምዝጋና ለውእቱ ገብር ለእመ
ገብረ ዘአዘዞ እግዚኡ ።

፱ በውኑ ያባርያ ጌታው ያዘዘውን ቢያደርግ
ይመሰግናልን ።

፲ ከማሁኬ አንትሙኒ ገቢረክሙ ኵሎ ዘአ
ዘዝኩክሙ በሉ አግብርት ጽሩዓን ንሕነ ።

፲ እንደዚህም እናንተም ያዘዝኋችሁን ሥራ
ሁሉ ሠርታችሁ ሥራ ፈት ባሮች ነን ።
ወዘይደልዎነ ለገቢር ገበርነ ።
ልንሠራው የሚገባንን ሠራን በሉ ። አንድም የር
ትዑን ሠርተን የትሩፋቱ ቀርቶናል በሉ ።
በእንተ ፲ቱ እለ ለምጽ ።

፲፩ ወእምዝ እንዘ የሐውር ኢየሩሳሌም ኃለፈ
ማዕከለ ሰማርያ ወገሊላ ።

፲፩ ከዚህ በኋላ ወደ ኢየሩሳሌም ሲሄድ በሰ
ማርያና በገሊላ መካከል ሄደ ።

፲፪ ወእንዘ ይበውእ አሐተ ሀገረ ተቀበልዎ
ዓሠርቱ ዕደው እለ ለምጽ ።

፲፪ ወደአንዲት አገር ሲገባ ለምጽ የያዛቸው
ዐሥር ሰዎች ተገናኙት ።
ወቆሙ እምርኁቅ ።
ርቀው ቆሙ ።

፲፫ ወይቤልዎ ወአውየው ኢየሱስ ሊቅ ተሣ
ሃለነ ።

፲፫ ኢየሱስ መምህር ሆይ እዘንልን ብለው
አሰምተው ተናገሩ ።

፲፬ ወርእዮሙ ወይቤሎሙ ሑሩ ኀበ ካህን
ወአፍትኑ ርእሰክሙ

፲፬ አይቷቸው ከካህን ሂዱችሁ ራሳችሁን አስ
መርምሩ አላቸው ።
ወእንዘ የሐውሩ ነጽሑ ።
እርሳቸውም ሲሄዱ ዳኑ ነጹ ።

፲፭ ወርእዮ አሐዱ እምኔሆሙ ከመ ነጽሐ
ተመይጠ እንዘ የአኵቶ ለእግዚአብሔር በዓቢይ
ቃል ።

፲፭ ከርሳቸውም አንዱ እንደ ዳነ አይቶ እግ
ዚአብሔርን በታላቅ ቃል እያመሰገነ ተመለሰ ።
ሐተታ ያዳነኝን ትቼ ወዴት እሄዳለሁ ብሎ ።

፲፮ ወሰገደ ታሕተ እገሪሁ ለእግዚእ ኢየሱስ
በገጹ ።

፲፮ ከጌታ እግር በታች በግንባሩ ሰገደ ።
ወአዕኰቶ ። አመሰገነው ።
ወሳምራዊ ብእሲሁ ።
ትውልዱ ነገዱ ሳምራዊ ነው ።

፲፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ አኮኑ
ዐሠርቱ እሙንቱ እንትሙ እለ ነጹሑክሙ ።

፲፯ ጌታም አለ የዳናችሁት ዐሥር አልነበራችሁምን ።
አይቴኑ እንከ ተስዓቱ ።
ዘጠኙ ወዴት አሉ አለው ።

፲፰ ሉሙሰ ተስእናሙኑ ተመይጦ ወአዕኲቶ ለእግዚአብሔር ዘእንበለ ዝንቱ ዘካልዕ ሕዝቡ ።

፲፰ ወገኑ ልዩ ከሚሆን ከዚህ በቀር ተመልሶ እግዚአብሔርን ማመስገን ለርሳቸው ተሳናቸውን ።

፲፱ ወእምዝ ይቤሎ ተንሥእ ወሑር ሃይማኖትከ አሕየወተከ ።

፲፱ ተነሥተህ ሂድ ሃይማኖትህ አድኖሃልና። ሐተታ ዐሥሩ ለምጻሞች ያሥሩ ሕሊናት ምሳሌ የቀሩት ዘጠኙ የክፉ ሕሊናት ፡ የተመለሰው እንዱ የበጐ ሕሊና ምሳሌ ። ለአዳም ተውህብዎ ዐሠርቱ ሕሊናት ወለከሰ አሐዱ እንዲል ።

በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር ወበእንተ ተመይጦቱ ለወልደ ዕጓለ እምሕያው ።

፳ ወዕቢዘ ተስእልዎ ፈሪሳውያን ወይቤልዎ ማዕዜ ትመጽእ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፳ ፈሪሳውያን የእግዚአብሔር መንግሥት መቼ ትመጣለች ማለት መቼ ትሰጣለች ብለው ጠየቁት።
ወአውሥአ ፡ መለሰ ።
ወይቤሎሙ ኢትመጽእ መንግሥተ እግዚአብሔር በተዓቅቦ ።
የእግዚአብሔር መንግሥት በጥንቃቄ አትሰጥም ።

፳፩ ወኢይብልዋ ነያ ዝየ ።
፳፩ ከወዲህ አለች ከወዲያ የለችም ።
ወነያ ከህከ ።
ከወዲያ አለች ከወዲህ የለችም አትባልም ።
መንግሥተ እግዚአብሔር ነያ ማዕከሌክሙ ይእቲ።
የእግዚአብሔር መንግሥት እነሆ በመካከላችሁ ነች ማለት እኔን ማመን ነው ሲል ።

፳፪ ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ይመጽእ መዋዕል እመ ትፈትው ትርአዩ ኖሐተ ዕለተ እምነ መዋዕሊሁ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፳፪ ለደቀ መዛሙርቱ ከሰው ልጅ ቀኖች አንዲቱን ቀን ታዩ ዘንድ የምትመኙበት ቀን ይመጣል ወኢትሬእዩ ።
ነገር ግን ኦታዩትም አላቸው ።

፳፫ ወለእመ ይብሉክሙ ነዋ ዝየ ወነዋ ከህከ።
ማቴ፥፳፬፥፳፫ ማር፥፲፫ ፥ ፳፩ ።

፳፫ እነሆ ከዚህ ነው ወይም ከዚያ ነው ይሏችኋል ።
ኢትሑሩ ። እትሂዱ።
ወኢትዴግኑ ። አትከተሉ።

፳፬ እስመ ከመ መብረቅ ዘይበርቅ ወያበርህ እምኦጽናፈ ሰማይ እስከ አጽናፈ ሰማይ ከማሁ ውእቱ ይከውን ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፳፬ ከሰማይ ዳር እስከ ሰማይ ዳር እንደሚበርቅና እንደሚያበራ መብረቅ የሰው ልጅ መምጣት እንዲሁ ይሆናልና ።

፳፭ ወባሕቱ እምቅድመ ዝንቱ ኵሉ ብዙኃ የሐምም ወትሜንኖ ።

፳፭ አስቀድሞ ግን ብዙ መከራ ይቀበላል ወታሜክሮ ዛቲ ትውልድ ።
ይህችም ትውልድ ትፈታተነዋለች ።

፳፮ ወበከመ ኮነ በመዋዕሊሁ ለኖህ ከማሁ ይከውን ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እምሕያው ።
ዘፍጥ፥፯፥፯ ማቴ ፳፬፥፴፯ ፡

፳፮ በኖኅ ዘመን እንደ ተደረገ የሰው ልጅ መምጣት እንዲህ ይደረጋል ።

፳፯ ወበሊዖ ኮኑ እንዘ ይበልዑ ወይሰትዩ ያወስቡ ወይትዋሰቡ እስከ እመ ዕለት ቦአ ኖኅ ውስተ ቅፍቀ ታቦት ።

፳፯ ኖኅ ከፍል ወዳለው መርከብ እስከሚገባበት ቀን ድረስ ሲበሉ ሲጠጡ ሲያገቡ ሲጋቡ።
ወመጽአ ማየ አይኅ ወእጥፍአ ኵሎ ኀቡረ ።
የጥፋት ውኅ መጥቶ ሁሉንም እንዳጠፋ ።

፳፰ ወበከመ ኮነ በመዋዕሊሁ ለሎጥ ።
፳፰ በሎጥ ዘመን እንደ ተደረገ ።
እንዘ ይበልዑ ወይሰትዩ የሐንጹ ወይተክሉ ዘፍ፥ ፲፱፥፳፭ ።
ሲበሉ ሲጠጡ ሲያንጹ ሲተክሉ ።
ይሠይጡ ወይሣየጡ ።
ሲገዙ ሲሸጡ እንደነበሩ ።

፳፱ እስከ አመ ዕለተ ወፅአ ሎጥ እምሰዶም።
፳፱ ሎጥ ከሰዶም እስከሚወጣበት ቀን ድረስ ወእዝነመ እግዚአብሔር እሳተ ወተየ እምሰማይ።
እግዚአብሔርም ከሰማይ ኦሳትና ዲን እስከሚያዘንምበት ቀን ድረስ ። ሐተታ እግዚአብሔር እሳት አዝንሚ ኣ መላእክት ዲን ነስንሰዋል እንዲያጸናው።
ወእጥፍአ ኵሎ ።
ሁሉንም ኦስከሚያጠፋበት ቀን ድረስ ።

፴ ከማሁ ውእቱ ምጽአቱ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ኢይትዓወቅ ።

፴ የሰው ልጅ መምጣትም እንደዚሁ አይታወቅም ።

፴፩ ይእተ አሚረ ዘሀሎ ውስተ ናሕስ ።
፴፩ ያን ጊዜ በሰገነት ላይ ያለ ።
ወንዋዮ ውስተ ቤት ።
በቤት ያለ ገንዘቡንም ።
ኢይረድ ይንሣእ ።
ያንሣ ዘንድ አይውረድ ።
ወዘሂ ገዳመ ሀሎ ኢይግባእ ድኅሬሁ ።
በምድረ በዳም ያለ ወደኋላው አይመለስ ።

፴፪ ተዘከርዋ ለብእሲተ ሎጥ ።
፴፪ የሎጥን ሚስት አብንት አድርጓት ። ሐተታ መላእክት ይዘዋቸው ሲወጡ ዞረሽ አትዩ ብለዋታል ከወጣች በኋላ የእሳቱን ድምፅ ሰምታ ወይ አገሬ ሰዶም ብላ ዞራ ብታይ ሐውልተ ጼው ሆናለች ያጼው ከንቱ እንደሆነ እናንተም ከመነናችሁ በኋላ ወደ ዓለም ብትመለሱ ከንቱ ትሆናላችሁ ለማለት እንዲህ አለ ።

፴፫ ዘይፈቅድ ያድኅና ለነፍሱ ስይግድፋ ። ማቴ፡፲፡፴፱ ማር፡፰፡፴፭ ሉቃስ ፱፡፳፬ ዮሐ፡፲፪፡፳፭።

፴፫ ሰውነቱን ሊያድናት የወደደ ሁሉ ይጣላት ።
ወዘሰ ገደፋ ስነፍሱ በእንቲአየ የሐይዋ ።
ሰውነቱንም ስለኔ የጣላት ያድናታል ።

፴፬ እብለከሙ በይእቲ ሌሊት ክልኤቱ ይስክቡ ውስተ አሐዱ ዓራት ።

፴፬ በዚያች ሌሊት ሁለቱ በአንድ አልጋ ይተኛሉ ።
አሐዱ ይነሥእ ።
አንዱን ይወስዳሉ ።
ወካልኡ የኃድጉ ።
ሁለተኛውንም ይተዋሉ ።

፴፭ ወክልኤቲ የኃርጻ በእሐቲ ማኅረጽ ።
፴፭ ሁለት ሴቶች ባንድ ወፍጮ ይፈጫሉ ።
እሐተ ይነሥኡ ።
አንዲቱን ይወስዳሉ ።
ወካልዕታ የኃድጉ ።
ሁለተኛይቱንም ይተዋሉ ።
ወክልኤቱ ይሄልዉ ውስተ አሐዱ ገራህት ።
ሁለቱ በአንድ እርሻ ይኖራሉ ።
አሐደ ይነሥኡ ።
አንዱን ይወስዳሉ ።
ወካልአ የኃድጉ ።
ሁለተኛውን ይተዋሉ ።

፴፮ ወአውሥኡ ወይቤልዎ ኀበ አይቴኑ እግዚእ ።

፴፯ እቤቱ ወዴት ነው ብለው ጠየቁት ። ወይቤሎሙ ኀበ ሀሎ ገደላ ህየ ይትጋብኡ አንስርት። ጥንብ ካለበት አሞሮች ይሰበሰባሉ አላቸው ።

በእንተ መኰንን አኩይ ።

ምዕራፍ ፲፰ ።

፩ ወመሰለ ሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ በምሳሌ ከመ ዘልፈ ይጼልዩ ወኢይትሀከዩ ሲራ ፲፰፡፳፪ ፩፡ ተሰ፡ ፭፡፲፯ ።

፩ ይጸልዩ ዘንድ ቸል እንዳይሉ ማለት ጸሎት መላልሶ መጸለይ እንዲገባ ፈጥኖ መተው እንዳይገባ ለጊዜው ሊያደርገው ያልወደደውን ተላጽቆተ ስኢል እንዲያደርግለት ምሳሌ መስሎ ይነግራቸዋል ።

፪ ወይቤሎሙ ሀሎአ አሐዱ መኰንን በአሐቲ ሀገር ዘኢይፈርሆ ለእግዚአብሔር ወኢያኃፍር ሰብአ ።

፪ ሰውን የማያፍር እግዚአብሔርን የሚፈራ አንድ ሹም በአንዲት አገር ነበር አላቸው

፫ ወሀለወት እሐቲ ዕቤርት በይእቲ ሀገር።
፫ አንዲት ደኅም እርሱ በተሾመበት አገር ነበረች ።
ወቦኣት ትመጽእ ኀቤሁ ወትቤሎ ኰንነኒ አምዕድውየ ።
ወደሱ እየመጣች ከባለጋራዬ ፈርደህ አድነኝ ትለዋለች ።

፬ ወእበያ ወአጕንደያ ።
፬ ቸል አላት ።
፭ ወእምዝ ሀለየ በልቡ ወይቤ እመ ኢይፈርሆ ለእግዚአብሔር ወኢየኃፍር ሰብአ ።

፭ እግዚአብሔርን ባልፈራ ሰውንም ባላፍር ።
፮ ከመ ኢታንጥየኒ ዛቲ እቤር እትቤቀል ላቲ።
፮ ይህች ደሀ እንዳትዘበዝበኝ እፈርድላታለሁ አለ ።
ከመ ኢትምጽአ ወኢታስርኃኒ ዘልፈ ።
ዘውትር እየመጣች እንዳትዘበዝበኝ ።

፯ ወይበሎሙ እግዚእነ ስምዑ ዘይቤ መኰንነ ዓመፃ ።

፯ ጌታም አለ ግፈኛ መኰንን ያሰውን ስሙ። እግዚአብሔርኑ እንከ ኢይፈትሕኑ ለኅሩያኒሁ እለ ይግዕሩ ኀቤሁ መዓልተ ወሌሊተ ያስንኪ ለዚያች ድኃ እፈርድላታለሁ ያለ እንኪያ እግዚአብሔር በመዓልትም በሌሊትም ወደሱ ለሚለምኑ አይፈ

ርድላቸውምን ።
ወይትዔገሦሙኑ ።
ቾል ይላቸዋልን ።

፰ እወ እብለክሙ ከመ ይፈትሕ ሎሙ ፍጡነ።
፰ አዎን ፈጥኖ ይፈርድላቸዋል ብዬ እነግ ራችኋለሁ ።

ወባሕቱ ሶበ መጽአ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ይረክብኑ እንጋ ሃይማኖተ በዲበ ምድር ።

ነገር ግን የሰው ልጅ በመጣ ጊዜ ማለት ሰው በሆነ ጊዜ ሌላን ሃይማኖት አስተማረን ቃል ሥጋ ኮነ በሉ ብሎ አይደለምን አንድም ይረክቡኑ። በኋላ በመጣ ጊዜ ሌላን ይጠይቃል ቃል ሥጋ መሆኑ አውቃችኋልን አላወቃችሁም ብሎ አይደለምን ።

በእንተ ፈሪሳዊ ወመጸብሐዊ ።

፱ ወይቤሎሙ ለእለ ያጸድቁ ርእሶሙ ወይሜንኑ ቢጾሙ ።

፱ ባልንጀራቸውን ለሚንቁ ራሳቸውንም ለሚያከብሩ ሰዎች ።

፲ ወመሰለ ሎሙ ከመዝ ፤
ምሳሌ መስሎ ነገራቸው ።
ወይቤሎሙ ክልኤቱ ኦዕያው ዓርጉ ቤተ መቅደሰ ይጸልዩ ።

፲ ሁለት ሰዎች ወደ ቤተመቅደስ ሊጸልዩ ገቡ ። ወዓርጉ ቤተ አዎን ። ወዓርጉ ጴጥሮስ ወዮሐንስ ጊዜ ተሱዓት ሰዓት ለጸሎት እንዲል ።
አሐዱ ፈሪሳዊ ።
አንዱ ፈሪሳዊ ነው ። ፈሪሳዊ ማለት እሉል ባሕታዊ ማለት ነው ።
ወካልዑ መጸብሐዊ ።
አንዱ ቀራጭ ነው ።

፲፩ ወቆመ ፈሪሳዊ ወጼለየ ።
፲፩ ፈሪሳዊ ቁሞ ጸለየ ።
ወይቤ አእኵተከ እግዚኦ ዘኢረሰይከኒ ከመ ባዕዳን ሰብእ ።
እንደ ሌሎች ሰዎች ያላደረግኸኝ አቤቱ አመሰግንሃለሁ ።
ሐያድያን ።                    እንደሚቀሙ ።
ወዓማፅያን ።                    እንደሚበድሉ
ወእለ የሐውሩ ብእሲተ ብእሲ ፤
እንደሚያመነዝሩ ።
ወኢከመ ዝንቱ መጸብሐዊ ።
እንደዚህም ቀራጭ ያላደረግኸኝ ።

፲፪ እንሰ እጸውም ክልኤተ ዕለተ በኵሉ ሰናብት ።

፲፪ በሳምንት ሁለት ቀን እጾማለሁ ። ሐተታ እሑድና ማክሰኞ ወይም ማክሰኞና ሐሙስ ይጾማሉ።
ወእበውእ ዐሥራተ እዴሁ እምኵሉ ዘአጥረይኩ ።
ከገንዘቤ ሁሉ ካሥር አንድ እሰጣለሁ ።

፲፫ ወመጸብሐዊሰ ቆመ እምርኁቅ ።
፲፫ ቀራጭ ግን ከሩቅ ቆመ ።
ወኢፈቀደ ያንሥእ አዕይንቲሁ ላዕለ ውስተ ሰማይ።
ዓይኑን አቅንቶ ወደሰማይ ሊያይ አልወደደም ።
ወጕድዓ እንግድዓሁ ።

ደረቱን ደቃ እንጂ ። ሐተታ መካነ አእምሮ ነውና።
ወይቤ ስረይ ሊተ እግዚኦ ፣
አቤቱ ይቅር በለኝ አለ ።

እስመ አነ ኃጥእ ዘኢይደልወኒ አቂም ውስተ መካነ መቅደስከ ።

በምትመሰገንበት በቤተ መቅደስ መቆም የማይቻለኝ ኃጥእ ነኝና ።

፲፬ እብለክሙ ዝንቱ አተወ ቤቶ እንዘ ይጸድቅ እምዝኩቱ ሉቃስ ። ፲፭፥፲፬ ማቴ ፳፫፥፲፪ ።

፲፬ ይህ መጸብሐዊ ከፈሪሳዊ ይልቅ በእግዚአብሔር ዘንድ ክብሮ ተመለሰ ብዬ እነግራችኋለሁ ። አንድም እንዘ ይጼደቅ ይህ ፈሪሳዊ ተመጻድቆበት ሄደ ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።
እስመ ኵሉ ዘአዕበየ ርእሶ የኃሥር ።
ራሱን ያከበረ ሁሉ ይዋረዳልና ወዘአትሐተ ርእሶ ይከብር ።
ራሱን ያዋረደ ሁሉ ይከብራልና ።

በእንተ ኢየሱስ ወሕፃናት ።

፲፭ ወእምዝ አምጽኡ ኀቤሁ ሕፃናተ ከመ ያንብር እዴሁ ላዕሌሆሙ ። ማቴ. ፲፱፥፲፫ ማር. ፲፥፲፫

፲፭ እጁን ይጭንባቸው ዘንድ ሕፃናትን ወደሱ አመጧቸው ።
ወርእዮሙ ኦርዳኢሁ ገሠጽዎሙ ።
ደቀ መዛሙርቱም አይተው ቱቆጧቸው ።

፲፮ ወጸወዖሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ኅድጉ ሕፃናተ ይምጽኡ ኀቤየ ።

፲፮ ጌታም ጠርቶ ኦላቸው ሕፃናትን ወደኔ ይመጡ ዘንድ ተዋቸው ።
ወኢትክልኦዎሙ ።
ኦትከልክሏቸው ኦላቸው ።
እስመ ለዘከመ እሉ ይእቲ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔር መንግሥት እንደዚህ ላሉ ናትና

፲፯ አማን እብለክሙ ዘኢተቀበላ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ከመ ሕፃናት ኢይበውኣ ፡

፲፯ የእግዚአብሔርን መንግሥት የማይቀበላት ሁሉ እንደ ሕፃናት አይገባባትም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ፡፡

በእንተ ወሬዛ ባዕል ፡፡

፲፰ ወተስእሎ አሐዱ መልአክ ፡፡ ማቴ፡፲፱፡፲፮፡፡

፲፰ ካለቆች አንዱ ጠየቀው ፡፡
ወይቤሎ ሊቅ ኄር ምንተ ሠናየ ገቢርየ እረክብ ሕይወተ ዘለዓለም ፡፡
ቸር መምህር ሆይ ምን በጎ ሥራ ሠርቼ የዘላለም ሕይወትን አገኛለሁ አለው ፡፡

፲፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ምንተ ትብለኒ ኄር ፡፡

፲፱ ጌታም ስምን ቸር ትለኛለህ ፡፡
አልቦ ኄር ዘእንበለ አሐዱ እግዚአብሔር ፡፡
ካንድ ከእግዚአብሔር በቀር ሌላ ቸር የለም ፡፡

፳ ለሊከ ታእምር ትእዛዛቲሁ ፡፡

፳ ትእዛዙን ታውቅ ዘንድ ፡፡
ኢትቅትል ነፍስ ፡፡
ነፍስ አትግደል ፡፡
ኢትሑር ብእሲተ ብእሲ ፡፡
ወደ ጎልማሳ ሚስት አትሂድ
ወኢትዘሙ ፡፡ አትሴስን ፡፡
ወኢትስርቅ ፡፡ አትስረቅ ፡፡
ወኢትኩን ስምዓ በሐሰት ፡፡
በሐሰት አትመስክር ፡፡
ወአክብር አባከ ወእመከ ፡
አባት እናትክን አክብር ፡

፳፩ ወይቤሎ ዘንተሰ ኵሎ ዓቀብኩ እምን እስየ እስከ ይእዜ ፡፡
ይህንስ ሁሉ ከሕፃንነቴ ጀምሬ እስከ ዛሬ ጠብቄ አለሁ ፡፡

፳፪ ወሰሚዖ ዘንተ እግዚእ ኢየሱስ ይቤሎ አሐቲ ተርፈተከ ፡፡

፳፪ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ይህን ሰምቶ አንዲት ቀረችብህ ፡፡
ሑር ወሢጥ ኵሎ ዘብከ ንዋየ ወሀብ ለነዳያን ፡
ሂደህ ያለህን ገንዘብህን ሁሉ ሸጠህ ለድሆች ስጥ ፡፡
ወትረክብ መዝገበ ዘበሰማያት ፡፡
በሰማይ መዝገብ ታገኛለህ ፡፡
ወነዓ ትልወኒ ፡፡
መጥተህ ተከተለኝ አለው ፡፡

፳፫ ወሰሚዖ ዘንተ ተከዘ ፈድፋደ ፡፡

፳፫ ይህን ሰምቶ ፈጽሞ አዘነ ፡፡
እስመ ባዕል ውእቱ ጥቀ ወብዙኅ ጥሪቱ ፡፡
እጅግ ባለጠጋ ነበር ገንዘቡም ብዙ ነበርና ፡፡

፳፬ ወርእዮ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይቴክዝ ይቤ እፎ ዕፁብ ለእለ ቦሙ ንዋይ በዊአ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ፡፡

፳፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ሲያዝን ባየው ጊዜ ገንዘብ ላላቸው ሰዎች ወደ መንግሥተ ሰማያት መግባት እንደምን ጭንቅ ነው አለ ፡፡

፳፭ ይቀልል ገመል ይኅልፍ እንተ ሰቅረተ መርፍዕ እምባዕል ይባእ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ፡፡

፳፭ ባለጠጋ ወደ መንግሥተ ሰማይ ከሚገባ ግመል በመርፌ ቀዳዳ ሊያልፍ ይቀላል ፡

፳፮ ወይቤሉ እለ ሰምዑ መኑ ይክል ድኂነ
፳፮ ለሰሙትም መዳን ማን ይችላል አሉ ፡
፳፯ ወይቤሎሙ ዘበኀበ ሰብእ ይሰአን በኀበ እግዚአብሔር ይትከሃል ፡፡

፳፯ በሰው ዘንድ የማይቻለው በእግዚአብሔር ዘንድ ይቻላል አላቸው ፡፡

በእንተ ተላውያነ ኢየሱስ ፡፡

፳፰ ወይቤሎ ጴጥሮስ ናሁ ንሕነ ኀደግነ ኵሎ ወተለውናከ ፡፡

፳፰ ጴጥሮስም አለ እነሆ እኛ ሁሉን ትተን ተከትለንሃል ፡፡
ምንተ እንጋ ንረክብ ፡፡
ምን እናገኛለን አለው ፡፡

፳፱ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ አልቦ መኑሂ ዘኃደገ ቤቶ ወአዝማዲሁ ወአኃዊሁ ወብእሲቶ ወውሉዶ በእንተ መንግሥተ እግዚአብሔር፡፡

፳፱ አባት እናቱን ወንድሞቹን ሚስቱን ልጆቹን ስለ እግዚአብሔር መንግሥት ብሎ የተወሁሉ በዚህ ዓለም ፡፡

፴ ዘኢይነሥእ ዕሴቶ ብዙኃ ፯ተ ምክእቢተ በዝንቱ ዓለም ፡፡

፴ ብዙ ዕጥፍ የማይወስድ የለም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ፡፡
ወበዓለምሰ ዘይመጽእ ሕይወተ ዘለዓለም ፡፡
በሚመጣው ዓለም ግን የዘለዓለም ሕይወትን ያገኛል ፡፡

በእንተ ትንቢት ዘሕማማት ።

፴፩ ወእምዝ ነሥኦሙ እግዚእ ኢየሱስ ለዐሠርቱ ወክልኤቱ አርዳኢሁ ። ማቴ ፳፡፲፯ ማር ፲ ፡ ፴፪ ።

፴፩ ዐሥራ ሁለቱንም ደቀ መዛሙርቱን ወስዳቸው ።
ወይቤሎሙ ናሁ ነዓርግ ኢየሩሳሌም ።
እነሆ ወደ ኢየሩሳሌም እንወጣለን አላቸው ።
ወይትፌጸም ኵሉ ዘጽሑፍ ውስተ መጻሕፍተ ነቢያት ላዕለ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
በነቢያት መጽሐፍ የተጻፈው ሁሉ በሰው ልጅ ክርስቶስ ላይ ይፈጸማል ።

፴፪ ወይሜጥውዎ ለአሕዛብ ።
፴፪ ለአሕዛብም አሳልፈው ይሰጡታል ።
ወይሳለቁ ላዕሌሁ ።
ይዘባበቱበታል ።
ወይጼዕልዎ ፡ ይሰድቡታል
ወይዌርቁ ውስተ ገጹ ።
ይተፉበታልም ።

፴፫ ወይቀሰፍዎ ፡ ይገርፉታል ።
ወይቀትልዎ ። ይገድሉታል ።

፴፫ ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ።
በሦስተኛው ቀን ይነሣል ።

፴፬ ወእሙንቱሰ አልቦ ዘለበው እምዝ ይቤሎሙ ።

፴፬ እርሳቸው ግን የነገራቸውን አላወቁትም ።
እስመ ስውር ውእቱ ዝንቱ ነገር እምኔሆሙ ወኢየአምሩ ዘይብል ።
ይህ ነገር ከርሳቸው ተሰውሮ ነበርና የሚናገረውን አያውቁም ነበር ።
በእንተ ዕውር ዘኢያሪኮ ።

፴፭ ወበጺሖሙ ኢያሪኮ ።
፴፭ ኢያሪኮ በደረሱ ጊዜ ።

ሀሎ አሐዱ ዕውር ይነብር ውስተ ፍኖት ወይስእል ማቴ፡፳፡፳፱-፴፭ ማር፡ ፲፡፵፮ ።
አንድ ዕውር ከመንገድ ተቀምጦ ይለምን ነበር።

፴፮ ወሰሚዖ ድምፀ ሰብእ ዘየኃልፍ ይቤ ምንትኑዝ ዘእሰምዕ ።

፴፮ የሚሄዱትን ሰዎች ድምፅ ሰምቶ ይህ የምሰማው ምድር ነው አለ ።
ወይቤልዎ ኢየሱስ ናዝራዊ የኃልፍ ።

፴፯ ወይቤልዎ ኢየሱስ ናዝራዊ የኃልፍ ።
፴፯ የናዝሬቱ እየሱስ እንዲያልፍ ነገሩት።

፴፰ ወአውየወ ወይቤ ኢየሱስ ወልደ ዳዊት ተሣሃለኒ ።

፴፰ የዳዊት ልጅ ኢየሱስ ሆይ እዘንልኝ አለው
፴፱ ወገሠጽዎ እለ ይመርህዎ ከመ ያርምም።
፴፱ የሚመሩት ዝም እንዲል ተቆጡት ።
ወአውየወ ፈድፋደ ወይቤ ወልደ ዳዊት ተሣሃለኒ።
እሱ ግን የዳዊት ልጅ ሆይ እዘንልኝ ብሎ አጅግ ጮኸ ።

፵ ወቆመ እግዚእ ኢየሱስ ወአዘዘ ያምጽእዎ ኀቤሁ ።

፵ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ቁሞ ወደርሱ ያመጡት ዘንድ አዘዘ ።
ወበጺሖ ኀቤሁ ይቤሎ ምንተ ትፈቅድ እግበር ለከ ።
ወደርሱም በደረሰ ጊዜ ምን ላድርግልህ ትወዳለህ አለው

፵፩ ወይቤሎ እግዚኦ ከመ ይርአያ አዕይንትየ።
፵፩ አቤቱ ላይ እወዳለሁ አለው ።
፵፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ርኢ ።
፵፪ ጌታም አለው እይ ።
ሃይማኖትከ አሕየወተከ ።
ሃይማኖትህ አዳነህ አለው ።

፵፫ ወርእየ ሶቤሃ ወተለዎ ።

፵፫ ያንጊዜም አይቶ ተከተለው ወአዕኰቶ ለእግዚአብሔር ።
እግዚአብሔርንም አመሰገነው
ወርእዮሙ ኵሉ ሕዝብ ሰብሕዎ ለእግዚአብሔር።
ሕዝቡም ሁሉ አይተው አመሰገኑት ።

በእንተ ዘኬዎስ መጸብሐዊ ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

፩ ወበዊአ እግዚእ ኢየሱስ ኢያሪኮ አንሶሰወ።
፩ ኢያሪኮ ገብቶ መላልሶ አስተማረ ።

፪ ወናሁ ረከበ ብእሴ ዘስሙ ዘኬዎስ መልአኮሙ ለመጸብሓን ።

፪ እነሆ የቀራጮች አለቃ የሚሆን ዘኬዎስ የሚባል ሰው አገኘ ።
ወባዕል ውእቱ ።
ባለጸጋም ነበረ ።

፫ ወየኃሥሥ ይርአዮ ለእግዚእ ኢየሱስ ከመ ያእምሮ መኑ ውእቱ ።

፫ ማናቸው እንደሆነ ያውቅ ዘንድ ጌታን ሊያየው ይወድ ነበር ።
ወኢያበውሖ ሰብእ ።
ሰው ግን አያሳየውም ነበር ።
እስመ ሐፂር ውእቱ በቆሙ ።
ቁመቱ አጭር ነበርና ።

፬ ወሮጸ ቅደሚሁ ወዓርገ ዲበ ሰግላ ።

፬ በፊቱ ሩጦ ከሾላ ላይ ወጣ ።
ከመ ይርአዮ ።
ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታን ያየው ዘንድ ።
እስመ እንተ ይእቲ ፍኖት ሀለዎ ይኅልፍ ።
በዚያች መንገድ ይሄድ ዘንድ አለውና ።

፭ ወበጺሖ ህየ ነጸሮ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ዘኬዎስ አፍጥን ወረድ ።

፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ከዚያ በደረሰ ጊዜ አይቶ ዘኬዎስ ፈጥነህ ውረድ አለው ።
እስመ ዮም ሀለወኒ እዓል ቤተከ ።
ዛሬ ከቤትህ እውል ዘንድ አለኝና ፤

፮ ወአፍጠነ ወረደ ።

፮ ፈጥኖ ወረደ ።
ወአግኀሦ ኀበ ቤቱ እንዘ ይትፌሣሕ ።
ደስ ብሎት ከቤቱ አገባው ።
ሐተታ ይሄድብኛል ብሎ ።

፯ ወርእዮሙ ዘንተ አንጐርጐሩ ወይቤሉ ኀበ ብእሲ ኃጥእ ቦአ የዓል ።

፯ ሁሉም ባዩ ጊዜ ከኃጥእ ሰው ቤት ይውል ዘንድ ገባ ብለው ነቀፉት ።

፰ ወቆመ ዘኬዎስ ወይቤሎ ለእግዚእን ናሁ እግዚእየ መንፈቀ ንዋይየ እሁብ ለነዳያን ።

፰ ዘኬዎስም ይህንን ሰምቶ ቁሞ ለጌታችን እነሆ ጌታዬ የገንዘቤን እኩሌታ ለደኃ እሰጣለሁ።
ወእመሂ ቦ ዘገፋእክዎ አፈደዮ ትርብዕተ ህየንተ አሐዱ ።
የበደልኩት ቢኖር በአንድ አራት እከፍለዋለሁ አለው ።

፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዮምስ ሕይወት ኮነ ለሰብአ ዝንቱ ቤት ።

፱ ኢየሱስም አለው ዛሬስ ለዚህ ቤት ሰው ድኅነት ተደረገ ።

፲ እስመ አንተሂ ወልደ አብርሃም አንተ ።

፲ አንተም የአብርሃም ልጅ ነህና ።
እስመ መጽአ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ይኅሥሥ ወያድኅን ዘተኃጕለ ።
ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስም የጠፋውን ሊሻ የተጐዳውን ሊያድን መጥቷልና ።

በእንተ ምሳሌ ዘምናናት ።

፲፩ ወእንዘ ይሰምዑ ዘንተ መሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ ።

፲፩ ይህን ሲሰሙ ምሳሌ መስሎ ነገራቸው እስመ ቅሩብ ውእቱ ለኢየሩሳሌም ።
ለኢየሩሳሌም አቅራቢያ ነበርና ። ሐተታ ወሰብአ ሀገሩ ይጸልዕዎ ያለውን ይሻል ።
ወይመስሎሙ ከመ ሶቤሃ ታስተርኢ መንግሥተ እግዚአብሔር ።
መንግሥተ ሰማያት ያን ጊዜ ፈጥና የምትሰጥ ይመስላቸው ነበርና ። ሐተታ አሐዱ ብእሲ ክቡር ሐረርትቀ ብሔረ ያለውን ይሻል ። አንድም ይህን ሲሰሙ ወእንዘ ይመስል ሎሙ ይላል እየመሰለ ሲነግራቸው መንግሥተ ሰማያት ትሰጥ ትገለጥ ባለ ጊዜ እንዳትውል እንዳታድር ፈጥና እንድትሰጥ ዕወቁ ። ይሰወጥ ያለውን ይሻል ።

፲፪ ወይቤ አሐዱስ ኦ ብእሲ ክቡር ሐረርትቀ ብሔረ ይንሣእ ሎቱ መንግሥተ ወይሰወጥ ።

፲፪ እንድ የከበረ ሰው መንግሥትን እጅ አድርጎ ይመለስ ዘንድ ወደሩቅ አገር ሄደ ።

፲፫ ወጸውዓ አግብርቲሁ ዐሠርተ ወወሀቦሙ ዓሠርተ ምናናተ ።

፲፫ ዐሥሩን ባሮቹን ጠርቶ ዐሥር ምናን ሰጣቸው ። ሐተታ ዐሥራ ሁለቱ ወቄት አንድ ነጥር ዐሥራ ሁለቱ ነጥር አንድ ምናን ዐሥራ ሁለቱ ምናን አንድ መክሊት ። መክሊቱ ፳፻፻፷፰፻ ወቄት ይሆናል ።
ወይቤሎሙ ተገበሩ እንከ እስከ እዓቱ ።
እስክመለስ ድረስ ውጡበት ውረዱበት ብሎ ሰጣቸው ።

፲፬ ወሰብአ ሀገሩ ይጸልእዎ ፤

፲፬ ያገሩ ሰዎች ይጠሉት ነበር አይወዱትም ነበርና ።
ወፈነዉ ተናብልተ እምድኅሬሁ እንዘ ይብሉ ኢንፈቅዶ ለዝንቱ ይንግሥ ላዕሌነ ።
ይህ በኛ ላይ ሊነግሥብን አንወድም ብለው ከወደ ኋላው መልክተኞችን ላኩ ።

፲፭ ወእምዝ አተወ ነሢኦ መንግሥተ ።

፲፭ ከዚህ በኋላ መንግሥትን እጅ አድርጎ ተመለሰ ።
ወአዘዘ ያምጽእዎሙ ለአግብርቲሁ ዘወሀቦሙ ወርቀ ከመ ያእምር ዘከመ ተገበሩ ።
እንዴት እንዳተረፉ ያውቅ ዘንድ ወርቁን የሰጣቸውን ባሮቹን ያመጧቸው ዘንድ አዘዘ ።

፲፮ ወመጽአ ቀዳማዊ ወይቤሎ እግዚኦ ምናንከ ዐሠርቱ ።

፲፮ አንዱ መጥቶ አቤቱ ምናንህ ዐሥር ነበር ።
ወዐሠርተ ምናናተ ረባሕኩ ።
ዐሥር ምናን አተረፍኩ አለው ።

፲፯ ወይቤሎ እግዚኡ አኅብር ኄር ወምእመን ዘበውኁድ ምእመነ ኮነከ ላዕለ ብዙኅ እስይመከ።

፲፯ አንተ የታመንከ በጐ ባሪያ በጥቂቱ ከታመንክ በብዙ ላይ እሾምሃለሁ ።
ተሠየም ላዕለ ዐሥሩ አህጉር ባሥሩ አገር ተሾም አለው በሠርቱን ቃላት ጠብቆ በሚገኝ ክብር መክበሩን መናገር ነው ።

፲፰ ወመጽአ ካልዑሂ ወይቤሎ እግዚእ ምናንከ ኃምስቱ ።

፲፰ ሁለተኛውም አቤቱ ገንዘብህ አምስት ምናን ነበር ።
ወኃምስተ ምናናተ ረባሕኩ ።
አምስት አተረፍኩ ።

፲፱ ወይቤሎ ሎቱኒ አንተኒ ተሠየም ላዕለ ኃምስቱ አህጉር ።

፲፱ እርሱን አንተም ባምስቱ አገር ተሾም አለው ። በአምስቱ አዕማደ ምሥጢር በሚገኝ ክብር መክበሩን መናገር ነው ።

፳ ወመጽአ ሣልሱኒ ወይቤሎ እግዚእ ነያ ምናንከ እንተ ኀቤየ እንበርክዋ ወጠብለልክዋ ፡ ውስተ ሰበንየ ።

፳ ሦስተኛም መጥቶ በመጠምጠሚያዬ የጠቀለልኳት ገንዘብህ እነሆ ይህች ናት ማለት ፡ ለራሴ ጠብቄ ለሌላው አላስተማርሁም ።

፳፩ እስመ ፈራህኩከ እስመ እእምረከ ከመ ዕፁብ ብእሲ አንተ ።

፳፩ የምታስጨንቅ ሰው እንደሆንህ ስላወቅሁ ፈርቻለሁና ።
ወትነሥእ ዘኢያንበርከ ።
ያላኖርከውን የምታነሣ ።
ወተአርር ዘኢዘራዕከ ።
ያልዘራኸውን የምትሰበስብ ጨካኝ እንደሆንክ ስላወቅሁ ።

፳፪ ወይቤሎ እግዚኡ በከመ ቃልከ እኴንነከ እ ገብር እኩይ ወወሐካይ ።

፳፪ አንተ ክፉ ሀኬተኛ ባሪያ እንደ ቃልህ አፈርድብሃለሁ ።

ተአምረኒኑ ከመ ዕፁብ ብእሲ አነ አነሥእ ዘኢያንበርኩ ወአአርር ዘኢዘራዕኩ ወአስተጋብእ ዘኢዘረውኩ ።
ያልበተንኩትን የምሰበስብ ያልዘራሁትን የማጭድ ያላኖርኩትን የማነሣ ጽኑ ጨካኝ መሆኔን ታውቃለህን ።

፳፫ ወለምንት ዘኢያግባእከ ወርቅየ ውስተ ማዕድየ ።

፳፫ ስለምን ገንዘቤን ወደለዋጮች ያላኖርህ ።
ወለልየ አቲውየ እምአስተገበርክዎ ምስለ ረባሑ ።
እኔ መጥቼ ለሚያስተርፍ እሰጠው ነበር ።

፳፬ ወይቤሎሙ ለእለ ይቀውሙ ሀየ ንሥኡ እምላዕሌሁ ዘንተ ምናነ ወወሀብዎ ለዘቦቱ ፲ቱ ምናናት ።

፳፬ ከዚያ ቆመው ያሉትን ይህን ገንዘብ ወስዳችሁ ዐሥር ላለው ስጡት አላቸው ።

፳፭ ወይቤልዎ እግዚእ አኮኑ ቦቱ ዐሠርቱ ምናናት ።

፳፭ አቤቱ ዐሥር ምናን ያለው አይደለምን አሉት ።

፳፮ ወይቤሎሙ እብለክሙ እስመ ለኵሉ ዘቦ ይሁብዎ ወይዌስክዎ ። ማቴ፡፲፫፥ ፲፪ ማር፡ ፬ ፡ ፳፭ ሉቃ፥ ፰ ፡ ፲፰ ።

፳፮ ላለው ሁሉ ይሰጡታል ይጨምሩለታልም።
ወለዘሰ አልቦ እለሂ ቦ ያሐይድዎ የሌለውን ግን ያለውንም ይወስዱበታል ።

፳፯ ወባሕቱ ለእልክቱስ ጸላዕትየ እለ ኢይፈቅዱ እንግሥ ላዕሌሆሙ አምጽእዎሙ ዝየ ወርግዝዎሙ በቅድሜየ ።

፳፯ ልነግሥባቸው የማይወዱ እኒህን ጠላቶቼን ግን አምጥታችሁ በፊቴ እየወጋችሁ ግደሏቸው አለ ።

በእንተ በአተ ኢየሱስ ኀበ ኢየሩሳሌም ።

፳፰ ወዘንተ ብሂሎ አምልአ ቅድመ ወዓርገ ኢየሩሳሌም ።

፳፰ ይህንም ተናግሮ በፊታቸው ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ ።

፳፱ ወሶበ በጽሐ ቤተ ፋጌ ። ማቴ፡፳፩ ፡ ፩ ማር፡፲ ፡ ፩

፳፱ ወደቤተ ፋጌም በቀረበ ጊዜ ፤
ወቢታንያ ኀበ ደብረ ዘይት ዘስሙ ኤሌዎን ።
ደብረ ዘይት ወደሚባል ቢታንያም በደረሰ ጊዜ ።
ፈነወ ፪ተ አምአርዳኢሁ ።
ከደቀ መዛሙርቱ ሁለቱን ላከ ።

፴ ወይቤሎሙ ሑሩ ሀገረ ዘቅድሜክሙ ።
፴ ወደፊታችሁ ካለ አገር ሂዱ ።
ወበዊአክሙ ትረክቡ ዕዋለ ዕሱረ ዘኢተፅዕኖ ሰብእ ።

በገባችሁም ጊዜ ሰው ያልተቀመጠበት ያህያ ግል
ገል ታገኛላችሁ ።
ፍትሕዎ ወእምጽእዎ ሊተ ።
ፈትታችሁ አምጡልኝ ።

፴፩ ወእመቦ ዘይቤለክሙ ለምንት ትፈትሕዎ።
፴፩ ለምን ትፈቱታላችሁ የሚል ሰው ቢኖር ።
በሉ እግዚኡ ይፈቅዶ ።
ጌታው ይሻዋል በሉ ።

፴፪ ወሐዊሮሙ እለ ተፈነዉ ረከቡ በከመ
ይቤሎሙ ።
፴፪ የተላኩትም እንደ ነገራቸው አገኙ ።
፴፫ ወፈትሑ ዕዋለ ።
፴፫ ያህያውን ግልገል ፈቱ ።
ወእንዘ ይፈትሑ ዕዋለ ይቤልዎሙ ኦጋእዝቲሁ
ለምንት ትፈትሑ ዕዋለ ።
ያህያውን ግልገል ሲፈቱ ጌቶቹ ለምን ትፈቱታላችሁ
አሏቸው ።

፴፬ ወይቤሉ እግዚኡ ይፈቅዶ ።
፴፬ ጌታው ይሻዋል አሉ ።
፴፭ ወነሥኡ ወወሰድዎ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፭ ወደጌታችን ይዘውት ሄዱ ።
ወረኀኑ አልባሲሆሙ ዲበ ዕዋል ።
ልብሳቸውን በአህያው ግልገል ላይ ጕዘጕዙ ።
ወአፅዓንዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ዲቤሁ ።
ጌታንም አስቀመጡት ።

፴፮ ወእንዘ የሐውሩ ነጸፉ አልባሲሆሙ ውስተ
ፍኖት ።

፴፮ ሲሄዱም ልብሳቸውን ከመንገድ ይጕዘ
ጕዙሉ ።

፴፯ ወበጺሖሙ ኀበ ሙራደ ዐቀበ ዘደብረ
ዘይት ።

፴፯ ወደ ደብረ ዘይት በሚወርደውም መንገድ
በደረሱ ጊዜ ሐተታ እሬ ቆላ ነው ከታች የመጣው
አቀበቱን ወጥቶ የሚያርፍበት ከላይ የመጣ መጥቶ
የሚያርፍበት ነው ከዚያ በደረሱ ጊዜ ።
አኀዙ ኵሎሙ አርዳኢሁ ይትፌሥሑ ወይሴብሕዎ
ለእግዚአብሔር በዓቢይ ቃል ።
ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ ደስ ብሏቸው እግዚአብሔርን
በታላቅ ቃል ያመሰግኑት ጀመር ።
በእንተ ኵሉ ኃይል ዘርእዩ ።
ስላዩት ኃይል ሁሉ ።

፴፰ እንዘ ይብሉ ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ
እግዚአብሔር ።

፴፰ በእግዚአብሔር ስም የሚመጣ እሱ የተ
ባረከ ነው ።

ወቡሩክ ንጉሠ እስራኤል ።
የእስራኤልም ንጉሥ የተባረከ ነው ።
ሰላም በምድር ።
በምድር ሰላም ።
ወስብሐት በአርያም ።
በአርያምም ምስጋና እያሉ ።

፴፱ ወቦ እምፈሪሳውያን ወእምሕዝብ እለ ይቤ
ልዎ ሊቅ ገሥጾሙ ለአርዳኢከ ።

፴፱ ከፈሪሳውያን ወገን ከሕዝቡ ወገን መም
ህር ሆይ ደቀመዛሙርትህን ተቆጣቸው ያሉትምአሉ።

፵ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ለእመ አርመሙ ።
እሉ እሉንቱ ኦእባን ይኬልሑ።
እኒህ ዝም ቢሉ እኒህ ድንጋዮች ይጮሀሉ ብሎ መለ
ሰላቸው ።

፵፩ ወበጺሖ ርእያ ለሀገር በከየ ላዕሌሃ ።
፵፩ በደረሰም ጊዜ አገሪቱን አይቶ ማለት
የአይሁድን ሰውነት አይቶ አለቀሰላት ።
፵፪ ወይቤላ ሶበሰ ተእምሪ ዮም ሰላምኪ ።
፵፪ እውቀሽስ ቢሆን የይቅርታሽ ቀን ዛሬ
ነበር ።
ወባሕቱ እምይእዜሰ ተሰወረ እምአዕይንትኪ ።
ዛሬ ግን ከዕውቀት ተገተሻል ማለት አላወቅሽም
እንጂ ።
፵፫ ወይበጽሕ መዋዕል እመ የዓግቱኪ ፀርኪ ።
፵፫ ጠላቶችሽ ከበውሽ የሚስፍሩብሽ ጊዜ ይደ
ርሳል ።
ወይትአየኑኪ ላዕሌኪ ።
ይከትሙብሻል ።
ወየኃጽሩኪ ።
ይከቡሻል ።
ወያስተጋብኡኪ እምኵለሄ ።
ካራቱ ማዕዘን ይሰበስቡሻል ።

፵፬ ወይነጽሑኪ ለኪ። ማቴ. ፳፬ ፡ ፪ማር. ፲፫፡፪
ሉቃ ፡ ፳፩ ፡ ፮ ።
፵፬ ይጥሉሻል ።
ወለውሉድኪኒ ምስሌኪ ።
ልጆችሽንም ካንች ጋራ እንዳንች ይጥሏቸዋል ።
ወኢየኃድጉ ዝየ እብነ ዲበ እብን በውስቴትኪ ።
ደንጊያንም በደንጊያ ላይ አይተውልሽም ።
እስመ ኢያእመርኪ መዋዕለ ሣህልኪ ።
የይቅርታሽን ወራት አላወቅሽምና ።

በእንተ ተሰዶቶሙ ለእለ ያረኵሱ ቤተ መቅደስ ።

፵፭ ወቦአ ምኵራበ ወሰደደ ኵሎ እለ ይሠይጡ
ወይሣየጡ በቤተ መቅደስ ።

፵፭ ከምኵራብ ገብቶ በቤተ መቅደስ የሚሸ
ጡትን የገዙትንም ሁሉ አስወጣ ።

ወገፍትዖ ማዕዳቲሆሙ ለመወልጣን ።
የለዋጮችንም ወንበር ገለበጠ ።
ወመናብርቲሆሙኒ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ገንጸለ ።
ርግብ የሚሸጡትንም ወንበር ገለበጠ ።

፴፮ ወይቤሎሙ ጽሑፍ ዘይብል ቤትየሰ ቤተ ጸሎት ይሰመይ ።

፴፮ ቤቴስ የጸሎት ቤት ይባላል የሚል ጽሑፍ አለ ።
ወአንትሙሰ ረሰይክምዎ በአተ ፈያት ወሠረቅት ።
እናንተ ግን የሌባ ዋሻ አደረጋችሁት አላቸው ።

፴፯ ወኵሎ አሚረ ይሜህሮሙ በምኵራብ ።
፴፯ ዘወትር በምኵራብ ያስተምራቸው ነበር።
ወየኃሥሡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወሊቃናተ ሕዝብ በዘይቀትልዎ ።
የካህናት አለቆችና ጸሐፊዎች የሕዝቡም አለቆች ይገሉት ዘንድ ይሹት ነበር ።

፴፰ ወኃጥኡ በዘይሬስይዎ ።
፴፰ የሚያደርጉትን አጡ ።
እስመ ኵሎሙ ሕዝብ ይሰቀሉ በአጽምዖቱ ።
ሕዝቡ ሁሉ ለትምህርቱ ይሳሱ ነበርና ።

ዘከመ ተሰእልዎ ኢየሱስ በእንተ
ጥምቀት ዘዮሐንስ ።

ምዕራፍ ፳ ።

፩ ወእምዝ አሐተ ዕለተ እንዘ ይሜህሮሙ ለሕዝብ በምኵራብ ወይነግሮሙ ቆሙ ላዕሌሁ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ወረበናት። ማቴ. ፳፩ ፥ ፳፫ ማር. ፲፩ ፥ ፳፯ ።

፩ ከዚህ በኋላ ባንድ ቀን በምኵራብ ለሕዝቡ ሲያስተምራቸው የምሥራችም ሲነግራቸው የካህናት አለቆችና ጸሐፊዎች የሕዝቡም አለቆች ተነሡበት ።

፪ ወይቤልዎ ንግረነ በመባሕተ መኑ ትገብር ዘንተ ።

፪ በማን ሥልጣን ይኸን ትሠራለህ ።
ወመኑ አብሐከ ትግበር ከመዝ ።
እንዲህስ ታደርግ ዘንድ ማን አሠለጠነህ አሉት ።

፫ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እሴአለክሙ አነሂ አሐተ ነገረ ።

፫ እኔም አንድ ነገር እጠይቃችኋለሁ ።
ወንግሩኒ ፤
እናንተም ንገሩኝ ።

፬ ጥምቀቱ ለዮሐንስ እምአይቴኑ ይእቲ ።
፬ የዮሐንስ ጥምቀቱ ከወዴት ናት ።
እምሰማይኑ ።
ከሰማይን ናት ።
ወሚመ እምሰብእኑ ።
ወይም ከሰው ናትን አላቸው ።

፭ ወተበሃሉ በበይናቲሆሙ ፤
፭ እርስ በራሳቸው እንዲህ አሉ ።
እመሂ ንብሎ እምሰማይ ይብለነ በእፎ ዘኢአመንክምዎ ።
ከሰማይ ነው ያልነው እንደሆነ ምነው ያላመናችሁበት ይለናል ።

፮ ወእመሂ ንብሎ እምሰብእ ይዌግሩነ ኵሉ ሕዝብ ።

፮ ከሰው ነው ያልነውም እንደሆነ ሕዝቡ ሁሉ ይጣሉናል ።
እስመ ኵሎሙ ተአመንዎ ለዮሐንስ ከመ ነቢይ ውእቱ ።
የ ሐንስ ነቢይ እንደሆነ ሕዝቡ ሁሉ አምነውታልና ።

፯ ወአውሥኡ ወይቤልዎ ኢነአምር እምኀበ ኮነት ።

፯ ከወዴት እንደሆነች አናውቅም ብለው መለሱ ።

፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አነሂ ኢይነግረክሙ በመባሕተ መኑ እገብር ከመዝ ።

፰ እኔም ይህን የምሠራ በማንም ሥልጣን እንደሆነ አልነግራችሁም አላቸው ።

በእንተ እኩያን ዐቀብተ ወይን ።

፱ ወአኃዘ ይመስል ሎሙ ለሕዝብ ዘንተ ምሳሌ ።

፱ ለሕዝቡም ይህን ምሳሌ ይመስልላቸው ጀመረ ።
ወይቤሎሙ ብእሲ ተከለ ወይነ ።
ሰው ወይን ተከለ ።
ወሢመ ሎቱ ዓቀብተ ለወይኑ ።
ለወይኑም ጠባቂ ሾመ ።
ወአከረየ ምክያደ ።
አውድማ አስቆፈረ ።
ወሐነጸ ማኅፈደ ።
ግንብም ሠራ ።
ወነገደ ርኁቀ ብሔረ ።
ወደሩቅ አገርም ሄደ ።
ወጐንደየ እቲወ ።
ብዙ ዘመንም ኖረ ።

፲ ወእመ ኮነ ጊዜ ፍሬሁ ፈነወ ገብሮ ኀበ ዓቀብተ ወይን ።

፲ በሚያፈራበት ጊዜ ባሪያውን ወደ ወይኑ ጠባቆች ላከ ።
ከመ ይፈንው ሎቱ እምፍሬ ወይኑ ።
ከወይኑ ይልኩለት ዘንድ ።
ወዘበጥዎ ዓቀብተ ወይን ለገብሩ ወፈነውዎ ዕራቆ ።
ወይን ጠባቆች ግን ባሪያውን ደብድበው ባዶውን ሰደዱት ።

፲፩ ወዳግመ ፈነወ ካልዓ ገብሮ ።
፲፩ ዳግመኛም ሌላውን ባሪያውን ላከ ።
ወኪያሁኒ ዘበጥዎ ወአሰርዎ ወፈነውዎ ዕራቆ ።
እርሱንም አስረው ደብድበው ባዶውን ሰደዱት ።
፲፪ ወካዕበ ፈነወ ሣልሳየ ገብሮ ።

፲፪ ዳግመኛም ሦስተኛውን ባሪያውን ላከ ።
ወኪያሁኒ ፈቅዕዎ ወወሰድዎ ።
እርሱንም አቁስለው አባረሩት ።

፲፫ ወይቤ በዓለ ወይን ምንተ እንከ እሬሲ ።
፲፫ የወይኑም ባለቤት እንግዲህ ምን ላድርግ አለ ።
እፌኑ ወልድየ ዘአፈቅር ።
የምወደውን ልጄን እልካለሁ ።
ለእመ ኪያሁ የኀፍርዎ ርእዮሙ ።
እርሱን አይተው ያፍሩት እንደሆነ ብሎ ።
ወፈነዎ ፤ ላከው ።

፲፬ ወሶበ ርእይዎ ዓቀብተ ወይን ተማከሩ በበይናቲሆሙ ወይቤሉ ዝንቱ ውእቱ ወራሲሁ ።

፲፬ የወይኑ ጠባቂዎችም አይተው ወራሽ ልጁ ይህ ነው ።
ንዑ ንቅትሎ ወንርከብ ርስቶ ።
ኑ እርሱን ገድለነው ርስቱን እጅ እናድርግ ብለው መከሩ ።

፲፭ ወአውፅእዎ እፍአ እምዓጸደ ወይን ወቀተልዎ ።

፲፭ ከወይኑ ቦታ ውጭ አውጥተው ገደሉት ።
ወሶበ መጽአ በዓለ ዓጸደ ወይን ምንተ እንከ ይሬስዮሙ ።
የወይኑ ባለቤት በመጣ ጊዜ ምን ያደርጋቸዋል አሳቸው ።

፲፮ ይመጽእ ወይቀትሎሙ ለእልከቱ ዓቀብተ ወይን ።

፲፮ መጥቶ የወይኑን ጠባቂዎች ይገድላቸዋል ።
ወይሁብ ወይናሂ ለካልዓን ዓቀብት ።
ወይኑንም ለሌሎች ጠባቆች ይሰጣል እንጂ አላቸው ።
ወሰሚዖሙ ቃሎ ይቤሉ ሐሰ ኢይከውን ከመዝ ።
ይኽንንም በሰሙ ጊዜ ይኽነንስ የሚያደርግ የለም አሉት ።

፲፯ ወነጸርሙ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ምንትኑ ጽሑፍ ዘይብል እብን እንተ መነንዋ ነደቅት ይእቲ ኮነት ውስተ ርእሰ ማዕዘንት ። መዝ ፤ ፻፲፯ ፤ ፳፩ ኢሳ ፤ ፳፰ ፤ ፲፮ ማቴ ፤ ፳፩ ፤ ፵፪ ግብ ፤ ፬ ፤ ፳፩ ሮሜ ፤ ፱ ፤ ፴፫ ፩. ጴጥ ፪ ፤ ፯ ።

፲፯ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ወደርሳቸው አይቶ አናጾች የናቁት ድንጊያ የማዕዘን ራስ ሆነች የሚለው ጽሕፈት ምንድነው አላቸው ።

፲፰ ወኵሉ ዘወድቀ ዲበ ይእቲ እብን ይትቀጠቀጥ ።

፲፰ በዚያችም ደንጊያ ላይ የወደቀ ሁሉ ይሰበራል ።
ወለዘኒ ወድቀት ዲቤሁ ትቀጠቅጦ ወትደምቆ ።
የወደቀችበትንም ትሰብረዋለች ።

በእንተ ጸባሕት ዘቄሣር ።

፲፱ ወፈቀዱ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ከመ የእኃዝዎ ሶቤሃ ወፈርህዎሙ ለሕዝብ ።

፲፱ የካህናት አለቆችና ጸሐፎችም ያን ጊዜም ሊይዙት ወደው ሕዝቡን ፈሩዋቸው ።
እስመ አእመሩ ከመ በእንቲአሆሙ መሰለ ዘንተ ።
ይህንም ምሳሌ እንደ መሰለባቸው ዐውቀዋልና ።

፳ ወተግኅሥሙ እምኔሁ አጽንሑ ሎቱ እለ ይትዓቀብዎ ወፈነዉ ኀቤሁ ሰብአ ዓይን እለ ያጸድቁ ርእሶሙ ከመ ያስሕትዎ በቃሉ ። ማቴ. ፳፪ ፤ ፲፭ ማር ፤ ፲፪ ፤ ፲፫

፳ ጻድቃን መስለው በነገር ያጸምዱበት ዘንድ ተጠባባቂዎች አኖሩበት ።
ወከመ ያግብእዎ ለመኳንንት
ላለቆችም አሳልፈው ይሰጡት ዘንድ ፤
ወለመሳፍንት ፤
ለሹማምንቱም ፤

፳፩ ወተሰእልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ነአምር ከመ ጽድቀ ትነግር ወትሜህር ።

፳፩ መምህር ሆይ እውነት እንድትናገር በውነትም እንድታሰተምር ፤
ወኢታደሉ ለገጽ ወኢለመኑሂ ።
ፊት አይተህ ለማንም ለማን እንዳታደላ እናውቃለን አሉት ።

ወርትዓ ትሜህር ፍኖተ እግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርን መንግሥት በውነት ታስተምራለህ እንጂ ።

፳፪ ይከውነነሁ ነሀብ ጸባሕተ ለቄሣር ።
፳፪ ለቄሣር ግብር ልንሰጥ ይገባልን ፤
ወሚመ አልቦኑ ፤
ወይም አይገባምን ብለው ጠየቁት ፤

፳፫ ወአእመሮሙ ትምይንቶሙ ፤
፳፫ ተንኮላቸውን አውቆባቸው ፤
ይቤሎሙ ለምንት ታሜክሩኒ ።
ለምን ትፈትኑኛላችሁ ።

፳፬ አርእዩኒ አላደ ዲናሩ ።
፳፬ ወርቁን አላዩኝ አላቸው ።
ወአምጽኡ ወአርአይዎ ፤
አምጥተው አሳዩት ።
ወደቤሎሙ ዘመኑ መልከዑ ወመጽሐፉ ።
ቅርጹ ጽሕፈቱ የማነው አላቸው ።
ወአውሥኡ ወይቤልዎ ዘቄሣር ።
የቄሣር ነው ብለው መለሱለት ።

፳፭ ወይቤሎሙ ዘቄሣር ሀቡ ለቄሣር ።
፳፭ የቄሣርን ለቄሣር ፤
ወዘእግዚአብሔር ለእግዚአብሔር ።
የእግዚአብሔርን ለእግዚአብሔር ስጡ አላቸው ።

፳፮ ወስእንዎ አስሕቶቶ በቃሉ በቅድመ ኵሉ ሕዝብ ።

፳፮ በሕዝቡ ሁሉ ፊት በነገሩ ማሳት ተሳናቸው ወአንከሩ ሣዕማአ አፉሁ ወአውሥኦቶ ወአርመሙ ። አከናውኖ መናገሩን ምላሹን ሰምተው አደንቁ ዝም አሉ ።

## በእንተ ሰዱቃውያን ወበእንተ ትንሣኤ ሙታን ።

፳፯ ወመጽኡ ኀቤሁ ሰዱቃውያን እለ ይብሉ ኢየሐይዉ ምውታን ።

፳፯ ሙታን አይነሡም የሚሉ ሰዱቃውያን ወደርሱ መጡ ።

፳፰ ወተስአልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ሙሴ ጸሐፈ ለነ እንዘ ይብል ለእመቦ ብእሲ ዘሞተ እኁኁ ወኀደገ ብእሲቶ ።

፳፰ መምህር ሆይ ሰው ልጅ ሳይወልድ ቢሞት እንዘ አልቦ ውሉድ ።
ልጅ ሳይኖረው ።
ያውስባ እኁኁ ለብእሲቱ ወያቅም ዘርዓ ለእኁኁ ።
ወንድሙ ሚስቱን አግብቶ ለወንድሙ ዘር ይተካ ብሎ ሙሴ ጻፈልን ።

፳፱ ወሀለዉ እንከ ኀቤነ ሰብዓቱ አኃው ።
፳፱ ሰባት ወንድማማች ከኛ ዘንድ ነበሩ ።
ወአውሰበ ዘይልሕቅ ብእሲተ ወሞተ እንዘ አልቦ ውሉድ ።
ታላቁ ሚስት አግብቶ ልጅ ሳይወልድ ሞተ ።

፴ ወከማሁ አውሰባ ካልዑ ።
፴ ሁለተኛውም እንዲሁ አገባት ።
ወሣልሱኒ ነሥአ ከማሁ ።
ሦስተኛውም አገባት ።
ወኢኀደጉ ውሉደ ።
ልጅ ግን አልነበራቸውም ።

፴፩ ወእስከ ሰብዓቲሆሙ ከማሁ አውሰብዋ ወሞቱ እንዘ አልቦሙ ውሉድ ።

፴፩ ሰባቱም እንዲሁ አያገቧት ልጅ ሳይወልዱ ሞቱ ።

፴፪ ወድኅረ ኵሎሙ ሞተት ይእቲ ብእሲት ።
፴፪ ከሁሉም በኋላ ሴቲቱ ሞተች ።

፴፫ ወእመ የሐይ ው ሙታን ለመኑ እምኔሆሙ ትከውኖ ብእሲተ ።

፴፫ ሙታን በሚነሡበት ቀን ለማናቸው ሚስት ትሆናለች ።
እስመ ሰብዓቲሆሙ አውሰብዋ ።
ሰባቱም አግብተዋታልና ፤

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ውሉደ ዝንቱዓለምያወስቡወይትዋሰቡ።
የዚህ ዓለም ልጆች ያገባሉ ይጋባሉ ።
ይወልዱ ወይትዋለዱ ።
ይወልዳሉ ይዋለዳሉ ።

፴፭ ወእለሰ ይደልዎሙ ይረከብዎ ለዝክቱ ዓለም ።

፴፭ ያን ዓለም ይወርሱት ዘንድ የሚገባቸው ሰዎች ግን ።
ኢመ የሐይዉ ምውታን ኢያወስቡ ወኢይትዋሰቡ ።
ሙታን በሚነሡበት ጊዜ አያገቡም አይጋቡም ።

፴፮ ወኢይትከሃሎሙ እንከ መዊት ።
፴፮ ሁለተኛም ሞት የለባቸውም ።
አላ ከመ መላእክተ እግዚአብሔር በሰማያት እሙንቱ ።
እንደ መላእክት ይሆናሉ እንጂ ።
ወውሉደ እግዚአብሔር ይከውኑ ።
የእግዚአብሔር ልጆች ይባላሉ ።
ወውሉደ ሕይወት እሙንቱ ።
የሕይወትም ልጆች ናቸው ።

፴፯ ወከመሰ የሐይዉ ምውታን ሙሴሂ ነገረ ዘከመ ይቤሎ እግዚአብሔር በኀበ ዕፀ ጳጦስ

አነ ውእቱ አምላከ አብርሃም ወአምላከ ይስሐቅ ወአምላከ ያዕቆብ ። ዘፀ፡ ፫ ፡ ፮ ።

፴፯ ሙታን ግን እንዲነሡ በቍጥቋጦው ዘንድ የአብርሃም አምላክ የይስሐቅ አምላክ የያዕቆብ አምላክ እኔ ነኝ ብሎ እግዚአብሔር እንደ ነገረው ሙሴም ተናግሯል ።

፴፰ ኢኮነኬ አምላከ ምውታን ።
፴፰ እርሱም የሙታን አምላክ አይደለም ።
አላ አምላከ ሕያዋን ውእቱ ።
የሕያዋን አምላክ ነው እንጂ ።
እስመ ኵሎሙ ሕየዋን እሙንቱ በኀቤሁ ።
በርሱ ዘንድ ሁሉም ሕየዋን ናቸውና ።

፴፱ ወአውሥኡ ሰብአ እምጸሐፍት ወይቤሉ ሊቅ ሠናየ ትቤ ።

፴፱ ከጸሐፊዎች ወገን የሚሆኑ ሰዎችም መምህር ሆይ መልካም ተናግረሃል ብለው መለሱ ።

፵ ወአልቦ እንከ መኑሂ ዘተሀበለ ይሰአሉ ።

፵ ማንም ማን ሊጠይቀው የወደደ የለም ።

ዘከመ ውእቱ መሲሕ ወልደ ዳዊት ።

፵፩ ወይቤሎሙ እፎኑ ይቤልዎ ለክርስቶስ ወልደ ዳዊት ።

፵፩ ክርስቶስን የዳዊት ልጅ እንደምን ይሉታል ።

፵፪ ወለሊሁ ይቤ በመጽሐፈ መዝሙር ይቤሎ እግዚእ ለእግዚእየ ንበር በየማንየ እስከ እገብእሙ ለጸላእትከ ታሕተ መከየደ እገሪከ ። መዝ ፡ ፻፲ ማቴ፡ ፳፪፡ ፵፬ ። ማር ፡ ፲፪ ፡ ፴፮ ።

፵፪ እርሱ ጌታዬ ጌታዬን ጸላቶችህን ከእግርህ በታች እስካደርግልህ በቀኜ ተቀመጥ አለው ።

፵፬ ዘለሊሁ እንከ ዳዊት እግዚእየ ይቤሎ እፎ እንከ ይከውኖ ወልዶ ።

፵፬ ዳዊት እርሱ ራሱ ጌታዬ ያለው እንደምን ልጁ ይሆናል ።

በእንተ ተመድልዎት ዘጸሐፍት ።

፵፭ ወእንዘ ኵሎሙ ሕዝብ ይሰምዑ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ተዓቀብዎሙ ለጸሐፍት እለ ይፈቅዱ ያንሶስዉ ተላቢሶሙ ።

፵፭ ሕዝቡ ሁሉ ሲሰሙ ለደቀ መዛሙርቱ ረጅም ልብስ ለብሰው ከሚመላለሱ ተጠበቁ አላቸው ።
ወያፈቅሩ ተአምኆ በምሥያጥ ።
ባደባባይ እጅ ሊነሡዋቸው ከሚወዱ ።
ወነበረ ፍጽም በውስተ አፅዋዳት ።
ባደባባይ ፊት ለፊት መቀመጥ የሚወዱ ።
ወርእሰ ምርፋቃት በውስተ ምሳሐት ።
በምሳም ጊዜ በራስጌ መቀመጥን ከሚወዱ ።

፵፮ እለ ይሠጕጥዎን ለአብያተ መበለታት ።
፵፮ የባልቴቶችን ገንዘብ ከሚበሉ ከጸሐፊዎች ተጠበቁ ።
ወይትሜየኑ በምክንያተ አንኆ ጸሎቶሙ ።
በምክንያት ጸሎታቸውን ያረዝማሉ ይተነኰላሉ ።
፵፯ እሙንቱ ይነሥኡ ዘየዓቢ ኵነኔ ።
፵፯ እኔህ ታላቅ ፍርድ ይቀበላሉ ።

በእንተ ጸሪቀ መበለት ነዳይት ።

ምዕራፍ ፳፩ ።

፩ ወነጸረ አብዕልተ ዘያበውኡ መባዖሙ ውስተ ሙዳየ ምጽዋት ።

፩ መባቸውን ከምጽዋቱ ሣጥን የሚያገቡ ባለጸጎችን አየ ።

፪ ወርእየ ዕቤረ መበለተ ዘአብእት ክልኤተ ጸራይቀ ።

፪ አንዲት ድኃ ባልቴትም ከዚያ ሁለት ነሐስ ስትጥል አየ ።

፫ ወይቤሎሙ አማን እብለከሙ ከመ ዛቲ ነዳይት ዕቤር አብዝኃት አብአ መባዕ ለእግዚአብሔር ።

፫ ይህች ድኃ ባልቴት ከሁሉ ይልቅ አብዝታ ለእግዚአብሔር መባዕ እንደሰጠች በውነት እነግራ ራችኋለሁ ።

፬ እስመ እሉ ኵሎሙ እምተረፈሙ አብሁ መባዖ ለእግዚአብሔር ።

፬ እኒህ ሁሉ ከተረፋቸው ለእግዚአብሔር መባዕ ሰጥተዋልና ።
ወዛቲሰ ኵሎ ጥሪታ ዘባቲ አብአት ።
ይህች ግን ያላትን ገንዘብ ሁሉ ሰጥታለች ።

በእንተ ትንቢተ ጥፍአተ ቤተ
መቅደስ ወህገረ ኢየሩሳሌም ።

፭ ወቦ እለ ይቤልዎ በእንተ መቅደስ ሠናይ ዕበኒሁ ወሥርግው ንድቁ ።

፭ ሕንጻው የተጌጠ ግንቡ ያማረ የቤተ መቅደስን ነገር የነገሩት አሉ ።

፮ ወይቤሎሙ ትሬዕዩኑ ዘንተ ።
ማቴ ፡ ፳፬ ፡ ፩. ማር. ፲፫ ፡ ፩. ሉቃ ፲፱ ፡ ፵፬ ።

፮ ይህን ታያላችሁ ።
ይመጽእ መዋዕል አመ ኢይትኃደግ ዝየ እብን ዲበ
እብን ዘኢይትነሣእ ።
ደንጊያ በደንጊያ ላይ ሳይፈርስ የማይቀርበት ዘመን
ይመጣል ።

፯ ወተስእልዎ ወይቤልዎ ሊቅ ማእዜ ይከውን
ዝንቱ ።

፯ መምህር ሆይ ይህ የሚደረገው ምን ጊዜ ነው
ወምንት ተአምሪሁ አመ ይከውን ዝንቱ ።
ይህ የሚደረግበትስ ምልክቱ ምንድነው ብለው ጠየ
ቁት ።
ወይቤሎሙ ዑቁ ኢያስሕቱክሙ ።
እንዳያስቷችሁ አስተውሉ ።

፰ ወብዙኃን ይመጽኡ በስምየ እንዘ ይብሉ
አነ ውእቱ ክርስቶስ ።

፰ እኔ ክርስቶስ ነኝ እያሉ ብዙ ሰዎች በስሜ
ይመጣሉ ።
ወበጽሐ ዕድሜሁ ።
ዘመኑም ደርሷል እያሉ ይመጣሉ ።
ወኢትሑሩ ወኢትትልውዎሙ ። አትከተሏቸው ።

፱ ወእመ ሰማዕክሙ ቀትለ ።
፱ ሰልፍን ።
ወሐከክ ኢትደንግፁ ።
ጩብ ክርክር በሰማችሁ ጊዜም አትፍሩ ።
እስመ ይከውን ቅድመ ከመዝ ።
አስቀድሞ እንዲህ ይደረጋልና ።
ወባሕቱ አኮ ሶቤሃ ዘየኃልቅ ።
ነገር ግን ያን ጊዜ አይፈጸምም ።

፲ ወይቤሎሙ ይትነሥኡ ሕዝብ ዲበ ሕዝብ ።
፲ ሕዝብ በሕዝብ ላይ ።
ወነገሥት ዲበ ነገሥት ።
ነገሥታትም በነገሥታት ላይ ይነሣሉ ።

፲፩ ወይመጽእ ዓቢይ ረኃብ ወድልቅልቅ በበ
ብሔሩ ።

፲፩ በየሀገሩም ታላቅ መናወጥ ረኃብ ይመጣል ።
ወፍርሃት ላዕለ ሰብእ ።
በሰውም ላይ ፍርሃት ።
ወተእምር ዓቢይ ይከውን ።
በሰማይም ታላቅ ምልክት ይሆናል ።

፲፪ ወእምቅድመ ዝንቱ ኵሉ ይእኅዙክሙ ወይ
ወስዱክሙ አዕዋዲተ ።

፲፪ ከዚህ ሁሉ አስቀድሞ ይዘው ወደ ዐደባባይ
ይወስዷችኋል ።
ወይሞቅሑክሙ ወይወስዱክሙ ኀበ ነገሥት በእ
ንተ ስምየ ።
ስለ ስሜ አስረው ወደነገሥት ይወስዷችኋል ።

፲፫ ወዝንቱ ይረክበክሙ ከመ ይከውን ስምዓ
ላዕሌሆሙ ።

፲፫ በርሳቸው ላይ ምስክር ሊሆናችሁ ይህ
ይደርስባችኋል ።

፲፬ ዑቁ ኢተሀልዩ በልብክሙ ዘትብሉ ።
፲፬ የምትናገሩትን በልቡናችሁ እንዳታስቡ
አስተውሉ ።

፲፭ አነ እሁበክሙ አፈ ወጥበበ በዘኢይክሉ
ተዋሥኦተክሙ ወተዋቅሦተክሙ እለ ይትነሥኡ
ላዕሌክሙ ፤

፲፭ የሚነሡባችሁ እናንተን መከራከርና መቋ
ቋም በማይቻላቸው ገንዘብ እኔ አፍና ጥበብ እሰጣች
ኋለሁና ፤

፲፮ ወያገብኡክሙ አዝማዲክሙ ወአኃዊክሙ
፲፮ ወንድሞቻችሁና አባቶቻችሁ ።
ወአዕርክቲክሙ ወቢጽክሙ ።
ወዳጆቻችሁና ባልንጀሮቻችሁም አሳልፈው ይሰ
ጧችኋል ።

፲፯ ወኵሉ ይጸልኡክሙ በእንተ ስምየ ።
፲፯ በስሜ ስለ አመናችሁ ሁሉ ይጠሏችኋል ።
ወይቀትሉክሙ ። ይገድሏችኋል ።

፲፰ ወኢትትኃጐል አሐቲ እምሥእርተ ርእ
ስክሙ ፤

፲፰ ከራሳችሁ ጠጉር አንዲቱ አትጠፋም ፤
፲፱ ወበትዕግሥትክሙ ታጠርይዋ ለነፍስክሙ።
፲፱ በትዕግሥታችሁ መከራውን ታግሣችሁ
በመቀበላችሁ ነፍሳችሁን ታድንዋታላችሁ ጥሪት
ታደርጓታላችሁ ።

ዘከመ በዓይ ጥፍአታ ለኢየሩሳሌም ወሕዝብ ።

፳ ወአመ የዐግትዋ ሠራዊት ለኢየሩሳሌም ።
ዳን ፱ ፥ ፳፯ ማቴ. ፳፬ ፤ ፲፭ ማር. ፲፫ ፤ ፲፬ ።

፳ ኢየሩሳሌምን ሊከቧት ባያችሁ ጊዜ የምት
ጠፋበት ጊዜ እንደ ደረሰ ዕወቁ ።

፳፩ ወይእተ አሚረ እለ ውስተ ይሁዳ ይጕዩ
ውስተ አድባር ።

፳፩ ያን ጊዜ በይሁዳ ያሉ ወደተራራ ይሸሻሉ ።
ወእለሂ ማእከላ ይወፅኡ እምኔሃ ።
በመካከሏም ያሉ ከእሷ ይወጣሉ ።

፳፪ ወእለ ውስተ በሐውርቲሃ ኢይበውእዋ ።
፳፪ ባውራጃዋም ያሉ ወደርሷ አይገቡም ።

እስመ ዕድሜሃ ውእቱ በዘይትቤቀልዋ ።
በሚፈርዱባትትገንዘብ ይፈርዱባት ዘንድ ጊዜዋ ነውና።
ከመ ይብጻሕ ኵሉ ዘጽሑፍ ላዕሌሃ ።
በርሷ የተጻፈው ሁሉ ይደርስባት ዘንድ ።

፳፫ ወባሕቱ አሌ ሎን ለፅኑሳት ወለለ የሐፅና በውእቱ መዋዕል ።

፳፫ ነገር ግን ለፀነሱ በዚያ ወራት ለሚያሳድጉም ወዮላቸው ።
እስመ ይከውን ዓቢይ ምንዳቤ በዲበ ምድር ።
በምድር ጽኑ መከራ ይሆናልና ።
ወመቅሠፍት ዲበ ዝንቱ ሕዝብ ።
በዚህም ሕዝብ ላይም መቅሠፍት ።

፳፬ ወይወድቁ በኲናት ።
፳፬ በጦርም ይወድቃሉ ።
ወይጼወው ውስተ ኵሉ አሕዛብ ።
ወደ አሕዛብ ይማረካሉ ።
ወይከይድዋ አሕዛብ ለኢየሩሳሌም ።
አሕዛብ በኢየሩሳሌም ይሰፍሩባታል ።
እስከ ይበጽሕ ዕድሜሆሙ ለአሕዛብ ።
የአሕዛብ ዘመናቸው እስኪፈጸም ድረስ አለ በሐሳዊ መሲሕ ጊዜ ቢሉ ፫ ዓመት ከ፫ ወር ነው ።

በእንተ እለ ይቀድሙ ትእምርታት ዘዕለተ
ደይን ወደኅሪት ምጽአቱ ለኢየሱስ ።

፳፭ ወይከውን ተአምር ውስተ ፀሐይ ወወርኅ ኢሳ. ፲፫፡ ፲ ሕዝ. ፴፪፡፯ ኢዮ. ፪፡፲ማቴ. ፳፬ ፡ ፳፱ ፡ ማር. ፲፫ ፳፬ ።

፳፭ በፀሐይና በጨረቃ ምልክት ይሆናል ።
ወከዋክብትኒ ይወድቁ እምሰማይ ዲበ ምድር ።
ከዋክብትም ከሰማይ ወደምድር ይወድቃሉ ።
ወይትመነደቡ አሕዛብ ወየኃሥሩ እምድምፀ ባሕር ።
አሕዛብም ከውቅያኖስ ድምፅ የተነሣ ይጨነቃሉ ይሸበራሉ ።

፳፮ ወትወፅእ ነፍስ ዕጓለ እመሕያው እምፍርሃት ወእምትሕዝብት ዘይመጽእ ለዓለም ።

፳፮ የሚመጣውን መከራ ከመመልከትና ከፍርሃት የተነሣ የሰው ነፍሱ ከሥጋው ትለያለች ።
እስመ ይትከወስ ኃይለ ሰማያት ይእተ አሚረ ።
የዚያን ጊዜ የሰማዮች ኃይል ይናወጣልና ፤

፳፯ አሜሃ ይሬእይዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ ይመጽእ በደመና ሰማይ ምስለ ኃይል ብዙኅ ወስብሐት ።

፳፯ ያን ጊዜ የሰው ልጅ ከታላቅ ኃይልና ምስጋና ጋራ በሰማይ ደመና ሲመጣ ያዩታል ።

፳፰ ወአመ ኮነ ዝንቱ ኵሉ ስግዱ ወአንሥኡ ርእሰክሙ ። ሮሜ. ፰ ፡ ፳፫ ።

፳፰ ይህ ሁሉ ከሆነ በኋላም የመረታ ስግደት ስገዱ ራሳችሁን አንሡ አለ እንደ አባ በትረ ማርያም ። ቅዱሳን ከበቁ በኋላ የሚሠሩትን አያውቁትም እንደ እንዝርት ራስ ይዞራሉ ።
እስመ በጽሐ ዘያድኅነክሙ ።
የሚያድናችሁ ደርሷልና ።

ዘከመ ይደልዎ ለክርስቲያን ተደልዎት
ለምጽአተ ክርስቶስ ኰናኒ ።

፳፱ ወመሰለ ሎሙ ወይቤሎሙ እምከመ ርኢክምዋ ለበለስ ወለኵሉ ዕፀው ከመ ሠረጹ ተአምሩ ከመ አልጸቀ ማዕረር ።

፳፱ በለስን ዛፍም ሁሉ እንደ ለመለመ ያያችሁ እንደሆነ መከር እንደ ደረሰ ዕወቁ ።

፴ ከማሁ አንትሙኒ እምከመ ርኢክሙ ከመ ኮነ ዝንቱ ሕእምሩ ከመ በጽሐት መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፴ እናንተም ይህ ሁሉ እንደ ተደረገ ያያችሁ እንደሆነየእግዚአብሔርመንግሥት እንደቀረበችዕወቁ

፴፩ አማን እብለክሙ ከመ ኢተኃልፍ ዛቲ ትውልድ እስከ አመ ይከውን ዝንቱ ኵሉ ።

፴፩ ይህ ሁሉ እስኪደረግ ይህች ትውልድ አታልፍም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፴፪ ሰማይ ወምድር የኃልፍ ።
፴፪ ሰማይና ምድር ያልፋሉ ።
ወቃልየሰ ኢየኃልፍ ።
ቃሌ ግን አያልፍም ።

ዘከመ ይደልዎሙ ለክርስቲያን
ተደልዎ ለሞት ።

፴፫ ዑቁ ርእሰክሙ ኢታክብዱ ልበክሙ በስታይ ወበፈጊዕ ወበህልዮ መንበርት ።

፴፫ በመብል በመጠጥ ይኽነንም ዓለም በማሰብ ልቡናችሁን እንዳታጠኑ ዕወቁ ።

፴፬ ወትበጽሐክሙ ይእቲ ዕለት ከመ መሥገርት እንተ ትወርድ ዲበ ኵሎሙ እለ ይነብሩ ዲበ ምድር ።

፴፬ በምድር ባሉ በአዕዋፍ ወጥመድ ድንገት እንዲመጣባቸው ያች ቀን ድንገት ትደርስባችኋለች

፴፭ ትግሁ እንከ በኵሉ ጊዜ ።
፴፭ በጊዜው ሁሉ ተግታችሁ ጸልዩ ።

ከመ ትክሀሉ አምሥጦ በጸሎትክሙ እምነ ዝንቱ ኵሉ ዘይመጽእ ።
በምትጸልዩት ጸሎት ከዚህ ከሚመጣው መከራ ሁሉ መዳን ይቻላችሁ ዘንድ ።
ወትቁሙ ቅድሜሁ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
በወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ፊት መቆም ይቻላችሁ ዘንድ ።

፴፯ ወኮነ መዓልተ ይውዕል በምኵራብ ወሌሊተ ይወፅእ ወይበይት ውስተ ደብረ ዘይት ዘስሙ ኤሌዎን ።

፴፯ ቀን በምኵራብ ሲያስተምር ሌሊት ኤሌዎን በሚባል በደብረ ዘይት ሲጸልይ ያድር ነበር ።

፴፰ ወኵሉ ሕዝብ ይገይሡ ኀቤሁ ውስተ ምኵራብ ወያጽምዕዎ ቃሎ ።

፴፰ ሕዝቡ ሁሉ ትምህርቱን ይሰሙት ዘንድ እርሱ ወዳለበት ወደ ምኵራብ ማልደው ይሄዳሉ ።

በእንተ ምክር ዘረ ወጀቱ ፈታሕያን ላዕለ ኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፳፪ ።

፩ ወቀርበ በዓለ መጸለት ዘስሙ ፋሲካ ። ማቴ ፣ ፳፮ ፤ ፪. ማር ፲፬ ፤ ፩ ።

፩ ፋሲካ የሚባለው በዓለ ናዕትም ቀረበ ።

፪ ወየኃሥሡ ሎቱ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት ፀዘይቀትልዎ ።

፪ የካህናት አለቆችና ጸሐፊዎችም ይገድሉት ዘንድ ፈለጉ ።
ወኮኑ ይፈርህዎሙ ለሕዝብ ።
ነገር ግን ሕዝቡን ፈሩ ።

በእንተ ተሰናዕዎቱ ለይሁዳ ምስለ አይሁድ ።

፫ ወቦአ ሰይጣን ውስተ ልበ ይሁዳ አስቆሮታዊ ዘእምዓሠርቱ ወክልኤቱ ትልቍ ። ማቴ ፣ ፳፮ ፤ ፲፬ ማር ፣ ፲፬ ፤ ፲ ።

፫ ቍጥሩ ካሥራ ሁለቱ ሐዋርያት በሚሆን በይሁዳ ልብ ሰይጣን አደረበት ። ሐተታ ተለይቶን ያውቃል ሥራ አሠራው ሲል እንዲህ አለ ።

፬ ወሖረ ወተናገሮሙ ለሊቃነ ካህናት ወለ ጸሐፍት ከመ ያግብኦ ሎሙ ።

፬ ሄዶ ያሲዛቸው ዘንድ ከካህናት አለቆችና ከጸሐፊዎችም ጋራ ተነጋገረ ።

፭ ወተፈሥሑ ወተሰነዓው ምስሌሁ ወተና ገርዎ የሀብዎ ፴ ብሩረ ።

፭ ደስ ብሏቸው ሠላሳ ብር እንሰጥሃለን ብለው ተነጋገሩት ።
ወአስተኃለቀ ነገረ ።
ነገር ቆረጡ ።

፮ ወተፈሥሐ ውእቱኒ ወየኃሥሥ ሰሀተ ያግብኦ ሎሙ እንዘ አልቦ ሰብእ ።

፮ እሱም ደስ አለው ሰው ሳይኖር ያሲዛቸው ዘንድ ምቹ ቦታ ይሻ ነበረ ።

በእንተ ደኀሪት ድራር ወበእንተ አስተዳልዎት ።

፯ ወበጽሐት ዕለተ መጸለት ዘስሙ ፋሲካ አመ ይጠብሑ ፍሥሐ ።

፯ ፋሲካ ያርዱበት የነበረ በዓለ ናዕትም ደረሰ ።
፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለጴጥሮስ ወለዮሐንስ ሑሩ ወአስተዳልው ለነ ፍሥሐ ዘንበልዕ ።

፰ ጌታም ኢየሱስ ክርስቶስ ጴጥሮስና ዮሐንስን ሂዳችሁ የምንበላውን ፋሲካ አዘጋጁ አላቸው ።

፱ ወይቤልዎ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ ለከ ፍሥሐ ።

፱ በግዐ ፋሲካውን ወዴት ልናዘጋጅልህ ትወዳለህ አሉት ።

፲ ወይቤሎሙ በዊእክሙ ሀገረ ትረክቡ ብእሴ ዘይጸውር ፃሕበ ማይ ።

፲ ወደ ሀገር በገባችሁ ጊዜም የውኃ ማድጋ የተሸከመ ታገኛላችሁ ።
ወትልውዎ ኪያሁ ኀበ ቦአ ቤት ።
እርሱ ወደሚገባበት ቤት ተከተሉት ።

፲፩ ወበልዎ ለበዓለ ውእቱ ቤት ይቤለከ ሊቅ አይቴኑ ኀበ እበልዕ ፍሥሐ ምስለ አርዳእየ ።

፲፩ የዚያን ቤት ባለቤት ከደቀ መዛሙርቴ ጋራ ፋሲካውን የምንበላበት የት ነው አለህ መምህር በሉት ።

፲፪ ወውእቱ ያርእየክሙ ጽርሐ ዓቢየ ወንጹፈ ወስርግወ ።

፲፪ እርሱ የተነጠፈ ያጌጠ ታላቅ አዳራሽ ያሳያችኋል ።
ወበህየ አስተዳልው ለነ ፤
በዚያ አዘጋጁልን ።

፲፫ ወሖሮሙ ረከቡ በከመ ይቤሎሙ ።
፲፫ በሄዱም ጊዜ እንደ ነገራቸው አገኙት ።
፲፬ ወአስተዳለው ፍሥሐ ።
ፋሲካውን አዘጋጁ ።

በእንተ ሠሪዓ ቅዱስ ቊርባን ።

፲፬ ወሶበ ኮነ ጊዜሁ ለድራር ረፈቀ እግዚእ ኢየሱስ ወሀሠርቱኒ ወክልኤቱ ሐዋርያቲሁ ምስሌሁ። ማቴ፡ ፳፮፡፳ ማር ፤ ፲፬፡፲፯ ።
ጊዜውም በደረሰ ጊዜ ጌታ ከርሳቸው ጋራ ለመብላት ተቀመጠ ።

፲፭ ወይቤሎሙ ፈቲወ ፈተውክዎ ለዝንቱ ፋሲካ እብላዕ ምስሌክሙ ።

፲፭ ይህን ፋሲካ ከናንተ ጋራ እበላ ዘንድ መውደድን ወደድኩ አላቸው ።
ዘእንበለ ይብጽሐኒ ሕማምየ ።
ከመከራዬ አስቀድሞ ።
ወነሥአ ኅብስተ እዕኰተ ወፈተተ ወወሀቦሙ ወይቤሎሙ ።
ዳቦውን አንሥቶ አመሰገነ ቆርሶ ሰጣቸው ።

፲፮ እብለክሙ ባሕቱ ከመ ኢይበልዕ እንከ እምኔሁ እስከ ይትፈጸም በመንግሥተ እግዚአብሔር ።

፲፮ በእግዚአብሔር መንግሥት እስኪፈጸም ድረስ ከርሱ እንግዲህ አልበላም ብዬ እንግራችኋለሁ አላቸው ።

፲፯ ወተመጦ ጽዋዓ ወእዕኰተ ።
፲፯ ጽዋውንም ተቀብሎ አመሰገነ
ወይቤሎሙ ንሥኡ ዘንተ ወተካፈልዎ ኵልክሙ ።
ይህን ተቀብላችሁ ሁላችሁ ተካፈሉት ።

፲፰ እብለክሙ አንሰ ኢይሰቲ እንከ እምዝ ንቱ እጺረ ፍሬ ወይን እስከ አመ እሰትዮ በመንግሥተ እግዚአብሔር ።

፲፰ በእግዚአብሔር መንግሥት እስከጠጣው ድረስ ከዚህ ወይን ጭማቂ አልጠጣም ብዬ እነግራችኋለሁ ።

፲፱ ወእምዝ ነሥአ ኅብስተ ወእዕኰተ ፩፡ ቆሮ ፲፩፡፳፬ ።

፲፱ ኅብስቱን ይዞ አመሰገነ ።
ባረከ ወፈተተ ወወሀቦሙ ።
ቆርሶ ሰጣቸው ።
ወይቤሎሙ ዝንቱ ውእቱ ሥጋየ ዘይትወሀብ በእንቲአክሙ ለቤዛ ብዙኃን ።
ለብዙ ሰዎች ቤዛ ስለናንተ የሚሰጥ ሥጋዬ ይህ ነው ።
ወከመዝ ግበሩ ተዝካርየ በእንቲአየ ።
መታሰቢያዬን እንዲህ አድርጉ

፳ ወከማሁ ጽዋዓኒ እምድኅረ ተደሩ
፳ ጽዋውንም እንዲሁ ከበሉ በኋላ ሰጣቸው ።
ወይቤሎሙ ዝንቱ ጽዋዕ ዘሐዲስ ሥርዓት
ደምየ ውእቱ ዘይትክዓው በእንቲአክሙ ወበእንተ ብዙኃን ።
ይህ ጽዋ ሐዲስ ሥርዓት የሚሆን ስለናንተ ስለ ብዙ ሰዎችም የሚፈስው ደሜ ይህ ነው ።

በእንተ ትእምርት ለዘያገብኦ ።

፳፩ ወባሕቱ ናሁ እዴሁ ለዘያገብአኒ ምስሌየ ውስተ ማዕድ ። ማቴ፡፳፮፡፳፪ ማር፡፲፬፡፳ ዮሐ፡ ፲፫ ፤ ፲፰ ።

፳፩ ነገር ግን አሳልፎ የሚሰጠኝ እጅ ከኔ ጋራ በማዕድ ነው ።

፳፪ ወወልደ ዕጓለ እምሕያውስ የሐውር በከመ ተሠርዓ በእንቲአሁ ። መዝ፡ ፵፡፲ ።

፳፪ የሰው ልጅ ክርስቶስ ግን ስለ እርሱ እንደ ተጻፈ ይሄዳል ።
ወባሕቱ አሌ ሎቱ ለውእቱ ብእሲ እምውስተ እዴሁ ይትሜጠውዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
ነገር ግን አሳልፎ ለሚሰጠው ለዚያ ሰው ወዮለት ።

፳፫ ወይቤሉ እርዳኢሁ በበይናቲሆሙ መኑ እንጋ ውእቱ እምኔሆሙ ዘዘንተ ይገብር ።

፳፫ ከርሳቸው ይህን የሚሠራ ማንም እንደ ሆነ እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ ።

በእንተ ትሕትና ዘክርስቲያን ።

፳፬ ወእምዝ ተዋከሁ በበይናቲሆሙ እንዘይብሉ መኑ እንጋ የዓቢ እምኔሆሙ ።

፳፬ ከዚህ በኋላ ከርሳቸው ማናቸው እንዲበልጥ እርስ በርሳቸው ተከራከሩ ።

፳፭ ወይቤሎሙ ነገሥቶሙ ለአሕዛብ ይኴንንዎሙ ። ማቴ ፳፡ ፳፭ ማርቆስ ፲፡ ፵፪ ።

፳፭ አሕዛብን ነገሥታቱ ይገዟቸዋል ።
ወመኳንንቲሆሙ ረዳእያነ ይብልዎሙ ።
ገገሮቻቸውንም ረዳቶች ይሏቸዋል ።

፳፮ ወለክሙስ አኮ ከመዝ ።
፳፮ ለናንተ ግን እንዲህ አይደለም
አላ ዘየዓቢ እምኔክሙ ይኩንከሙ ከመ ዘይንእስ።
ከናንተ ታላቁ እንደ ታናሽ ይሁን ።
ወሊቅኒ ከመ ላእከ ።
አለቃውም እንደ ሎሌ ይሁን እንጂ ፤

፳፯ መኑ ውእቱ ዘየዓቢ ።
፳፯ ማን ይበልጣል ።
ዘይረፍቅኑ ።

ተቀምጦ የሚበላው ነውን ።
ወሚመ ዘይትለአክ ፤
ወይም የሚያገለግለው ።
አኮኑ ዘይረፍቅ ።
ተቀምጦ የሚበላው ጌታ ይበልጥ የለምን ።
ወአንሰ ናሁ ከመ ላእክ ማእከሌሆሙ ።
እነሆ እኔ ዘይረፍቅ እግዚእ ስሆን አገለግልኋችሁ ።

፳፰ ወአንትሙሰ ባሕቱ እለ በእንቲአየ ተዓገሥክሙ ምስሌየ በሕማምየ ።

፳፰ እናንተስ በመከራ ታግሣችሁ ስለኔ መከራዬን የተቀበላችሁ ናችሁ ።

፳፱ አነኒ አስተዳሉ ለክሙ መንግሥተ በከመ ወሀበኒ ሊተ አቡየ ።

፳፱ አባቴ ለእኔ እንዳዘጋጀ እኔም ለናንተ መንግሥት አዘጋጅላችኋለሁ ። እንድም በነቢይ አድሮ ስአል እምኔየ እሁበከ አሕዛበ ለርስትከ ብሎ እንደ ተናገረልኝ ። ልጅነትን አዘጋጅላችኋለሁ ።

፴ ከመ ትብልዑ ወትስትዩ በማዕድየ በመንግሥትየ ።

፴ በነገሥኩ ጊዜ በማዕዱ ተቀምጣችሁ ትበሉ ትጠጡ ዘንድ ።
ወትነብሩ ዲበ መናብርት ወትኰንኑ ፲ተ ወ፪ተ ሕዝበ እስራኤል ።
በዐሥራ ሁለት ዙፋን ተቀምጣችሁ ባሥራ ሁለቱ ነገደ እስራኤል ትፈርዳላችሁ ።

፴፩ ወይቤሎ እግዚእ ስምዖን ስምዖን ስምዖን ናሁ ሰኢሎ ሰአለ ሰይጣን የሐንጽጽክሙ ወየሐንፍጽክሙ ከመ ዕለስ ።

፴፩ ስምዖን ሆይ ሰይጣን እንዳጃ ሲጠረጥራችሁ ከኔ አንድነት ሊለያችሁ ፈጽሞ ተካሷል ። ሐተታ ደጊመ ቃል ለዕብራውያን ልማዳቸው ነው አብርሃም አብርሃም ማርታ ማርታ አልዓዛር አልዓዛር እንዳለ ስምዖን ስምዖን አለ ። አንድም ለአጽንዖተ ነገር ። አንድም የነፍስህ የሥጋህ ፈጣሪ ነኝ ሲል ።

፴፪ ወአንሰ ሰአልኩ በእንቲአክሙ ከመ ኢይድክም ሃይማኖትክሙ ።

፴፪ እኔ ግን ሃይማኖታችሁ ሕጹጽ እንዳይሆን ስለናንተ ፈጽሞ ተካሰስኩ ።
ወአንተኒ ተመይጠከ ጽንዖሙ ለአኃዊከ ።
አንተም ከፍርሃት ወደ ጥብዓት ተመልሰህ ወንድሞችህን አጽናቸው ።

፴፫ ወይቤሎ እግዚኦ እንሰኬ ጥቡዕ ለሐዊር ። ምስሌከ ውስተ ኢየሩሳሌም እመኒ ተሞቅሖ ወእመኒ ለመዊት ።

፴፫ አቤቱ ኦ እኔስ ለመታሰርም ቢሆን ለሞትም ቢሆን ካንተ ጋር ኢየሩሳሌም ለመሄድ ቆርጫለሁ ።

፴፬ ወይቤሎ ኦ ጴጥሮስ ዮም ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ሥልሰ ትክሕደኒ ከመ ዘኢተአምረኒ ። ማቴ. ፳፮፥፴፬ ማር. ፲፬፥፴ ።

፴፬ ጴጥሮስ ሆይ ዛሬ ዶሮ ሳይጮህ እንደማታውቀኝ አድርገህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ብዬ እነግርሃለሁ ።

፴፭ ወይቤሎሙ አመ ፈነውኩክሙ ዘእንበለ ቍናማት ወጽፍነት ወአሣዕን ቦኑ ዘተጸነስክሙ ። ማቴ ፲፱፥፴፭ ።

፴፭ ያለ ከረጢት ያለ ስንቅ ያለ ጫማም በላክኋችሁ ጊዜ በውኑ የተቸገራችሁት መቸገር አለን በውኑ ተቸገራችሁን አላቸው ።

፴፮ ወይቤልዎ አልቦ ፤
፴፮ አልተቸገርንም አሉት ፤
ወይቤሎሙ ይእዜሰኬ ዘቦ ቍናማት ይንሣእ ሎቱ።
ዛሬ ግን ከረጢት ያለው ይያዝ
ወዘሂ ጽፍነት ፣ ስንቅም ያለው ።
ሐተታ መግቦቱን እስኪያውቁ ድረስ አትያዙ ይላል መግቦቱን ካወቁ በኋላ ግን ቢይዙም ባይዙም አይጐዱምና ።
ወዘሰ አልቦ መጥባሕት ይሢጥ ልብሶ ወይሣየጥ ሎቱ መጥባሐተ ሰይፍ የሌለው ልብሱን ሽጦ በልብሱ ዋጋ ሰይፍ ይግዛ ።
አንድም ፈቃደ ነፍስን ያልያዘ ሰው ፈቃደ ሥጋውን ትቶ ፈቃደ ነፍሱን ይሥራ ።

፴፯ እብለክሙ ከመ ይብጽሐኒ ዘጽሑፍ ወይትፌጸም በላዕሌየ ዘይብል ምስለ ኃጥአን ተኈለቁ ።

፴፯ ከኃጥአን ጋር ተቈጠረ ተብሎ የተነገረው በኔ እንዲደርስ በውነት እነግራችኋለሁ ።
ወኵሉ ዘበእንቲአሃ ይትፌጸም ።
ስለኔ የተነገረው ይፈጸማል ።

፴፰ ወይቤልዎ ነዋ ሀለዉ ኀቤነ ክልኤቱ መጣብሕ ዝየ ።

፴፰ አቤቱ ከዚህ ከኛ ዘንድ እነሆ ሁለት ሰይፎች አሉ አሉት ።
ወይቤሎሙ የአክለነ እንከሰ ።
ሁለት ሰይፍስ ካለ ይበቃናል አላቸው ።
አንድም የአከለከሙ ያበቃችኋል አላቸው ።
አንድም ብሉይንና አዲስን ግንዘብ አድርገናል አሉት ብሉይ ሐዲስ ከያዛችሁስ ይበቃችኋል አላቸው ።

ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ በደብረ ዘይት ።

፴፱ ወወፂኦ ሖረ በከመ ያለምድ ይጸሊ ደብረ ዘይት ።

ማቴ፡ ፳፮፡፴፮ ማር፡ ፲፬፡፴፪ ዮሐ፡ ፲፰፡፩ ፡

፴፱ እንደ ለመደ ሊጸልይ ወጥቶ ደብረ ዘይት ሄደ ።
ወተለውዎ አርዳኢሁ ።
ደቀ መዛሙርቱም ተከተሉት ።

፵ ወበጺሖ ህየ ይቤሎሙ ጸልዩ ከመ ኢትባኡ ውስተ መንሱት

፵ ከዚያም በደረሱ ጊዜ ወደ መከራ እንዳትገቡ ጸልዩ አላቸው ።

፵፩ ወተአተተ እምኔሆሙ መጠነ ሙጋረ እብን ወሰገደ ወጸለየ ማቴ፡፳፮፡፴፱ ማር፡ ፲፬፡፴፭ ።

፵፩ የደንጊያ ውርወራ ያህል ማለት ደንጊያ ወርውሮ እስከሚደርስበት ድረስ ከርሳቸው እልፍ ብሎ ሰገደ ጸለየ ።

፵፪ እንዘ ይብል አባ ለእመ ትፈቅድ አግኅሥ እምኔየ ለዛንቱ ጽዋዕ ።

፵፪ አባቴ ሆይ ከወደድህስ ይህን ጽዋዕ ከኔ አርቀው እያለ ።
ወባሕቱ ፈቃድከ ይኩን ወአኮ ፈቃደ ዚአየ ።
ነገር ግን ፈቃድህ ይሁን እንጂ የኔ ፈቃድ አይደለም ።

፵፫ ወአስተርአዮ መልአከ እግዚአብሔር ዘይጌንዮ ።

፵፫ ለከ ኃይል ለከ ጽንዕ እያለ የሚያመሰግነው መልአክ ታየው ።
አንድም ዘያጸንዖ የሚያጸናው መልአከ እግዚአብሔር ከወደ ሰማይ ተነጋገረው ።
ወውእቱሰ ፈርሃ ።
እርሱ ግን ፈራ ። ሐተታ በሰው ልማድ ፈራ ፤ ሶበሰ ኢፈርሃ እምኢሰሰለ ፍርሃት እምኔነ ለካሣ ። እንዲል ወአውተረ ጸልዮ ።
መላልሶ ጸለየ ። ወጸርሐ ኀበ አቡሁ ከመ ትምጽእ ረድኤቱ እንዲል ።

፵፬ ወኮነ ሐፉ ከመ ነጸፍጸፈ ደም ዘይወርድ ዲበ ምድር ።

፵፬ ወዙ እንደ ደም ሆነ ማለት በዝቶ ወይቦ ምድሩን አራሰው

፵፭ ወተንሢኦ እምኀበ ይጼሊ ሖረ ኀበ አርዳኢሁ ።

፵፭ ከሚጸልይበት ተነሥቶ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ሄደ ።
ወረከቦሙ እንዘ ይነውሙ እምኃዘን ።
ከኃዘንም የተነሣ ተኝተው አገኛቸው ።

፵፮ ወይቤሎሙ ምንትኑ ያነውመክሙ ።
፵፮ ምን አስተኛችኋል ።
ተንሥኡ ወጸልዩ ከመ ኢትባኡ ውስተ መንሱት ።
ወደጥፋት እንዳትገቡ ተነሥታችሁ ጸልዩ አላቸው ።

በእንተ አግብኦት ዘይሁዳ
ወተእኅዞት ዘኢየሱስ ።

፵፯ ወእንዘ ዘንተ ይቤሎሙ በጽሑ ሕዝብ።
፵፯ ይህን ሲነግራቸው ሕዝቡ ደረሱ ።
ወይሁዳ ፩ እምዓሠርቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ እንዘ ይመርሆሙ ።
ካሥራሁለቱ ሐዋርያት አንዱ ይሁዳ እየመራቸው።
ወቀርበ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወሰዓሞ ።
ወደ ጌታ ቀርቦ ሳመው ።
ወዝውእቱ ትእምርት ዘወሀቦሙ ፤
የነገራቸውም ምልክት ይህ ነበርና ።
ወይቤሎሙ ዘሰዓምክዎ ውእቱ ኪያሁ አኀዙ ወሰድዎ አጽኒእክሙ ።
የምስመው እርሱ ነውና አጽንታችሁ ያዙት አላቸው ።

፵፰ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለይሁዳ በስኢምኑ ታገብኦ ለወልደ ዕጓለ ዕመሕያው ። ማቴ፡ ፳፮ ፵፯ ማር፡ ፲፬፡፵፫ ዮሐ፡ ፲፰፡፫ ።

፵፰ ጌታም ይሁዳ ሆይ የሰውን ልጅ በመሳም አሳልፈህ ትሰጠዋለህን ።
አኮኑ ከመ ታቀትሎ ።
ልታስገድለው አይደለምን አለው ።

፵፱ ወርእዮሙ እለ ምስሌሁ ዘኮነ ይቤልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እግዚኦ ትፈቅድኑ ንዝብጦሙ በመጥባሕት ።

፵፱ ከርሱም ጋራ ያሉት አይተው አቤቱ በሰይፍ ልንገድላቸው ትወዳለህን አሉት ።

፶ ወዘበጦ አሐዱ እምኔሆሙ ለገብረ ሊቀ ካህናት ።

፶ አንዱ የሊቀ ካህናቱን ባሪያ መታው ።
ወመተሮ እዝኖ ዘየማን ።
ቀኝ ጆሮውን ቆረጠው ።

፶፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፶፩ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ኅድግ ዘንተ ።
ይህንስ ተው አለው ።
ወገሠሦ እዝኖ ሶቤሃ ።

ያንጊዜውንም ጆሮውን ዳሶ አዳነው ።

፶፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ክርስቶስ ለእለ መጽኡ ኀቤሁ እምኀበ ያእኀዝዎ ሊቃነ ካህናት ወመ ኀብተ ምኵራብ ወረበናት ከመ ዘሰራቂኑ ተአኀዙኒ መጻእክሙ ምስለ መጣብሕ ወእብትር ፤

፶፪ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም የምኵራብ አዛዦችንና ሊቃነ ካህናትን ሽማግሌዎችን ሌባን እንደምትይዙ በሾተል በጐመድ መጣችሁብኝ አላ ቸው ።

፶፫ ወእንዘ ሀሎ አሚረ ህሎኩ ምስሌክሙ። ውስተ ምኵራብ እዴክሙ ጥቀ ኢሰፋሕክሙ ላዕሌየ።

፶፫ ዘወትር ከናንተ ጋራ ስኖር እጃችሁን ስንኳ አልዘረጋችሁብኝም ።
ወባሕቱ ዝንቱ ውእቱ ሰዓትክሙ ወሥልጣኑ ለመ ኰንነ ጽልመት ።
ነገር ግን ጊዜያችሁ ዛሬ ነው የጨለማ አበጋዝ የሚ ሆን የዲያብሎስም ጊዜው ዛሬ ነው ።

በእንተ ክህደታት ዘጴጥሮስ ።

፶፬ ወአኀዝዎ ወወሰድዎ ቤተ ሊቀ ካህናት ማቴ፣ ፳፮ ፶፬ ፣ ማር፣ ፲፬፣ ፶፫ ።

፶፬ ይዘው ከሊቀ ካህናቱ ቤት ወሰዱት ፤
ወተለዎ ጴጥሮስ እምርኁቅ ።
ጴጥሮስም በሩቅ ተከተለው ።

፶፭ ወአንደዱ እሳተ ማዕከለ ዓጸድ ወነበሩ ።
ማቴ፣ ፳፭፣፳፱ ማር፣ ፲፬፣፳፯ ዮሐ፣ ፲፰፣፳፭ ።

፶፭ ባደባባይ መካከል እሳት አንድደው ተቀ መጡ ።
ወጴጥሮስኒ ነበረ ምስሌሆሙ
ጴጥሮስም ከርሳቸው ጋራ ተቀመጠ ።

፶፮ ወርእየቶ ወለት እንዘ ይነብር መንገለ በርሀ ።

፶፮ የእሳቱ ጸዳል በወደቀበት በኩል ተቀምጦ ሳለ አንዲት ብላቴና አየችው ።
ወጠየቀቶ ።     አስተዋለች ።
ወትቤዝኒ ምስሌሁ ።
ይህም ከርሱ ጋራ ነበረ አለች ።

፶፯ ወክህደ ወይቤላ ኦ ብእሲቶ ኢየአምር ዘት ብሊ ።

፶፯ አንቺ ሴት የምትይውን አላውቀውም ብሎ ካደ ።

፶፰ ወእምድኅረ ኅቀ ርእዮ ካልዕ ።
፶፰ ጥቂት ቆይቶም ሌላው አየው ።
ወይቤሎ አንተኒ እምኔሆሙ አንተ ።
አንተም ከርሳቸው ወገን ነህ አለው ።
ወይቤሎ አንተ ብእሲ ኢኮንኩ አንሰ ።
አንተ ሰው አይደለሁም አለው ።

፶፱ ወኃሊፎ መጠነ አሐቲ ሰዓት አጥዎቀ አሐዱ ካልዕ እንዘ ይብል አማን ዝንቱ ሀሎ ምስሌሁ ዮሐ. ፲፰፣ ፳፯ ።

፶፱ አንድ ሰዓት ከቆየም በኋላም ሌላው ይህም ከርሱ ጋራ ነበር ።
ወገሊላዊ ብእሲሁ ።
የገሊላ ሰው ነው ብሎ አስጨነቀው ።

፷ ወይቤሎ ጴጥሮስ አንተ ብእሲ ኢየአምሮ ዘትብል ።

፷ አንተ ሰው የምትለውን አላውቀውም አለ ።
ወእንዘ ውእቱ ይትናገር ዘንተ ነቀወ ዶርሆ ሰቤሃ ።
ይህን ሲናገር ዶሮ ጮኸ ።

፷፩ ወተመይጠ እግዚእነ ኢየሱስ ወነጸሮ ለጴ ጥሮስ ። ማቴ. ፳፮ ፴፯ ማር፣፲፬፣ ፴ ዮሐ ፲፫ ፣ ፴፰ ።

፷፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ተመልሶ ጴጥሮስን አየው ።
ወተዘከረ ጴጥሮስ ቃሎ ለእግዚእነ ኢየሱስ ዘይ ቤሎ ሥልሰ ትክህደኒ ዮም ።
ጴጥሮስም ዛሬ ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛ ለህ ያለውን የጌታን ነገር አሰበ ።
ወወፂአ ጴጥሮስ አፍአ ወበከየ መሪረ ።
ጴጥሮስም ወደውጭ ወጥቶ መራራ ልቅሶ አለቀሰ ።

ዘከመ ተሣለቁ አይሁድ ላዕለ ኢየሱስ ።

፷፪ ወዐደውኒ እለ አኀዝዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ኮኑ ይሣለቁ ላዕሌሁ ።

፷፪ ጌታን የያዙት ሰዎችም ዘበቱበት ።
፷፫ ይዘብጥዎ ።
፷፫ መቱት ።
ወይገለብብዎ ወይጸፍዕዎ ።
ፊቱን ሸፍነው ጸፉት ።
ወይቤልዎ ተነበይ ለነ መኑ ውእቱ ዘጸፍአከ ወኰር ዓከ ።
የመታሕ ማነው ንገረን አሉት ።

፷፭ ወባዕድኒ ብዙኃ ዘይጸርፉ ላዕሌሁ ወይት ናገሩ በእንቲአሁ ።
፷፭ ሌላም የሚሰድቡት ብዙ አለ ።

በእንተ ቀዊሞተ ኢየሱስ ውስተ ዓውድ ።

፷፮ ወጸቢሖ ተጋብኡ ሊቃነ ካህናት ወጸሐ ፍት ወሊቃናተ ሕዝብ ወወሰድዎ ውስተ ዓውዶሙ

፷፮ ሲነጋ የካህናቱ አለቆችና ጸሐፊዎች የሕዝቡም አለቆች ተሰብስበው ወደደባባይ ወሰዱት ።

፷፯ ወይቤልዎ እመ አንተሁ ክርስቶስ ንግረነ ገሃደ ። ማቴ ፳፯ ፩ ማር ፲፭ ፩ ዮሐ ፲፰ ፳፰ ።

፷፯ ክርስቶስ አንተ እንደሆንክ ገልጸህ ንገረን አሉት ።

፷፯ ወይቤሎሙ እይዳዕኩክሙ ፡ ወኢ.ተአምኑኒ ።

፷፯ ብነግራችሁ አትቀበሉኝ ።

፷፰ ወእመኒ ተሰአልኩክሙ ኢትነግሩኒ ወኢታወሥኡኒ ።

፷፰ ብጠይቃችሁ ፡ አትመልሱልኝ ።
ወኢ.ሂ ፡ ኢ.ተኃድጉኒ ።
ወይ አትተውኝ አላቸው ።

፷፱ ወባሕቱ እብለክሙ እምይእዜሰ ትሬእይዎ እንዘ ይነብር ለወልደ ዕጓለ እመሕያው በየማነ እግዚአብሔር ።

፷፱ ነገር ግን ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ከዛሬ ጀምሮ በእግዚአብሔር በቀኝ ኃይል ሲቀመጥ ታዩታላችሁ ።

፸ ወይቤልዎ ኵሎሙ አንተኑ ውእቱ እንከ ወልደ እግዚአብሔር ።

፸ ሁሉም እንኪያ የእግዚአብሔር ልጅ አንተነህ አሉት ።

፸፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አንትሙ ትብሉ ከመ አነ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ።

፸፩ የእግዚአብሔር ልጅ እኔ እንደሆንኩ እናንተ ትናገራላችሁ ።

፸፪ ወይቤሉ ምንተ እንከ ንፈቅድ ሰማዕት በእንቲአሁ ።

፸፪ እንግዲህ ስለ እርሱ ምን ምስክር እንሻለን።
ናሁ ሰሊነ ሰማዕነ እምአፉሁ ።
እነሆ ካፉ ሰምተናል አሉ ።

## በእንተ ቀዊሞተ ፡ ኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ወሄሮድስ ።

## ምዕራፍ ፳፫ ።

፩ ወተንሥኡ ኵሎሙ በምልዖሙ ወወሰድዎ ኀበ ጲላጦስ ።

፩ ወገኖቻቸው ተነሥተው ወደ ጲላጦስ ወሰዱት ።

፪ ወአኀዙ ያስተዋድይዎ ወይቤሉ ረከብናሁ ለዝንቱ እንዘ የዓልዎሙ ለሕዝብነ ። ማቴ ፳፪ ፣ ፳፩ ማር ፲፫ ፣ ፪ ዮሐ ፣ ፲፰ ፣ ፴፫ ።

፪ ይኸን ሰው ወገኖቻችንን ሲያሳምጽ አገኘነው ብለው ያካስሱት ጀመር ።
ወይከልዖሙ ኢ.ያሀቡ ጸባሕተ ለቄሣር ።
ለቄሣር ግብር እንዳይሰጡ ይከለክላቸዋል ።
ወይሬሲ ርእሶ ክርስቶስሃ ንጉሠ እስራኤል ።
የእስራኤል ንጉሥ ክርስቶስም ነኝ ይላል ብለው አሳጡት ።

፫ ወሐተቶ ጲላጦስ። ማቴ፡፳፯ ፣ ፲፩ ማር ፣ ፲፭ ፣ ፪ ዮሐ ፣ ፲፰ ፣ ፴፫ ።

፫ ጲላጦስም መረመረው ።
ወተስእሎ ወይቤሎ አንተኑ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሣቸው አንተ ነህ ብሎ ጠየቀው ።
ወአውሥአ ወይቤሎ አንተ ትብል ከመ አነ ውእቱ ።
እኔ እንደሆንኩ አንተ ትናገራለህ ብሎ መለሰ ።

፬ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ለሊቃነ ካህናት ወለሕዝብ አልቦ ዘረከብኩ አበሳ ላዕለ ዝንቱ ብእሲ ።

፬ ጲላጦስም የካህናት አለቆችና ሕዝቡን በዚህ ሰው ያገኘሁበት በደል የለም አላቸው ።

፭ ወአውየው ወይቤሉ የሀውኮሙ ለሕዝብ ።
፭ ሕዝቡን ያውካቸዋል ያሳዝናቸዋል ብለው ጮኸው ተናገሩ ።
ወይሜህር በኵሉ ይሁዳ እኂዞ እምገሊላ እስከ ዝየ ።
ከገሊላ ጀምሮ እስከዚህ በይሁዳ ሁሉ ያስተምራል ።

፮ ወሰሚዖ ጲላጦስ ስመ ገሊላ ወተስእለ ገሊላውያን ለእመ ገሊላዊ ብእሲሁ ።

፮ ጲላጦስም እኂዞ እምገሊላ ያሉትን ሰምቶ የገሊላ ሰው መሆኑን ጠየቀ ።

፯ ወአእሚሮ ከመ እምኵናኔ ሄሮድስ ውእቱ ፈነዎ ኀበ ሄሮድስ ።

፯ ከሄሮድስ ግዛት ወገን እንደሆነ ዐውቆ ወደ ሄሮድስ ላከው ።

እስመ ሀሎ ውእቱ በኢየሩሳሌም በውእቱ መዋዕል ።
እርሱ በዚያ ወራት በኢየሩሳሌም ነበርና ።

፰ ወሶበ ርእዮ ሄሮድስ ለኢየሱስ ተፈሥሐ ፈድፋደ ።

፰ ሄሮድስም ጌታን ባየው ጊዜ ፈጽሞ ደስ አለው ።
እስመ ይፈቅድ ይርአዮ እምጕንዱይ ዕለት ።
ከብዙ ቀን ጀምሮ ሊያየው ይወድ ነበርና ።
እስመ ይሰምዕ ነገሮ ወይሴፎ ይርአይ እምኔሁ ተአምረ ዘይገብር ።

ነገሩን ስለ ሰማ የሚያደርገውን ተአምራት ሊያይ ይመኝ ነበርና ።

፱ ወሐተቶ በብዙኅ ነገር ።
፱ መላልሶ ጠየቀው ።
ወአልቦ ዘተሰጥዎ አሐተ ቃለ ።
አንዲት ቃል ስንኳ አልመለሰለትም ።

፲ ወኮኑ ይቀውሙ ሊቃነ ካህናት ወጸሐፍት።
፲ የካህናት አለቆችና ጸሐፊዎች ቁመው ነበር።
ወአስተዋደይዎ ብዙኃ ።
አሳጡት ማለት ወዶ ሊመልስልህ አሉት ።

፲፩ ወአስተአከዮ ሄሮድስ ።
፲፩ ሄሮድስም ክፉ ነውሳ አለ ።
ወተሳለቁ ላዕሌሁ ወዓልያኒሁ ።
ብላቴኖቹም ዘበቱበት ።
ወአልበስዎ ልብሰ ቀይሐ ።
የሚብለጨለጭ ልብስ አለበሱት ።
ወፈነዎ ኀበ ጲላጦስ ።
ወደ ጲላጦስም ላከው ።

፲፪ ወይእተ አሚረ ተኳነኑ ሄሮድስ ወጲላጦስ በበይናቲሆሙ ።

፲፪ ሄሮድስና ጲላጦስም ያን ጊዜ እርስ በርሳቸው ተፋቀሩ ።
እስመ ጋዕዝቦሙ እምቅድም ።
ከጥንት ጀምሮ ጸብ ነበራቸውና ሐተታ እኔ ልግዛ እኔ ልግዛ በማለት በዳኝነት ምክንያት ፤ አሁን በጌታ ሞት እርቅ እንደተጀመረ ለማጠየቅ ።

፲፫ ወጸውዖሙ ጲላጦስ ለሊቃነ ካህናት ወለመኳንንተ ሕዝብ ።

፲፫ ጲላጦስ የሕዝቡን ገዢዎችና የካህናቱን አለቆች ጠራቸው ።

፲፬ ወይቤሎሙ አምጻእክምዎ ኀቤየ ለዝ ብእሲ ከመ ዓላዌ ሕዝብ ። ዮሐ ፲፰ ፥ ፴፰

፲፬ ሕዝቡን እንደሚያሳምጽ አስመስላችሁ ይህን ሰው ወደኔ አመጣችሁት ።
ወናሁ ሐተትክዎ በቅድሜክሙ ።
እነሆ በፊታችሁ መረመርኩት ።
ወአልቦ ዘረከብኩ ጌጋየ ላዕለ ዝንቱ ብእሲ እምዘ አንትሙ አስተዋደይክምዎ ።
በምታጣሉት ነገር ሁሉ በዚህ ሰው ምክንያት አላገኘሁበትም ።

፲፭ ወኀበ ሄሮድስኒ ፈነውክዎ ።
፲፭ ወደ ሄሮድስም ላክሁት ።
ወውእቱ ፈነዎ ኀቤነ ።
እርሱም ወደኛ ላከው ።
ወናሁ አልቦ ዘገብረ በዘይመውት ።
እነሆ ይሙት በቃ ይፈረድበት ዘንድ በደል አላገኘሁበትም ።

፲፮ እቅሥፎኬ ወእኅድጎ ።
፲፮ ቀጥቸ ልተወው አለ ።

ዘከመ ኀረዩ በርባንሃ እምነ
ኢየሱስ ወዘከመ ኰነንዎ ።

፲፯ ወግብር በበዓል ያሕዩ ሎሙ አሐደ ሙቁሐ እምነ ሙቁሐን ።

፲፯ በየበዓሉ አንዳንድ ሰው ይፈታላቸው ዘንድ ልማድ ነበረ ።

፲፰ ወዓውየው ኵሉሙ ሕዝብ በምልዖሙ ።
፲፰ መላው ጮሁ ።
ወይቤሉ አእትቶ ወስቅሎ ለዝ ።
ይህን አርቀው ሰቀለው ።
ወአሕዩ ለነ በርባንሃ ።
በርባንንም ፍታልን አሉት ።

፲፱ ወውእቱሰ በርባን ዘገብረ ሀከከ በውስተ ሀገር ፤ ወበቀቲለ ነፍስ ተሞቅሐ ።

፲፱ ይህም በርባን በሀገር ሁከት ያደረገ ። በነፍስ መግደልም የታሰረ ነበር ።

፳ ወካዕበ ይቤሎሙ ጲላጦስ ትፈቅዱኑ አሕይዎ ለክሙ ለኢየሱስ ።

፳ ዳግመኛም ጲላጦስ ኢየሱስን ላድንላችሁ ትወዳላችሁን አላቸው ።

፳፩ ወአውየው ወይቤሉ ስቅሎ ስቅሎ ።
፳፩ ስቀለው ስቀለው ብለው ጮሁ ።

፳፪ ወይቤሎሙ ጲላጦስ በሣልስ ምንተ እኩየ ገብረ ። ማቴ ፥ ፳ ፥ ፯ - ፳፫ ማር ፲፭ ፥ ፲፬

፳፪ ጲላጦስም በሦስተኛው ምን ክፉ ሥራ ሠራ አላቸው ።
ናሁ አልቦ ዘረከብኩ በላዕሌሁ ጌጋየ በዘይመውት ።
እነሆ የሚሞትበት በደል አላኝሁበትም ።
እቅሥፎኬ እንከ ወአሕይዎ ።
እንግዲህስ ገርፌ ልተወው አለ ።

፳፫ ወአውየው በዐቢይ ቃል ወሰአሉ ወይቤሉ ይሰቅልዎ
፳፫ ስቀለው ብለው ጮኹው ለመኑት ።
፳፬ ወኃየለ ቃሎሙ ወቃለ ሊቃነ ካህናት ።
፳፬ የሊቃናትና የሕዝቡም አለቃ ጩኸታቸው በረታ ጸና ።

ወኰነኖ ጲላጦስ ከመ ይኩኖሙ ፈቃዶሙ ።
ጲላጦስም ልመናቸውን ይፈጽምላቸው ዘንድ ፈረደበት ።

፳፭ ወአሕየወ ሎሙ ዘሰአልዎ በቀቲለ ነፍስ ወበገቢረ ሁከከ ተሞቅሐ ።

፳፭ ነፍስ በመግደልና ሁከት በማድረግ የታሰረውን ይፈታላቸው ዘንድ የለመኑትን ፈታላቸው ። ወኢየሱስሃ መጠዎሙ ለፈቃዶሙ በከመ ኀሠሡ ። ኢየሱስን ግን ለፈቃዳቸው ሰጣቸው ።

በእንተ ፍኖት ዘኃዘን ።

፳፮ ወሶበ ወሰድዎ ይሰቅልዎ አኃዝዎ ለስምዖን እትወቶ እምሐቅል ። ማቴ ፳፯ ፣ ፴፪ ማር ፲ ፣ ፳ ፳፩ ።

፳፮ ሊሰቅሉት ይዘውት ሲሄዱ ስምዖን የሚባል ሰው ከበረሃ ሲገባ አገኙ ።

፳፮ወአጸርዎ መስቀሎ ወተለዎ ለእግዚእ ኢየሱስ
፳፮ ጌታንም ይከተለው ዘንድ መስቀሉን አሸከሙት ።
ወተለውዎ ብዙኃን ሕዝብ ።
ብዙ ሰዎችም ተከተሉት ።
ወአንስትኒ ይበክያሁ ወያስቆቅዋሁ ።
ሴቶችም ያለቅሱለት ያዝኑለት ነበር ።

፳፰ ወተመይጠ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎን እዋልደ ኢየሩሳሌም ኢትብክያኒ ኪያየሰ ።

፳፰ ጌታም ተመልሶ እናንተ የኢየሩሳሌም ልጆች ለኔስ አታልቅሱልኝ ።
እላ ብከያ ላዕለ ርእስክን ወላዕለ ውሉድክን ።
ለራሳችሁ ለልጆቻችሁ አልቅሱ እንጂ ።

፳፱ እስመ ይመጽእ መዋዕል አመ ይብሉ ብፁዓት መካናት እለ ኢወለዳ ።

፳፱ ያልወለዱ መካኖች የተመሰገኑ ናቸው ።
ወከርሥኒ እንተ ኢወለደት ።
ያልወለደችም ማኅፀን የተመሰገነች ናት ።
ወአጥባት እለ ኢሐፀና ።
ያላጠቡም ጡቶች የተመሰገኑ ናቸው የሚሉበት ጊዜ ይደርሳልና ።

፴ ወይእተ አሚረ ይብልዎሙ ለአድባር ደቁ ላዕሌነ ። ኢሳ. ፪ ፣ ፲፱ ሆሴ ፲፰ ራእ ፮ ፣ ፲፯ ።

፴ ያንጊዜ ተራሮች ወድቀው በተጫኑን ።
ወለአውግርኒ ድፈኑነ ።
ኮረብቶች ተከፍተው ባሰጠሙን ይላሉ ። ሐተታ የመከራውን ጽናት መናገር ነው ሰው መከራ ሲጸናበት ሰማዩ ተንዶ በተጫነኝ ምድር ተከፍቶ ባሰጠመኝ ይላል ።

፴፩ በዝ ዕፅ ርጡብ ከመዝ ዘገብሩ እፎኑመ እንጋ ይከውን በይቡስ ።

፴፩ በዚህ በርጥብ ዕንጨት እንዲህ ያደረጉ በደረቅማ እንዴት ይሆን ማለት ፤ መለኮት በተዋሐደኝ በኔ እንዲህ ያደረጉ እሩቅ ብእሲ ቢያገኙ እንደምን ባደረጉ ። አንድም በኔ እንዲህ ያደረጉ እርሳቸው ለመከራው እንደምን ይስማሙት ይሆን ።

፴፪ ወወሰዱ ካልዓነ ክልኤተ ፈያተ ገባርያነ እከይ ይሰቅሉ ።
፴፪ ከርሱም ጋራ ሊሰቅሏቸው ሌሎች ሁለት ወንበዴዎች ወሰዱ ።

በእንተ ተሰቅሎት ኢየሱስ ።

፴፫ ወበጺሖሙ ብሔረ ዘስሙ ቀራንዮ በሀየ ሰቀልዎ ። ማቴ ፡ ፳ ፣ ፳-፴፫ ማር ፣ ፲፭ ፣ ፳፪ ዮሐ ፣ ፲ ፣ ፲-፳ ።

፴፫ ቀራንዮ ከሚባል ቦታም በደረሱ ጊዜ በዚያ ሰቀሉት ።
ወእልክቶኒ ክልኤተ ፈያተ ገባርያነ እከይ አሐደ በየማኑ ወአሐደ በጸጋሙ ሰቀሉ ።
እነዚያንም ሁለቱን ወንበዴዎች አንዱን በግራው አንዱን በቀኙ ሰቀሉ ።

፴፬ ወይቤ እግዚእ ኢየሱስ አባ ኅድግ ወስረይ ሎሙ እስመ በዘኢየአምሩ ይገብሩ ።

፴፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አባት ሆይ ባላወቁት ይሠራሉና ይቅር በላቸው አለ ። ሐተታ ከዚያ ነቢይ ግፍዖሙ ጽብእሙ እለ ከዚህ ኅድግሎሙ እለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ከዚያ የማይመለሱ አሉና ግፍእሙ እያለ ይጸልይባቸዋል ። የሚመለሱ እሉና ከዚህ ስረይ ሎሙ አለ ። ከዚያ እሙንቱሰ ጠይቆሙ ወተዓወሩኒ ይላል ። ከዚህ በዘኢየአምሩ ይገብሩ እለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም እያወቁ ቸል ብለው የሰቀሉት አሉና፤ ነቢይ እሙንቱሰ ጠይቆሙ አለ ሳያውቁ የሰቀሉት አሉና ከዚህ በዘኢየአምሩ ይገብሩ አለ ።
ወተዓፀው ዲበ አልባሲሁ ወተካፈሉ ።
በልብሱ ዕፃ ተጣጥለው ተካፈሉ ።

፴፭ ወይቀውሙ ሕዝብ ወይሬእዩ ።
፴፭ ሕዝቡም ቆመው ያዩት ነበር ።
ወመላእክትኒ ይዘነጕግዎ ።
አለቆችም ያፌዙበት ነበር ።
ወይቤልዎ ዘባዕደ ያድኅን ርእሶ ያድኅን ።
ሌላውን የምታድን ራስህን አድን ።
እመሰ ክርስቶስ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ወኅሩዩ ለእግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር የመረጠው የእግዚአብሔር ልጅ ክርስ ቶስ ከሆንክ ፡፡
ለያድኅን ርእሶ ፡፡
ራሱን ያድን ፡፡

፴፮ ወይሣለቁ ላዕሌሁ ሐራ ወይቀርቡ ፡፡
፴፮ ጭፍሮቹም ቀርበው ይዘብቱበት ነበር ፡፡
ወአምጽኡ ሎቱ ብሒአ ይስተይ ፡፡
መጻጻም አመጡለት ይጠጣ ዘንድ ፡፡

፴፯ ወይቤልዎ እመ ንጉሦሙ ለአይሁድ አድ ኅን ርእሰከ ፡፡

፴፯ የአይሁድ ንጉሣቸው ከሆንክ ራስክን አድን አሉት ፡፡

፴፰ ወጸሐፉ መጽሐፈ ላዕሌሁ ፡፡
፴፰ ጽሕፈትም በላዩ ጽፈውበት ነበር ፡፡
ወጽሕፈቱ በሮማይስጥ ወበጽርእ ወበዕብራይስጥ ዘይብል ዝንቱ ውእቱ ንጉሦሙ ለአይሁድ ፡፡
ጽፈቱም በጽርእና በሮማይስጥ በዕብራይስጥ ቋንቋ የአይሁድ ንጉሣቸው ይህ ነው የሚል ነው ፡፡

፴፱ ወአሐዱ ፈያታዊ እም እለ ተሰቅሉ ምስ ሌሁ ፀረፈ ወይቤሎ እመሰ አንተ ክርስቶስ አድኅን ርእሰከ ወኪያነሂ ፡፡

፴፱ ከርሱ ጋራ ከተሰቀሉት አንዱ ዳክርስ አንተ ክርስቶስ ከሆንክ እኛንም ራስክንም አድን ብሎ ሰደበው ፡፡

፵ ወአውሥአ ካልኡ ወገሠጾ ፡፡
፵ ሁለተኛውም ተቆጣው ጥጦስ ነው ፡፡
ወይቤሎ ኢትፍርሆን ለእግዚአብሔር አምላክከ አንተ ወአነ እንዘ ውስተ ዝንቱ ኵነኔ ህለውነ ፡፡
እኔና አንተ በእንደዚህ ያለ ፍርድ ሳለን እግዚአብ ሔርን አምላክህን አትፈራምን ፡፡

፵፩ ወለነሰ ዘበርቱዕ ረከብነ ዘይደልወነ ፡፡
፵፩ እኛስ በሚገባ ተፈርዶብናል ፡፡
ወበከመ ምግባሪነ ተፈደይነ ፡፡
እንደ ሥራችን ተፈርዶብናል ፡፡
ወዝንቱሰ አልቦ እኩይ ዘገብረ ወኢምንተኒ ፡፡
እርሱ ግን የሠራው ክፉ ሥራ የለም አለው ፡፡

፵፪ ወይቤሎ ለእግዚእ ኢየሱስ ተዘከረኒ እግ ዚኦ አመ ትመጽእ በመንግሥትከ ፡፡

፵፪ ጌታንም አቤቱ በጌትነትህ በመጣህ ጊዜ በቸርነትህ አስበኝ አለው ፡፡

፵፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፡፡
፵፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰ ፡፡
ወይቤሎ አማን እብለከ እመን ፊድፋደ ከመ ዮም ትሄሉ ምስሌየ ውስተ ገነት ፡፡
ዛሬ ከኔ ጋራ በገነት እንድትኖር በውነት እነግርሃለሁ አለው ፡፡

በእንተ ገዐሩ ወሞቱ ለኢየሱስ ፡፡

፵፬ ወቀቲሮ ጊዜ ስሱ ሰዓት ሞተ ፀሐይ ፡፡
፵፬ ቀትር ሲሆን በስድስት ሰዓት ፀሐይ ከብ ርሃን ተሰየ ፡፡
ወጸልመ ኵሉ ዓለም እስከ ጊዜ ተሱዓት ሰዓት ፡፡
እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ ጨለማ ሆነ ፡፡

፵፭ ወጸልመ ፀሐይ ፡፡
፵፭ ፀሐይም ጨለመ ማብራቱን ተወ ፡፡ ታሪክ ከቤተልሔም ሲነሡ ሁለት ወንበዴዎች አይተዋ ቸው ከዱር ሲደርሱ ሊቀሟቸው ተከትለዋቸው ሄዱ ስድስት ቀን ሲፈልጓቸው ሰንብተው በሰባተኛው ቀን አገኙዋቸው ስንፈልጋችሁ ሰንብተን አጥተ ናችሁ ወዴት ሄዳችሁ ኑሯል ብለው ደብድበው ልብሳቸውን ገፈው ሄዱ ፡፡ ከሄዱም በኋላ ጥጦስ ይህች ሴት ከአዝማደ መንግሥት ወገን ናት መሰለኝ አሳ ዘነችኝ ይህም ሕፃን አሳዘነኝ እንመልስላቸው አለው፡፡ ዳክርስ ከሕፃንነትህ ጀምረህ ይህን ያስተማርከን አንተ ነህ ይህን ያህል ርኅራኄ ከማን አገኘኸው በዚያውስ ላይ በማን ፈንታ ታዛለህ አለው ከቤተ ልሔም እስከዚህ የቀማነው ላንተ ይሁን እኔ በፈን ታዬ እቆጠርበታለሁ ተውልኝ ብሎ መለሰላቸው ፡፡ ጥጦስ ጌታን ከመቤታችን ተቀብሎ አቀፈው ፡፡ ኦጥጦስ አንተ ትቀድሞ ለአዳም አቡከ በዊአ ውስተ ገነት አለው ፡፡ እንዲህ ቢለው ደስ ብሎት ይህ ብላቴና ከደቂቀ ነቢያት ወገን ይመስለኛል አለ ፡፡ ዳክርስ ከደቂቀ ነቢያት ወገን ቢሆን ነው አንተን ወንበዴውን ከአዳም አስቀድሞ ገነት ትገባለህ ያለህ ብሎ ዘበተበት ስሎሜም እመቤታችንም ቢሉ ሕፃኑን ተቀብለውት ሲሸኙቸው አነቀፈው ወደቀ ፡፡ ሰይፉ ብጥልጥል ብላ ወደቀች አዘነ ሰብስበህ አምጣ አለው እንደ ጥንቱ አድርጐ ሰጥቶታል ከሄዱ በኋላ ለመቤታችን በዕለተ ዓርብ ከኔ ጋራ የሚሰቀሉ እኒህ ናቸው ይህ ያባቴ ፈንታ ነው ያ የዲያብሎስ ፈንታ ነው ብሎ ነግሯቸዋል ፡፡
ወተሠጠ መንጦላዕተ ምኵራብ እማእከሉ እምላዕሉ እስከ ታሕቱ ፡፡
የቤተ መቅደስ መጋረጃ ከላይ እስከ ታች ተቀደደ ፡፡

፵፮ ወጸርሐ እግዚእ ኢየሱስ በዓቢይ ቃል ወይቤ አባ አመሐፅኑ ነፍስየ ውስተ እዴከ ፡፡ መዝ ፴፩ ፡፡

፵፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አባት ሆይ ነፍሴን በጅህ አደራ እሰጣለሁ ብሎ ጮሆ ተናገረ ፡፡

ወዘንተ ብሂሎ መጠወ ነፍሶ ።
ይህንም ተናግሮ ነፍሱን ሰጠ ።

፵፯ ወርእዮ መስፍነ ምእት ዘኮነ አዕኰቶ ለእግዚአብሔር ።

፵፯ የመቶው አለቃም የሆነውን አይቶ እግዚአብሔርን አመሰገነው ።
ወይቤ አማን ጻድቅ ውእቱ ዝንቱ ብእሲ ።
ይህ ሰው በውነት ጻድቅ ኑሯል አለ ።

፵፰ ወኵሎሙ ሕዝብ እለ ኮኑ ጉቡአነ ሶበ ርእዩ ዘኮነ ጐድኡ እንግደዓቲሆሙ ወተሠውጡ ወአተው ቤቶ እንዘ ያነከሩ ።

፵፰ ሕዝቡም ሁሉ የተደረገውን ባዩ ጊዜ ደረታቸውን እየመቱ ተመልሰው ገቡ ። ሐተታ መካነ አኰምሮ ነውና ።

፵፱ ወይቀውሙ ኵሎሙ እለ የአምርዎ እምርኁቅ ።

፵፱ የሚያውቁት ሁሉ ርቀው ቆሙ ወአንስትኒ እለ ተለዋሁ እምገሊላ ርእያ ዘንተ ።
ከገሊላ ጀምሮ የተከተሉት ሴቶችም ይህን ያዩ ነበር ።

## በእንተ ተቀብሮቱ ለኢየሱስ

፶ ወመጽአ ብእሲ ዘስሙ ዮሴፍ ።
፶ ዮሴፍ የሚባል ሰው መጣ።
ብእሲ ባዕል ወሥዩም ዘቦቱ ምክር ሠናይ ኄር ።
ማቴ ፣ ፳፯ ፣ ፶፯ ማር ፣ ፲፭ ፣ ፵፫
ቸር ሰው ባለጠጋ ።
ወጻድቅ ፤ ደግ
ወጠቢብ ፤ ዐዋቂ ።

፶፩ ወውእቱ ኢህሎ ውስተ ምክሮሙ ወምግባሮሙ ለአይሁድ ። ዮሐ ፲፱ ፣ ፴፰ ።

፶፩ እርሱም በአይሁድ ምክርና ሥራ አልተባበረም ነበር ጠቢብ ላለው ።
ወህገሩ አርማትያስ ዘእምህገረ ይሁዳ ።
ሀገሩም የዮሁዳ ክፍል የምትሆን አርማትያስ ነበረች ።
ወኮነ ይሴፈዋ ውእቱ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ።
እርሱም መንግሥተ ሰማይን ተስፋ ያደርግ ነበረ ጻድቅ ላለው ።

፶፪ ወሖረ ኀበ ጲላጦስ ወሰአለ ሥጋሁ ለኢየሱስ ።
፶፪ ወደ ጲላጦስም ሄደ የጌታን ሥጋ ላውርድ ብሎ ለመነ ኄር ላለው ።

፶፫ ወአውረደ ሥጋሁ ወገነዞ በሰንዱናት ።
፶፫ ሥጋውን አውርዶ በድርብ በፍታ ከፈነው ባዕል ላለው ።

ወቀበሮ ውስተ መቃብር ሐዲስ ዘወቅርዎ አውቀረ ዘአልቦ ተቀብረ ውስቴቱ ።
እሱ ባሳነጸው ሰው ባልተቀበረበት በታነጸ መቃብርም ቀበረው ።
ወአንከርከረ እብነ ዓቢየ ወአንበረ ውስተ አፈ መቃብር ወኃለፈ ።
ታላቅ ደንጊያ አንላብጦ መቃብሩን ገጥሞት ሄደ ።

፶፬ ወዓርብ ውእቱ ዕለት አሚሁ ለጸቢሐ ሰንበት ።

፶፬ ያም ቀን የሰንበት አጥቢያ ዓርብ ነበር ።
፶፭ ወተለዋሁ ፪ቲ አንስት እለ መጽአ እምገሊላ ።

፶፭ ከገሊላ የመጡ ሁለት ሴቶችም ተከትለውታል ።
ወርእያ መቃብሮ ወዘከመ ተወድየ ሥጋሁ ።
መቃብሩንም አዩ ሥጋው እንዴትም እንደ ተጨመረ ።
ወእምድኅረ ቀበርዎ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ሥጋውንም ከቀበሩት በኋላ ፤

፶፮ ወአተዋ ወአስተዳለዋ አፈዋተ ።
፶፮ ተመልሰውም ሽቱ አዘጋጁ ።
ወኃደጋ በሰንበት ወኢሖራ ።
በሰንበት ግን አልሄዱም ።
እስመ ከማሁ ሕጎሙ ።
ሕጋቸው እንዲህ ነበርና ።

## በእንተ ተንሥኦቱ ለኢየሱስ

### ምዕራፍ ፳፬

፩ ወበእሑድ ሰንበት በጽባሕ አሌለያ ገይሠ ወሖራ ኀበ መቃብር ወወሰዳ ውእተ አፈዋተ ዘአስተዳለዋ ። ማቴ ፣ ፳፰ ፣ ፩ ማር ፣ ፲፮ ፣ ፩፡ዮሐ ፣ ፳ ፣ ፩ ።

፩ በመጀመሪያው ሰንበት ማለዳ ያዘጋጁትን ሽቱ ይዘው እጅግ ማልደው ወደ መቃብር ሄዱ።
ወካልዓትኒ አንስት ምስሌሆን ።
ሌሎችንም ሴቶች ከርሳቸው ጋራ ሄዱ ።

፪ ወረከባሃ ለይእቲ እብን ኀበ አንከርከረት እምነ መቃብር ።

፪ ያችንም ደንጊያ ከመቃብሩ ተንሥታ አገኙዋት ።

፫ ወቦአ ወኢረከባ ሥጋሁ ለእግዚእነ ኢየሱስ ።
፫ ገብተውም የጌታችንን የኢየሱስን ሥጋ አላገኙም ።

፬ ወእንዘ ያንከራ ወየኃጥአ በእንተ ዝንቱ ፡፡
፬ ስለዚህም ነገር የሚሉትን አጥተው ሲያ
ደንቁ ፡፡
አስተርአይዎን ፪ቱ እደው ወቆሙ ኀቤሆን ፡፡
ሁለት ሰዎች ባጠገባቸው ቁመው ታዩዋቸው ፡፡
ወይበርቅ አልባሲሆሙ ፡፡
የሚያንጸባርቅ ልብስ ለብሰው ነበር ፡፡ ወርኃ ትፍ
ሥሕት ነው ሲሉ ፡፡

፭ ወፈርሃ ወአትሐታ አዕይንቲሆን ውስተ
ምድር ፡፡

፭ ፈርተውም ዓይናቸውን ወደ ምድር ዝቅ
አድርገው አዩ ፡፡
ወይቤልዎን ምንተ ተኃሥሣሁ ለሕያው ምስለ ምው
ታን ፡፡
ሕያውን ከሙታን ጋራ ለምን ትሹታላችሁ ፡፡

፮ ተንሥአ ኢሀሎ ዝየሰ ፡፡ ማቴ ፳፰ ፤ ፳፩
ማር ፲፮ ፤ ፴፩ ሉቃ ፱ ፤ ፳፪

፮ ከዚህ ግን የለም ተነሥቷል ፡፡

፯ ተዘከራ ቃሎ ዘይቤለክን በገሊላ ሀለም
ለወልደ ዕጓለእመሕያው ይግባእ ውስተ እደ ሰብእ
ኃጥአን ፡፡

፯ በገሊላ ሳለ ለሰው ልጅ ክርስቶስ በኃጥአን
እጅ ይሰጥ ዘንድ አለው ፡፡
ወይሰቅልዎ ፤ ይሰቅሉታል ፡፡
ወይቀትልዎ ፤ ይገድሉታል ፡፡
ወይትነሣእ በሣልስት ዕለት ፡፡
በሦስተኛው ቀን ይነሣል ያላችሁን አስቡ አሏቸው ፡፡

፰ ወተዘከራ ቃሎ ፡፡
፰ ነገሩንም አሰቡ ፡፡
፱ ወአቲዎን እምኀበ መቃብር ነገራሆሙ
ዘንተ ለ፲፩ቱ ወ፩ዱ አርዳኢሁ ፡፡

፱ ከመቃብሩም ተመልሰው ለዐሥራ አንዱ
ነገሩዋቸው ፡፡
ወለቢጸሙኒ ኵሎሙ እለ ተርፉ ፡፡
ለቀሩት ባልንጀሮቻቸውም ሁሉ ፡፡

፲ ወእማንቱሰ ማርያም መግደላዊት ወዮ
ሐና ፡፡

፲ እርሳቸውም የመግደላዊቱ ማርያምና
ዮሐና ናቸው ፡፡
ወማርያም እንተ ያዕቆብ ፡፡
የያዕቆብ እናት ማርያምም ናት ፡፡
ወቢጽንሂ ምስሌሆን ነገራሆሙ ዘንተ ለሐዋርያት ፡፡
ከርሳቸውም ጋራ ያሉ ባልንጀሮቻቸው ይህን ለሐ
ዋርያት ነገሩዋቸው ፡፡

፲፩ ወኮነ ዝንቱ ነገር ዘሰምዑ በቅድሜሆሙ
ከመ ዝኒጋዔ ፡፡

፲፩ የዝንጋታ መስሏቸው ማለት አእምሮ የማ
ጣት መስሏቸው ፡፡

፲፪ ወኢአምንዎን ፤
፲፪ አልተቀበሏቸውም ፡፡
ወአክሐድዎን ፤
አሉ አሏቸው ሐሰት አሏቸው ፡፡
ወተንሥአ ጴጥሮስ ወሮጸ ወሖረ ኀበ መቃብር ፡፡
ጴጥሮስም ተነሥቶ ወደመቃብር ሮጦ ሄደ ፡፡
ወሐወጸ ፤ ዘልቆ ተመለከተ ፡፡
ወርእየ መዋጥሐ ባሕቲቶ ንቡረ ፡፡
በፍታውንም ብቻውን ተቀምጦ አየ ፡፡
ወአተወ እንዘ ያንክር ዘኮነ ፤
የተደረገውን እያደነቀ ተመለሰ ፡፡

በእንተ አርድዕት ዘኤማሑስ ፡፡

፲፫ ወይእተ ዕለተ እንዘ የሐውሩ ፪ቱ እምው
ስቴቶሙ ሀገረ እንተ ርኅቅት እምኢየሩሳሌም መጠነ
፷ ምዕራፍ እንተ ስማ ኤማሑስ ፡፡ ማር ፲፮ ፤ ፲፪፡፡

፲፫ በዚያን ቀን ከርሳቸው ሁለቱ ከኢየሩ
ሳሌም ስሳ ምዕራፍ ያህል የሚርቅ ኤማሑስ ወደ
ምትባል አገር ሲሄዱ ፤ ሐተታ ፪ቱ ያላቸው ሉቃ
ስና ቀለዮጳ ናቸው ፡፡ ሉቃስንስ ዘውእቱ ቀለዮጳ ይሉ
ዋል ብሎ ሉቃስና ኒቆዲሞስ ናቸው ፡፡
፲፬ ወይትናገሩ በበይናቲሆሙ በእንተ ኵሉ
ዘኮነ ፡፡

፲፬ ስለተደረገውም ነገር ሁሉ ሲጫወቱ ፡፡
፲፭ ወእንዘ እሙንቱ ይትናገሩ ወይትኀሠሥዎ፥
ለዝንቱ ፡፡
፲፭ ይህን ሲነጋገሩ ሲመራመሩ ፡፡
ቀርቦሙ እግዚእ ኢየሱስ ወሖረ ምስሌሆሙ ፡፡
ጌታችን ኢየሱስም ቀርቦ ከርሳቸው ጋራ ሄደ ፡፡

፲፮ ወተእኀዘ አዕይንቲሆሙ ከመ ኢያእምርዎ፡፡
፲፮ እንዳያውቁት ዓይናቸው ከዕውቀት ተገታ፡፡

፲፯ ወይቤሎሙ እግዚእነ ምንትኑ ዝንቱ ነገር
ዘትትናገሩ በበይናቲክሙ እንዘ ተሐውሩ ትኩዛ
ኒክሙ ፡፡

፲፯ እያዘናችሁ ስትሄዱ እርስ በርሳችሁ የም
ትነጋገሩት ይህ ነገር ምንድነው አላቸው ፡፡

፲፰ ወአውሥአ ፩ዱ እምኔሆሙ ዘስሙ ቀለ
ዮጳ ፡፡

፲፰ ከርሳቸው አንዱ ቀለዮጳ የሚባለው መለሰ፡፡
ወይቤሎ አንተኑ ባሕቲትከ ነግድ ዘኢሀለውከ
በኢየሩሳሌም ፡፡
አንተ ብቻህን በኢየሩሳሌም አልነበርህምን ፧

ወኢያእመርከኑ ዘኮነ በውስቴታ በዝንቱ መዋዕል ።
በዚህ ወራት በርሷ የተደረገውን አላወቅህምን አለው

፲፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ምንትኑ ውእቱ
፲፱ ጌታም ምንድነው አለው ።
ወይቤልዎ በእንተ ኢየሱስ ናዝራዊ ።
የናዝሬቱን የኢየሱስን ነገር ይነግሩት ጀመር ።
ብእሲ ጻድቅ ፤ ደግ ሰው ።
ወነቢይ ፤ ዐዋቂ የሆነ ።
ዘኮነ ከሃሌ በቃሉ ወበምግባሩ በቅድመ እግዚአ ብሔር ወበቅድመ ሰብእ ።
በተናገረው ነገር በሚሠራው ሥራ በእግዚአብሔር ዘንድ በሰውም ዘንድ ማድረግ የሚቻለው ።

፳ ወዘከመ አግብእዎ ሊቃነ ካህናት ወመኳንንቲነ ።

፳ የካህናት አለቆችና አለቆቻችን አሳልፈው እንደሰጡት ።
ወኰነንዎ ለሞት ።
ለሞት ፍርድ አሳልፈው ሰጡት ።
ወሰቀልዎ ፤ ሰቀሉት ።

፳፩ ወንሕነሰ ነአምን ቦቱ ከመ ውእቱ ሀለዎ ያድኅኖሙ ለእስራኤል ።

፳፩ እኛ ግን እርሱ እስራኤልን ያድናቸው ዘንድ እንዳለው እናምናለን ።
ወምስለ ዝንቱ ኵሉ ሠሉስ ዮም እምዘኮነ ዝንቱ ።
ከዚህም ሁሉ ጋራ ይህ ከተደረገ ዛሬ ሦስተኛ ቀን ነው ።

፳፪ ወባ አንስትኒ እለ እምኔነ ወነገራነ እለ ጌሣ ኀበ መቃብር ወኢረከባ ሥጋሁ ።

፳፪ ወደ መቃብር ገሥግሠው ሂደው ሥጋውን ባያገኙ አድንቀው የነገሩን ሴቶች አሉ ።

፳፫ ወተሠውጣ ወነገራነ ከመ ርእያ ርእየተ መላእክት እለ ይቤልዎን በእንቲአሁ ከመ ሐይወ ።

፳፫ ተመልሰውም እንደ ዳነ የነገሩዋቸውን የመላእክትን መልክ እንዳዩ ነገሩን ።

፳፬ ወቦ እምኔነሂ እለ ሖሩ ኀበ መቃብር ወረከባ ከማሁ በከመ ይቤላ አንስት ።

፳፬ ከኛም ወገን ወደ መቃብር የሄዱ ሴቶች እንዳሉት ሆኖ ያገኙት አሉ ።
ወሎቱሰ ኢረከብዎ ።
እርሱን ግን አላገኙትም ።

፳፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ዓብዳን ወጉንዱያነ ልብ ለኢአሚን በኵሉ ዘይቤሉ ነቢያት ።

፳፭ ነቢያት በተናገሩት ነገር ሁሉ ልቡናችሁ ከማመን የዘገየ እናንት ያላስተዋላችሁ ።

፳፮ አኮኑ ከመዝ ጽሑፍ ከመ ሀለዎ ለክርስቶስ ከመ ይትቀተል ወይባእ ውስተ ስብሐቲሁ ።

፳፮ ክርስቶስ መከራ ይቀበል ዘንድ ወደክብሩም ይገባ ዘንድ ይገባው የለምን ።

፳፯ ወአኀዘ ይፈክር ሎሙ እምነ ሙሴ ወዘነቢያት ።

፳፯ ከኦሪት ከመጻሕፍተ ነቢያት እየጠቀሰ ።
ወእምኵሉ መጻሕፍት ዘበእንቲአሁ ።
ስለ እርሱ የተጻፉ ስለ ርሱ የሚናገሩ መጻሕፍትን እየጠቀሰ እየተረጐመ ይነግራቸው ጀመር ።

፳፰ ወቀርቡ ሀገረ ኀበ የሐውሩ ባቲ ።
፳፰ ወደሚሄዱበት አገር ወደኤማሁስ ቀረቡ ።
ወአኀዘ ይትረኃቆሙ ።
ይርቃቸው ጀመር ።

፳፱ ወአገበርዎ ወይቤልዎ ንበር ምስሌነ ።

፳፱ ግድ ከኛ ጋራ እደር ብለው ማለዱት ።
እስመ መስየ ወተቆልቆለ ፀሐይ ።
መሽቶ ፀሐይ ገብቷልና ።
ወቦአ ከመ ይኅድር ምስሌሆሙ ።
ከርሳቸውም ጋራ ሊያድር ገባ ።

፴ ወእምዝ እንዘ ይረፍቅ ምስሌሆሙ ነሥአ ኅብስተ ባረከ ወፈተተ ወወሀቦሙ ።

፴ ከርሳቸው ጋራም ተቀምጦ ሲበላ ዳቦውን ይዞ ጸሎተ ማዕድ ጸልዮ ቆርሶ ሰጣቸው ።

፴፩ ወተከሥታ አዕይንቲሆሙ ።
፴፩ አእምሮዋቸው ተገለጠላቸው ።
ወአእመርዎ ፤ ዓወቁት ።
ወጠፍአ ፤ ነገሩን አጡት ።
ወእምዝ ተሰወረ እምኔሆሙ ፤ ተሰወረባቸው ።
ወኃጥእዎ ፤ እንዳላወቁት ሆኑ ።

፴፪ ወይቤሉ በበይናቲሆሙ አኮኑ ይነድደነ ልብነ ።

፴፪ እርስ በርሳቸው እንዲህ አሉ ልቡናችን ያዝን ይጸጸት የለምን ።
ወይርኅቀነ እንዘ ይነግረነ በፍኖት ።
በመንገድ እየነገረን ሲርቀን ።
ወይፌክር ለነ መጻሕፍተ ።
መጻሕፍትን ሲተረጕምልን አናውቅ ብለን ።

፴፫ ወተንሥኡ ሶቤሃ ይእተ ሰዓተ ወተሠውጡ ኢየሩሳሌም ።

፴፫ በዚያን ሰዓት ፈጥነው ወደኢየሩሳሌም ተመለሱ ።
ወረከብዎሙ ለ፲ ወ፩ዱ አርዳኢሁ ጉቡአኒሆሙ ።

ዐሥራ አንዱን ሐዋርያት ተሰብስበው አገኙዋቸው ።
ወለእለሂ ምስሌሆሙ ።
ከርሳቸው ጋራ ያሉትን ።

፴፬ ወይቤልዎሙ አማን ተንሥአ እግዚእነ ወአስተርአዮ ለስምዖን ።

፴፬ ጌታችን በውነት ተነሥቶ ለስምዖን ታየው።
፴፭ ወነገርዎሙ እሙንቱሂ ዘበፍኖት ።
፴፭ እርሳቸውም በመንገድ የሆነውን ነገሯቸው ።
ወዘከመሂ አእመርዎ ለእግዚእነ እንዘ ይፌትት ኅብስተ ።
ጌታንም ዳቦውን ሲቆርስ እንዳወቁት ።

፴፮ ወእንዘ ዘንተ ይትናገሩ ቆመ እግዚእ ኢየሱስ ማእከሎሙ ።
ወይቤሎሙ ሰላም ለከሙ ። ማር ፲፮ ፡ ፲፬ ዮሐ ፳፡ ፲፱

፴፮ ይኸንም ሲናገሩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዝግ ቤት ገብቶ በመካከላቸው ቆሞ እንደምን ሰነበታችሁ አስታረቅኋችሁ ።
ወኢትፍርሁ አነ ውእቱ ።
እኔ ነኝ አትፍሩ አላቸው ።

፴፯ ወደንገፁ ወፈርሁ ወመሰሎሙ ከመ ዘመንፈስ ይሬእዩ ።

፴፯ እርሳቸው ግን ምትሐት ያዩ መሰላቸው። ምትሐት እንዳዩ አድርገው ፈሩ ደነገጡ ።

፴፰ ወይቤሎሙ ምንት ያደነግፀከሙ ።
፴፰ ጌታም አላቸው ለምን ትደነግጣላችሁ ።
ወለምንት የዐርግ ሕሊና እኩይ ውስተ ልብክሙ ።
በልባችሁስ ክፉ አሳብ ለምን ይወጣል ይወርዳል ።

፴፱ ርእዩ እደውየ ወእገርየ ከመ አነ ውእቱ ወእእምሩኒ ።

፴፱ እጄን እግሬን እይታችሁ እኔ እንደሆንኩ ዕወቁ ።
እስመ ለመንፈስስ ሥጋ ወዓፅም አልቦቱ በከመ ትሬእዩኒ ብየ ።

በኔ እንደምታዩት ለምትሐት ሥጋ ዓፅም የለውምና፤ ሐተታ በነፍስ መደብ ሆኖ ብየ አለ ለኔ ግን ሥጋ ዓፅም አለኝ ማለቱ ነው ።

፵ ወዘንተ ብሂሎ አርአዮሙ እደዊሁ ወእገሪሁ ።

፵ ይኸን ተናግሮ በችንካር የተወጋውን እጁን እግሩን አሳያቸው ።

፵፩ ወእንዘ ዓዲ ኢአምኑ እምድንጋጼ ።
፵፩ ከድንጋጼ የተነሣ ገና ሳያምኑ ፤
ወእንዘ ያንከሩ በትፍሥሕት ።
ደስ ብሏቸውም ሲያደንቁ ።
ይቤሎሙ ደቂቅየ ቦኑ ብከሙ ዝየ ዘንበልዕ ።
ልጆቼ የምንበላው አላችሁ አላቸው ።

፵፪ ወወሀብዎ መክፈልተ ዓሣ ጥቡስ ።
፵፪ የተጠበሰ ዓሣ ፤
ወጸቃውዓ መዓር ።
ሰፈፍ የሌለው ወለላ ማር ሰጡት ።

፵፫ ወበልዓ በቅድሜሆሙ ።
፵፫ በፊታቸው በላ ። ሐተታ ለልማዱ ሲመገብ ስድስቱ ይቆማሉ ስድስቱ ይቀመጣሉ በዚህ ቀን ግን ዐሥራ አንዱ እንደ ቆሙ ተመገበዋል ። ትንሣኤውን እንዲረዱት ምትሐት እንዳይደለ ለማጠየቅ ።
ወነሥአ ዘተርፈ ወወሀቦሙ ።
የተረፈውን አንሥቶ ሰጣቸው ።

፵፬ ወይቤሎሙ አኮኑ ዝንቱ ነገርየ ዘእቤለከሙ እንዘ ሀሎኩ ምስሌክሙ ።

፵፬ ከናንተ ጋራ ሳለሁ የነገርኋችሁ ነገሬ ይህ አይደለምን ።
ከመ ሀለዎ ይብጻሕ ኦሪተ ሙሴ ወነቢያት ወመዝሙር በእንቲአየ ።
ኦሪት ነቢያት ዳዊት ስለኔ የተናገሩት ነገር ይደርስ ዘንድ እንዳለው ።

፵፭ ወእምዝ ከሠተ ልቦሙ ከመ ይለብዉ መጻሕፍተ ።

፵፭ ከዚህ በኋላ መጻሕፍትን ያውቁ ዘንድ አእምሯቸውን ገለጠላቸው ።
ወለበዉ ፤　　ዓወቁ ።
ወዖበ ተንሥአ እምነ ምውታን ከሠተ ሎሙ መጻሕፍተ ወለበዉ ወኮኑ ከመ ሰብል እንዲል ።

፵፮ ወይቤሎሙ ከማሁ ጽሑፍ ከመ ይትቀተል ክርስቶስ ወይትነሣእ እምውታን በሣልስት ዕለት

፵፮ ክርስቶስ እንዲሞት በሦስተኛውም ቀን ከሙታን እንዲነሣ እንዲሁም ተጽፏል ብሎ ነገራቸው ።

፵፯ ወይሰብኩ በስሙ ለንስሐ ።
፵፯ ስሙ ሕይወት መድኃኒት እንደሆነ ሊያምኑ ወለኅድገተ ኃጢአት ።
ኃጢአት ሊሰረይ ያስተምሩ ፤
ወለኵሉ ሕዝብ እኒዞሙ እምኢየሩሳሌም ።
ከኢየሩሳሌም ጀምረው ለሕዝቡ ሁሉ ሊያስተምሩ ።

፵፰ ወአንትሙሰ ሰማዕቱ ለዝንቱ ነገር ።
፵፰ እናንተም ለዚህ ነገር ምስክሮች ናችሁ ።
፵፱ ወናሁ እፌኑ ተስፋሁ ለአቡየ ላዕሌክሙ። ዮሐ ፲፬ ፡ ፳፮ ።

፵፱ እኔም እስወጥ እምነ መንፈስየ ዲበ ኵሉ ዘሥጋ ብሎ ያናገረውን ተስፋ መንፈስ ቅዱስን እሰድላችኋለሁ ።

ወአንትሙሰ ንበሩ ሀገረ ኢየሩሳሌም እስከ ትለብሱ ኃይለ እምአርያም ።
እናንተ ግን ከሰማይ ኃይል እስክትለብሱ ማለት ሰማያዊ ሀብትን ሰማያዊ ዕውቀትን ገንዘብ እስክ ታደርጉ ድረስ በኢየሩሳሌም ኑሩ ።

፶ ወእምዝ አውፅኦሙ አፍአ እስከ ቢታንያ ወአንሥአ እደዊሁ ላዕሌሆሙ ወባረኮሙ ።

፶ ወደ አፍአ እስከ ቢታንያ ድረስ አውጥቶ በአንብሮተ እድ እስከ ፓትርያርክነት ያለውን ማዕ ርግ ሾማቸው ።

፶፩ ወእንዘ ይባርኮሙ ተረኃቆሙ ወዓርገ ሰማየ ። ማር. ፲፮ ፡ ፲፱ ግብ/ ሐ. ፩ ፡ ፱ ።

፶፩ ሾሚቸው የርቀት ያይደለ የርኅቀት ተሰ ውሯቸው ወደ ሰማይ ዓረገ ።

፶፪ ወእሙንቱሰ ሰገዱ ሎቱ ወተሠውጡ ኢየ ሩሳሌም በዓቢይ ፍሥሐ ።

፶፪ እርሳቸው ግን ደስ ብሏቸው እጅ ነሥተው ሰግደው ኢየሩሳሌም ተመለሱ ።

፶፫ ወነበሩ በቤተ መቅደስ እንዘ ዘልፈ ይባ ርክዎ ለእግዚአብሔር ።

፶፫ ዘወትር እግዚአብሔርን ሲያመሰግኑት ሲያገለግሉ በቤተ መቅደስ ኖሩ ።
መልአ ጽሕፈተ ብሥራቱ ለሉቃስ ወንጌላዊ አሐዱ እምሰብአ ወክልኤቱ አርድዕት ዘጸሐፎ በልሳነ ዮናኒ ለሰብአ ሀገረ መቄዶንያ እምድኅረ ዕርገቱ ለእግዚእነ ውስተ ሰማይ በዕሥራ ወአሐዱ ዓመት ወበ፲ቱ ወ፱ቱ ዓመተ መንግሥቱ ለአቅሎንድዮን ቄሣር ።

ከሰባ ሁለቱ አርድእት አንዱ ሉቃስ አቅሎንድዮስ ቀላውዲዎስ ቄሣር በነገሠ በዐሥራ አራት ዓመት ጌታችን ወደ ሰማይ ባረገ በሃያ አንድ ዓመት ለመቄዶንያ ሰዎች በዮናኒ ቋንቋ የጻፈው ወንጌል ደረሰ ተፈጸመ ።
ወስብሐት ለእግዚአብሔር ።
አስጀምሮ ላስጨረሰኝ ለእግዚአብሔር ክብር ምስ ጋና ይግባው ። አሜን ።

## ትልቁ ምዕራፍ ዐቢይ ዘወንጌለ ሉቃስ ።

ምዕራፍ ፩ እስመ ብዙኃን እለ አኀዙ ።
ም ፪ ። ወኮነ በውእቱ መዋዕል ወፅአ ትእዛዝ
ም ፫ ። ወእመ ዐሠርቱ ወኃምስቱ ።
ም ፬ ። ወመልአ መንፈስ ቅዱስ ላዕለ ኢየሱስ ።
ም ፭ ። ወሀለዉ ሰብእ ብዙኃን ።
ም ፮ ። ወእምዝ ካዕበ ወረረ እግዚእ ኢየሱስ ።
ም ፯ ። ወፈጺሞ ነጊሮቶሙ ቃሎ ለሕዝብ ።
ም ፰ ። ወእምዝ በሳኒታ አንሶሰወ ውስተ አህጉር
ም ፱ ። ወጸውዖሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሐዋርያት ።
ም ፲ ። ወእምዝ አርአየ ካልዓነ ሰብአ ።
ም ፲፩ ። ወእምዝ ጸለየ በአሐቲ መካን ።
ም ፲፪ ። ወተጋብኡ ኅቤሁ አእላፍ ሰብእ ።
ም ፲፫ ። ወቦ እለ መጽኡ ኀቤሁ አሚሃ ።
ም ፲፬ ። ወእምዝ ሖረ ወኮነ ሶበ በጽሐ ።
ም ፲፭ ። ወሀለዉ ይቀርብዎ መጸብሐን ።
ም ፲፮ ። ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለአርዳኢሁ
ም ፲፯ ። ወይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ግብር ይመጽእ መንሱት ።
ም ፲፰ ። ወይቤሎሙ በምሳሌ ከመ ዘልፈ ይጸልዩ።
ም ፲፱ ። ወበዊአ ኢያሪሆ አንሶሰወ ።
ም ፳ ። ወእምዝ አሐተ ዕለተ እንዘ ይሜህሮሙ
ም ፳፩ ። ወነጸረ ወርእየ አብዕልተ ዘከመ ያበውኡ መባዓ ።
ም ፳፪ ። ወቀርበ በዓለ መጸለት ።
ም ፳፫ ። ወተንሥኡ ኵሎሙ በምልአሙ ።
ም ፳፬ ። ወበእሑድ ሰንበት በጽባሕ ።

## የሉቃስ ወንጌል የዐቢይ ምዕራፍ ቍጥር ።

ወንጌልን ሊጽፉ የዠመሩ ብዙ ናቸውና ።
በዚያ ወራት ትእዛዙ ወጣ ።
በዐሥራ አምስተኛው ።
በጌታ መንፈስ ቅዱስ መላ ።
ብዙ ሰዎች ነበሩ ።
ዳግመኛ ጌታ ሔደ ።
ለሕዝብ አስተምሮ ከጨረሰ በኋላ ።
ከዚህ በኋላ በነጋው ባውራጃው ሁሉ ተመላለሰ ።
ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት ጠራቸው ።
ከዚህ በኋላ ሌሎች ሰብዓን መረጠ ።
ከዚህ በኋላ ባንዲት ቦታ ጸለየ ።
ብዙ ሰዎች ተሰበሰቡ ።
ያንጊዜ ወደሱ የመጡ ሰዎች አሉ ።
ከዚህ በኋላ ሔዶ በደረሰም ጊዜ ።
መጸብሐን ይቀርቡት ነበሩ ።
ጌታ ለተማሪዎቹ እንዲህ አላቸው ።

ለተማሪዎቹ ግድ ጥፋት ይመጣል አላቸው ።
ዘወትር እንዲጸልዩ በምሳሌ ነገራቸው ።
ኢያሪሖ በገባ ጊዜ ተመላለሰ ።
ከዚህ በኋላ አንድ ቀን ሲያስተምራቸው ።

መባ የሚያገቡትን ባለጠጎች አየ ።
የቂጣ በዓል ቀረበ ።
ሁሉም በመላው ተነሡ ።
እሑድ ማለዳ ።

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌለ ሉቃስ ። | | የሉቃስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|
| እስመ ብዙኃን እለ አኀዙ ይጽሐፉ ፤ ምዕ ፩ | ቍ ፩ | ወንጌልን ሊጽፉ የሞከሩ ብዙ ናቸውና ። |
| በእንተ ዘከመ አይድዓ ገብርኤል መልአክ ልደቶ ለዮሐንስ ፤ | ቍ ፲፩ | ገብርኤል የዮሐንስን ልደት እንደ ተናገረ ። |
| በእንተ ዘከመ አብሠራ ለማርያም ሥጋዌሁ ለቃል | ቍ ፳፮ | የጌታን ሰው መሆን ለማርያም እንደ ነገራት ። |
| በእንተ ብጽሐት ኀበ ኤልሳቤጥ | ቍ ፴፱ | ወደ ኤልሳቤጥ እመቤታችን እንደ ደረሰች ። |
| በእንተ ልደተ ዮሐንስ መጥምቅ ፤ | ቍ ፶፯ | ስለ ዮሐንስ መወለድ ። |
| በእንተ ልደተ ኢየሱስ ፤ ም ፪ | ቍ ፩ | ስለ ኢየሱስ መወለድ ። |
| በእንተ ዘከመ ተገዝረ ኢየሱስ ወዘከመ አቀምዎ ውስተ ቤተ መቅደስ ፤ | ቍ ፳፩ | ስለ ጌታ መገዘርና ከቤተ መቅደስ ውስጥ ስለ አቆሙት ። |
| በእንተ ኢየሱስ ሕፃን | ቍ ፴፱ | ስለ ሕፃን ኢየሱስ ። |
| በእንተ ዘከመ ረፈቀ ኢየሱስ ማእከለ ሊቃውንት | ቍ ፵፮ | ስለ ጌታ መቀመጥ ከሽማግሎች መካከል ። |
| በእንተ ስብከት ዘዮሐንስ መጥምቅ ፤ ም ፫ | ቍ ፩ | ስለ ዮሐንስ ማስተማር ። |
| በእንተ ዘከመ ተሞቅሐ ዮሐንስ መጥምቅ | ቍ ፲፱ | ስለ ዮሐንስ መታሰር ። |
| በእንተ ጥምቀቱ ለኢየሱስ ፤ | ቍ ፳፩ | ስለ ጌታ መጠመቅ ። |
| በእንተ መጽሐፈ ትውልድ ዘኢየሱስ ፤ | ቍ ፳፫ | ስለ ጌታ ትውልድ ቍጥር ። |
| በእንተ ተመክሮት ዘኢየሱስ ም ፬ | ቍ ፩ | ስለ ጌታ መፈተን ። |
| በእንተ ዘከመ አኀዘ ኢየሱስ ይስብክ በገሊላ። | ቍ ፲፬ | ስለ ጌታ ማስተማር በገሊላ ። |
| በእንተ ዘከመ ሰበከ ኢየሱስ በናዝሬት ። | ቍ ፲፮ | ስለ ጌታ ማስተማር በናዝሬት ። |
| በእንተ ዘከመ ኀደጋ ኢየሱስ ለናዝሬት ወዘከመ ሖረ ቅፍርናሆም ። | ቍ ፴፩ | ጌታ ናዝሬትን ስለ ተዋት ፤ ወደ ቅፍርናሆምም ስለሔደ ። |
| በእንተ ዘከመ አሕየወ ኢየሱስ ዘቦቱ ጋኔን ። | ቍ ፴፫ | ጌታ ጋኔን ያደረበትን ስለ አዳነ ። |
| በእንተ ዘከመ አሕየዎሙ ኢየሱስ ለሐማተ ጴጥሮስ ወለካልዓን ሕሙማን ። | ቍ ፴፰ | ጌታ የጴጥሮስን አማትና ፤ ሌሎች በሽተኞችን ስለ አዳነ ። |
| በእንተ ዘከመ አኀዙ በተአምር ብዙኃ ዓሣ ። ምዕራፍ ፭ | ቍ ፩ | ብዙ ዓሣን በታምራት ስለ ያዙ ። |
| በእንተ ተጸውዖቶሙ ለሐዋርያት ቀዳማውያን ። | ቍ ፱ | የቀደሙ ሐዋርያት ስለ ተጠሩ ። |
| በእንተ ዘከመ አሕየዎሙ ኢየሱስ ለሰ ምጻዊ ወለመፃጕዕ ። | ቍ ፲፪ | ጌታ ለምጻሙንና መፃጕዑን ስለ አዳነ ። |
| በእንተ ተኀርዮተ ሌዊ ። | ቍ ፳፯ | ስለ ሌዊ መመረጥ ። |
| በእንተ ጾም ዘክርስቲያን ። | ቍ ፴፫ | ስለ ክርስቲያን ጾም ። |
| በእንተ ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ በእንተ ሰዊት ወዕለተ ሰንበት ። ም ፮ | ቍ ፩ | ጌታ ስለ እሸትና ስለ ሰንበት እንደ ተናገረ ። |
| በእንተ ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ ለዘየብሰት እዴሁ ። | ቍ ፮ | ጌታ እጁ የደረቀችውን ስለ አዳነው ። |
| በእንተ ዘከመ ሰመዮሙ ለ፲ቱ ወ፪ቱ ሐዋርያት ። | ቍ ፲፪ | ዐሥራ ሁለቱን ሐዋርያት እንደ ሾማቸው ። |

| መክሥተ እርእስት ዘወንጌለ ሉቃስ ። | | | የሉቃስ ወንጌል እርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|---|
| በእንተ ተራኅርኆተ ሳምራዊ | | ቍ ፳፰ | ስለ ሳምራዊ መራራት ማዘን ። |
| በእንተ ማርያ ወማርታ ። | | ቍ ፴፰ | ስለ ማርያና ማርታ ። |
| በእንተ ጸሎት ክርስቲያናዊት ። | ም ፲፩ | ቍ ፩ | ስለ ክርስቲያን ጸሎት ። |
| በእንተ ጽሙም ዘአኀዞ ጋኔን | | ቍ ፲፬ | ጋኔን ስለያዘው ደንቆሮ ። |
| በእንተ መናፍስት እኩያን ። | | ቍ ፳፬ | ስለ ክፉዎች አጋንንት ። |
| በእንተ ዘከመ ብፁዕ ውእቱ ዘይሰምዕ ቃለ እግዚአብሔር ። | ምዕራፍ፡ ፲፩ | ቍ ፳፯ | ወንጌልን የሚሰማ ብፁዕ እንደሆነ ። |
| በእንተ ትእምርተ ዮናስ ። | | ቍ ፳፱ | ስለ ዮናስ ምልክት ። |
| በእንተ ኢየሱስ ወፈሪሳውያን | | ቍ ፴፯ | ስለ ጌታና ስለ ፈሪሳውያን ። |
| በእንተ ብኍዕ ዘፈሪሳውያን ። | ም ፲፪ | ቍ ፩ | ስለ ፈሪሳውያን እርሾ ። |
| በእንተ ትዝሕርት ወበእንተ እኩይ ባዕል፤ | | ቍ ፲፫ | ስለ ትዕቢትና ስለክፉ ባለጠጋ ። |
| በእንተ ዘከመ ኢይደልዎ ለክርስቲያን ተፀፅቦት በከንቱ ። | | ቍ ፳፪ | ለክርስቲያን በከንቱ መቸገር እንዳይገባ ። |
| በእንተ ተጊሆት ። | | ቍ ፴፭ | ስለ መትጋት ። |
| በእንተ ዕርቅ ። | | ቍ ፶፰ | ስለ ዕርቅ ። |
| በእንተ ዘከመ ይደልዎ ለክርስቲያን ገቢረ ንስሐ በጐርሕ ። | ም ፲፫ | ቍ ፩ | ለክርስቲያን በግድ ንስሐ እንዲገባው ። |
| በእንተ በለስ ዘእልባቲ ፍሬ ። | | ቍ ፮ | ፍሬ ስለሌላት በለስ ። |
| በእንተ ብእሲት ዘድኅነት እምደዌሃ በዕለተ ሰንበት ። | | ቍ ፲ | በሰንበት ከደዌዋ ስለዳነች ሴት ። |
| በእንተ ኅጠተ ሰናፔ ወበእንተ ብኍዕ ። | | ቍ ፲፰ | ስለ ሰናፍጭ ቅንጣትና ስለ እርሾ ። |
| በእንተ ኍልቈ ኅሩያን ። | | ቍ ፳፫ | ስለ ተመረጡ ቍጥር ። |
| በእንተ ጽልዕ ዘሄሮድስ ። | | ቍ ፴፩ | ስለ ሄሮድስ ጥል ። |
| በእንተ ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ ተኀድጎታ ለኢየሩሌም ። | | ቍ ፴፬ | ጌታ ኢየሩሳሌም እንድትቀር እንደተናገረ ። |
| በእንተ ዘከመ ፈወሶ ኢየሱስ ለቅብው በሰንበት ። | ም ፲፬ | ቍ ፩ | ጌታ በሰንበት ሆዱ ያበጠውን ስለ ፈወሰው ። |
| በእንተ ዘከመ መሀረ ኢየሱስ ትሕትና ወፍቅረ ለእለ ይረፍቁ ። | | ቍ ፯ | ጌታ ለተቀመጡ ትሕትናንና ፍቅርን ስለአስተማረ ። |
| በእንተ ምሳሌ ዘዕሡራን ። | | ቍ ፲፮ | ስለ ተቀጠሩ ሰዎች ምሳሌ ። |
| በእንተ ዘከመ ይደሉ ተሊዎተ ኢየሱስ ። | | ቍ ፳፭ | ጌታን ስለ መከተል ። |
| በእንተ ተገድፎተ በግዕ ፤ | ም ፲፭ | ቍ ፩ | ስለ በግ ጥፋት |
| በእንተ ትረክቦተ ገመስ ። | | ቍ ፰ | ስለ ቀለበት መገኘት ። |
| በእንተ ተኀጕሎቱ ወተመይጦቱ ለወልድ ፤ | | ቍ ፲፩ | ስለ ልጅ መጥፋትና መመለስ ። |
| በእንተ መጋቢ ዘኢይትአመን | ም ፲፮ | ቍ ፩ | ስለ የማይታመን ሹም ። |
| በእንተ ተመድልዎት ዘፈሪሳውያን ። | ም ፲፮ | ቍ ፲፬ | ስለ ፈሪሳውያን ግብዝነት ። |
| በእንተ ባዕል ። | | ቍ ፲፱ | ስለ ባለጠጋው ፤ |
| በእንተ ዘከመ ተናገረ ኢየሱለ ላዕለ ዕቅፍት ። | ም ፲፯ | ቍ ፩ | ስለ መጠራጠር እንደተናገረ ፤ |
| በእንተ ገሥጾተ አኃው ። | | ቍ ፫ | ስለ ወንድሞች ምክር ። |
| በእንተ ኃይል ዘሃይማኖት ወዘከመ ይደሉ ፈጽሞቱ ለግብር ። | | ቍ ፭ | ስለ ሃይማኖት ኃይል ስለ ሥራ መፈጸም ። |
| በእንተ ፲ቱ እለ ለምጽ ። | | ቍ ፲፩ | ስለ ዐሥሩ ለምጻሞች ። |

| መክሥተ አርእስት ዘወንጌል ሉቃስ ። | | የሉቃስ ወንጌል አርእስት ማውጫ ። |
|---|---|---|
| በእንተ ሠሪዖተ ቍርባን ቅዱስ ። | ቍ ፲፱ | ስለ ቅዱስ ቍርባን ። |
| በእንተ ትእምርት ለዘያገብእ ፤ | ቍ ፳፩ | ስለ ሚያሲዘው ይሁዳ ምልክት ። |
| በእንተ ትሕትና ለክርስቲያን ። | ቍ ፳፬ | ስለ ክርስቲያን ትሕትና ። |
| በእንተ ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ በደብረ ዘይት ። | ቍ ፴፱ | ስለ ጌታ ጸሎት በደብረ ዘይት ። |
| በእንተ አግብኦት ዘይሁዳ ወተእኅዞቱ ለኢየሱስ ። | ቍ ፵፯ | ስለ ይሁዳ መስጠትና ስለ ጌታ መያዝ ። |
| በእንተ ክህደት ዘጴጥሮስ ። | ቍ ፶፬ | ስለ ጴጥሮስ መካድ ። |
| በእንተ ዘከመ ተሣለቁ እይሁድ ላዕለ ኢየሱስ ፤ | ቍ ፷፫ | ስለ አይሁድ በጌታ መዘበት ። |
| በእንተ ቀዊሞተ ኢየሱስ በውስተ ዐውድ ። | ቍ ፷፮ | ስለ ጌታ በሸንጎ መቆም ። |
| በእንተ ቀዊሞተ ኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ወሄሮድስ | ም. ፳፫ ቍ ፩ | ስለ ጌታ መቆም በጲላጦስና በሄሮድስ ፊት ። |
| በእንተ ዘከመ ኀረዩ በርባንሃ እምነ ኢየሱስ ወዘከመ ኰነንዎ ፤ | ቍ ፲፫ | ስለ በርባን መመረጥና ስለ ጌታ መፈረድ ። |
| በእንተ ፍኖት ለኀዘን ፤ | ቍ ፳፯ | ስለ ኀዘን መንገድ ። |
| በእንተ ተሰቅሎተ ኢየሱስ ፤ | ቍ ፴፫ | ስለ ጌታ መሰቀል ። |
| በእንተ ጸዕሩ ወሞቱ ለኢየሱስ ። | ቍ ፵፮ | ስለ ጌታ መጮህና ሞት ፤ |
| በእንተ ተቀብሮቱ ለኢየሱስ ፤ | ቍ ፶ | ስለ ጌታ መቀበር ፤ |
| በእንተ ተንሥኦቱ ለኢየሱስ ፤ | ም ፳፬ ቍ ፩ | ስለ ጌታ መነሣት ፤ |
| በእንተ እርድእት ዘኤማኁስ ፤ | ቍ ፲፫ | ስለ ኤማኁስ ተማሪዎች ፤ |
| በእንተ ዘከመ አስተርአዮሙ ኢየሱስ ለሐዋርያት ። | ቍ ፴፮ | ስለ ጌታ መታየት ለሐዋርያት ። |
| በእንተ ዘከመ ዐርገ ኢየሱስ ውስተ ሰማይ ። | ቍ ፶፩ | ስለ ጌታ ወደ ሰማይ መውጣት ፤ |

## የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ወንጌል ።
## ቅዱስ ዮሐንስ እንደ ጻፈው ።

ብሥራተ አብ ትሩፍ ረድዕ ተናጋሪ በመለኮት ዮሐንስ ወልደ ዘብዴዎስ ፍቁረ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ።

ጸሎቱ ወበረከቱ የሃሉ ምስሌነ ለዓለመ ዓለም አሜን ።

ይህ ቃል የሠለስቱ ምእት ነው ጥንተ ነገሩ እንደምን ነው ቢሉ እንደ ማቴዎስ ተርከ ዮሐንስ እንዳባቶቹ እንደ ነቢያት እንደ ወንድሞቹ እንደ ሐዋርያት አይጽፍም ። አባቶቹ ነቢያት በሥነ ፍጥረት በዋዌ ባገባብ ይጀምራሉ ። በሥነ ፍጥረት በቀዳሚ ገብረ እግዚአብሔር ሰማየ ወምድረ ብለው ባገባብ እኮን አንተ ትቤ እመ ፈጠርካሃ ለምድር ብለው በዋዌ ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ ብሔረ አውሲጢድ ዘስሙ ኢዮብ ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ በብሔረ አርማቴም እምደብረ ኤፍሬም ዘመሴፋ ዘስሙ ሕልቃና ። ወሀሎ ፩ዱ ብእሲ በብሔረ ባቢሎን ዘስሙ ኤልያቄም ብለው እንዳባቶቹ እንደ ነቢያትስ ይሁን ። እንደ ወንድሞቹ እንደ ሐዋርያት አለመጻፉ ስለምን ነው ቢሉ ፤ እንደ ማቴዎስ ወልደ ዳዊት ወልደ አብርሃም ብሎ ከአብርሃም ከዳዊት መወለዱን ተናግሮ ቢሆን ከዳዊት ከአብርሃም የተወለዱ ብዙ ነገሥታት አሉ የኒያ ይብቃው ባሉት ነበርና ። እንደ ማርቆስ ወልድየ አንተ ብሎ የባሕርይ ልጅነቱን ቢናገር ።

እስራኤል ወልድየ ዘበኵርየ ይባላሉ በጸጋ የሚወለዱ የምእመናን ልደት ይብቃው ባሉት ነበርና እንደ ሉቃስ መንፈስ ቅዱስ ይመጽእ ላእሌኪ ወኃይለ ልዑል ይጼልለኪ ብሎ በኅቱም ድንግልና ተፀንሶ በኅቱም ድንግልና መወለዱን ቢናገር አዳም ቅሉ ከኅቱም ምድር ተገኝቶ የለምን የርሱ ይብቃው ባሉት ነበርና ፤ መስተጻርር መስተቃርን የሌለበት ደረቅ ቃል ቀዳሚሁ ቃል አለ ይህን አርእስት ፫ቱ ምእት ሰጥተዋል ፤ እንደ ማቴዎስ ተርከ ብሥራተ ማቴዎስብሥራተ ማርቆስብሥራተ ሉቃስ፤ብሥራተ እብ ትሩፍ ረድዕ ተናጋሪ በመለኮት ዮሐንስ ወልደ ዘብዴዎስ ፍቁረ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ እያሉ ስለምን ነው ቢሉ ጥንቱን የጻሐፈው ደግነት የታወቀ እንደሆነ የመጽሐፉም ደግነት ይታወቃልና ይደልዎ ለዘያነብብ ቅድመ ይዝክር ስሞ ለበዓለ መጽሐፍ ወእምዝ ያንብብ ወይምሐር እንዲል ። ወንጌል ስብከት ብሥራት ቢል አንድ ነው ። ወንጌል ብሂል በልሳነ ጽርእ ወትርጓሜሁ ስብከት እንዲል። ዲያብሎስ እንደተሻረ ወልደ እግዚአብሔር እንደ ነገሠ ። ሞተ ሥጋ ሞተ ነፍስ እንደጠፋ ትናገራለችና ። አብ አለ በትምህርት ይወልደናልና እስመ አነ ወለድኩክሙ በትምህርተ ክርስቶስ እንዲል፣ ትሩፍ አለ ። በክብርም በግብርም ፍጹም ነውና ረድዕ አለ ። መጠኑ ለረድ እምከመ ኮነ ከመ ሊቁ ያለው የተፈጸመለት ከርሱ በቀር ሌላ የለምና ተናጋሪ በመለኮት መለኮተ ሲል ነው ። በግእዝ የገባ ነው ፤ ወአንተሰ ኢቀባዕከኒ በዘይት ርእስየ እንዲል ። ያንድነትን የሦስትነትን ነገር የተናገረ ፣ አንድም እንዳለው ተናጋሪ በመለኮት። በመለኮት ድሕንፃ ተቃኝቶ ያንድነትን የሦስትነትን ነገር የተናገረ ። በዚህ ታዖጎሎስ ተብሏል ። ነባቤ መለኮት ማለት ነው ። ጎርጎርዮስ ምሥጢረ ሥላሴን እምልቶ አስፍቶ አብዝቶ ቢናገር ነባቤ መለኮት እንደ ተባለ። ልመናው ክብሩ ይደርብንና የዘብዴዎስ ልጁ የክርስቶስ ወዳጁ ካሥራ ሁለቱ ሐዋርያት እንዱ ዮሐንስ የተናገረው ወንጌል ስብከት ብሥራት ብትል ይህ ነው ፍቁረ እግዚእነን ፫ቱ ፪ት ከራሳቸው አንቅተው አልተናገሩትም ከወንጌል ከውስጡ ረድዕ ዘያፈቅሮ ያለውን አግኝተው ተናግረውታል እንጂ

በእንተ ከዊኖቱ ለቃል መለኮታዊ ወቀፊን ዎቱ ለዮሐንስ ።

### ምዕራፍ ፩ ።

፩ ቀዳሚሁ ቃል ውእቱ ።

ጌታ ወንጌላውያንን ሲያጽፍ በመዋቅር ጀመረ በመሠረት ጨረሰ ነገር ግን ቤት ከመዋቅሩ እስከ መሠረቱ ከመሠረቱ እስከ መዋቅሩ የተያያዘ ነው እንጂ የተለያየ አይደለም ተጠመቀ ለማለት ተወለደ ማለት ጥንቱ ነው ። ተወለደ ለማለት ተፀነሰ ማለት ጥንቱ ነው ። ተፀነሰ ለማለት በቅድምና ነበረ ማለት ጥንቱ ነው ።

፩ ያቃል በቅድምና የነበረ ነው ወእንተሰ ጥበብ እምላዕሉ ቀዳሚሃ ንጽሕት ይእቲ ወሰውእቱ

መቅድመ ቃል ይባርከዎ እንዲል የት ተናግሮት ነበርና ውእቱ ብሎ አጸፈ ቢሉ ከወንድሞቼ አያይዞ፥ እንደ ወንድሞቹስ አይጽፍም ብለናል ብሎ በጥንተ ስብከት ላስተማራቸው ውእቱ ብሎ አጸፈላቸው በጥንተ ስብከት ያስተማርኳችሁ ያ ቃል በቅድምና የነበረ ነው ። እንድም ቀዳሚሁ ለፍጥረት ለየ ቀረው ነው ከሥነ ፍጥረት አስቀድሞ የነበረ ነው አእትሪኮን በርፎሪኮን አተርግዋን የሚባሉ ዝርዋን ቃላት እሉ ቃለ ሰብእ ቃለ እንስሳ ቃለ መላእክት

ስለ ሦስት ነገር ቃል ብሎታል ህልውናቸውን ቅድምናቸውን ለመናገር ፈጠረበትም ለማለት ህልውናቸውን ለመናገር ከልብ ከትንፋሽ ተለይቶ በአፍአ የሚገኝ ቃል የለም ። ህልዋን እሙንቱ በአብ እንዘ ይሄልዉ በበ አካላቲሆሙ ነአምን በአብ ከመ ህልው በወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ወነአምን በወልድ ከመ ህልው በአብ ወመንፈስ ቅዱስ ወነአምን በመንፈስ ቅዱስ ከመ ህልው በአብ ወወልድ እንዲል ቀድምናቸውን ለመናገር ። ልብ እስትንፋስ ቀድመው ወደኋላ የሚገኝ ቃል የለም ፣ አሐቲ ቅድምና ሆሙ ለሥላሴ ወዕሩያን እሙንቱ በቅድምና እንዲል ። ፈጠረበትም ለማለት አብኒ ፈጠረ በቃሉ ዘውእቱ እምነ መለኮቱ ወኵሎ ፈጠርከ በቃልከ እንዲል ። እምላከ ወልድ አይለውምን ቢሉ አምላከ ቢለው እንስ እቤ አማልክት አንትሙ ያላቸው እሉ የኒያ ይብቃው ባሉት ነበርና ። ወልድም ቢለው እሥራኤል ወልድየ ዘበኵርየ ይባላሉ ምእመናን በጸጋ የሚወለዱት ልደት እለ የነዚያ ይብቃውባሉት ነበርና ዳግመኛም ወልድ ብሎት ቢሆን የሁለቱን አንድነት ነው እንጂ የሦስቱን አንድነት አያስረዳምና ወዝስም ዘውእቱ ወልድ ያጤይቅ ኅብረተ ህላዌሆሙ ለአብ ወለወልድ እንዲል ። ቃል ግን የሦስቱን አንድነት ያስረዳልና ቃለ አብ ወቃለ መንፈስ ቅዱስ ወልድኒ ቃሎሙ ለአብ ወለመንፈስ ቅዱስ እንዲል ያውስ ቢሆን የሦስቱን አንድነት በሚያስረዳ እዱ መዝራዕቱ የማኑ አይለውምን ቢሉ የአፍአ አንድነታቸውን ነው እንጂ የውስጥ አንድነታቸውን አያስረዳምና ውሳጣዊ አንድነታቸውን በሚያስረዳ ጥበቡ ምክሩ ሕሊናሁ አይለውምን ቢሉ የምክር የሕሊና መዲናቸው መገለጫቸው ቃል ነውና በመዲናቸው በመገለጫቸው በቃል ተናገረው እንድም ቃል ከልብ ተገኝቶ በልብ ህልው ሁኖ ሲኖር ልገለጽ ባለ ጊዜ ባንደበት እንዲገለጽ እርሱም ከአብ ተገኝቶ በአብ ህልው ሆኖ ሲኖር ልገለጽ ባለ ጊዜ በሥጋ ተገልጧልና ዳግመኛ ለምሳሌ ይመቸኝ ብሎ ለቃል እርምም ጽርአት የለውም በልቡና ሲወጣ ሲወርድ ይኖራል ጸሐፊ ቀለም በጥብጦ ብርዕ ቀርጾ ብራና ደምጦ በጻፈ ጊዜ ረቂቁ ቃል ከልቡና ሳይለይ በቀለም ገዘፎ እንዲታይ ረቂቅ አካላዊ ቃልም ከአብ አንድነት ሳይለይ በሥጋ ገዘፎ ታይቷልና በዚህም ቃል ኃደረ በብእሲ የሚል ሳምሳጤ ጳውሎስ ለፈ እማርያም የሚሉ እለፎጢኖስ ተረተውብታል ።

ወውእቱ ቃል ኀበ እግዚአብሔር ውእቱ ። በቅድምናም ነበረ ያልሁት ያ ቃል በእግዚአብሔር አብ ህልው ነው ጸዳል በከበብ ነበልባል በእሳት ርጥበት በስፍሐት ቃል በልብ ህልው ሁኖ እንዲኖር ህልዋን እሙንቱ በአብ እንዘ ይሄልዉ በበአካላቲሆሙ ነአምን በአብ ከመ ህልው በወልድ መንፈስ ቅዱስ። ወነአምን በወልድ ከመ ህልው በአብ ወመንፈስ ቅዱስ ወነአምን በመንፈስ ቅዱስ ከመ ህልው በአብ ወወልድ እንዲል ። በዚህም ቃል መዓርገ መንግሥት የሚሰጡ እለ አቡሊናርዮስ መዓርገ ርቀት የሚሰጡ እለ አርጌንስ አንድ ገጽ የሚል ሰባልዮስ ተረተውብታል ። ወእግዚአብሔር ውእቱ ቃል ፣ ያቃል እግ እግዚአብሔር ነው ማለት ጸዳል በከበብ ርጥበት በስፍሐት ነበልባል በእሳት ቃል በልብ ህልው ሆኖ እንዲኖር አይደለም ። በተለየ አካሉ ፈጥሮ የሚገዛ ነው ። ይህስ እንዳይሆን ለምሥጢረ ሥላሴ ምሳሌ ነው ምሳሌ ያፈርሳል ብሎ ደቀ መዝሙር ከመምህሩ ሎሌ ከጌታው ተጠግቶ እንደሚገዛው አገዛዝ ያይደለ በተለየ አካሉ ፈጥሮ የሚገዛ ነው ፣ በዚህም ቃል ምትሐት የሚሉ እነ ማኒ ዋልጦስ ዝርው የሚሉ እለ መርቅያን ወልድ ፍጡር በመለኮቱ የሚል አርዮስ ተረተውብታል

፪ ወከማሁ ቀዳሚሁ እምቀዲሙ ኀበ እግዚአብሔር ውእቱ ።

፪ ያ ቃል በእግዚአብሔር አብ ህልው ነው እንዳልኩ በእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስም ህልው ነው ። እንድም ወዝንቱ ቀዳሚሁ እምቀዲሙ ይላል ይህ ቃል ከጥንት ጀምሮ በእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ህልው ነው በዚህም ቃል መንፈስ ቅዱስ ሕጹጽ የሚሉ እለ መቅዶንዮስ ተረተውብታል ቀዳሚሁ ቃል ባለው በቀዳሚ ኮነ ቃል ይላል ። እስመ ውእቱ ይቤ ወኮኑ ካለው ጋራ ንባብ ቢያሳብረው ምሥጢር አያሳብረውም እኒያን ተፈጠሩ ሲላቸው ነው ። እርሱን ግን በቅድምና ነበረ ሲለው ነውና ። በቀዳሚ ኮነ ቃል ባለው በቀዳሚ ሀሎ ቃል ይላል ፣ በቀዳሚ ገብረ እግዚአብሔር ሰማየ ወምድረ ካለው ጋራ ንባብ ቢያሳብረው ምሥጢር አያሳብረውም እኒያን በቀዳማይ ዕለት በቀዳማይ ሰዓት ተፈጠሩ ሲላቸው ነው ። ጥንት አላቸው ጥንታቸው ዕለተ እሑድ ናት ፣ እርሱን ግን በቅድምና ነበረ ሲለው ነውና በቀዳሚ ሀሎ ቃል ፣ ወውእቱ ቃል ኀበ እግዚአብሔር ሀለወ ወእግዚአብሔር ውእቱ ቃል ወከማሁ ቀዳሚሁ እምቀዲሙ ኀበ እግዚአብሔር ሀለወ ይላል ። እግዚአብሔር ብሎ ሦስትነታቸውን ተና

ገረ አንበ ሶበ እቤ እግዚአብሐር እብል በአንተ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ እንዲል አንድም ኅበ ኅበ ኅበ ብሎ ሦስትነታቸውን እግዚአብሔር እግዚአብሔር እግዚአብሔር ብሎ አንድነታቸውን ተናገረ ፤ ከዚህም አያይዘው ሊቃውንት ምሥጢረ ሥላሴን አምልተው አስፍተው አብዝተው ተናግረዋል ተርጕመዋል ። አምላክ ውእቱ አብ አምላክ ውእቱ ወልድ አምላክ ውእቱ መንፈስ ቅዱስ ። ወኢይትበሀሉ ሠለስተ አማልክተ አላ አሐዱ አሙንቱ ምሥጢረ ሥላሴ ይትከፈል ወኢይትከፈል ፤ ይትከፈሉ በአካላት ወኢይትከፈሉ በመለኮት ሥላሴ በተዋሕዶ ወተዋሕዶ በሥላሴ ተጋብኦ በተከፍሎ ወተከፍሎ በተጋብኦ ኅቡራን እንበለ ተሌልዮ ወሊሉያን እንበለ ተድምርት እንዘ አሐዱ ሠለስቱ ወእንዘ ሠለስቱ አሐዱ ይሜለሱ በአካላት ወይትወሐዱ በመለኮት ህልዋን እሙንቱ በአብ እንዘ ይሄልዉ በበአካላቲሆሙ ነአምን በአብ ከመ ህልው በወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ወነአምን በወልድ ከመ ህልው በአብ ወመንፈስ ቅዱስ ወነአምን በመንፈስ ቅዱስ ከመ ህልው በአብ ወወልድ እንዲል አንድም ምሥጢረ ሥላሴ ከጥንት ሲነገር ሲያያዝ የመጣ ነው እንጂ እንደ እንግዳ ደራሽ እንደ ወኀ ፈሳሽ አይደለም በጥንተ ፍጥረት ንግበር ሰብአ በአርአያነ ወበአምሳሊነ ብለዋል ። ንግበር ፡ የሦስትነት ፡ አርአያነ ያንድነት ይህማ አንዱ አንዱን ንግበር ቢለው ይሆን የለምን ብሎ ከዚህ ይልቅ የጎላ ከዚህ ይልቅ የሚያስረዳ ንዑ ንረድ ወንከዓው ነገሮሙ ለዕንለ እመ ሕያው እስመ አሐዱ ዘመድ እሙንቱ ብሲዋል ንዑ የሦስትነት ነገሮሙ ያንድነት ይህስ ቢሆን አንዱ አምላውኝ ሰላውን ንዑ ቢላቸው ይሆን የለምን ብሎ ከዚህ ይልቅ የጎላ ከዚህ ይልቅ የሚያስረዳ አነ ውእቱ እግዚአብሔር አምላክከ አምላከ አበዊከ አምላከ አብርሃም አምላከ ይስሐቅ ወአምላከ ያዕቆብ ብለዋል ። አነ ያንድነት አምላከ አምላከ አምላክ የሦስትነት ፤ ዳዊትም ሣህሉ ለእግዚአብሔር መልአ ምድረ ወበቃለ እግዚአብሔር ጸንዓ ሰማያት። ወእምእስትንፋሰ አፉሁ ኵሉ ኃይሎሙ ብሏል ። ፀልጁ ህልው ሁኖ ሥራ ስለ ሠራ።ዳግመኛም ዓቢይ እግዚአብሔር ወዓቢይ ኃይሉ ወአልቦ ኍልቍ ለጥበቢሁ ። ዓቢይ እግዚአብሔር ። እግዚአብሔር አብ ወዓቢይ ኃይሉ እግዚአብሔር ወልድ ኃይሉ ስለ ተገለጸበት ። ወኍልቊ ፡ ኍልቍ ለጥበቢሁ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ስለ ሀብቱ ብዛት ዳዊት ይህን በተናገረ በ፪፻ ዘመን ኢሳይያስ በዓመተ ሞተ ዖዝያን ንጉሥ ርኢክዎ ለእግዚአብሔር እንዘ ይነብር ዲበ መንበሩ ነዋህ ወብሩህ ወምሉእ ቤተ ስብሐቲሁ ወሱራፌል ይቀውሙ ዓውዶ ለለ፩ በበ፮ ክነፊሆሙ በ፪ ክነፊሆሙ ይከድኑ ገጾሙ ወበ፪ቱ ክነፊሆሙ ይከድኑ እገሪሆሙ ወበ፪ቱ ክነፊሆሙ ይሠሩ እንጸረ ኅቡረ እንዘ ይብሉ ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ እግዚአብሔር ጸባኦት ፍጹም ምሉእ ሰማያተ ወምድረ ቅድሳተ ስብሐቲከ ብሏል ። ቅዱስ ቅዱስ ቅዱስ የሦስትነት ምሉእ ያንድነት ። መልአኩም መንፈሰ እግዚአብሔር ቅዱስ ይመጽእ ላዕሌኪ ብሏል ። ባለቤቱም ወእንዘ ታጠምቅዎሙ በሉ በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ብሏል ከዚህም አያያዘው ምሥጢረ ሥላሴን አምልተው አስፍተው አብዝተው ተናግረዋል አምላክ ውእቱ አብ ብለህ ህልው በወልድ እስኪል ጥቅስ እንዲህ በጥቂት ንባብ ብዙ ምሥጢር አናገረ ። እስመ ጸጋ መንፈስ ቅዱስ ዘከመዝ አምሳሊሁ ያመጽእ ብዙኃ ፍካሬ አኮ በብዙኅ ንባብ አላ በኅዳጥ እንዲል ።

፫ ወኵሉ ቦቱ ኮነ ።

፫ ሁሉ በርሱ ህልውና በርሱ አንድነት ተፈጠረ ወዘእንበሌሁሰ አልቦ ዘኮነ ወኢምንትኒ እምዘ ኮነ ከተፈጠረው ፍጥረት ግን ያለርሱ ህልውና ምንም ምን የተፈጠረ የለም ። በሐልዮ በአርምሞ የተፈጠረውን ለአብ የነቢብ የገቢሩን ለወልድ ሰጥተው የሚናገሩ አሉና በእርዮስም ያሳይቡታል ። ሸክላ ሠሪ መኖሪያዋን ሠርታ እንድትሠራ ፈጥሮ ፈጠረበት ካለ እርሱን በማን ፈጠረው ያሰኝበታልና ።

፬ ወዘኒ ኮነ በእንቲአሁ ቦቱ ሕይወት ውእቱ

፬ እርሱን ለማስመስገን እርሱን ለማስታወቅ በርሱ ሥልጣን የተፈጠረ ፍጥረት ሁሉ ሕይወት ነው ።

ወሕይወትሰ ብርሃኑ ለዕጓለ እመሕያው ውእቱ ። ሕይወትነቱም ለሰው ዕውቀት መሆን ነው ።

፭ ወብርሃንሰ ዘውስተ ጽልመት ያበርህ ወያርኢ

፭ በሥነ ፍጥረት ተመራምሮ የማያውቁት ዕውቀት በሰዋሬ ያለ ምሥጢርን ይገልጻል ። ለእመ ፈቀድከ ታእምር ዘንተ ብከ ሰማዕት ወካልዕ መምህር እምአፍአ ዘይመርሐከ ኀበ ዝንቱ ወኵሉ ዘተፈጥረ ለመፍቅደ ነባብያን ቦ እምኔሆሙ ለምህሮ ወቦ ለተገብሮ እንዘ ኢየኃድግ ርእሶ ዘእንበሊ ሰማዕት ። ወዘኢያስተርኢ እግዚአብሔር እምፍጥረተ ዓለም ይትዓወቅ ለፍጥረቱ በፍጥረቱ እንዲል ። በሥነ ፍጥረት ተመራምረው ያመኑ ብዙ ናቸው ከዚያው ግን ከቀደሙ ሰዎች አብርሃም ከኋላ ሰዎች ሙሴ ጸሊም ።

ወጽልመትኒ ኢይረክቦ ።
በሥነ ፍጥረት የሚመራመርን ሰው ድንቁርና አያገኘውም ። ወኢይቀርቦ ።

ስንኳን ሊያገኘው አይደርሰበትም ። አንድም ወዘኒ ኮነ በእንቲአሁ ብለህ መልስ ። እርሱን ለማስመስገን እርሱን ለማስታወቅ በርሱ ሥልጣን የተፈጠረፍጥረት

ሁሉ ሕይወት ነው ። ወሕይወትሰ ሕይወትነቱም በመመላለስ ። እፍራሲከኒ ሕይወት ውእቱ እንዲል ይህ አይወርድም ከዚህ ይቀራል ። እንድም ወዘሂ ኮነ እርሱን ለማመስገን እርሱን ለማስታወቅ በርሱ ሥልጣን የተፈጠረ ፍጥረት ሁሉ ሕይወት ነው ። ወሕይወትሰ ሕይወትነቱም ምግብ በመሆን እንድም ያበላልጣል ። ወሕይወትሰ ። ሕይወትስ ባለኝ አእምሮ ጠባይዕ ። ክብራስ ለጠባይዕ ነቢብ ወአእምሮ እንዲል ። ወብርሃንሰ ። በአእምሮ ጠባይዕ ተመራምሮ የሚያውቁት በሰዋሬ ያለ ምሥጢርን ይገልጣል ። እንዳባ ማቴዎስ በሥነ ፍጥረት ተመራምሮ በአእምሮ ጠባይዕ ዐውቆ ምግባረ ትሩፋት ሠርቶ በቅቶ ከመዓርገ ነጽሮ ደርሶ ከዚህ ሁኖ ሽቅብ ባየ ጊዜ እስከ ጽርሐ አርያም ቍልቍል ባየ ጊዜ እስከ በርባሮስ ያይ ነበር ወሶበ ሠረቀ ብርሃን አምላካዊ ውስተ ነፍስ ወተዋሐደት ነፍስ ምስሌሁ ያበውእ ለነፍስ ውስተ ኵሎን ጠባይዓት እለ ውስተ ሰማይ ወእለ ውስተ ምድር እንዲል ።

ወጽልመትኒ ኢይረክቦ በአእምሮ ጠባይዕ የሚመራመር ሰውን ድንቁርና አያገኘውም ስንኳን ሊያገኘው አይደርስበትም እንድም ወዘሂ ኮነ በእንቲአሁ ቦቱ ሕይወት ውእቱ ቦቱና በእንቲአሁ አንድ ወገን በርሱ ቃል የተነገረ ሃይማኖት ሕይወት ነው ። ወሕይወትሰ ሕይወትነቱም ለሰው ዕውቀት መሆን ነው ወብርሃንሰ በሃይማኖት ተመራምሮ ያወቁት ዕውቀት በስዋሬ ያለ እግዚአብሔርን ይገልጻል ። እበዊነኒ ይሰምዩከ ቀባረ ወዓውሎ በእንተ ስዋሬከ እንዘ ደመናተ ብርሃን የዓውዱከ ወረሰየ ጽልመተ ምስዋሮ እስመ እሚን ትሬስዮ ለሀኢሀለወ ከመ ዘሀለወ እንዲል ። ወጽልመትሰ ኢይረክቦ በሃይማኖት ያወቀን ሰው ክህደት አያገኘውም ወኢይቀርቦ ስንኳን ሊያገኘው አይደርስበትም እንድም በርሱ ቃል የተሰጠ ሥጋው ደሙ ሕይወት ነው ። ወሕይወትሰ ሕይወትነቱም ለሰው ዕውቀት መሆን ነው ። ወብርሃንሰ በሥጋው ደሙ ያወቁት ዕውቀት በሰዋሬ ያለ ምሥጢርን ይገልጣል ወሶበ ይበውእ ውስተ ልበ ንጹሕ ሶቤሃ ያነቅሆ ለተናግሮ እንዲል ከኃጢአት ነጽተው ቢቀበሉት ምሥጢር ይገልጣልና ወጽልመትኒ ሥጋውን ደሙን የተቀበለን ሰው ፣ ኃጢአት ኢይመውእ ወኢይኄይሎ ኃጢአት አይሠለጥንበትም ድል አይነሣውም ። እንድም ወቦቱ ኮነ ሕይወት ወቦቱ ሕይወት ውእቱ። ይላል በመጀመሪያው እንደ ሥነፍጥረት ባ፪ኛው እንደ ሃይማኖት ያስተረጕማል ። ዘወስተ ጽልመት ባለው በውስተ ጽልመት ይላል የላይ ቤት አብነት በጽልመተ ልብ በአይሁዳዊ አድሮ ምሥጢርን ይገልጣል ማለት ነው ።

፮ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ዘተፈነወ እምኀበ እግዚአብሔር ዘስሙ ዮሐንስ ።

፮ ስለ ሦስት ነገር ያመጣዋል ከወንድሞቹ ለማያያዝ ስሙን ለመናገር ምስክር ሦስት ለማድረግ ራሱ ዮሐንስ መጥምቅ እብ ከእግዚአብሔር የታዘዘ ዮሐንስ የሚባል አንድ ሰው ነበር ።

፯ ወውእቱ መጽአ ስማዕተ ይኩን በእንተ ብርሃን ።

የብርሃንን ነገር ይመሰክር ዘንድ የመጣ ። እንድም ለስምዕ ይላል አብነት የብርሃንን ነገር ለመመስከር የመጣ ።

ከመ ዙሉ ይእመን እምኔሁ ሰው ሁሉ ከርሱ ተምሮ ያምን ዘንድ ። እንድም በዘእምኔሁ ከርሱ በተገኘ ትምህርት ያምን ዘንድ እንድም ቦቱ ሰው ሁሉ በርሱ ያምን ዘንድ ።

፰ ወሊሊሁሰ ኢኮነ ብርሃን ።
፰ እርሱ ብርሃን አይደለም ።
ዳዕሙ ስማዕተ ይኩን በእንተ ብርሃን ።
የብርሃንን ነገር ይመሰክር ዘንድ እንጂ ዝንቱ ማኅቶት ብሎ ያመጣው የለምን ቢሉ የዮሐንስ ብርሃንነት የጸጋ ነው ። የጌታ ግን የባሕርይ ነውና ። እንድም በዮሐንስ ብርሃን ሕጸጽ አለበት ። በጌታ ብርሃንነት ግን ሕጸጽ የለበትምና ።

፱ ወብርሃን ጽድቅሰ ዘያበርሀ ለኵሉ ሰብእ ዘመጽአ ውስተ ዓለም ።

፱ ለሰው ሁሉ ዕውቀትን የሚገልጥ እውነተኛ ብርሃንስ ወደዚህ ዓለም የሚመጣው ነው እንድም ወሊሊሁሰ ኢኮነ ብርሃን እርሱ ግን ብርሃን አይደለም ዮሐንስ ስማዕቱ ከልሐ በእንቲአሁ ብሎ እስኪያመጣው ሌላ ነገር አገባበት ወብርሃን ጽድቅኒ ለሰው ሁሉ ዕውቀትን የሚገልጥ እውነተኛ ብርሃንም ወደዚህ ዓለም መጣ ።
ወውስተ ዓለም ሀሎ ።

መጽአ ብሎ ነበርና እንደ እንግዳ ደራሽ እንደ ውኅ ፈሳሽ በዓለሙ የሌለ ሁኖ አይደለም በዓለም ምሉእ ነው ።

ወዓለምኒ ቦቱ ኮነ ።
ሀሎ ብሎ ነበርና ሰው ቤት ሠርቶ በዚያ ተወስኖ እንዲኖር አይደለም ከዓለም በአፍአ ነው ማለት ምሉእ ነው ።

ወዓለምሰ ኢያእመሮ ።
ዓለም ግን አላወቀውም ። ላይኛው ዓለም ሌላ ይህ ዓለም ሌላ ነው ።
፲፩ ውስተ ዘአሁ መጽአ ንግበር ሰብአ በአርአያነ

፲፩ ብሎ ወደ ፈጠራቸው ወገኖች መጣ ባሕርይ ለማንግት ።
ወእሊአሁሰ ኢተወከፍዎ ።
እርሳቸው ግን አላመኑበትም ።

፲፪ ወለእለሰ ተወከፍዎ ወሀቦሙ ሥልጣነ ውሉደ እግዚአብሔር ይኩኑ ለእለ አምኑ በስሙ ።

፲፪ ባያምኑበትስ ምን ይጎዳል ቢያምኑበትስ ምን ይጠቀማል ትሉኝ እንደሆነ ላመኑበትስ በስሙ ያመኑ የእግዚአብሔር ልጆች ይባሉ ዘንድ ግእዛንን ሰጣቸው ። ግእዛንማ የሚሰጥ በተፈጥሮ አይደለ ምን ቢሉ ወደኃጢአት ወደጣዖት ሂደው አሳድፈ ውት ነበርና አይሰላቸው ሲል ነው ። ከጥቀርሻ የተሰቀለውን ጋሻ ጦር አውርደው ወልውለው ሰን ግለው ሥራ እንዲሠሩበት ።

፲፫ እለ ኢኮኑ እምነ ዘሥጋ ወደም
፲፫ ከሥጋዊ ከደማዊ ግብር ያልተገኙ ።

ወኢ እምሥምረተ ብእሲ ወብእሲት ።
ሴትና ወንድ ተዋደው ከሚሠሩት ሥራ ያልተገኙ ። አላ እምእግዚአብሔር ተወልዱ በመንፈስ ቅዱስ ከእግዚአብሔር ተወልደዋል እንጂ እንደም ውስተ ዚአሁ መጽአ ብለህ መልስ ወልድየ ዘበኵርየ ወዳ ላቸው ወደእስራኤል መጣ ። ወሐረ እምቅድመ ባዕ ዳን ነበ እለ እምደመ እስራኤል እንዲል ወእሊአሁሰ ወልድየ ዘበኵርየ ያላቸው እስራኤል ግን አልተቀ በሉትም ማለት አላመኑበትም ወለእለሰ ተወከፍዎ ቢያምኑበትስ ምን ይጠቀማል ባያምኑበትስ ምን ይጎዳል ትሉኝ እንደሆነ ላመኑበትስ ልጅነት ሰጣቸው ለእለሰ ተወከፍዎ ለእለ አምኑ በስሙ እንድ ወገን እለ ኢኮኑ ። ከሥጋዊ ከደማዊ ግብር ያልተገኙ ወኢእምሥምረተ ብእሲ ወብእሲት ሴትና ወንድ ተዋደው ከሚሠሩት ሥራ ያልተገኙ በሃይማኖት ከእግዚአብሔር ተወልደዋል እንጂ ከዚህ ያልተገኘ ምን አለ ቢሉ ሥራውን ከተውት ብሎ እስመ ኀደ ግነ አበ ቀዳማዌ ዘውእቱ አዳም ዘቦቱ ማሰነ እንዲል
፲፬ ወውእቱ ቃል ሥጋ ኮነ ማቴ ፡ ፩ ፲፰ ፡ ሉቃ፡ ፪፥ ፯ ።

፲፫ እምእግዚአብሔር ተወልዱ ብሎ ነበርና ግዙፉኑ ከረቂቁ እንደምን ይወለዳሉ ትሉኝ እንደ ሆነ ረቂቁም እንጂ ገዘፈ ረቂቁም ከገዘፈ ግዙፉኑም ከረቂቁ ይወለዳሉ ለማለት እንዴህ አለ እንድም መጽአ ብሎ ነበርና እንደ ወትሮ የረድኤት ያይደለ ያ ቃል የኵነት ሥጋ ሆነ ። እንድም ቀዳሚሁ ቃል ብሎ ነበርና በቅድምና የነበረ ያ ቃል ሥጋ ሆነ ። ወኀደረ ላዕሌነ ።

በኛም አደረ ። የኵነት የተዋሕዶ ኅድረት ። ኮነ ያለውን ይዘው ተለወጠ እንዳይሉ ኀደረ አለባቸው ኀደረ ያለውን ይዘው ኅድረት እንዳይሉ ኮነ አለ ባቸው ። ኮነና ኀደረ እንደ አለቃና እንደጠበቃ ይጠ ባበቃሉ ። ላዕሌነ ማለቱ ግን ሥጋ በቅድምና ነበረ ባሕርዩን አግዝፎ ታየ ምትሐት ውላጤ የሚሉ መና ፍቃን አሉና ላዕሌነ አለባቸው።ላዕሌነ ባለው በውስ ቴትነ ይላል በጽርእ ምላሽ እንደ መስኖ ውሀ ገብቶ ወጣ እንጂ ነፍስን ኢልተዋሐደም የሚሉ መናፍቃን አሉና ላዕሌነ ባለው ሥጋን ። በውስቴትነ ባለው ነፍስን እንደ ተዋሐደ ሰማጠየቅ ላዕሌነ በውስቴትነ አሉ ። ወሰወሮ እምኔነ በዘእምኔነ ቃልን በኛ ባሕርይ ሰወረው በተሰውሮተ ቃለ እግዚአብ ሔር በዘመድነ እንዲል ። እንድም ሥጋን ከኛ ሰወ ረው በተዋሕዶ የባሕርይ አምላክ አደረገው እንድም ሥግው ቃልን በርቀቱ ኢጸናው ። እፎኑ ኢየአምኑ እሙራን ሰብእ ከመ እምድኅረ ተሠገወ ነበረ ከመ ቃለ እንዲል ።

ወርኢነ ስብሐቲሁ ከመ ስብሐተ ፩ዱ ዋሕድ ለአቡሁ ላባቱ አንዳንድ ልጅ ክብር የሚሆን ክብሩን አየን ለት ። ልጅ ላባቱ አንድ የሆነ እንደሆነ ደጃፍ የመሰሰው ማጀት የጐረሰው ገንዘቡ ነው ። እሱም እስመ ኵሉ ዘቦ ለአቡየ ዚአየ ውእቱ እንዲል ያባቱ ገንዘብ ሁሉ ገንዘቡ ነውና ። እንድም ወይሰገድ ከመ ዋሕድ እንዲል ። እንዳንድ ልጅነቱ ክብሩን አየንለት። እንደም ስብሐቲሁ ለዋሕድ ከመ ስብሐተ አሐዱ አቡሁ ፡ ያባቱን ጌትነት በደብረ ሲና እንዳ የነ የርሱንም ጌትነት በዮርዳኖስ በደብረ ታቦር አየነ ። እንድም አባቱ በኤልያስ አድሮ አንድ ምውት በኤልሳዕ አድሮ ሁለት ምውት ሲያሥነሣ እንዳየነ እርሱም ሰው ሁኖ ያራት ቀን ሬሳ አልዓ ዛርን የለት ሬሳ ወልደ መበለትን ወለተ ኢያዒሮስን ሲያሥነሣ አየንለት ። ለሐዲሰ ይሁን ለብሉዩ ወዴት ነበርና ርኢነ አለ ቢሉ የነሙሴን ዓይን ዓይን አድርጐ አባ ሕርያቆስ እርሱ ሳይኖር የሐዋርያትን መብል መብል አድርጎ ንሕነ እሙንቱ እለ በላዕነ ምስሌሁ እንዳለ ።

ዘምሉእ ጸጋ ።
ጸጋን የተመላ ። ጸጋ አለው የባሕርይ ክብሩን ለኛ የሚሰጠው ስለሆነ ወዘመለኮቱ ጸጋ ምሉእ እንዲል ወጽድቀ ። ጽድቀ አሚንን

ወሞገሰ ። ስርየተ ኃጢአትን ። እን ድም ዘምሉእ ወፍጹም በጸጋ ወበጽድቅ ወበሞገስ ይላል አብነት ።

፲፭ ዮሐንስ ሰማዕቱ በእንቲአሁ ከልሐ ወይቤ
፲፭ ወለሊሁሰ ኢኮነ ብርሃነ ብሎ ሌላ ነገር አግብቶበት ነበርና ከነገሩ ተመለሰ ። እንድም ሌላም ማግባት አይደለም እንዴህ እንደሆነ እገሌ ታው ቁልኝ ብሎ ምስክር እንደማብዛት ያለ ነው ምስክሩ ዮሐንስ የርሱን ነገር ጮሆ ተናገረ መጮህስ የለም ጮሆ የተናገሩት ከሩቅ እንዲሰማ የርሱም ነገሩ ጽንፍ

እስከ ጽንፍ ተሰምቷልና ።
ዝውእቱ ዘእቤለክሙ አነ በእንቲአሁ ይመጽእ አምድኅሬየ ብእሲ ዘሀሎ እምቅድሜየ ። ከኔ አስቀድሞ የነበረ ከኔ በኋላ ይመጣል ያልኋችሁ ሰው ይህ ነው ። ሀሎ እምቅድሜየ እንደአምላክነቱ ፡ ብእሲ ይመጽእ እምድኅሬይ እንደሰውነቱ ።

እስመ አምቅድሜየ ውእቱ ኮነ ከኔ በፊት ነበርና ማለት የባሕርይ አምላክ ነውና ።

፲፮ እስመ እምተረፈ ዚአሁ ንሣዕነ ኵልነ ጸጋ በዲበ ጸጋ ። ፩. ጢሞ ፮ ፡ ፲፯ ።

፲፮ ከፍጹም ጌትነቱ ከተፈጸመለት ሀብቱ በዐሥርቱ ቃላት ላይ ወንጌልን ። በመንፈስ ረድኤት ላይ መንፈስ ልደትን ። በአእምሮ ጠባይዕ ላይ መንፈሳዊ አእምሮን ተቀበልን ። አንድም ነሣእነ ጸጋ ሀየንተ ጸጋ ይላል ። ነሣእነ ጸጋ ። ወንጌልን ባሠርቱ ቃላት ስለ ጸናን ፈንታ ። ነሣእነ ጸጋ ። መንፈስ ልደትን በመንፈስ ረድኤት ስለ ጸናን ፈንታ ነሣእነ ጸጋ አእምሮ መንፈሳዊን። በአእምሮ ጠባይዕ ስለ ጸናን ፈንታ ። አንድም ነሣእነ ጸጋ በዲበ ጸጋ ሀየንተ ጸጋ ይላል ፡ በዐሠርቱ ቃላት ላይ ወንጌልን ። ባሠርቱ ቃላት ስለጸናን ፈንታ ። ዮሐንስ መጥምቅ ወዴት ነበርና ነሣእነ አለ ቢሉ እንዳይቀርበት ያውቃልና ወእምተረፈ ዚአሁ ይላል ።
ርኢነ ላለው ዋዌ ።

፲፯ እስመ ኦሪት በሙሴ ተውህበት ለነ ።

፲፯ ኦሪት በሙሴ ተሠርታልናለችና ። በዲበ ጸጋ ላለው ።

ወጸጋሰ ወጽድቅ በኢየሱስ ክርስቶስ ኮነ ለነ ።
ጸጋ ጽድቅ ወንጌል ግን በኢየሱስ ክርስቶስ ተሠርታልናለችና ። ነሣእነ ጸጋ አንድም ኦሪት በሙሴ ተሰርታልናለች እኮን ፡ ጸጋ ጽድቅ ወንጌል ግን በኢየሱስ ክርስቶስ ተሠርታልናለች ።

፲፰ ለእግዚአብሔርሰ አልቦ ዘርእዮ ግሙራ። ፩ ጢሞ ፮ ፲፮ ፩ ፡ ዮሐ ፬ ፲፪ ።

፲፰ ርኢነ ብሎ ነበርና እግዚአብሔርን ማን ያየው አለ ትሉኝ እንደሆነ እውነት ነው እግዚአብሔርንስ ከቶ በባሕርዩ ያየው የለም ። እስመ በአንጽሖ መንፈስ ርእይዎ ነቢያት ለእግዚአብሔር ወተናጸሩ ገጸ በገጽ ይል የለምን ቢሉ ባሕር አየሁ እሳት አየሁ ሰማይ አየሁ ማለት ነው እንጂ በባሕርዩ ያየው የለም ። ኢላ ወልድ ዋሕድ ዘሀሎ ውስተ ሕፅነ አቡሁ ውእቱ ነገረ ባባቱ ዕሪና ያለ ወልድ በባሕርዩ አይቶ ነገረን እንጂ አንድም ከነቢያት ወገን ልጅ ሆኖ ያየው የለም ልጁ ልጅ ሆኖ በባሕርይ አይቶ ነገረን እንጂ ።

በእንተ ስምዐ ለዮሐንስ መጥምቅ ።

፲፱ ወዝንቱ ውእቱ ስምዐ ለዮሐንስ ።
፲፱ የዮሐንስ ወንጌላዊ ምስክርነቱ ይህ ነው ።

ርኢነ ስብሐቲሁ ያለው አመ ለአኩ ብለህ ለዮሐንስ መጥምቅ ስጥ ። አንድም የዮሐንስ መጥምቅ ምስክርነቱ ይህ ነው ይመጽእ እምድኅሬየ ዘሀሎ እምቅድሜየ ያለው ። ወአመ ለአኩ ብለህ ያለፈውንም የሚመጣውንም ለዮሐንስ መጥምቅ ስጥ ። አንድም የዮሐንስ መጥምቅ ምስክርነቱ ይህ ነው ። ዝ ያለውን ያመጣዋል ።

አመ ለአኩ ኀቤሁ አይሁድ እምኢየሩሳሌም ካህናተ ወሌዋውያነ ።

አይሁድ ከኢየሩሳሌም ካህናት ሌዋውያንን በላኩ ጊዜ ሌዋውያን ካህናትማ ይልኩን ይላኩ ቢሉ ደግን ሰው ከደግ መላክ ልማድ ነው ። ታሪክ የሁለቱን ነገድ ተኩል በዮርዳኖስ ማዶ ግንብ መሥራት ጀመሩ ጣዖት ለማምለክ ግንብ ይሠሩ ጀመሩ ብለው ለኢያሱ ነገሩት ቦታ ጠቧችሁ እንደሆነ ወደኔ ኑ እንጂ ጣዖት አታምልኩ ብሎ ዐሥሩን የቤት አለቆች ፊንሐስን ሊቀ ካህናቱን ላከ ። ጣዖትስ እንዳናመልክ አምላከ እስራኤል ያውቃል ነገር ግን ከዘመን ብዛት የተነሣ ልጆቻችሁ ልጆቻችንን እናንተ ከዚህ ምን አላችሁ አባቶቻችሁ በዮርዳኖስ ዳር ቀርተው የለም እንዳይሏቸው በቤተ መቅደስ አንጻር ይሁንልን ብለን ነው እንጂ ብለውታል ። አንድም መልከተኞችን በቃል አምጣ ። አይሁድ ካህናት ሌዋውያን ወደርሱ በላኩ ጊዜ ።
ከመ ይስአልዎ ወይቤልዎ መኑ አንተ ።
አንተ ማነህ ብለው ይጠይቁት ዘንድ ወአመ ይቤልዎ ይላል ለአኩ ላለው ዋዌ በላኩበት እንዲህም ባሉት ጊዜ ።

፳ አምነ ወኢክህደ ከመ ኢኮነ ውእቱ ክርስቶስሃ ።

፳ አመነ እንጂ አልካደም ማለት ክርስቶስ ነህ ቢሉት አይደለሁም አለ እንጂ ነኝ አላለም ። በዝንቱ ስም ተሰምዩ ነቢያት ቅቡዓነ እንዲል ። ነኝ አይላቸውም ቢሉ ለልቡናቸው ምላሽ አይደለምና
፳፩ ወይቤልዎ መኑ አንተ
፳፩ አንተ ማነህ ።
ኤልያስኑ አንተ ።
ኤልያስን ነህ አሉት ።
ወይቤ ኢኮንኩ ። አይደለሁም አለ ።
እመሰ ትፈቅዱ ትትወከፍዎ ዝውእቱ ኤልያስ ዘሀለዎ ይምጻእ ፡ ይል የለምን ቢሉ ለልቡናቸው ምላሽ አይደለምና ወይቤልዎ ነቢይኑ አንተ ።

ሙሴ ኢያሱ ነህ ።
ወይቤ አልቦ ።
አይደለሁም አለ ። ወወህበ ኃይለ ተነብዮ ለመጥ ምቅ እንዲል እኒያም ማስተማር ማጥመቅ ነው እርሱም ያስተምራቸዋል ያጠምቃቸዋል ነኝ አይ ላቸውም ቢሉ ለልቡናቸው ምላሽ አይደለምና ።

፳፪ ወይቤልዎ መኑመ አንተ እንከ ከመ ናይ ድእሙ ወናጠይቆሙ ለእለ ለአኩኑ ወፈነውነ

፳፪ ለአኩን በነገር ፈነውነ በእግር ለላኩን እንነግራቸው እናስረዳቸው ዘንድ እንኪያ ማነህ ።
መኑ ትብል ርእሰከ ።
ማንኝ ትላለህ አሉት ።

፳፫ ወይቤ አንሰ ቃለ ዓዋዲ ዘይሰብከ በገዳም ወይብል ጺሑአ ፍኖቶ ለእግዚአብሔር በከመ ይቤ ኢሳይያ ስነቢይ።ኢሳ፡፵፡፫ማቴ፡፴፡፫ማር፡፩፡፫ሉቃ.፫፡፬

፳፫ አኔስ ኢሳይያስ እንደ ተናገረ የእግ[?]አብ ሔርን መንገድ ጥረጉ ብዬ በገዳም የማስተምር ዐዋጅ ነጋሪ ነኝ ።

፳፬ ወእለሰ ተፈነዉ እምፈሪሳውያን እሙንቱ
፳፬ የተላኩት ግን ከፈሪሳውያን ነበሩ ።
፳፭ ወተስእልዎ ወይቤልዎ በእፎ አንከ ታጠ ምቅ ለእመ ኢኮንከ ክርስቶስሃ ።

፳፭ ቢሰጡን አንነዳ ቢነሱን አናረዳ የማይሉ ዶጋማ ናቸውና ። መላልሰው ይጠይቁታል ። ለም ንት ሲል ነው ። በእፎ ትጼእል ሊቀ ካህናቲሁ እንዲል ። ክርስቶስን ካይደለህ ለምን ታጠምቃ ለህ ብለው ጠየቁት ክርስቶስ በመጣ ጊዜ እንዲያ ጠምቅ እነዝሕከሙ በማይ ንጹሕ ተብሎ ተነግሯል ወኢ ኤልያስሃ ። ኤልያሯን ካይደለህ ለምን ታጠምቃለህ አለ ዮርዳኖስን ከፍሎ መሻገ ሩን ጥምቀት ብሎለት ።
ወኢነቢየ ሙሴን ኢያሱን ካይደለህ ለምን ታጠምቃለህ ለኒያ እስመ ለኵሎሙ አበዊነ አጥመቆሙ ሙሴ በደመና ወበባሕር ወተጠምቃ እገሪሆሙ ስካህናት ተብሎ ተነግሮላቸዋል ።

፳፮ ወአውሥአ ዮሐንስ ወይቤሎሙ አንሰ አጠ ምቀክሙ በማይ ማቴዎስ ፫ ፣ ፲፩ ።

፳፮ እኔስ ለጠጅ ብርሌን ለልብስ ገላን እንዲ ያጥቡለት ለርሱ ጥምቀት በሚያበቃ ጥምቀት ለርሱ ተአምኖ ኃጣውእ በሚያበቃ ተአምኖ ኃጣውእ አጠምቃችኋለሁ አንድም በእፎ ብለህ መልስ ክር ስቶስ ካይደለህ ለምን ሥርዓት ለዋውጠህ ታስተ ምራለህ ክርስቶስ በመጣ ጊዜ ሥርዓት ለዋውጦ እንዲያስተምር መቅደስ ትትሐነጽ እስከ ክርስቶስ ንጉሥ ወእምዝ ትትመዘበር ተብሎ ተነግሮለታል ለኤልያስም ከመ ይሚጥ ልበ አበው ኀበ ውሉድ ተብሎ ። ለኢያሱም ፣ ነቢየ ያነሥእ ለክሙ እምአኃ ዊክሙ ተብሎ ተነግሮለታል ። ወአውሥአ ዮሐንስ ወይቤሎሙ አንሰ አጠምቀክሙ በማይ ምን ሥር ዓት ለዋውጬ አስተማርኩ ። እኒያም በውኃ ያጠ ምቋችሁ ነበር ። እኔም በውኃ አጠምቃችኋለሁ ። ወማእከሌክሙ ህሎ ይቀውም ዘኢ.ተአምርዎአንትሙ ሥርዓት ለዋውጦ የሚያስተምር እናንተ የማታ ውቁት ከመካከላችሁ ቁሟል ፣ ኢተአምርዎ አንደ አምላክነቱ ይቀውም ። አንደ ሰውነቱ ።

፳፯ ዘይመጽእ እምድኅሬየ ውእቱ ዘሀሎ እም ቅድሜየ ። ማር፡፩፡፯ ሉቃስ፡፫ ፲፯፡ ግብ ፲፫፡፲፭፡ ፲፯ ፲፱ ፬ ።

፳፯ ከኔ በኋላ የሚመጣው ከኔ አስቀድሞ የነ በረው ነው አለ ፣ የባሕርይ አምላክ ነው ።
ዘኢይደልወኒ እፍታሕ ቶታነ አሣእኒሁ እምገሪሁ። የአግሩን ጫማ ልፈታ የማይገባኝ ። ዕጼር ማቴዎስ አድንን ማርቆስ ፡ እፍታሕ ሉቃስ ፣ መገናኛው ዮሐንስ እንዲህ ግን ስለሆነ አድንን ይቀድማል እፍታሕ ይከተላል ዕጼር መጨረሻ ነው ይህን ተካ ፍለው ጽፈዋል ።

፳፰ ወከመዝ ኮነ በቢታንያ በቤተ ራባ በማ ዕዶተ ዮርዳኖስ በኀበ ሀሎ ያጠምቅ ዮሐንስ ።

፳፰ ዮሐንስ ያጠምቅበት በነበረ በዮርዳኖስ ማዶ ቢታንያ ቤተራባ በሚባሉ አገገር እንዲህ ያለ ጉባኤ እንዲህ ያለ ክርክር ተደረገ ። አንድም ቀድሞ አንያ ራባ የሚባሉ ነገሥታት ከተማ ሠርተ ውበት ኋላ ተፈትቷል ቀድሞ ከተማ ተሠርቶበት ነበር ኋላ ከተፈታ ዮሐንስ ያጠምቅበት በነበረ በዮርዳኖስ ማዶ እንዲህ ያለ ጉባኤ እንዲህ ያለ ክር ክር ተደረገ ።

፳፱ ወእመ ሳኒታ ርእዮ ዮሐንስ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይመጽእ ኀቤሁ ።
ወከመዝ ኮነ በቢታንያ በቤተራባ በማዕዶተ ዮር ዳኖስ በኀበ ሀሎ ዮሐንስ ያጠምቅ ብሎ ነበርና ለዚያ ሳኒታ አለ ።
አንድም ሕዝቡ ሊጠመቁ በዋዜማው ተሰብስበ ዋልና ለዚያ ሳኒታ አለ ። አንድም ጌታ ባሥረ ኛው ስዓተ ሌሊት ተጠምቆ ሁለቱን ተቦታው ሂዶ አንግቷል ቢነጋ ለመሰናበት መጥቷል ላሥሩ ስዓት ሁለቱን ሳኒታ አለው ።

፳፱ በነጋው ዮሐንስ ጌታ ወደርሱ ሲመጣ ባየ ጊዜ ።
ወይቤ ነዋ በግዑ ለእግዚአብሔር ዘያእትት ወያ ሴስል ኃጢአተ ዓለም ።
የሰውን ኃጢአት የሚያስተሰርይ የእግዚአብሔር መሥዋዕቱ እነሆ አለ ። እንዲሁም ባለጊዜ የሕዝቡን ቢሉ መሥዋዕታቸውን የካህናቱን ቢሉ

ሕጋቸውን እንዳሳሳፈባቸው ያጠይቃል ። ያአትት ወያሴስል ማለቱ ግን ስለ ጊዜው ስለዘላለሙ ስለ ሥጋ ስለ ነፍስ ስለ ሕዝብ ስለ አሕዛብ ለማለት የአትት ባለው ዘይጸውር የሚል አብነት ይገኛል ቀድሞ የብሉይ ሊቀ ካህናት እጁን ከበጉ ራስ አድ ርጎ ይጸልይ ነበር ኃጢአታችን ባንተ ምክንያት ይሰረያል ሲል በዚያ ግሥ እንዲህ አለ ።

፴ ዝንቱ ውእቱ ዘእቤለክሙ እነ በእንቲአሁ ይመጽእ እምድኅሬየ ብእሲ ዘሀሎ እምቅድሜየ ።

፴ ከኔ አስቀድሞ የነበረው ከኔ በኋላ ይመጣል ያልኳችሁ ሰው ይህ ነው ።
እስመ እምቅድሜየ ውእቱ ኮነ
ከኔ አስቀድሞ ነበርና ማለት የባሕርይ አምላክ ነውና ።

፴፩ ወአንሰ ኢየአምሮ ።
፴፩ እኔ ግን አላውቀውም ። ቃል ለቃል ተጨዋ ውቶ ማማለጃ በልቶ ተዘምዶተ ሥጋ ኑሮት አድልቶ ይሉኛል ብሎ ። አንድም የዮሐንስ አስተዳደግ በገ ዳም ። የጌታ አስተዳደግ በዓለም ነውና ። አንድም ካንድ ቀን በቀር አይቶት ባያውቅ ። ታሪክ ከግብጽ ከወጡ በኋላ ጌታ ወደ ደብረ ሲና እያቀና ሲያይ አይታ እመቤታችን ልጄ ወደዚያ ምን ታያለህ አለችው ። ኤልሳቤጥ እኅትኪ አዕረፈት አላት ፤ ደመና አድርጊቸዋል ስምዖንና ዘካርያስ በአካለ ነፍስ መጥተው ቀብረዋት ሄደዋል ። እመቤታችን እንዲህ ከሆነ ይዘነው እንሂድ አለችው ። ሰማያዊ አባቱ ያዘዘለት ቦታው ይህ ነው አይሆንም አላት ያን ጊዜ ዐሥራ አንድ ዓመት ሁኖት ነበር ቢሉ ዓሥራ ዘጠኝ ዓመት ኑሮ ይገናኛሉ።ያን ጊዜ ዘጠኝ ዓመት ሁኖች ነበር ያሉ እንደሆነ ሃያ አንድ ዓመት ኑረው ይገናኛሉ። ያላንድ ቀን አይቶት ባያውቅ። አንድም እኔ የማላውቀው ሁኖ አይደለም ፤
ዳዕሙ ከመ ያእምርዎ እሥራኤል በእንተዝ መጻእኩ እነ ከመ አጥምቅ በማይ ።
እስራኤል ያውቁት ዘንድ ስለዚህ በውኃ ላጠምቅ መጣሁ ማለት ላስተምር ታዝዤአለሁ እንጂ ።

፴፪ ወነገረ ስምዖ ዮሐንስ ። ማቴ፡፫፡፲፮ ማር፡ ፩፡፲ ሉቃ ፫ ፡ ፳፪ ።

፴፪ አብ ለወልድ የመሰከረውን ። አንድም ለወልድ የተመሰከረውን ። አንድም ዮሐንስ ምስ ክርነቱን ተናገረ ።
ወይቤ ርኢኩ መንፈሰ ቅዱሰ እንዘ ይወርድ እም ሰማይ ከመ እንተ ርግብ ወይነብር ዲቤሁ ርኢኩን ቢያዩ መንፈሰ ቅዱሰ ይወርድን ቢያዩ መንፈስ ቅዱስ በርግብ አምሳል ወርዶ ሲቀመጥበት አየሁ ብሎ መሰከረ ።

፴፫ ወአንሰ ኢየአምሮ ።
፴፫ እኔ ግን አላውቀውም ።
ወባሕቱ ዘፈነወኒ ከመ አጥምቅ በማይ ውእቱ ይቤለኒ ዲበ ዘርኢከ ይወርድ መንፈስ ቅዱስ ወይነብር ዲቤሁ ውእቱኬ ዘያጠምቅ በመን ፈስ ቅዱስ ።
ማየት በፊት መንገር ወደ ኋላ ነው ብሎ መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ በራሱ ላይ ሲቀ መጥበት ባየኸው ማየት ላይ ። አንድም ዲቤሁ ዘርኢከ ። ያየኸው እርሱ በመንፈስ ቅዱስ የሚያ ጠምቅ እርሱ ነው አለኝ እንጂ ። አንድም መንገር በፊት ማየት ወደኋላ ነው ብሎ ። ዲበ ዘትሬኢ ፤ መንፈስ ቅዱስ በአምሳለ ርግብ ወርዶ ሲቀመጥ በት በምታየው ማየት ላይ ። አንድም ዲቤሁ ዘት ሬኢ የምታየው እርሱ በመንፈስ ቅዱስ የሚያ ጠምቅ እርሱ ነው አለኝ እንጂ ።

፴፬ ወሰልየ ርኢኩ ወአነ ሰማዕቱ ።
፴፬ እኔ አየሁ መሰከርኩ ።
ከመ ዝንቱ ውእቱ ወልዱ ለእግዚአብሔር ።
ይህ የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ ።

በእንተ ቀዳማውያን አርድእተ ኢየሱስ ።

፴፭ ወበሳኒታ ካዕበ እንዘ ይቀውም ዮሐንስ ወክልኤቱ እምአርዳኢሁ ።

፴፭ ተራ ሳኒታ ። አንድም የሳኒታ ሳኒታ ። አንድም የሄደባትን ለተመለሰበት ሳኒታ አለው በነጋውም ዮሐንስ ከሁለቱ ደቀ መዛሙርት ጋራ ቁሞ ሳለ ። ሐተታ ዮሐንስና እንድርያስ ናቸው ።

፴፮ ርእዮ ለኢየሱስ እንዘ የሐውር ።
፴፮ ጌታን ሲሄድ አይቶት ።
ወይቤ ነዋ በግዑ ለእግዚአብሔር ዘያአትት ወያ ሴስል ኃጢአተ ዓለም ።
የእግዚአብሔር በግዑ ማለት የዓለምን ኃጢአት የሚያስተሰርይ የእግዚአብሔር መሥዋዕቱ እነሆ አላቸው ።

፴፯ ወሰምዕዎ ክልኤሆሙ አርዳኢሁ እንዘ ይብል ከመዝ ።

፴፯ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱም እንዲህ ሲል ሰምተው ።

ወተለውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ከዳረገኸንማ ብለው ጌታን ኢየሱስን ተከተሉት ።
፴፰ ወተመይጦ እግዚእ ኢየሱስ ርእዮሙ እንዘ ይተልውዎ ፪ሆሙ አርዳኢሁ ለዮሐንስ ።

፴፰ ጌታም ሁለቱ የዮሐንስ ተማሪዎች ሲከ ተሉት ተመልሶ አያቸው ።
ወይቤሎሙ ምንተ ተኀሥሡ ምን ትሻላችሁ አላ

ቸው ሰው ሲከተል ዝም ማለት አይገባምና ።
ወይቤልዎ ረቢ ዘበትርጓሜሁ ሊቅ ብሂል ፡
ትርጓሜው መምህር ሆይ ማለት ነው ።
አይቴ ተኃድር ።
ወዴት ታድራለህ አሉት ። ደግን ሰው ከመንገድ አቁሞ ማነጋገር ፈሊጥ አይደለምና ።

፴፱ ወይቤሎሙ ንዑ ትርአዩ ኀበ እኀድር።
፴፱ ታዩ ዘንድ ኑ አላቸው ። ወይቤሎሙ ንዑ ትርአዩ ፡ መጥታችሁ እዩ አላቸው ።
ወሖሩ ወርእዩ ኀበ የኃድር ።
ሂደውም የሚያድርበትን አዩ ወወዓሉ ኀቤሁ ይእተ ዕለተ እስከ ዓሥሩ ሰዓት ።
በዚያን ቀን እስከ ዐሥር ሰዓት ከእርሱ ዘንድ ዋሉ አለ ሲማሩ ። ምነው በሚያመጣው አኮኑ ዐሠርቱ ወክልኤቱ ሰዓቱ ለዕለት ይል የለምን ቢሉ አንዱ የሄዱበት አንዱ የተመለሱበት ነው ። አንድም ሁለት ሰዓት አሳልፈው ሄደው ሲመሽ ተመልሰዋል ። እንድም ማለዳ ሄደው ሁለት ሰዓት ሲቀር ተመልሰዋል ። አንድም አይቴ ተኃድር ብለህ መልስ ፡ እንደምን ባለ ሰውነት ታድራለህ አሉት ንዑ ትርአዩ እስራኤል ዘነፍስ ትባሉ ዘንድ እመኑ አላቸው ወሖሩ ወርእዩ፡እስራኤል ዘነፍስ ተባሉ ወወአሉ ኀቤሁ እስከ ዓሥሩ ሰዓት ። እስከ ዐሥሩ ማዕርጋት ደረሱ

፵ ወእሐዱ ውእቱ እንድርያስ እኁሁ ለስምዖን ጴጥሮስ እምክልኤቱ እለ ሰምዑ በኀበ ዮሐንስ ወተለውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፵ ዮሐንስ ነዋ በግዑ ሲል ሰምተው ጌታን ከተከተሉት ከሁለቱ አንዱ የስምዖን ጴጥርስ ወንድም እንድርያስ ነው ፡ የርሱን ሳይናገር ቀረ ስለ ትሕትና ። ይህስ እንዳይሆን የርሱንም ረድዕ ዘያፈቅሮ ብሎ በኋላ ያመጣዋል ብሎ እርሱ ከዚህ ነገር የለውም ። እንድርያስን ግን ጴጥሮስን ሳበ የሚለው ነውና ።

፵፩ ወሰሲሁ አቅደመ ረከበ እኁዋሁ ለስምዖንሃ ።

፵፩ እርሱ አስቀድሞ ወንድሙን ስምዖንን አገኘ ።
ወይቤሎ ረከብናሁ ለመሲሕ ዘይብልዎ ክርስቶስ።
ክርስቶስ የተባለ መሲሕን አገኘነው ። ማስያስ በዕብራይስጥ ክርስቶስ በጽርእ ። መሲሕ በዓረብ ቅቡዕ በግእዝ ።

፵፪ ወውእቱ ወሰዶ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ።
፵፪ እርሱም ወደጌታችን ወደ ኢየሱስ ክርስቶስ ይዞት ሄደ ።
ወሶበ ርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ለስምዖን ይቤሎ አንተኑ ስምዖን ወልደ ዮና ።
ጌታም ባየው ጊዜ የዮና ልጅ ስምዖን አንተ ነህ አለው ። አባቱን ካወቀ አከብሮ ያኖረኛል ብሎ እንዲከተለው ። አንድም ወልደ ዮሐንስ ዘዮና ይላል። የዮሐንስ ልጅ የዮና ልጅ ስምዖን አንተ ነህ አለው ። አንተሰኬ ትሰመይ ኬፋ የሚለው ነውና አባቱን እያቱን ማወቁ የባሕርይ አምላክ እንጂ ቢሆን ነው ብሎ ነገሩን እንዲቀበለው ።
አንተኬ ትሰመይ ኬፋ ።
አንተስ መሠረት ትባላለህ ዘበትርጓሜሁ ጴጥሮስ በትርጓሜው ጴጥሮስ ማለት ነው ። ኬፋ በዕብራይስጥ ጴጥሮስ በጽርእ ። ኵኵሕ በዓረብ ። በግእዝ እብን ኵኵሕና እብንስ አንድ ወገን ነው ብሎ በዓረብ እልሐጅር ይላል ።

፵፫ ወበሳኒታ ፈቀደ ይሑር ገሊላ ።
፵፫ የሳኒታ ሳኒታ ተራ ሳኒታ ። አንድም አርድእተ ዮሐንስ ለመጡበት ሳኒታ አለ ። በነጋውም ወደ ገሊላ ሊሄድ ወደደ ።
ወረከቦ እግዚእ ኢየሱስ ለፊልጶስ ።
ጌታ ፊልጶስን አገኘው ።
ወይቤሎ ትልወኒ ።
ተከተለኝ አለው ። ለጊዜው በእግር ፍጻሜው በግብር ምሰለኝ አለው ።

፵፬ ወውእቱ ፊልጶስ ዘቤተ ሳይዳ ዘገሊላ እምሀገረ እንድርያስ ወጴጥሮስ ።

፵፬ ይህ ፊልጶስም የእንድርያስና የጴጥሮስ አገር የምትሆን የቤተ ሳይዳ ሰው ነው ። እኒያ ሲያምኑ አይቶ አመነ ለማሰት ።

፵፭ ወረከቦ ፊልጶስ ለናትናኤል ዘፍ፡፵፱፡ ፲ ዘዳ፡ ፲፰፡፲፰ ኢሳ፡ ፵፡፲ ። ኤር ፳፫፡፭ ሕዝ፡ ፴፬፡፳፫ ዳን፡ ፱፡፳፬

፵፭ ፊልጶስም ናትናኤልን አገኘው መሳሳብ ሆነ ።
ወይቤሎ ረከብናሁ ለኢየሱስ ወልደ ዮሴፍ እምናዝሬት ዘጸሐፈ ሙሴ ውስተ ኦሪት ወነቢያት ተነበዩ በእንቲአሁ ። ሙሴ በኦሪት የጻፈለትን ። ነቢያትም ትንቢት የተናገሩለትን የዮሴፍን ልጅ የናዝሬቱን ኢየሱስን አገኘነው አለ ። ያላዋቂ ወታደር አነጋገር እንድም ዐውቋል ብሎ አይሁድ የዮሴፍ ልጅ የሚሉትን የናዝሬቱን ኢየሱስን ሙሴ በኦሪት የጻፈለት ነቢያትም ትንቢት የተናገሩለት ሁኖ አገኘነው ።

፵፮ ወይቤሎ ናትናኤል ቦኑ ይትከሃል እምናዝሬት ከመ ይፃ እኄር ብእሲ ።

፵፮ ናትናኤልም በውኑ ከናዝሬት ደግ ሰው ይገኝ ዘንድ ይቻላልን አለው ፡ እንደ ጭልጋ የወንበዴ የቀጥቃጭ አገር ናትና ። ዘቦቱ ሠናይት ይላል ። ሀብትኬ ሠናይ መንፈስ ቅዱስ እንዲል ። ልጅነትን ለራሱ ገንዘብ አድርጎ ለሌላው የሚያድል ደግ ሰው ይገኝ ዘንድ ይቻላልን
ወይቤሎ ፊልጶስ ነዓ ትርአይ ፡
ተከራክሮ ማስረዳት ባይቻለው መሆኑንም አለመ ሆኑንም መጥተህ እይና ተረዳ አለው ።

፵፯ ወሰበ ርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ለናትናኤል እንዘ ይመጽእ ኀቤሁ ።

፵፯ ኢየሱስም ናትናኤልን ወደርሱ ሲመጣ አየው ።
ወይቤ በእንቲአሁ ነዋ ዘበአማን እስራኤላዊ ዘአልቦ ጽልሑት ውስተ ልቡ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ወደርሱ ሲመጣ ናትናኤልን ባየው ጊዜ በውነት ክዳት ተንኮል የሌለበት እስራኤላዊ እነሆ ብሎ ስለርሱ ተናገረ ። እስራኤል ማለት ሕሊና ዘይሬእዮ ለእግዚአብሔር ፡ ነጸሪ ከሃሊ ምስለ አምላኩ ፡ ሕዝበ እግዚአብሔር ማለት ነው ።
ወይቤሎ ናትናኤል በአይቴ ተአምረኒ ።
ናትናኤልም ወዴት ታውቀኛለህ አለው ።

፵፰ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ እም ቅድመ ይጸውዕከ ፊልጶስ ርኢኩከ በታሕተ ዕፀ በለስ

፵፰ ጌታም ፊልጶስ ሳይጠራህ ከበለስ በታች ሳለህ አየሁህ አለው በቅትለተ ሕፃናት ጊዜ እናቱ በቀፎ አድርጋ ከበለስ ሥር ሰውራው ነበርና ። ያን ጊዜ ያዳንኩህ እኔ ነኝ ሲል ፡ አንድም ሰው ገድሎ አስቀብሮ ነበርና የጎልማሳ ሚስት ቀምቶ የማይገባ ሥራ ሲሠራ ነበርና ዐውቅብሃለሁ ሲለው ነው። አንድም ባለጸጋ ነው ከዚያ ሁኖ ወይፋፍን ሲያ ስፈትን ፈረስ በቅሎ ሲያስገራ ይውል ነበርና ። አንድም ምሁረ ኦሪት ነው ከዚያ ሁኖ የተነገረው ትንቢት ደረሰ የተቈጠረው ሱባኤ ቀረ እያለ ሲያ ወጣ ሲያወርድ ይውል ነበርና ዐውቅልሃለሁ ሲለው ነው አንድም የበለስ ቅጠሉ ሰፊ እንደሆነ ኃጢአት ሰፍናብህ አየሁህ ሲለው ነው ።

፵፱ ወአውሥአ ናትናኤል ።
፵፱ ናትናኤልም መለሰ ።

ወይቤሎ ረቢ አማን አንተ ውእቱ ወልደ እግዚአ ብሔር ። መምህር ሆይ በውነት አንተ የእግዚአብ ሔር ልጅ ነህ ።
ወንጉሥ እስራኤል አንተ ።
የእስራኤልም ንጉሣቸው አንተ ነህ አለው ።
፶ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፶ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎ እስመ እቤለከሁ ርኢኩከ በታሕተ ዕፀ በለስ ተአምን ከዕፀ በለስ ሥር አየሁህ ብልህ አመ ንክ ። አንድም ሶበ እቤለከሁ ። ከበለስ ሥር አየሁህ ብየ ብልህ አመንክ ።

እምይእዜሰ ዘየዓቢ እምዝ ትሬኢ ።
ከአንግዲህስ ወዲህ ከዚያ የበለጠ ታያለህ አለው ። ሦስት ዓመት ከሦስት ወር የሚደረገውን ተአምራት። አንድም ዕውቀቱ ከሌዋውያን ካህናት ጌትነቱ ከም ድራውያን ነገሥታት እንዲበልጥ ለማጠየቅ፡ ትሬ እዩ እንዘ ይትረኃዋ ሰማያት የሚል ነውና

፶፩ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ እምይእዜሰ ትሬእዩ እንዘ ይትረኃዋ ሰማያት ።

፶፩ ሰማያት ሲከፈቱ ።
ወመላእክት እግዚአብሔር እንዘ የዓርጉ ወይወርዱ ኀበ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
የእግዚአብሔር መልክተኞችም ወደ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ሲወጡ ሲወርዱ ታያላችሁ ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ። በሰማይስ መከፈት መዘጋት የለበትም ደጅ በተከፈተ ጊዜ የውስጡ እንዲታይ ያልተገለጠ ምሥጢር ሲገለጥ ተርኅወ ይላል እንጂ እርሱ ሰው ከመሆኑ አስቀድሞ መላ እክት ሰው የጸለየውን ጸሎት የሠዋውን መሥዋ ዕት ለማሳረግ አይወጡም አይወርዱም ነበር ። እርሱ ሰው ከሆነ ወዲህ ግን የሚወጡ የሚወርዱ ሁነዋልና ። አንድም አምላክ ሰው ሆነ ሰው አምላክ ሆነ እያሉ ርደቱን ዕርገቱን ለመንገር ።

ዘከመ ተገብረ ከብካብ በቃና ዘገሊላ ።

ምዕራፍ ፪ ።

፩ ወአመ ሣልስት ዕለት ከብካብ ኮነ በቃና ዘገሊላ ።

፩ ወእመ ሳኒታ እንዘ ይቀውም ዮሐንስ ያለው እሑድ ። ወበሳኒታ ፈቀደ ይሑር ገሊላ ሰኞ ወአመ ሣልስት ማክሰኞ ። አንድም ከታች ውረድ ወአመ ሳኒታ ርእዮ ዮሐንስ ፡ እሑድ ጌታ ማክሰኞ ተጠ ምቆ ዕለቱን ሂደ አርባው ቅዳሜ ይፈጸማል ። እሑድ ገብቶ ያድራል አርባውን ቀን እንዳንድ ቀን አድርጎ እሑድን ሳርባው ቀን ሳኒታ አለው ። በማ ቴዎስ ሃያ ኦምስቱን ዘመን እንዳንድ አድርጎ ወበ ውእቱ መዋዕል እንዳለ ። ወአመ ሳኒታ እንዘ ይቀ ውም ሰኞ ወአመ ሳኒታ ፈቀደ ያለውና ወአመ ሣል ስት ፡ ማክሰኞ ሣልስትነቱ ለእሑድ ሳኒታነቱ ለሰኞ ፡ የገሊላ ክፍል በምትሆን በቃና በሦስተኛው ቀን ምሳ ሰርግ ትደረገ ።
ወሀለወት ሀየ እሙ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
እመቤታችን ከሰርግ ቤት ነበረች ። ቤተ ዘመድ ናትና ። አንድም ደግ ናትና ተጠርታ ።

፪ ወጸውዖ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
፪ ጌታን ጠሩት እናት ጠርቶ ልጅን መተው ሥርዓት አይደለምና ።

ወለአርዳኢሁኒ ውስተ ከብካብ ጸውዖሞ ያለበት ነው ደቀ መዛሙርቱንም ሰርግ ጠሯቸው መም ሀር ጠርቶ ደቀ መዛሙርቱን መተው ሥርዓት አይ ደለምና ።

፫ ወሶበ ኀልቀ ወይኖሙ ትቤሎ እሙ ለእግ ዚእ ኢየሱስ ወይንኬ አልቦሙ ።
፫ ጠጅ ባለቀባቸው ጊዜ እመቤታችን ጠጅ አልቆባቸዋል ኣኮን አለችው እርሱ የማያው ቀው ሁኖ አይደለም ፡ ዙሎ ዘይቤለከሙ ግበሩ ለማ ለት ነው እንጂ ።

፬ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ምንት ብየ ምስ ሌኪ ኦ ብእሲቶ ።

፬ ካንች ጋራ ምን አለኝ ማለት ወኀውን ጠጅ አድርግላቸው ብትዪኝ አይሆንም እልሽ ዘንድ ካንች ጋራ ምን ጸብ አለኝ እንድም ውኀውን ጠጅ አድር ግላቸው ብትዪኝ አይሆንም እልሽ ዘንድ ውኀውን ጠጅ ላላደርግላቸው ከሰርግ ቤት ተጠርቼ መጥቻ ለሁን ውኀውን ጠጅ ላላደርግላቸው ነውን አላት ። እንድም በአምላክነቱ አገብሮ ተአዝዞ እንደሌለ በት ለማጠየቅ ። እንድም ውኀውን ጠጅ አድርጌ የማጠጣቸው በኔ ፈቃድ ነው እንጂ ባንቺ ትእዛዝ ነውን አላት ።
ዓዲ ኢበጽሐ ጊዜየ ፡
ነገር ግን ጊዜዬ አልደረሰም ጊዜ ግቢር ለእግዚአብ ሔር እንዲል ። ሥራውን የሚሠራበት ጊዜ አለውና በቀትር የሚሠራውን በሠለስት አይሠራውምና በሠ ለስት የሚሠራውን በነግህ አይሠራውምና ። እን ድም ጠጁ ፈጽሞ አላለቀም ነበር ያለውንም አበ ርክቶት ቢሆን ያኑ አበረከተው ተብሎ ተአምራቱ ድንቅ ባልተባለም ነበርና ። እንድም ይሁዳ ወጥቶ ነበርና ከተአምራቱ እንጂ ቢለየኝ ከሞቱ ገባሁበት እንዳይል ።

፭ ወትቤሎሙ እሙ ለእግዚእ ኢየሱስ ለእለ ይትለአኩ ዙሎ ዘይቤለከሙ ግበሩ ።

፭ እመቤታችን የሚሠሩትን ያዘዛችሁን ሁሉ ሥሩ አለቻቸው ።

፮ ወሀለዋ ህየ መሳብክት ስድስቱ እለ እብን በዘያጥኀሩ ቦቶን አይሁድ ንቡራት ህየ ።

፮ ሀለዋና ንቡራት አንድ ወገን ። አይሁድ በሚያጠምቁባቸው ገንዘብ ያጠምቁባቸው ዘንድ የሚያጠምቁባቸው ስድስት የደንጊያ ጋኖች ከዚያ ነበሩ እንደምን አድርገው ይሠሩታል ቢሉ ያነ ጥጡታል ፡ ይሀስ ሲነሣ ጭቃ እየሆነ ያውካል ብሎ እብነ አልማስ የሚባል አለ ። ደንጊያውን ሁሉ እየሰበሰቡ ያቀረቡለት እንደ ሆነ ያቀልጠዋል እያ ስማሙ ይሠሩታል ።
ወያገምራ ለለ፩ በበ፪ቱ ወበበ፫ቱ መሥፈርተ ዘቀ ሙት ሁለት ሁለት ሦስት ሦስት ማድጋ ይይዛሉ ሦስቱ ሁለት ሁለት ሦስቱ ሦስት ሦስት ዓሥራ አምስት ይሆናል ።
አንድም ስድስቱ በታናናሽ ሦስት ሦስት ይይዛሉ ዐሥራስምንት ይሆናል ። አንድም ስድስቱ በታላ ላቅ ሁለት ሁለትይይዛሉ። ዐሥራ ሁለት ይሆናል ።

፯ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለእለ ይት ለአኩ ምልእዎንኬ ለእላ መሳብክት ማየ ።

፯ ጌታችን ኢየሱስ እኒህን ጋኖች ውኀ ሙሏ ቸው አለ ።
ጠመልእዎን እስከ ላዕሉን ።
ኣስከ ጉረሮዋቸው ።
ወእስከ አፉሆን ።
እስከ ከንፈራቸውም መሏቸው ። አንድም እስከ አፉሆን እስከ ከንፈራቸው ። ወእስከ ላእሉን ፡ እንደ ማር እንደ ቅቤ ቀለል እስኪል ።

፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ቅድኀዎንኬ ይእዜ ወስዱ ወሀብዎ ለሊቀ ምርፋቅ ።

፰ ቀድታችሁ ወስዳችሁ ላሳዳሪው ስጡት አላቸው ። ተአምራትስ ያደርጋል ነገር ግን አስተዳ ደር አያውቅም እንዳይሉት ። እንድም ሁሉ ጠጥቶ ስከሯል ጣዕም አያውቅም እርሱ ግን አልጠጣምና ጣዕም ያውቃል ብሎ ወወሰዱ ወወሀብዎ ።
ቀድተው ወስደው ሰጡት ።

፱ ወጥዒሞ አንከረ ሊቀ ምርፋቅ ውእተ ማየ ዘኮነ ወይነ ።

፱ የምርፋቁ አለቃ ጠጅ የሆነውን ውኀ ቀምሶ አደነቀ ።

ወኢያአመረ እምኀበ አምጽእዎ ።
ካመጡበት ግን አላወቀም ።
ወገዛዕትስ እለ ቀድኀዎ የአምሩ ውእተ ማየ ዘኮነ ወይነ ሠራተኞች ግን ጠጅ የሆነውን ውኀ ያውቃሉ እስመ እሙንቱ መልዑ ማየ ምሉ ብሏቸው መልተ ዋልና ወጸውዖ ሊቀ ምርፋቅ ለመርዓዊ ።
የምርፋቁ አለቃ ሙሽራውን ዶኪማስ ብሎ ጠራው።

፲ ወይቤሎ ዙሉ ሰብእ ዘይሤኒ ወይነ ያቀድም አስትዮ ።

፲ ሰው ሁሉ ሸሎውን በርዳዳውን አስቀድሞ ያጠጣል ።
ወእምድኀረ ሰከሩ ያሰቲ ዘይቴሐት ።
ከጠገቡ በኋላ ግን ተራውን ያጠጣል ። ቢጠጡ

ይጠጡት ባይጠጡ ቀምሰው ለብላቴኖቻቸው ይስ ጡዋቸው ብሎ ።

ወአንተሰ ዘይሴኒ ወይነ ዓቀብከ እስከ ይእዜ ። አንተ ግን ሽሎውን በርዳዳውን እስካሁን አቆ የሀ ። አንድም ዓቀብከ ወአስተደኃርከ ይላል ፈጽ መህ አቆየህ ።

፲፩ ወዝንቱ ውእቱ ቀዳሚ ተአምር ዘገብረ እግዚእ ኢየሱስ በቃና ዘገሊላ ።

፲፩ የገሊላ ክፍል በምትሆን በቃና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያደረገው የተአምራቱ መጀመሪያ ይህ ነው ። ሦስት ዓመት ከሚያደርገው አንድም ደገኛ ተአምራቱ ይህ ነው ቀዳሚሆሙ ለአሕዛብ አማሌቅ ቀዳሚ ተግባሩ ለእግዚአብሔር ብሂሞት እንዲል ። ሙሴ ውኃውን በሐልዮ ደም እንዳደ ረገው ። በሐልዮ ነውና ውሀውን ጠጅ ያደረገው ። ሙሴኒ ሚጦ ለማይ እምከዊነ ማይ ኀበ ከዊነ ደም እንዘ ኢይትናገር በአፉሁ ዳዕሙ በሕሊናሁ እንዲል። ወእርአየ ስብሐቲሁ ። ተአምራቱን አሳየ ። አንድም ጌትነቱን ገለጠ ። ወአምኑ ቦቱ አርዳኢሁ ። ደቀ መዛሙርቱ አመኑበት ። ሊጸፍ ባይቻል ነው እንጂ ጠይቀውታል ጠይቀዋቸዋል እርሱን ። ጠየቁት አላውቅም አለ እርሳቸውን ጠየቋቸው ውኀምሉ አለን መላን ቀድታችሁ ስጡ አለን ቀድተን ሰጠን እኛ ምን እናውቃለን ብለዋል ። አንድም ወኢመ ጫልስት ዕለት ብለህ መልስ ። በሦስተኛው ክፍለ ዘመን ሥጋዌ ተደረገ ወሀለወት እሙ ጥበቡ ከሥጋዌ አስቀድሞ ነበረች ወጸውዕዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወለአርዳኢሁ ነቢያት ጌታችንን ሐዋርያትን በትንቢት ጠሯቸው አነሷቸው ። ወሶበ ኃልቀ ወይ ኖሙ ትቤሎ እሙ ስቴ ሕይወት ስቴ መድኃኒት ባለ ቀባቸው ጊዜ ጥበቡ ስቴ ሕይወት ስቴ መድኃኒት አልቆባቸዋልና ተሰቅዬ ስቴ ሕይወት ስቴ መድኃ ኒት ልሁናቸው አሰኘችው ወይቤላ ምንት ብየ ። አንች ሆይ ተሰቅለህ ስቴ ሕያወት ስቴ መድኃኒት ሁናቸው ብትዪኝ አይሆንም እልሽ ዘንድ ተሰቅዬ ስቴ ሕይወት ስቴ መድኃኒት ልሆናቸው ሰው ሁኛ ለሁ እንጂ ተሰቅዬ ስቴ ሕይወት ሰቴ መድኃኒት ላልሆናቸው ሰው ሆኛለሁ አላት ።

ዓዲ ኢበጽሐ ጊዜየ ። ነገር ግን የምሰቀልበት ጊዜ አልደረሰም ። ጌታ የሚሰቀል ባራተኛው ፋሲካ ነውና ። ወትቤሎሙ እሙ ። ጥበቡ መምህራን ያዘዟችሁን ሁሉ ሥሩ አለቻቸው ወሀለዋ መሳብክት ስድስቱ ። በስድስተኛው ሽህ የነበረ ሰው ሁሉ አእ ምሮው እንደ ደንጊያ መፍዘዙን መናገር ነው ። ወያገምራ በበክልኤቱ ወበበሠለስቱ ። አንብብ መጻ ሕፍተ በበክልኤቱ ወበበሠለስቱ እንዲል ፡ በበክል ኤቱ መጻሕፍተ ነቢያትን ወበበሠለስቱ መጻሕፍተ ሐዲሳትን መቀበላቸውን መናገር ነው ። ዐሥራ አምስት ባለው ዓሥርቱ ቃላትን አምስቱ አዕማደ ምሥጢርን መቀበላቸውን መናገር ነው ዐሥራ ስምንት ባለው ያሥራሁለቱን ሐዋርያት ትምህርት ስድስቱን ቃላት ። ዐሥራ ሁለት ባለው ያሥራሁለ ቱን ሐዋርያት ትምህርት መቀበላቸውን መናገር ነው ወይቤሎሙ ምልእዎን ፡ አስተምሯቸው አላቸው ። ወመልእዎን ፡ ፍጹም ትምህርት አስተማሯቸው። ወይቤሎሙ ቅድኅዎን ፡ምሳሌውን ለአብርሃም ንገ ሩት አላቸው ። ወወሰዱ ወወሀብዎ ፡ ነገሩት ። ወጥዒሞ አንከረ ። ምሳሌውን ሰምቶ አደነቀ ወኢ ያእመረ እምኀበ እምጽእዎ ። ከመጡበት ግን አላ ወቀም ። ወገዛእትሰ እለ ቀድኅዎ መምህራን ግን ያውቃሉ ። እስመ እሙንቱ መልኡ ገልጠላ ቸው አስተምረዋልና ። ወጸውዖ ሊቀ ምርፋቅ ። አብርሃም ጌታን ሰው ሁሉ ደገኛውን ሕግ አስቀድሞ ይሠራል ። ወእምድኅረ ሰክሩ ያን ከጠበቁ በኋላ ግን ተራውን ሕግ ይሠራል ቢጠበቁ ይጠብቁት ባይጠብቁ አያስጐዳም ብሎ ፡ ወአንተሰ ዘይሜኒ ወይነ ዓቀብከ ፡ አንተ ግን ደገኛውን ሕግ እስካሁን አቆየህ አንድም ፈጽመህ አቆየህ ። ወዝንቱ ቀዳሚ ተአምር ይህ አያለወጥም ።

ዘከመ ዐርገ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ።

፲፪ ወእምድኅረ ዝንቱ ወረደ ቅፍርናሆም ውእቱ ወእሙ ወአኃዊሁ ወአርዳኢሁኒ ምስሌሁ ።

፲፪ ከዚህ በኋላ እርሱ እናቱም ደቀመዛሙ ርቱም ወደ ቅፍርናሆም ወረዱ ።
ወነበሩ ህየ ኅዳጠ መዋዕለ ።
ከዚያም ጥቂት ቀን ኖሩ ። ወአኮ ብዙኃ ። ብዙም አይደለም የቁጥር መጽሐፍ ዐሥራ አንድ ቀን ይለዋል

፲፫ ወቀርበ በዓለ ፋሲካሆሙ ለአይሁድ ።

፲፫ አይሁድ ፋሲካን የሚያከብሩበት ቀን ደረሰ መጀመሪያ ፋሲካ ነው ፡ ጌታ የሚሰቀል ባራተኛው ፋሲካ ነውና ዮሐንስ ፋሲካውን ጠንቅቆ ይቈጥራል
ወዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ።
ጌታ ወደ ኢየሩሳሌም ወጣ ።
ዘከመ ተሰዱ ሠየጥ እምኵራብ

፲፬ ወረከበ በምኵራብ እለ ይሠይጡ ወይሣየጡ አልሕምተ ወአባግዐ ወአርጋበ ወመወልጣነ እንዘ ይነብሩ ።

፲፬ በመቅደስ ላም በግ ርግብ የሚሸጡትን ተቀምጠው ማስት ገበያ አድርገው አገኘ ።

፲፭ ወገብረ መቅሠፍተ ጥብጣቤ ዘሐብል ።

፲፭ ዘሐዊን እለና ዘሐብል አለ ማሰሪያ አበጀ እርሱ እላበጀም ሐዋርያት አብጅተው

ሰዋተውታል የጭፍራውንም ላሊቃው ሰጥቶ መናገር ልማድ ነው ።

ወከመዝ ገብረ ሙሴ በዘሚር ወበአከሲኖዶስ እን ዲል ።
ወሰደደ ኵሎ እምኵራብ አባግዕኒ ወአልሕምተኒ ። ላሙን በጉን ሁሉ ከምኩራብ አሰወጣ ማለት ገበ ያውን ፈታ ወዘረወ ወርቆሙ ለመወልጣን የሰዋ ሙችን ገንዘባቸውን በተነባቸው ። የሰው ገን ዘብ አታበላሹ ይል የለም ቢሉ ለሰውነታቸው ቤዛ ሁኑዋቸዋል ። ማዕስ ቤዛ ማዕስ እንዲል ። አንድም በተአምራት ገንዘብ ገንዘባቸውን ለይቶ ይሰጣቸዋል አንድም ከዛፍ ላይ እንደ ሰፈረ ንብ ከዕቃ ከዕቃቸው ላይ እየተጣበቀ ተገኝቷል ።

ወገፍትዓ ማዕዳቲሆሙ ።
ድርድራቸውን ሰፈራቸውን አፈረሰ ።
ወመናብርቲሆሙ ለእለ ይሠይጡ ርግበ ገንጸለ ። ርግብ የሚሸጡትንም ፣ ወንበራቸውን ገለበጠባቸው ቋንጤ ወንበር አላቸው ከዚያ ሁነው ርግብ ይሸጣሉ የከተማ ቅሬ በወን በር ሁና ዶሮ እንድትሸጥ

፲፮ ወይቤሎሙ ለእለ ይሰይጡ ርግበ አሰስሉ ወአውፅኡ ዘንተ እምዝየ ።

፲፮ አንሡ አላቸው ርግቦች በትር አይችሉ ምና ።
ወኢትረስዩ ቤተ አቡየ ቤተ ምሥያጥ ።
ባባቴ ቤት ገበያ አታድርጉ ።

፲፯ ወተዘከሩ ፣ርዳኢሁ ከመ ጽሑፍ ውእቱ ዘይብል ቅንዓተ ቤትከ በልዓኒ ። መዝ. ፷፰ ፣ ፲ ።

፲፯ ደቀ መዛሙርቱም የቤትህ ቅናት አቃ ጠለኝ የሚል ጽሑፍ እንዳለ አሰቡ ።

፲፰ ወአውሥእዎ አይሁድ ።
፲፰ አይሁድም መለሱ ።
ወይቤልዎ ምንተ ትእምርተ ታርኢ ዘዘንተ ትገ ብር ።
ይህን የምትሠራ ምን ምልክት ታሳያለህ ማለት ከምድራውያን ነገሥታት ከሌዋውያን ካህናት ወገን ያይደለህ ገበያ መፍታትን ማን አሰናብቶህ ነው አሉት ።

፲፱ ወአሥውአ እግዚእ ኢየሱስ
፲፱ ጌታም መለሰ ። ወይቤሎሙ
ንሥትዎ ለዝንቱ ቤተ መቅደስ ። ማቴ. ፳፮ ፣ ፷፩ ። ማር ፣ ፲፬ ፣ ፶፰ ።
ይህን ቤተ መቅደስ አፍርሱት ፡
ወበሣልስት ዕለት አነሥእ ።

በሦስተኛው ቀን እንጸዋለሁ ።

፳ ወይቤልዎ አይሁድ በ፵ ወ፮ ዓመት ተሐ ንጸ ዝንቱ ቤተ መቅደስ ።

፳ ይህ ቤተ መቅደስ በአርባ ስድት ዓመት ተሠርቶ ነበር ።

ወአንተሰ በሠሉስ መዋዕል ታነሥእ ።
አንተስ በጐ በሦስተኛው ቀን አንጸዋለሁ አልክ ምን ይዘው እንዲህ አሉ ቢሉ ትሩፋን በባቢሎን ሳሉ ይህ ሁሉ መከራ ባባቶቻችን የተ ደረገባቸው ቤተ መቅደስን ባያሠሩ እንጂ ነው ። እኛ ሚጡቱ ለተደረገልን እንደሆነ ቤት ሳንሠራ ዘር ሳንዘራ ቤተ መቅደስን እንሠራለን ብለው ብፅ ዓት ገቡ ። ኋላ ሚጡቱ ተደረገላቸው ። ዘር ሲዘሩ ቤት ሲሠሩ ሁለት ዓመት ኑረዋል በሦስተኛው ጀምረው ባርባ ስድስት ዓሙት ሠርተው ፈጽመዋል። ይህም በዘሩባቤል መንግሥት ይታወቃል የዘሩባ ቤል መላ ዘመነ መንግሥቱ አርባ ዘጠኝ ነው ። ሳይታነጽ ሁለት ዓመት ከታነጸ በኋላ አንድ ዓመት ኑሮ አርፏል ። አንድም ዘመን ያጠራጥራሉ መሥ ራት በጀመሩ በስድስተኛው ዓመት አጀም ኮንታ መጥተው አግቡን እናግራችሁ አሏቸው። አሪታቸው ኢይባእ ሞአባዊ ወአሞናዊ ትላለችና አይሆንም አሉአቸው ።ጽርእ ከአርጤክስስ ዘንድ ሂደው ነገር ሠሩባቸው ያች ሀገር አሳዊተ ነገሥት ናት ልታምጽ ግንብ ትሠራለች ብለው ፡ አትሥሩ ብሎ ዐዋጅ ነገረባቸው ተጀምሮ ቀረ። ዓቢይ አርጤክስስ ሙቶ ካልዕ አርጤክስስ ነገሠ፤ በእናቱ አይሁዳዊ ነው የአርጤክስስ ልጅ ነው ከቃቤት ገብቶ ታሪክ ሲመለከት የቤተ መቅደስን ሥርዓት ሞዓብ አሞን መገበራቸውን አገኘ ። ዛሬ እንደምን ሁነዋል ብሎ ጠየቀ መሥራት ጀምረው ነበር አዋጅ ተነግሮባ ቸው ተጀምሮ ቀርቷል አሉት። ይሥሩ ሞዓብ አሞ ንም እንደጥንቱ ይገብሩላቸው ብሎ ዐዋጅ ነገረ ላቸው ሠላሳ ዘመን ሠርተው ጨርሰዋል ። ዐሥሩ ተየት ይመጣል ቢሉ ሄሮድስ ወልደ ሐንደፌር በእናቱ አይሁዳዊ ባባቱ አረማዊ ነው ለገቢረ በዓል ወጥቶ ሳለ ሠላሳ ስድስት ዓሙት የሠሩትን አይቶ ባባቶቻችን ዘመን የተሠራው ደግ ነበር ይሉናል አላማረምሳ አላቸው አባቶቻችንማ ሞአብ አሞን እየገበሩላቸው በተድላ በደስታ ሁነው ነው የሠሩት እኛማ በግራ እጃችን ጋሻ ጦር በቀኝ እጃችን ጭቃ ደንጊያ እያቀበልን ነው የሠራነው አሉት ።

አፍርሼ ልሠራላችሁ አላቸው በእናቱ አይሁዳዊ ቢሆን ባባቱ አረማዊ ነው አፍርሶ ቢተውብንሳ ብለው ጠርጥረውት ዝም አሉ ። እሱም ዐውቆባቸው ጠርጥ ረውኝ እንጂ ነው ብሎ ስምንት ዓሙት አዘጋጅቶ

በሁለት ዓመት ሁለት ዓመት አዘጋጅቶ በስምንት ዓመት ሠርቶ ጨርሶታል ።

፳፩ ወውእቱሰ በእንተ ቤተ ሥጋሁ ይቤሎሙ
፳፩ ስለ ሥጋው መቅደስ ማለት እሱ ግን ማኅደር ስለሚባል ሰውነቱ እንዲህ አላቸው ።

፳፪ ወአመ ተንሥአ እምነ ምውታን ተዘከሩ አርዳኢሁ ከመ በእንተዝ ይቤ ። መዝ ፴፮ ፣

፳፪ ከሙታን ተለይቶም ከተነሣ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ እንዲህ ያላቸው ማኅደር ስለሚባለው ሰውነቱ እንደሆነ ዐወቁ ። ወሶበ ተንሥአ እምነ ምውታን ሶቤሃ ከሠተ ሎቱ አእመሩ ወለበውወኮኑ ከመ ሰብል እንዲል እንደ ተደመጠ ብራና ሁነዋል ወአምኑ በቃለ መጻሕፍት ።

በመጻሕፍት ቃል አመኑ ። ወተንሥአ እግዚአብሔር ከመ ዘንቃሕ እምንዋም ። ይትነሣእ እግዚአብሔር ወይዘረው ፀሩ ባለው ወበቃለ እግዚእ ኢየሱስ ዘይቤሎሙ ።

ጌታችን ኢየሱስ በተናገረውም ነገር ንሥትዎ ለዝንቱ ቤተ መቅደስ ባለው ። አንድም ወቀርበ በዓለ ፋሲካሆሙ ለአይሁድ ብለህ መልስ ። አይሁድ የተባሉ ። ምእመናን ናቸው ። ጌታ ከሕይወት ወደ ሞት የሚሄድበት ምእመናንም ወደ ሕይወት የሚሄዱበት ዘመን በደረሰ ጊዜ ዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ጌታ ተሰቀለ ፣ ኢየሩሳሌም ማለት ሀገረ ሰላም ማለት ነው ። ሀገረ ሰላምም የተባለ መስቀል ነው። ወረከበ በምኵራብ መሥዋዕተ ኦሪትን ሲሠውአገኝ ። ወመወልጣነ ። በኦሪት ሥርዓት የሚለውጡትን ። ወገብረ መቅሠፍተ ጥብጣቤ ሥልጣነ ክህነትን ገንዘብ አደረገ ። ወሰደደ ኵሎ መሥዋዕተ ኦሪትን አሳለፈ ። ወዘረወ ወርቆሙ በኦረት ሥርዓት ጸንተው ሥርዓት የሚለዋውጡትን ሕጋቸውን አሳለፋባቸው ። ወገፍትዓ ። ከልዕልናቸው አዋረዳቸው ከሹመታቸው ሻራቸው ።

ወይቤሎሙ ለእለ ይሰይጡ ርግበ መሥዋዕተ ኦሪት የሚሠውትን መሥዋዕተ ኦሪት አትሠው አላቸው ። ወኢትረስዩ ባባቴ ቤት መሥዋዕተ ኦሪት አትሠው ። ወተዘከሩ አርዳኢሁ ከመ ጽሑፍ በቤትህ የቀናሁት ቅናት እንደ እሳት አቃጠለኝ የሚል ጽሑፍ እንዳለ ደቀ መዛሙርቱ ዐወቁ ። ወአውሥእዎ አይሁድ ። አቡየ የምትል ምን ምልክት አለህ አሉት ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ይህንስ ብላችሁ ግደሉኝ አላቸው። እርሱስ አይዛቸውም እንዳይተውት ያውቃልና እንዲህ አለ እንጂ ። ወበሠሉስ ዕለት እነሥኦ በሦስተኛው ቀን አሥነሣዋለሁ እፈጽመዋለሁ ። በ፵ወ፮ ዓመት ተሐንጸ ፣ ሥጋዌ በአርባ ስድስቱ ብሉያት ተነግሮ ነበር ፣ ወአንተሰ አንተስ በ፫ ቀን አሥነሣዋለሁ እፈጽመዋለሁ አልከ ። ወውእቱሰ እርሱም ማኅደር ስለሚባል ሰውነቱ ነው እንዲህ ያላቸው ወአመ ተንሥአ እምነ ምውታን ተዘከሩ እንዲህ ያላቸው ማኅደር ስለሚባል ሰውነቱ እንደ ሆነ ከተነሣ በኋላ ዐወቁ ፣ ወአምኑ በቃለ መጻሕፍት ቅንዓተ ቤትከ በልዓኒ ባለው አመኑ ፣ ወበቃለ እግዚእ እየሱስ ፣ እንዲህ ሲል ያውካል አቡየ ያለ ውንም ብታደርገው ይሆናል ።

በእንተ ቀዳሚት ፋሲካ ዘኢየሱስ ።

፳፫ ወእንዘ ሀሎ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም በበዓለ ፋሲካ ብዙኃን አምኑ ቦቱ ሶበ ርእዩ ተአምረ ዘገብረ ።
፳፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ለበዓል ኢየሩሳሌም ወጥቶ ሳለ ያደረገውን ተአምራት ባዩ ጊዜ ብዙ ሰዎች አመኑበት ።

፳፬ ወውእቱሰ ኢየሱስ ኢየአምኖሙ
፳፬ እርሱ ግን አላመናቸውም ። ማለት እንዲመኑ ይቀራሉ አላለም ። ኢያየቀ ሎሙ ርእሶ ኢያግኃደ ሎሙ ርእሶ ኢከሠተ ሎሙ ርእሶ ይላል፣ እስመ የአምሮሙ በኵሉ ለለአሐዱ ። አንዱንም አንዱን ያውቀዋልና ።

፳፭ ወኢይፈቅድ ይንግርዎ ግዕዞ ለሰብእ ።
፳፭ የሰውን ግብሩን ሊነግሩት አይሻምና።

ወውእቱሰ የአምር ሕሊና ሰብእ እምቅድመ ኩነታ እንዲል ።
እስመ ለሊሁ የአምሮ ለሰብእ እርሱ ጥቂቱን በሰው ያለውን ሁሉ ያውቅ ነበርና ። እምቅድመ ይፍጥሮ ለአዳም የአምር ግብሮ እንዲል ።

በእንተ ኢየሱስ ወኒቆዲሞስ ።

ምዕራፍ ፫ ።

፩ ወህሎ አሐዱ ብእሲ እምፈሪሳውያን ዘስሙ ኒቆዲሞስ ።

፩ ብዙኃን አምኑ ቦቱ ብሎ ነበርና ፣ ብዙኃን ካላቸው ከፈሪሳውያን ወገን የሚሆን ኒቆዲሞስ የሚባል አንድ ሰው ነበር መልአኮሙ ለአይሁድ የአይሁድ አለቃ መልአኮሙ በትምርት በሹመት በባለጸግነት ።

፪ ወውእቱ መጽአ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ቀዲሙ ሌሊተ ።

፪ አስቀድሞ በሌሊት ወደ ጌታ የመጣ ለግንዘት መጣ የሚለው ነውና ከዚያ አስቀድሞ አንድም በመዓልት ከሚመጡት አስቀድሞ አንድም ከማመን አስቀድሞ በሌሊት አለ ውዳሴ ከንቱ ሽቶ መምህር ነኝ

እያለ እስከ ዛሬ ድረስ ትምህርት ሳይከታተል ኑሯል ይሉኛል ብሎ ። እንድም የቀን ልቡና ባካና ነው ። የሌሊት ልቡና ከት ነውና ትምህርት እንዲ ረዳው ። አንድም እመቦ ዘአምነ ቦቱ ከመ ከር ስቶስ ይሰደድ እምኵራብ ብለው ዐዋጅ ነግረው ነበርና አይሁድን ስለፈራ ። ያም ሆነ ያም ሆነ ከሣላ አሬት እንዳልተላቀቀ በመንፈስ ቅዱስ እንዳ ልታወቀ ያጠይቃል ።

ወይቤሎ ረቢ ነአምር ከመ እምኀበ እግዚአብሔር መጻእከ ከመ ትኩን መምህረ ።

አላመነም ብሎ መምህር ከእግዚአብሔር ታዘህ ልታስተምር እንደመጣህ እናውቃለን። እስመ አልቦ ዘይክል ይግበር ዘንተ ተአምረ ዘአንተ ትገብር አንተ የምታደርገውን ተአምራት ሊያደርግ የሚቻ ለው የለምና፡ እንደም ኢይክል አሐዱሂ ይላል አብነት አንዱ ስንኳን ሊያደርገው አይቻለውምና ። ዘእንበለ ዘእግዚአብሔር ምስሌሁ ።

እግዚአብሔር ካደረብህ ካንተ በቀር ። አንድም አምኑዋል ብሎ መምህር ከእግዚአብሔር አካል ዘእ ምአካል ባሕርይ ዘእምባሕርይ ተወልደህ ልታስ ተምር እንደመጣህ እናውቃለን ። እስመ ዘይክል አንተ የምታደርገውን ተአምራት ሊያደርገው የሚ ቻለው የለምና ። ኢይክል አሐዱሂ ። አንዱ ስን ኳን ሊያደርገው አይቻለውምና ። ዘእንበለሂ ዘእግ ዚአብሔር በሕልውናው ከርሱ ጋር ካለህ ካንተ በቀር ።

፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።

፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ አማን አማን እብለከ ዘኢተወልደ ዳግመ ኢይሬእያ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ። ዳግመኛ ያልተወለደ ሃይማኖትን አያውቃትም ብዬ እንዳያው ቃት በውነት እነግራችኋለሁ።ሃይማኖት አይቀደምም ልጅነት አይከተልም ቢሉ ወአልቦ ዘይክል ብሂለ እግዚእ ኢየሱስ ዘእንበለ መንፈስ ቅዱስ ሳዕሌሁ እንዲል ። መጽናቱን መጉላቱን መገለጡን ሲያይ እንዲህ አለ እንጂ እውነት ነው ሃይ ማኖት ይቀድማል ልጅነት ይከተላል ። አንድም ዳግመኛ ካልተወለደ መንግሥተ ሰማይ አይወርስም ብዬ እንዳይወርስ በውነት እነግርሃለሁ ። ያልተ ካከለ ዳግመ ነው ለልደት ሥጋው ልደተ ነፍሱን ዳግመ አለው ። አንድም የተካከለ ዳግመ ነው ። ልደተ ነፍሱን ለልደተ ነፍሱ ዳግመ አለው ።

፬ ወይቤሎ ኒቆዲሞስ እፎ ይክል ብእሲ ዳግመ ተወልዶ እምድኅረ ልሒቀ ።

፬ ኒቆዲሞስም ካደገ በኋላ ሁለተኛ መወለድ ለሰው እንደምን ይቻለዋል አለው ።

ይክልኑ በዊአ ወገቢአ ውስተ ከርሠ እሙ ወይት ወለድ ዳግመ ።

ሁለተኛማ ይወለድ ዘንድ ወደ አባቱ አብራክ ወደ እናቱ ማኅፀን መግባት ይቻለዋልን አንድም ይገባዋልን ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ጌታም መለሰ።
፭ ወይቤሎ አማን አማን እብለከ ዘኢተወልደ ዳግመ እማይ ወእመንፈስ ቅዱስ ኢይክል በዊአ ውስተ መንግሥተ እግዚአብሔር ።

፭ ልደቱን ነግሮት መወለጃውን አልነገረውም ነበርና ሁለተኛ ከአብራክ መንፈስ ቅዱስ ከማኅፀነ ዮርዳኖስ ካልተወለደ መንግሥተ ሰማያት መግባት አይቻለውም ብዬ እንዳይቻለው በውነት እነግርሃ ለሁ ።

ሦስትነቱን በዚህ ነገረው ፡ እማይ ብሎ ወልድን እመን ፈስ ቅዱስ ብሎ መንፈስ ቅዱስን ፡ መንግሥተ እግዚአብሔር ብሎ እግዚአብሔር አብን ።

፮ እስመ ዘተወልደ እምሥጋ ሥጋ ውእቱ ።
፮ ከግዙፍ ሥጋ የሚወለድ ግዙፍ ነውና ይክ ልኑ ላለው ወዘተወልደ እመንፈስ መንፈስ ውእቱ ።

ከረቂቅ መንፈስ ቅዱስ የምትወለድ ነፍስ ረቂቅ ናትና እመንፈስ ላለው ።

፯ ወበእንተዝ ኢታንክር እስመ እቤለከ ህለ ወከሙ ትትወለዱ ዳግመ ።

፯ ሁለተኛ ትወለዱ ዘንድ አላችሁ ስላልኩህ አታድንቅ ። አንድም እንድታደንቅስ ግዱን ትወለዱ ዘንድ አላችሁ ።

፰ እስመ መንፈስ ኀበ ፈቀደ ይነፍሕ ።
፰ ነፋስ በወደደው ይነፍሳል ።

ፈቀደ ሲል አይመችም ግዕዛን የለውምና ።
ወቃሎ ትሰምዕ ፥
ባሕር ሲገሥጽ ዛፍ ሲያናውጽ ድምፁን ትሰማዋለህ ወኢተአምር እምኀበ ይመጽእ ወኀበሂ የሐውር ። የሚመጣበትን የሚሄድበትንም አታውቀውም ። በምሥራቅ ፮ በምዕራብ ፮ መስኮት አሉት በዚህ ይወጣል በዚህ ይገባል አትለውም ።
ከማሁኬ ውእቱ ኵሉ ዘይትወለድ እመንፈስ ቅዱስ ከመንፈስ ቅዱስ የሚወለዱት ልደት እንዲህ ነው ። አንድም እስመ መንፈስ እያልክ መልስ መንፈስ ረድኤት በወደደው ያድራል ። ወቃሎ ትሰምዕ ። ትንቢት ሲናገር ሱባዔ ሲያስቈጥር ትሰማዋለህ። ወኢተአምር ህብተ ሙሴ በኢያሱ ። ሀብተ ኤልያስ በኤልሳዕ ሲያድር አታውቅም ። ከማሁኬ ። ከመ ንፈስ ቅዱስ የሚወለዱትም ልደት እንዲህ ነው ።

እንድም መንፈስ ቅዱስ በወደደው ያድራል ወቃሎ ትሰምዕ ። ቋንቋ ሲያናግር ምሥጢር ሲያስተረጕም ትሰማዋለህ ። ወኢተአምር ከወዴያ አለ ከወዴህ የለም ከወዴህ ወዴየ ይሄዳል ከወዴህ አለ ከወዴያ የለም ከወዴህ ወዴያ ይሄዳል አትለውም ። ከማሁኬ ከመንፈስ ቅዱስ የሚወለዱት ልደት አሁን እንደ ተናገርኩት ነው ።

፱ ወአውሥአ ኒቆዲሞስ ወይቤሎ ይትከሃል ዝንቱ ይኩን ።

፱ ኒቆዲሞስም እንዴህ መሆን እንደምን ይቻላል ብሎ መለሰ ነገሩ ቢረቅበት ።

፲ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎ አንተ ሊቆሙ ለእስራኤል ።
አንተ የእስራኤል መምራቸው ነህ ።
ወዘንተ ነገረ ኢተአምር ፡
ነገር ግን ይህን ነገር አታውቅም ።
ሊቆሙ ብሎ ማለምለም ። ኢተአምር ብሎ መገሠጽ እንድም የእስራኤል መምህር ያታውቅ ።

፲፩ አማን አማን እብለከ ከመ ዘነአምር ንነግር ።

፲፩ ራሱን ከዮሐንስ አግብቶ ያየነውን የስማነውን እናስተምራለን ብዬ እንድናስተምር በውነት እነግርሃለሁ ።
ወስምዓነሰ ተአብዩነ ነሢአ ፡
ምስክርነታችንን ግን አትቀበሉንም ።

፲፪ ሶበ እንዘ ዘበምድር እነግረክሙ ኢተአምኑኒ ወእፎ እንከ ተአምኑኒ እመ ነገርኩክሙ ዘበሰማያት ።

፲፪ ምድራዊ ልደታችሁን ስነግራችሁ ብነግራችሁ ያልተቀበላችሁኝ ሰማያዊ ልደታችሁን ብነግራችሁ እንደምን ትቀበሉኛላችሁ ለዚህ ምክንያት አለው በጥምቀት በንፍሐት ይሰጣል ። ለዚያ ግን ንቃሕ ዘትነውም ባለው ነው ምክንያት የለውምና።

፲፫ ወአልቦ ዘዓርገ ውስተ ሰማይ ዘእንበለ ዘወረደ እምሰማይ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።

፲፫ ወደሰማይ የወጣ የለም ወደ ሰማይ የወጣው ከሰማይ የወረደው ክርስቶስ ነው እንጂ ይኸንስ ለምን ይሻዋል ቢሉ የወጣውም የወረደውም አንድ አካል አንድ ባሕርይ ነው ለማለት ። እንድም አማን አማን እብለከ ብለህ መልስ። ራሱን ከአብ ጋራ አንድ አድርጎ በሀልውና ያየነውን በሀልውና የሰማነውን እናስተምራለን ብዬ እንድናስተምር በውነት እነግራችኋለሁ ወስምዓነሰ ምስክርነታችንን ግን አትቀበሉትም ። ወሶበ እንዘ በምድር ምድራዊ ልደቴን ብነግራችሁ ስነግራችሁ ያልተቀበላችሁኝ ሰማያዊ ልደቴን ብነግራችሁ እንደምን ትቀበሉኛላችሁ ። ሁሉስ አንድ አይደለምን ቢሉ ይህ ምክንያት አለው ባጭር ቁመት በጠባብ ደረት ተወስኖ ሰው ሁሉ ያየዋል ሰው ሲሆን ያየው የለምና ። በአምሳለ ሊቀ መላእክት ታየኋቸው እስከ ሣልስ ሰማይ ሸኙኝ ይል የለምን ቢሉ መዳረሻው ስለ አልታወቀ ።
ወአልቦ ዘዓርገ ውስተ ሰማይ ሰማያዊ ህብትን ሰማያዊ ዕውቀትን ገንዘብ ያደረገ የለም ።
ዘእንበለ ሰማያዊ ህብትን ሰማያዊ ዕውቀትን ገንዘብ ያደረገ ከሰማይ የወረደው ክርስቶስ ነው እንጂ ።

፲፬ ወበከመ ሙሴ ሰቀሎ ለአርዌ ምድር በገዳም ። አሪት ዘኍ. ፳፩ ፡ ፱

፲፬ ሙሴ እባብ በምድረ በዳ እንደሰቀለ ።
ከማሁ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ይሰቀል
የሰው ልጅ ክርስቶስ ይሰቀል ዘንድ አለው ። ጌታ መሰቀሉ ስለምን ነው ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊደርስ ሊፈጸም ። ትንቢት ስቅለተ ትሬእያ እሥራኤል ለሕይወትከ ወኢትትአመና ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም ጌታ እሥራኤልን ከደመና መና አውርዶ ከጭንጫ ውኀ አፍልቆ ቢመግባቸው ከዚህ ምድሩ ብቅ ሰማዩ ዝቅ ቢልለት ከደጋ ላይ ቢሆንለት የውርጭ ሰደቃ እያበጀ ውኀውን እያረጋ መና መገብኳችሁ ይላል እንጂ ይከልኑ እግዚአብሔር ሠሪዓ ማዕድ በገዳም ። ቆላ በሆነማ ባልተቻለውም ነበር ብለዋል ጌታም የርሱን ከሃሊነት የርሳቸውን ሐሰት ለመግለጥ ሙሴን አውርዶሙ ቆላተ ሐራሴቦን አለው ነቅዓ ማይ የሌለበት በረሃ ነው ይዟቸው ወርዷል መናም ዘንሞላቸዋል ወ ኀውም ፈልቆላቸዋል ። ነገር ግን ነዘር የሚባል እባብ እየነከሰ ይፈጃቸው ጀመረ ሙሴን ከኛ ስሕተት ኃጢአት አይታጣምና ወደ እግዚአብሔር አመልክትልን አማልደን አሉት ወደ እግዚአብሔር ቢያመለከትላቸው ጽሩዩን ብርት አርዌ አስመስለህ ሠርተህ አንብር ሎሙ ኀበ ኵሉ ይትዔመሩ ከሚገናኙበት ዐደባባይ ከዕንጨት ላይ ስቀልላቸው ያልጸናባቸው መልኩን እይተው የጸናባቸው ድምፁን ብቻ ሰምተው ይዳኑ አለው እንዳዘዘው አደረገው ያልጸናባቸው መልኩን እይተው የጸናባቸው ድምፁን ብቻ ሰምተው ድነዋል ። አርዌ ምድር የዲያብሎስ አርዌ ብርት የጌታ ምሳሌ በአርዌ ምድር መርዝ እንዳለበት በዲያብሎስ ፍዳ ኃጢአት አለበት ። በአርዌ ብርት መርዝ እንደሌለበት በጌታም ፍዳ ኃጢአት የለበትም ጽሩይ እንደሆነ ጌታም ጽሩየ ባሕርይ ነው ። አርዌ ብርት በአርዌ ምድር አምሳል መሰቀሉ ጌታም በአርአያ እኩያን ለመሰቀሉ ምሳሌ ተኍለቈ ምስለ ጊጉያን

እንዲል ። ይኸንም ሊቁ ከመ ይደምረነ ምስለ ነፍስ ጻድቃን ብሎ ተርጉሞታል መልኩን አይተው ድምፁን ሰምተው የዳኑ ከቃሉ ሰምተው ያመኑ የዳኑ ድምፁን ብቻ ሰምተው የዳኑ ከርሱ በኋላ ከተነሡ መምህራን ሰምተው ያመኑ የዳኑ የምእመናን ምሳሌ

፲፭ ከመ ኵሉ ዘአምነ ቦቱ ኢይትኃጐል ።
፲፭ በርሱ ያመነ ሁሉ እንዳይጎዳ አላ ይሕየው ሕይወተ ዘለዓለም ።

ለዘለዓለም ይድን ዘንድ እንጂ አንድም አይጐዳም አላ የሐዩ ይድናል እንጂ ።

፲፮ እስመ ከመዝ አፍቀሮ እግዚአብሔር ለዓለም እስከ ወልዶ ዋሕደ መጠወ ወወሀበ ቤዛ ኵሉ ፩ ፡ ዮሐ ፡ ፬ ፡ ፱ ።

፲፮ አንድ ልጁን ለሁሉ ቤዛ አድርጎ እስከ መስጠት ደርሶ እግዚአብሔር ዓለሙን ወዶታልና። ከመ ኵሉ ዘየአምን ቦቱ ኢይትኃጐል ።

በርሱ ያመኑ ሁሉ እንዳይጐዱ አላ ይረክብ ሕይወተ ዘለዓለም፥ የዘላለም ደህንነት ያገኝ ዘንድ ነው እንጂ አንድም በርሱ ያመነ ሁሉ አይጐዳም ። አላ ይረክብ ። የዘላለም ደኅንነት ያገኛል እንጂ ።

፲፯ እስመ ኢፈነዎ እግዚአብሔር ለወልዱ ውስተ ዓለም ከመ ይኰንኖ ለዓለም ።

፲፯ እግዚአብሔር በዓለሙ ሊፈርድበት ልጁን ወደዚህ ዓለም አልሰደደውም ።

ዘእንበለ ከመ ያሕይዎ ለዓለም በእንቲአሁ ።
እርሱ ስለ ካሰለት ያድነው ዘንድ እንጂ ። አንድም አስቀድሞ ያልተፈረደበት ሁኖ ሊፈርድበት አልሰደደውም ዘእንበለ ከመ ያሕይዎ ። ተፈርዶበታልና ከተፈረበት ፍርድ ሊያድነው ነው እንጂ አንድም በሥጋው ሊፈርድበት አላከውምና እጅ ለሌለው እጅ እግር ለሌለው እግር ። ዓይን ለሌለው ዓይን ሊሰጠው ነው እንጅ ።አንድም በመንፈሳዊው ቅሉ ሊፈርድበት አልሰደደውም ተኃድገ ለኪ ኃጢአትኪ ተኃድገ ለከ ኃጢአትከ እያለ ስርየተ ኃጢአትን ሊሰጥ ነው እንጂ ።

፲፰ ዘየአምን ቦቱ ኢይትኴነን ።
፲፰ በርሱ ያመነ አይፈረድበትም ወዘሰ ኢአምነ ቦቱ ወጽአ ተኰንነ በርሱ ባላመነ ግን ፈጽሞ ይፈረድበታል ።

እስመ ኢአምነ በስመ ወልደ እግዚአብሔር ዋሕድ ባንድ በእግዚአብሔር ልጅ አላመነምና ዋሕድ ለሁሉ ሳቱም ቅጽል ።

፲፱ ወዝውእቱ ኵነኔሁ ። ዮሐ ፡ ፩፥ ፱
፲፱ ፍርዱም ይህ ነው ።

እስመ ብርሃን መጽአ ውስተ ዓለም ።
ብርሃን ክርስቶስ ወደ ዓለም መጥቷልና ።
ወአብደረ ሰብእ ጽልመተ እምብርሃን ።
ሰውም ከብርሃን ጨለማን ከዕውቀት ድንቁርናን ከክርስቶስ ሰይጣንን ከወንጌል ኦሪትን ወዷልና ።
እስመ እኩይ ምግባሩ ።
ሥራው ክፉ ስለሆነ ።

፳ እስመ ኵሉ ዘእኩይ ምግባሩ ይጸልዕ ብርሃነ ።

፳ ምግባሩ ክፉ የሆነ ሰው ሁሉ ብርሃንን ይጠላልና ።
ወኢይመጽእ ኀበ ብርሃን
ወደ ብርሃን አይመጣም ።
ከመ ኢይትከሠቶ ምግባሩ ።
ሥራው እንዳይገለጥበት እስመ እኩይ ውእቱ ሥራው ክፉ ስለሆነ ዓይነ ዘማዊ ይጸንሕ ጽልመተ ወያጤልል ዲበ ገጸ ማይ ያለውን ለውጦ አነበበው ።

፳፩ ወዘሰ ጽድቀ ይገብር ይመጽእ ኀበ ብርሃን
፳፩ ሥራው በጐ የሆነ ሰው ግን ወደ ብርሃን ይመጣል ።

ከመ ያስተርኢ ምግባሩ ።
ሥራው ይገለጥ ዘንድ ።
እስመ በእንተ እግዚአብሔር ይገብር ።
ለለ እግዚአብሔር ብሎ ይሠራዋል ። ማለት ሥራው በጐ ስለሆነ አንድም እስመ ኵሉ ዘእኩይ ምግባሩ እያልክ መልስ ሥራቸው ክፉ የሆነ ጸሐፍት ፈሪሳውያን አንድም ሥራቸው ክፉ የሆነ አይሁድ አንድም ሥራቸው ክፉ የሆነ አሕዛብ ጌታን ይጠላሉ ወኢይመጽእ ፤ በጌታ አያምኑም ከመ ኢይትከሠቶ ሥራቸው እንዳይገለጥ እስመ እኩይ ውእቱ ሥራቸው ክፉ ስለሆነ ወዘሰ ሥራቸው በጐ የሆነ ሐዋርያት አንድም ሥራቸው በጐ የሆነ አይሁድ፡ አንድም ሥራቸው በጐ የሆነ አሕዛብ ግን በጌታ ያምናሉ ሥራቸው ይገለጥ ዘንድ ሥራቸው በጐ ስለሆነ ።

በእንተ ዳግማዊ ስምዑ ለዮሐንስ

፳፪ ወእምዝ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ወአርዳኢሁ ምስሌሁ ውስተ ምድረ ይሁዳ ዮሐ. ፬ ፩ ።

፳፪ ከዚህ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ወደ ምድረ ይሁዳ ሄደ ። ወሀየ ነበረ ምስሌሆሙ እንዘ ያጠምቅ ።

በዚያም ከርሳቸው ጋራ ሲያጠምቅ ኖረ እርሱስ አላጠመቀም ወለሊሁሰ ኢያጥመቀ ብሎ ያመጣዋል የሐዋርያትን ስርሱ ሰጥቶ መናገር ነው እንጂ ። ወከመዝ ንብረ ሙሴ በዞሚር ወበአክሲኖዶስ እንዲል

፳፫ ወሀሎ ዮሐንስኒ ያጠምቅ በሄኖን በቅሩብ ሳሌም በማዕዶተ ዮርዳኖስ ።

፳፫ በ ና በ አንድ ወገን ዮሐንስም የሳሌም አቅራቢያ በምትሆን በሄኖን ያጠምቅ ነበር ። እስመ ቦቱ ሆየ ብዙኀ ማያት ብዙ የማዋት ውኀ ነበርና በከተማ አቅራቢያ መሆኑ ለዕውር ሳንካሳ እንዲመች ነው ።

ወይመጽኡ ኀቤሁ ብዙኃን ወያጠምቆሙ ።
ብዙ ሰዎች ወደርሱ እየመጡ ያጠምቃቸው ነበር

፳፬ እስመ ዓዲሁ ኢተወድየ ዮሐንስ ውስተ ቤተ ሞቅሕ ።

፳፬ ዮሐንስ ገና አልተጋዘም ነበርና

፳፭ ወእምዝ ኮነ ተኃሥሦ ማእከለ አርዳኢሁ ለዮሐንስ ምስለ አይሁድ በእንተ አጥህሮ

፳፭ ከዚህ በኋላ አርድእተ ዮሐንስና አርድእተ ክርስቶስ በማጥመቅ ምክንያት በአይሁድ ዳኝነት ተከራከሩ ። ማጥመቅ የሚገባ ለኛ ነው እንጂ ለናንተ መቼ ይገባችኋል መምህራችሁ መስክሮለቆ የለም ብለው በአይሁድ ዳኝነት ይዘዋቸዋል ። አይሁድም ይህን ሰምተው እውነታቸው ነው ማጥመቅ የሚገባ ለኒህ ነው የናንተማ መምህር መስክሮ ለቆ የለም አሏቸው ። አይሁድ ይህን ያሉ እውነት ተናገርን ብለው አይደለም ዮሐንስ ይህን የሰማ እንደሆነ ተናዶ ነገር ይለውጥልናል ብለው ነው እንጂ ። አንድም አርድእተ ዮሐንስና አይሁድ በጥምቀት ምክንያት ተከራከሩ አርድእተ ዮሐንስ አይሁድን ወደ ጌታ ሲሄዱ አገኙዋቸው የኛ መምህር እያለ ወዴት ትሄዳላችሁ አሏቸው ማጥመቅ የሚገባ ለርሱ ነው እንጂ የናንተማ መምህር መስክሮ ለቆ የለም ብለዋቸው ሄዱ መጥተው ይህን ይነግሩታል ምክንያቱ እንዳለፈው ።

፳፮ ወሐሩ ኀበ ዮሐንስ ወይቤልዎ ዝኩ ዘምርሌከ ሀሎ በማዕዶተ ዮርዳኖስ ዘአንተ ስማዕተ ኮንከ በእንቲአሁ ናሁ ሀሎ ውእቱሂ ያጠምቅ ።

፳፮ ወደ ዮሐንስ ሂደው በዮርዳኖስ ማዶ ካንተ ጋራ የነበረ አንተ የመስከርህለት ያ እነሆ ያጠምቅ ጀመር ብለው ነገሩት ።
ዝኩ ቃለ ጽብእ ነው ዝኩ ወልደ ዕሤይ እንዲል።
ወኵሉ የሐውር ኀቤሁ ።
ሰው ሁሉም ወደርሱ ይሄድ ጀመር አሉት።

፳፯ ወአውሥአ ዮሐንስ ወይቤ ኢይክል ሰብእ ነሢአ ጸጋ ለሊሁ ወኢምንትኒ እመ ኢትውህበ ሎቱ እምሰማይ ። ዮሐ ፩፥፲፪ ።

፳፯ ከሰማይ ካልተሰጠው ማለት ከእግዚአብሔር ካልተሰጠው መምህርነትን ገንዘብ ማድረግ ለሰው አይቻለውም ።

፳፰ አንትሙኒ ለሊክሙ ስማዕትየ ከመ እቤለክሙ አንሰ ኢኮንኩ ክርስቶስሃ ።

፳፰ መሆኑንማ ክርስቶስ ነኝ እንዳላልኳችሁ እናንተም ቅሉ ምስክሮቼ ናችሁ ።
ዳዕሙ ተፈኖኩ ቅድሜሁ እስብክ ።
በፊቱ ተልኬአለሁ ማለት መንፈቅ ተቀድሜ ላስተምር ታዝዣለሁ እንጂ ።

፳፱ ዘቦቱ መርዓት መርዓዊ ውእቱ
፳፱ ሙሽራ ያለችው ሙሽራ ነው ማለት ያጨ እንጂ ያገባል ።
ወአርኩሰ ለመርዓዊ ዘይቀውም ወይሰምዖ ፍሥሐ ይትፌሣሕ በእንተ ቃለ መርዓዊ ወመርዓት ወፍሥሐ ዘአየሰ ናሁ ተፈጸመት ።

አርከ ላእክ ኀሩይ ይላል ግልገል መሪ ቀባጣሪ አማጭ ። የሙሽራና የሙሽራይቱ ነገር ሲወሰን ሰምቶ ደስ ይለዋል አንድም እልቦ ዘይክል ብለህ መልስ ። ከእግዚአብሔር ካልተሰጠው ሰማያዊ ዕውቀትን ገንዘብ ማድረግ ለሰው አይቻለውም።

፴ ወእንቲአሁሰ ትበዝኅ ወእንቲአየሰ ተሠልጠት ።

፴ የኔ መምህርነት አለፈች ተፈጸመች የሱ ግን አታልፍም አትፈጸምም ። አንተሙኒ ለሊክሙ ሰማዕትየ ። ነኝ እንዳላልኳችሁ እናንተ ቅሉ ምስክሮቼ ናችሁ ። ዳዕሙ ተፈኖኩ ላስተምር ታዘዝኩ እንጂ ። ዘቦቱ መርዓት ። ምእመናን ያሉት ክርስቶስ መምህር ነው ወአርኩሰ ለመርዓዊ ይትፌሣሕ በእንተ ቃለ መርአዊ ። የክርስቶስ ባለሟል የምሆን እኔ ክርስቶስ ሲያስተምር ምእመናን ትምርቱን ሲቀበሉት ሰምቼ ሲያድርባቸው ሲዋሐዳቸው አይቼ ደስ ይለኛል ። ወፍሥሐ ዘአየሰ ናሁ ኃልቀት ወተፈጸመት የኔ መምህርነት መንፈቅ ነበረች አለፈች ተፈጸመች ። ወእንቲአሁሰ ትቡዝኅ የርሱ ግን መምህርነቱ አትፈጸምም ። ወእንቲአየሰ ተሠልጠት ። የኔ የተሰጠችኝ መንፈቅ ነበረች ያችውም ተፈጸመች ።

፴፩ እስመ እምላዕሉ መጽአ መልዕልተ ኵሉ ውእቱ ።

፴፩ ከሰማይ የመጣ እርሱ ከሁሉ በላይ ነው ። ማለት የባሕርይ አምላክ ነውና ። ትበዝኅ ።

ወዘእምድርሰ ምድራዊ ውእቱ ወዘበምድር ይነግር ።
ከምድር የተገኘሁ እኔ ግን ምድራዊ ነኝና የምድራዊን ነገር አስተምራለሁ ። ማለት ዘካርያስ አባቴ ኤልሳቤጥ እናቴ እያልኩ አስተምራለሁ ።
ወዘእምሰማይ መጽአ መልዕልተ ኵሉ ውእቱ ።

ከሰማይ የመጣ እሱ ግን የባሕርይ እምላክ ነው ።
፴፪ ወበዘርአየ ወበዘሰምዓ ስማዕተ ይከውን

፴፪ በሀልውና ያየውን ያስተምራል
ወስምዖሰ አልቦ ዘይትዌከፎ
ምስክርነቱን ግን የሚቀበለው የለም ።
፴፫ ወለዘሰ ተወክፎ ስምዖ ዓተቦ እግዚአብሔር ። ሮሜ ፫፥ ፬ ።

፴፫ ባይቀበሉትስ ምን ይጐዳል ቢቀበሉትስ ምን ይጠቅማል ትሉኝ እንደሆነ የተቀበለውንስ እግዚአብሔር እተመው ማለት ራሱን አስመስሎታል ።

እስመ ጻድቅ ውእቱ ።
እውነተኛ ማለት የባሕርይ አምላክ ነውና ።

፴፬ ወዘእግዚአብሔር ፈነዎ ቃለ እግዚአብሔር ይነግር ።

፴፬ እግዚአብሔር የሾመው እውነተኛ መምህርም የእግዚአብሔርን ነገር ያስተምራል ።
እስመ አኮ በመሥፈርት ዘይሁብ እግዚአብሔር መንፈሶ ።

እግዚአብሔር ስጦታ ተከፍሎበት ሀብተ መንፈስ ቅዱስ በልክ የሚሰጠው አይደለምና አተቦ። አንድም ወለዘሰ ተወክፎ ስምዖ ብለህ መልስ ባይቀበሉትስ ምን ይጐዳል ቢቀበሉትስ ምን ይጠቅማል ትሉኝ እንደሆነ የተቀበለውንስ ከኢአማንያን ለየው ። እስመ ጻድቅ እውነተኛ መምህር ነውና ወዘእግዚአብሔር ፈነዎ ቃለ እግዚአብሔር ይነግር ከእግዚአብሔር አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእምባሕርይ ተወልዶ የመጣ እሱን የእግዚአብሔርነቱን ነገር ያስተምራል ። እስመ አኮ በመሥፈርት ። ሀብተ መንፈስን በልክ የሚሰጥ አይደለምና ።

፴፭ አብሰ ያፈቅር ወልዶ ወኵሎ ኰነኔሁ አወፈዮ ውስተ እዴሁ

፴፭ አብ ልጁን ይወደዋልና ሁሉን በጁ ጭብጥ በእግሩ እርግጥ አድርጐ አስገዛለት ።

፴፮ ዘየአምን በወልድ ቦ ሕይወት ዘለዓለም
፴፮ በወልድ ያመነ የማታልፍ መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል ። ፩.ዮሐ ፭ ፣ ፲ ።

ወዘሰ ኢየአምን በወልድ ኢይሬእያ ለሕይወት ዘለዓለም ።

በወልድ ያላመነ ግን የማታልፍ መንግሥት ሰማይን አይወርስም ።
አላ መቅሠፍተ መዓቱ ለእግዚአብሔር ይነብር ላዕሌሁ ።

የእግዚአብሔር የቁጣው መቅሠፍት ማለት ፈርዶ ያመጣበትን ፍዳ ሲቀበል ይኖራል እንጂ ።

በእንተ ኢየሱስ ወሳምራዊት ።

ምዕራፍ ። ፬

፩ ወአአሚሮ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ሰምዑ ፈሪሳውያን ከመ በዝኁ አርዳኢሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ወእብዝኁ አጥምቆ እምዮሐንስ ።

፩ አርድእተ ክርስቶስ ከአርድእተ ዮሐንስ እንደበዙ ። ከአርድእተ ዮሐንስ አርድእተ ክርስቶስ አብዝተው እንዳጠመቁ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ሰምተው እንዳዘኑ ዐውቆ ።

፪ ወባሕቱ ሰሊሁ እግዚእ ኢየሱስ ኢያጠምቅ ዳዕሙ አርዳኢሁ ።

፪ ነገር ግን ደቀ መዛሙርቱ ናቸው እንጂ እሱ አላጠመቀም

፫ ወኅደጋ ለምድረ ይሁዳ ወሖረ ካዕበ ገሊላ።
፫ የይሁዳን አገር ትቶ ሁለተኛ ወደገሊላ ሄደ ሰው የሚጠላባችሁን ሥራ አትሥሩ አትጠናቀሉ ለማለት አብነት ለመሆን ።

፬ ወእንዘ ሀለዎ ይኅልፍ እንተ ሰማርያ ።
፬ ሰማርያን ተረግጦ በሰማርያ በኩል ይሄድ ዘንድ ሳለው ።

፭ ወበጽሐ ሀገረ ሳምር እንተ ስማ ሲካር ዘፍ. ፴፫ ፣ ፲፱ ፡ ዘሌ. ፳፬ ፣ ፴፪ ።

፭ ሰማርያ ደረሰ ፡ ሐተታ ፍርቃን ተረግጦ በፍርቃ በኩል በጌምድር ይሄድ ዘንድ ሳለው ፍርቃ ደረሰ እንደማለት ።

ሴምር ይለዋል ። ለዘንበሪ በሁለት መቶ ብር ሸጦ ሊታል ዋጋ አነሰኝ አለው በስምህ ትጠራልህ አለው በሱ ስም ሰማርያ ተብላለች ።
ታሪክ ለኤርምያስ ባሮክ አቤሜሌክ የሚባሉ ደቀ መዛሙርት ነበሩት ፣ የጌዋዌን ነገር ሲናገር እየሰሙ ኢታርእየነ ሙስናሃ ለኢየሩሳሌም እያሉ ሲጸልዩ ይኖሩ ነበር ። ጌዋዌ በደረሰ ጊዜ ፣ ጌታ ኤርምያስን ባሮክን መቃብረ ነገሥት አስጠብቀው አቤሜሌክን ለድውያን የምንቀባው ዕጽቀ በለስ ቆርጠህ አምጣ በለው አለው ። እንዳዘዘው እደረገ በዚህ ጊዜ እስራኤል ተማርከው ባቢሎን ወረዱ፣ አቤሜሌክም ዕጽቀ በለሱን ቆርጦ በሙዳይ አድርጎ በሚሄድበት ጊዜ ቀትር ነበርና ዋዕይ ተሰማው ከዛፍ ሥር ከጥላ ዐረፈ ፣ ዕንቅልፍ መጥቶበት ተኛ ለተኛበት ሰዓት ጊዜ ገጥሞት ጥቂት እልፍ ብሎ ነቃ ዘማይቻለሁ መምህሬ ይቆጣኛል

ብሎ መንገድ ጀመረ መንገዱ ጠፍቶ አገሩ ተፈቶ የማያስሄደው ሆነ ዕንቅልፉስ ባይለቀኝ ነው ወይስ አእምሮዬ ተነሥቶኛል እያለ ሲያወጣ ሲያወርድ አንድ አረጋዊ ታየው ፡ አገር በጠፋ በ፷፮ ዘመን ሰው የለም ተመትሯል ብሎ መልአክ በአምሳለ አረጋዊ ተገልጦለታል ። ሄዶ የናፍቆት አነጋገር አይቴ ሀለዉ ኤርምያስ ወአኃውየ መምህሬ ኤርምያስ ወንድሞቼ እስራኤል የት ነው ያሉ አለው ። አንተኑ ነግድ ለኢየሩሳሌም እነ ኤርምያስ ያሉ ፋርስ ባቢሎን በስደት ። ኢየሩሳሌም ከተፈታች ፷፮ ዓመት አንተ ለኢየሩሳሌም እንግዳ ነህ አለው ። አረት አክብር ገጸ አረጋዊ ባትል ይህ ጅጁ አእምሮውን ያጣ ሽማግሌ ብዬ በስደብኩህ ነበር ። እነሆ መምህሬ ኤርምያስ ለድውያን የምንቀባው ዐጽቀ በለስ ቆርጠህ አምጣ ብሎኝ ደሟ ይንጠፈጠፋል ። ቅጠሏ አልጠወለገም ። አለው እስኪ አሳየኝ አለው ።

ቢያይ ደምዋ እየተንጠፈጠፈ ቅጠሏ ሳይጠወልግ አየ ። ላንተ ተአምራት ቢደረግልህ ነው እንጂ ሲልከህ ምን ወራት ኑሯል አለው ። ወርኃ ዘርዕ ነው ቢለው ወርኃ ጽጌ ሁኖብሃልሳ ይለዋል ወርኃ ጽጌ ነው ቢለው ወርኃ ዘርዕ ሁኖብሃልሳ ይለዋል ። ነገሩን በዚህ ይረዳዋል ፡ ይልቅስ ና ከወንድምህ ክባሮክ ላገናኝህ ብሎ ወስዶ አገናኘው ። የሚጠትን ነገር ግለጥልን ብለው ቀኖና ቢገቡ አራት አመት እንደ ቀረው ተገለጠላቸው። ዘ ወረቀት ጽፈው ማን በወሰደልን ሲሉ የታዘዘ ንስር ቀረበ ። ወረቀቱን ከአንገቱ አስረው ዐጽቀ በለሱን ጨምረው ሰደዱት ። ኤርምያስም ከወገኑ ሰው ሙቶበት ከንጉሡ መቃብር ተካሶ ሊያስቀብር ሲሄድ ከፈረስ ግምብ ሥር አሳርፎ ሳለ ኤርምያስ ኤርምያስ ብሎ በቃለ ሰብአዊ ጠርቶ ወረቀቱን ጣለለት ። ወዲያው ወኬዶ ለምውት በእገሪሁ ይላል ምውቱን ቢረግጠው ተነሥቶ የወረቀቱን ቃል መስክሮ ዐርፏል ። ቃሉም ለሚጠት ፬ ዓመት ቀርቶታልና የተጋባችሁ ተፋቱ ያልተጋባችሁ ተጠበቁ የሚል ነው ከፋዎቹ ማን ሚጠቱ ይደረግ እንጂ አገራችንን ማን ነሥቶን ሚስታችንንስ ማን አፋቶን ብለው ዝም ብለው ኖሩ ። ጊዜው ሲደርስ ኤርምያስ ደጋጎቹን ይዞ ጉዞ ጀመረ እኒዮም ተከተሉት አትከተሉኝ አትምጡብኝ ቀድሞ እንዲህ ብላችሁ አይሆንም ብላችኋል አላቸው ፡ አሕዛብም እንዲህ ሲጠሏችሁ አትቀሩም የሚስት የልጅ አገርስ አገር አይደለምን አሏቸው ፡ ሳንገባስ አንቀርም አይሆንም ብለው ሄዱ ። ፈለገ ኤፍራጥስ ሲደርሱ ባሮክን አቤሜሌክን አስረድቶ ገጠማቸው ። ድል አድርጎ ሰደዳቸው ተመልሰው ወደነበሩበት ሄዱ እንግዲህ ወዲህስ አትምጡብን አይሆንም ስንላችሁ እምቢ ብላችሁ ሄዳችኋል ።

የወደዱትን ቢያጡ ያጡትን ይቀላውጡ እንዲሉ ፡ ብለው ሰደዷቸው እግራቸው እንዳደረሳቸው ሄደው አገር አቅንተው ኑረዋል ። ሠመርናሃ ብለዋታል ስለ ዚህ ሰማርያ ተብላለች ብዙ ስም አላት ሰማርያ ሲካር ቀራንዮ ሎዛ ቴምናስራህ ቤቴል ሰቂማ ወለም ንሀሳ ተብላለች

፭ ቅሩበ ዐጸደ ወይን ዘወሀቦ ያዕቆብ ለዮሴፍ ወልዱ ።

፮ ዛቲ ሀብት እንተ ተዓቢ እምሀብት ዘነ ግእከዋ በቀስትየ ብሎ ያዕቆብ በበረከት ጊዜ ለልጁ ለዮሴፍ ለሰጠው ለወይኑ ቦታ አቅራቢያ የምትሆን ። ወወፅአት ዲና እንተ ተወልደት ሎቱ ለያዕቆብ ከመ ትርአይ አዋልደ ውእቱ ብሔር ይላል ባሥራሁለቱ መካከል የተወለደች የዛብሎን መንትያ ናት አሕዛብ መልከ መልካሞች ናቸው ዘፈን ያውቃሉና ልታይ ወጥታ ሳለች የሀገረ ገዢው ልጅ ነጥቆ ወስዶ ከከብር አሳነሳት ወአፍቀራ በነፍስታ ይላል ። ግዝርት ናትና መልከ መልካም ናትና ከቤት አኑሯት ሥርዓት ከጉል በት አባቴ ይህችን ብላቴና ወድጃታለሁና ተናገርልኝ አለው ። ሂዶ ለያዕቆብ ሴኬም ወልድየ አፍቀራ ለወለትክሙ ሀብዎ ከመ ትኩኖ ብእሲተ አለው ልጆቹ የሉም ሲመጡ መክሬ እነግርሃለሁ አለው ። መጡ ነገራቸው ፡ ነገራቸውን በልባቸው አድርገው እኛ ግዙራን እነሱ ቆላፋን ግዙራን ከቆላፋን ጋራ መጋባት እንደምን ይሆናል ተገዘሩ በላቸው አሉት በግዝረት ምስሉን አለው እርሱም እኒህ ሰዎች ገንዘብ ያላቸው ናቸው እሳ ቀድመን በግዝረት እንምስላቸው ከዚያ በኋላ ትኛ በውራጃ እርሳቸው በግምጃ አንድ ሁነን የኛን ሴቶች ልጆች ከእርሳቸው ወንዶች ልጆች የርሳቸውን ወንዶች ልጆች ከኛ ሴቶች ልጆች አጋብተን እንኖራለን አላቸው ። ያገሩም ሰዎች ተገዘሩ ።

ወእንዘ ጽሉአን እሙንቱ ይላል ቁስል የሚጸና በሦስተኛው ቀን ነውና ፡ ስምዖን ወሌዊ ቦኡ ተኃቢአሙ ይላል ። ስምዖንና ሌዊ አይዞህ አይዞህ ተባብለው አፍ አፋቸውን ይዘው አርደው አርደው ፈጅተዋቸው እኅታቸውን ይዘው ወጥተዋል እስራኤል ጥቃት አይወዱምና ። ያዕቆብም ይህን ሰምቶ ደቂቅየ ለምንተ ከመዝ ረስይክሙኒ ወአጽላእክሙኒ በኀበ ኵሉ ብሔር ውሑድ አነ በኍልቍየ ዳዕሙ እትቀጠቀጥ አነ ወቤትየ ብሏል፡ እንዲህ ስላለ በአሕዛብ ፍርሃት አድሮባቸው በጠ

ላትነት የተነሣባቸው የለም ።
ወሀሎ ህየ ዓዘቅተ ማየ ዘያዕቆብ ።
ከዚያ የያዕቆብ የውኀ ቦታ ነበር በሙቶ በግ የዋ
ጀው ። አንድም ለራሱ ብሎ ያስቆፈረው ወደ
ኪሞ እግዚእ ኢየሱስ በሐዊረ ፍኖት ነበረ ፀየ
ኀበ ውእቱ ዓዘቅት ።

ጌታችን መንገድ በመሄድ በደከመ ጊዜ ከዚያ ውኀ
ዳር ዐረፈ ። በነጋዲያን ልማድ ጠል ለማንሣት።
አንድም ሳምራዊትን አሳመነ የሚለው ነውና ፤
ወቀትር ሶቤሃ ጊዜ ስሱ ሰዓት ያውም ድልድል
ቀትር ነበር ቀትር ሲሆን ዋዕይ ይጸናል ከናላ
ላይ ይወድቃል ሐሞት ይበትናል ሰውነት ይዝ
ላልና ። ፮ም ሳምራዊት ውኀ ልትቀዳ መጣች
የሚል ነውና ውኀ የሚቀዱበት ሰዓት ስዓት አላ
ቸው ኢያውብርን በሠርክ አገኘ ይለዋል ፤
ሳኦልን በሠለስት አገኘ ይለዋል ወረከብኩ አዋልደ
ይወፅአ ሐዋርያተ ማይ እንዲል ።

፯ ወናሁ መጽአት ብእሲት እምሰማርያ ከመ
ትቅዳኀ ማየ ።

፯ አንዲት ሴት ውኀ ልትቀዳ ከሰማርያ መጣች
ወይቤላ ኢየሱስ አስተዪኒ ማየ ውኀ አጠጭኝ
አላት ።

፰ እስመ አርዳኢሁስ ሖሩ ሀገረ ከመ ይሳ
ይጡ ኀብስተ ሲሳዮሙ

፰ ደቀ መዛሙርቱ ምግባቸውን እንጀራ
ሊገዙ ወደ አገር ገብተው ነበርና ፤ አስትዪኒ ።
አንድም ደቀ መዛሙርቱስ ትሉኝ እንደሆነ ደቀ
መዛሙርቱስ ምግባቸውን ሊገዙ ወደ ሀገር ሄደው
ነበር ።

፱ ወትቤሎ ይእቲ ሳምራዊት እፎኑ እንዘ
አይሁዳዊ አንተ ትስእል እምኀቤየ ትስትይ ማየ
እንዘ ሳምራዊት አነ ።

፱ ያችም የሰማርያ ሴት እንዴት አንተ አይ
ሁዳዊ እኔ ሳምራዊት ስሆን ውኀ አጠጭን ትላ
ለህ አለችው ። አንድም እፎ ትስእል ፤ አንተ አይ
ሁዳዊ እኔ ሳምራዊት ስሆን እንደምን ወኀ አጠ
ጭኝ ትላለህ አለችው ። በምን ዐውቃ እንዲህ
አለች ቢሉ ባነጋገሩ ባጠማጠሙ ።

እስመ ኢየኀብሩ ሕርመተ አይሁድ ምስለ ሳም
ራውያን ።

አይሁድ ከሳምራውያን ጋራ በሥርዓት አንድ አይ
ሆኑም ነበርና ።
ወኢይትህወሉ ።                በበዓል
ወኢይዴመሩ ።
በግቢ አንድ አይደሉምና ።

፲ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፲ ጌታም መለሰ ።
ወይቤላ ሶበስ ተአምሪ ጸጋሁ ለእግዚአብሔር ወመኑ
ውእቱ ይስእለኪ ወይብለኪ አስትዪኒ ማየ ።
ወኀ አጠጭኝ ብሎ የለመነሽ ማንም እንደሆነ
የእግዚአብሔርንስ ቸርነቱን ብታውቂ ። አን
ቲኒ ዓዲ እምስአልኪዮ ። አንችም በለመንሽው
ነበር ። ወውእቱኒ እምወሀበኪ ማየ ሕይወት ።
እርሱም የሕይወት ውኀን በሰጠሽ ነበር ። አን
ድም ውኀ አጠጭኝ ብዬ የምለምንሽ እኔ ኃይሉ
ሰኢብ ወጸጋ ዘአሕዛብ ተብሎ የተነገረልኝስ እን
ደሆንኩ ብታውቂ አንችም በለመንሽኝ እኔም ማየ
ሕይወትን በሰጠሁሽ ነበር ፤

፲፩ ወትቤሎ ይእቲ ብእሲት እግዚእየ ማኀ
የብኒ አልብከ ።

፲፩ ያችም ሴት ጌታዬ መቅጃ አልያዝኩም
ለልማዱ ነጋድያን ወኀ በመንቀል ይይዛሉ። ኪያ
ዝከው ታጠጣኛለህ እንዳልል ወኀ በመንቀል እል
ያዝክ ፤
ወዓዘቅቱኒ ዕሙቅ ውእቱ ። በጅህ ታፍነህ ታጠ
ጣኛለህ እንዳልልም ምንጩ ጥልቅ ነው እምአ
ይቴ እንከ ለከ ማየ ሕይወት ።
የሕይወት ወኀ ከወዴት አለህ አለችው ።

፲፪ አንተኑ ተዐቢ እምያዕቆብ አቡነ ዘወሀበነ
ዘንተ ዓዘቅተ ።

፲፪ የነቀፈብኝ መስኳት በዚያውስ ላይ ይሆን
ምንጭ ከሰጠን ከያዕቆብ አንተ ትበልጣለህን ወው
እቱኒ ሰትየ እምኔሃ ። እርሱ ከርሷ ጠጣ ፤
ወደቂቁኒ ።                ልጆቹም ።
ወአንስቲያሁኒ ።                ሚስቶቹም ።
ወእንስሳሁኒ ።                ከብቶቹም ።
ወጥሪቱኒ ።                ባሮቹም ።
ከርሷ ጠጡ ተወልዳለች ቢሉ የተመቸ አልተወ
ለደችም ቢሉ በልማድ ። ስልምናሶር በሰማርያ
አጀም ኮንታ የሚባል ጭፍራ ሠርቷል ። አንበሳ
ተነሥቶ ይፈጃቸው ጀመር እንደምን ሁነዋል ብሎ
ጠየቀ ኢያእመሩ ሕገ ለአምላክ ውእቱ ብሔር ።
ሥርዓቱን አላወቁበትም ፤ በዚያ አገር ያዕቆብ
አቡነ እግዚአብሔር አምላከነ የማይል እንጂ አይ
ኖርበትም አንበሳ ተነሥቶ ይፈጃቸው ጀመር አሉት
ምናሴ የሚባል ካህን በዔዋዌ ከርሱ ሄዶ ይኖራል
አስተምራቸው ብሎ ሰዶት አሥተምሯቸው ያዕ
ቆብ አቡነ እግዚአብሔር አምላከነ የሚሉ ሁነ
ዋልና በልማድ ። አንድም ከርሱ ተወልዳለች።
አንድም ምናሴ የሚባል ካህን በዔዋዌ ሂዶ ከሰ
ንባላጥ ንጉሠ ምስር ተጋብቶ ይኖራል ፤ እሰና

ብተኝ አገሬ ልሂድ አለው ። ምን አሳጣሁህ ግድ ኑር አለው አይሆንም አለው ። ሂድ ብሎ አሰና በተው ። ቢሄድ ዘመዶቹ ከአሕዛብ ተጋብተህ ኑረሃል ብለው መልሰው አባረው ሰደዱት ተመ ልሶ ሂደ ። እኔማ ቀድሞስ አትሂድ ብየህ አል ነበረም ወይም እንጂ እወዲ እዴየ ዲበ ደብረ ከርሜልም ያለው ይፈጸም ይሆናል ብሎ በምት ወደው በሀገርህ ቤተ መቅደስ ሥርተህ ካህን ሁነህ ኑር ብሎ ገንዘብ ሰጥቶ ሰዶታል ከዚህ ተወል ዳለች ።

፲፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፫ ጌታም መለሰ ፡
ወይቤላ ኵሉ ዘይሰቲ እምዝ ማይ ይጸምዕ ዳግመ።
ከዚህ ውኃ የሚጠጣ ሁሉ ሁለተኛ ይጠማል ።
ወዘሰ ይሰቲ እማይ ዘእሁብ አነ ኢይጸምዕ ለዓለም።
እኔ ከምሰጠው ውኃ የሚጠጣ ግን ለዘለዓለም አይጠማም ።

፲፬ አላ ውእቱ ማይ ዘእሁቦ አነ ይከውን ውስ ቴቱ ነቅዓ ማይ ዘይፈለፍል ለሕይወት ዘለዓለም ።

፲፬ እኔ የምሰጠው የዘላለም ሕይወት ውኃ ከርሱ ሲፈልቅ ሲፈስ ይኖራል እንጂ ። አንድም ወዘሰ ይሰቲ ብለህ መልስ እኔ ያስተማርኩትን ትምህርት እኔ የሰጠሁትን ልጅነት በተቀበለ ጽምዓ ነፍስ የለበትም ።
አላ ውእቱ ማይ ።
እኔ የማስተምረው ትምህርት በርሱ ቃል ሲነገር እኔ የሰጠሁት ልጅነት በርሱ ምክንያት ሲሰጥ ይኖ ራል እንጂ ።

፲፭ ወትቤሎ ይእቲ ብእሲት እግዚእየ ሀበኒዮ እምውእቱ ማይ

፲፭ ያችም ሴት ጌታዬ ከዚያ ውኃ ስጠኝ ።
ሀበኒ ኪያሁ እርሱን ስጠኝ ።
ከመ ኢይጽማዕ ።
እንዳልጠማ ።
ወኢይምጻእ ዝየ ዳግመ እቅዳሕ ማየ ።
ዳግመኛ ውኃ ልቀዳ እንዳልመጣ አንድም ኢይጸ ምዕ ዳግመ ብሎ ነበርና ሁለተኛ እንዳልጠማ ።

፲፮ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ሑሪኬ ጸውዒ ምተኪ ወንዒ ዝየ ።

፲፮ ጌታም ሄደሽ ባልሽን ጠርተሽ ይዘሽው ነይ አላት ።

፲፯ ወአውሥአቶ ይእቲ ብእሲት ።
፲፯ ያችም ሴት መለሰች ።
ወትቤሎ አልብየ ምት ።
ባልም የለኝ አለችው ።

፲፰ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ሠናየ ትቤሊ አልብየ ምት ።

፲፰ ጌታም አላት ባልም የለኝ ማለትሽ እው ነትሽ ነው ።
ቀዲሙስ ኃምስቱ አደው ነበሩ ምስሌኪ ።
አስቀድሞ አምስት ባሎች ነበሩሽ ።
ወይእዜሰ ዘሀሎ ምስሌኪ ኢኮነ ምተኪ ።
ዛሬ ግን ካንች ጋራ ያለው ባልሽ አይደለም በሳራ ወስተ ራጉኤል አስማንድዮስ የሚባል ጋኔን በጭ ንዋ አድሮ ፯ቱን ባሎቹዋን እንደ ገደለባት ። ይህ ችንም አምስቱን ባሎቹዋን ገድሎባታል ስለዚህ ልብስ ቀለብ እየሰጠች በጕረቤት ታኖረው ነበር አንድም ኃምስቱ አደው ብለህ መልስ ። አምስቱን መጻሕፍተ ሙሴ ተቀብለሻል ። ወይእዜሰ ዘሀሎ በኵር እኔን ግን በኵር አላደረግሽኝም ።

ወዘንተሰ አማን ትቤሊ ።
አልተወለደችም ቢሉ አልብየ ምት ማለትሽ እው ነትሽ ነው ያይወልድሽ ያዕቆብን ። ያዕቆብ አቡነ ማለትሽ ሐሰትሽ ነው እንጂ ። ተወልዳለች ቢሉ ያዕቆብ አቡነ ማለትሽ እውነትሽ ነው እግዚእ ያዕቆብ እኔን ከያዕቆብ ጋራ እነጻጽረሽ አንተኑ ተዓቢ እምያዕቆብ አቡነ ማለትሽ ሐሰትሽ ነው እንጂ ። አንድም ማኅየብኒ አልብከ ማለትሽ እው ነትሽ ነው ። ማየ ሕይወት እኔን እምአይቴ እንከ ለከ ማየ ሕይወት ማለትሽ ሐሰትሽ ነው እንጂ ።

፲፱ ወትቤሎ ይእቲ ብእሲት እግዚእየ እሬእየከ ከመ ነቢይ አንተ ።

፲፱ ያችም ሴት ጌታዬ ዐዋቂ ትመስለኛለህ አለችው ።

፳ አበዊነሰ በዝንቱ ደብር ሰገዱ ዘዳ፡፲፪፡፳ ።
፳ አባቶቻችን በዚህ ተራራ ይሰግዱ ነበር ተወልዳለች ቢሉ ሎዛን ቀራንዮን እያሳየች ፡ አል ተወለደችም ቢሉ ማናቸውንም ተራራ እያሳየች ።

ወአንትሙሰ ትብሉ ከመ በኢየሩሳሌም መካን ውእቱ ኀበ ይሰግዱ ።

እናንተ የኋላ ልጆች ግን የሚሰግዱ በኢየሩሳሌም ብቻ እንደሆነ ትናገራላችሁ ።

፳፩ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ እመንኒ ብእ ሲቶ ከመ ትመጽእ ሰዓት ወይበጽሕ ጊዜሁ አመ ኢዝንቱ ደብር ወኢበኢየሩሳሌም ዘይሰግዱ ለአብ አላ በበዝንቱ መካን ይሰግዱ ።

፳፩ አንች ሆይ በዚህም ተራራ ሁኖ በኢየ ሩሳሌም ሁኖ ለአብ የሚሰግዱበት ጊዜ እንዲደርስ ዕወቂ ። አንድም አመ ኢበዝንቱ ደብር ወኢበኢ የሩሳሌም በዚህም ተራራ ብቻ በኢየሩሳሌም ብቻ አመ ኢይሰግዱ ለአብ የማይሰግዱበት ጊዜ እንዲ

ደርስ ዕወቂ ፣ አላ በኵሉ ገጸ መካን ይላል ባራቱ ማዕዘን ነው እንጂ ።

፳፪ አንትሙሰ ትሰግዱ ለዘኢተአምሩ ። ፬ ነገ ፲፯፥፴፩ ።

፳፪ እናንተ በሥራ ለማታውቁት ትሰግዳላችሁ።
ወንሕነሰ ንሰግድ ለዘነአምር ።
እኛ ግን በሥራ ለምናውቀው እንሰግዳለን ።
እስመ መድኃኒት እምነ አይሁድ ውእቱ ።
ተስፋ በሀገረ ተስፋ አምልኮ በሀገረአምልኮ ነውና።
አንድም አንትሙሰ ትሰግዱ እናንተስ በአካል ሦስት በባሕርይ በህልውና አንድ ብላችሁ ለማታውቁት ትሰግዳላችሁ ። እኛ ግን በአካል ሦስት በባሕርይ በህልውና አንድ ብለን ለምናውቀው እንሰግዳለን።
እስመ መድኃኒት እምነ ይሁዳ መድኅነ ዓለም ክርስቶስ ከነገደ ይሁዳ ተወልዷልና ።

፳፫ መባሕቱ ትመጽእ ሰዓት ።
፳፫ ባሕቱ ዋዌ ነው ጊዜም ይደርሳልና ።

ወይእዜ ይእቲ አመ እለ በርቱዕ በአማን ሰጋድያን ይሰግዱ ለአብ በመንፈስ ወጽድቅ ።
በውነት በሚገባ ለአብ የሚሰግዱ በመንፈስና በጽድቅ ማለት በእብራክ ነፍስ ሁነው በንጽሐ ጠባይዕ ጸንተው ለአብ የሚሰግዱበት ጊዜም ዛሬ ነው።
አንድም በመንፈስ ቅዱስ ልጆች ሁነው በጽድቀ አሚን ጸንተው ። አንድም በመንፈስ ቅዱስ በወልድ አምነው የሚሰግዱበት ጊዜ ዛሬ ነው ።
እስመ አብኒ ዘከመዝ የኃሥሥ እለ ይሰግዱ ሎቱ።
አብ እንዲህ የሚሰግዱለትን ይወዳልና ።

፳፬ እስመ እግዚአብሔር መንፈስ ውእቱ ። ፪ ቆሮ ፫፥፲፯ ።

፳፬ እግዚአብሔር ረቂቅ ስለሆነ ።
ወእለሂ ይሰግዱ ሎቱ በመንፈስ ወበጽድቅ ሀለዎሙ ይስግዱ ሎቱ ።
የሚሰግዱለት በእብራክ ነፍስ ሁነው በንጽሐ ጠባይዕ ጸንተው ይሰግዱለት ዘንድ አላቸው ።

፳፭ ወትቤሎ ይእቲ ብእሲት አእምር ከመ ይመጽእ ማስያስ ዘይብልዎ ክርስቶስ ።

፳፭ ነግሬት ሳለ ያልነገራት መስሏት ለጠየቅሁህ መልስልኝ እንጂ ይኸንስ ክርስቶስ የሚባል ማስያስ እንዲመጣ አውቃለሁ ።
ወአመ መጽአ ውእቱ ይነግረነ ኵሎ።
በመጣም ጊዜ ሁሉን ያስተምረናል ። አንድም እንትሙሰ ትሰግዱ ለዘኢተአምሩ ። ብሏት ነበርና ምነዋ እናውቅ እናውቃለን እንጂ ክርስቶስ የሚባል ማስያስ እንዲመጣ ።
ወአመ መጽአ በመጣም ጊዜ እንዲነግረንእናውቃለን።

፳፮ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ዘእትናገረኪ ።

፳፮ ክርስቶስ የሚባል ማስያስ ይመጣል ። በመጣም ጊዜ ሁሉን ይነግረናል የምትዪው የምናገርሽ እኔ ነኝ አላት ። አንድም ክርስቶስ የሚባል ማስያስ ይመጣል የምትዪው እኔ ነኝ ። በመጣም ጊዜ ሁሉን ይነግረናል የምትዪው የምነግርሽ ነገር ነው ።

፳፯ ወእምዝ መጽኡ አርዳኢሁ ።

፳፯ ሖሩ ብሎ ነበርና ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ መጡ ።
ወአንከርዎ ።　　　　　አደነቁት ።
እስመ ምስለ ብእሲት ይትናገር ።
ከሴት ጋራ ሲነጋገር አይተውታልና ብዙ ምሑራን መጻሕፍት ያላመኑበት ይህች ሴት ታምንብኛለች ብሎ ነው ብለው ። አንድም ለትሕትናው ሴት ወንድ ታናሽ ታላቅ አይለይለትም ብለው ።
ወባሕቱ አልቦ ዘይቤሎ ምንተ ተኃሥሥ ወምንተ ትትናገር ምስሌሃ ።
ነገር ግን ከርሷ ምን ትሻለህ ከርሷ ጋራ ምን ትነጋገራለህ ብሎ ደፍሮ የጠየቀው የለም ።

፳፰ ወኀደገት ቀሡታ ይእቲ ብእሲት ወሖረት ወአተወት ሀገረ ።

፳፰ ያችም ሴት ማድጋዋን ትታ ከከተማው ገባች ። ልብ ቀርቷት ፈጥና እንድትመለስ።

ወነገረት ለሰብእ ።
ለጐረቤቶችዋ ነገረች ለሰብእ ቤታ ይላል ለቤተ ሰዎቹዋ ነገረች ቤተ ስብእ እያላት ውኃ ትቀዳለች ቢሉ በሀገራቸው በሥራ መለያየት የለም ።

፳፱ ወትቤሎሙ ንዑ ትርአዩ ብእሴ ዘነገረኒ ኵሎ ዘገበርኩ ።

፳፱ የሠራሁትን ሥራ የነገረኝን ሰው ታዩ ዘንድ ኑ ።

፴ እንዳኢ ለእመሁ ክርስቶስ ።

፴ ክርስቶስም እንደሆነ እንጃ አለቻቸው ።

፴፩ ወወፅኡ እምሀገር ወሖሩ ኀቤሁ ።

፴፩ ከከተማው ወጥተው ወደሱ ሄዱ ።
፴፪ ወእምዝ ይቤልዎ አርዳኢሁ ረቢ ብላዕ እክለ።

፴፪ መጽኡ ብሎ ነበርና ። ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱ መምህር ሆይ እህል ብላ አሉት ። ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አንሰ ብየ መብልዕ ዘእበልዕ ዘኢተአምርዎ እንትሙ ።

ጌታም አሳቸው የምበላው መብል አለኝ እናንተ የማታውቁት ።

፴፫ ወተበሀሉ አርዳኢሁ በበይናቲሆሙ ቦኑ እንጋ ሰብእ ዘአምጽአ ሎቱ መብልዓ ዘይበልዕ

፴፫ ደቀ መዛሙርቱም እርስ በርሳቸው እን ዳች የሚበላው ያመጣለት ሰው ይኖር ይሆን ተባባሉ። ወሚመ ዛቲ ብእሲት ። ወይም ይህች ሴት አመጣልሃለሁ ብላው ይሆን ።

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ ሊተሰ መብልዕየ ውእቱ ከመ እግበር ፈቃዶ ለዘ ፈነወኒ ።

፴፬ የኔስ ምግቤ የላከኝ ያባቴን ፈቃድ አደ ርግ ዘንድ ነው ።
ወከመ እፈጽም ግብሮ ።
ሥራውንም እፈጽም ዘንድ

፴፭ አኮኑ አንትሙ እለ ትብሉ አስከ ራብዕ ወርኅ ይከውን ማዕረር ።

፴፭ እናንተ እስከ አራት ወር ። ድኅረ ራብዕ ወርኅ ይላል ካራት ወር በኋላ መከር ይደርሳል ትሉ የለምን ።

ወናሁ እብለክሙ አንሥኡ አዕይንቲክሙ ወነጽሩ ኅበ በሐውርት ከመ ፃዕድው ወበጽሐ ማዕረር ። እንዲህም የምትሉ እናንተ ዓይናችሁን አራምዳችሁ መከር እንደ ደረሰ አስተውሉ ።

እኔ ግን ዕለቱን ዘርቼ ዕለቱን አድርሼ አሳያችኋለሁ። እስከባለው በሀገራችን ሐምሌ ነሐሴ መስከረም ጥቅምት ድኅረ ባለው ከሰኔ አምስት ሐምሌ ነሐሴ መስከረም ፣ ድኅረ ጥቅምት ነው ፣ በሀገራቸው እስከ ባለው ጥር የካቲት መጋቢት ሚያዝያ ፣ ድኅረ ባለው ከታኅሣሥ አምስት ጥር የካቲት መጋቢት ፣ ድኅረ ሚያዝያ ነው እንድም እስካራተኛው ክፍለ ዘመን ሥጋዌ ይደረጋል ትሉ የለምን።እንደም ድኅረ ራብዕ ወርኅ ፣ ካራተኛው ክፍለ ዘመን በኋላ ሥጋዌ ይደ ረጋል ትሉ የለምን አንሥኡ አዕይንቲክሙ እን ዲህ የምትሉ ዓይነ ልቡናችሁን አራምዳችሁ ሥጋዌ እንደ ደረሰ ዕወቁ እኔ ግን ዕለቱን አስተምሬ ዕለቱን ከፍጹምነት አድርሼ አሳያችኋለሁ ። እስከ ባለው ዘመነ አበው ዘመነ መሳፍንት ዘመነ ነገሥት ዘመነ ካህናት ድኅረ ባለው ዘመነ አበው ዘመነ መሳፍ ንት ዘመነ ነገሥት ድኅረ ዘመነ ሥጋዌ ነው ።

፴፮ እስመ ዘየአጽድኒ ይነሥእ አስበ ማቴ ፱፡፴፯ ሉቃ፡ ፲፱ ።

፴፮ የሚያጭድም ዋጋውን ያገኛል ወያስተ ጋብእ ፍሬ ለሕይወት ዘለዓለም ። ለዘላለም ሕይወት ፍሬንም ይሰበስባል ። ወይ ምሥ ጢር ሂዶ ለሕይወት ዘለዓለም አለ ። አንድም እስመ ዘየአጽድኒ ። የሚያስተምር ሐዋርያ ዋጋ ውን ያገኛል ። ወያስተጋብእ ፍሬ የዘላለም ክብር ሲሆነው ፍሬ ክብርን ይሰበስባል ።

ከመ ኅቡረ ይትፌሥሑ ዘሂ ይዘርዕ ወዘሂ የአርር። የሚዘራም የሚያጭድም አንድ ሁነው ደስ ይላ ቸው ዘንድ

፴፯ ወበዝንቱ ነገር ቃል ጽድቅ እሙን ውእቱ ከመ ካልዕ ዘይዘርዕ ወካልዕ ዘየአርር ።

፴፯ የሚዘራ ሌላ የሚያጭድም ሌላ እንደ ሆነ ይህ ነገር በውነት የታመነ ነው አለ ። በሀገራቸው በሀገራችን ታሞ ሙቶ እገር ጥሎ ሂዶ በደንቢያ ግን የዘራውን አያጭደውም የርሱን ሲ ያ ሳ ጭ ድ አጊጦ ጥላ ይዞ ሲያሳጭድ ይው ላል በነጋው ማጭዱን ይዞ ለሌላው ሊያጭድ ይሄዳል ። አንድም ከመ ኅቡረ ይትፌሥሑ ብለሀ መልስ ይወርዳል ይወለዳል ብለው ትንቢት የተ ናገሩ ነቢያት ወረደ ተወለደ ብለው ያስተማሩ ሐዋርያት አንድ ሁነው ደስ ይላቸው ዘንድ ። ወዝንቱ ነገር፡ይወርዳል ብለው ትንቢት የተናገሩ ነቢ ያት ወረደ ተወለደ ብለው ያስተማሩ ሐዋርያት አንድ ሊንደሆኑ ይህ ነገር እውነት ነው ፡ ነቢያ ትን በክረምት ገበሬ ። ሐዋርያትን በበጋ ገበሬ መስሎ ይናገራል ። የክረምት ገበሬ ጧት ሲወጣ ምሳ ሳይበላ ይወጣል ቀን ከዋለበት ከውኀ ሳይ ቆም ከላይ ውኀ ሲወርድበት ይውላል ማታም በተመለሰ ጊዜ ምግቡ ተዘጋጅቶ አይቀርብለትም ኅሠን ጠምቆ ያድራል ። የበጋ ገበሬ ጥዋት ሲ ወ ጣ ም ሳ ው ን በልቶ ይ ወ ጣ ል ከዋ ለበትም እሸቱን እንኩቶውን ሲበላ ይውላል ። ማታም በተመለሰ ጊዜ ምግቡ ተዘጋጅቶ ይቆ የዋል እ ን ጀ ራ ው በሌማት ጠላው በማቶት የክረምት ገበሬ ጧት ሲወጣ ምሳ ሳይበላ እንዲ ወጣ ነቢያትም ልጅነትን አላገኙም ከዋለበት ውኀ ላይ ቁሞ ውኀ ሲወርድበት እንዲውል ፣ መከራ ጸንቶባቸዋል ። በተመለሰም ጊዜም እራቱ ተዘጋጅቶ እንዳይቀርብለት ፣ ርድተ ገሃነም አልቀረ ላቸውም ፣ የበጋ ገበሬ ጧት ሲወጣ ምሳውንበልቶ እንዲወጣ ፡ ልጅነት አግኝተዋል ። ከዋለበት እሸት እንኩቶ ሲበላ እንዲውል ፡ ተአምራት ተድርጎ ላቸዋል ። ማታ በተመለሰ ጊዜም እራቱ ተዘጋ ጅቶ እንዲቀርብለት ርደተ ገሃነም አላገኛቸውም።

፴፰ ወአንስ ፈነውኩክሙ ከመ ትእርሩ በዘ ኢጻመውክሙ ዘባዕድ ጻመወ ።

፴፰ እኔስ እናንተ ያልደከማችሁበትን ሌላ የደ ከመበትን ልትሰበስቡ ላክኋችሁ ።
አንትሙ ትባኡ ውስተ ጻማሆሙ ለእልክቱ ።
እኒያ በደከሙበት እናንተ ትገቡ ዘንድ ። አንድም አንሰ ብሰሀ መልሰ እናንተ ይወርዳል ይወለዳል ብላችሁ ትንቢት ያልተናገራችሁለትን ነቢያት ይወርዳል ይወለዳል ብለው ትንቢት የተ ናገሩለትን ወረደ ተወለደ ብላችሁ ታስተምሩ ዘንድ ላክኋችሁ ። ነቢያት በመደመዱ ሐዋርያት ገደገዱ እንዲሉ ሁሉ ።

፴፱ ወብዙኃን እምይእቲ ሀገረ ሳምር እለ አምኑ ቦቱ በእንተ ዘትቤሎሙ ይእቲ ብእሲት ዘስምዓ ኮነት እንዘ ትብል ነገረኒ ኵሎ ዘገበርኩ ።

፴፱ የሠራሁትን ነገር ሁሉ ነገረኝ ብላ ያች ሴት ስለ ነገረቻቸው ከሰማርያ ሰዎች ያመኑበት ብዙ ናቸው ።

፵ ወበጺሖሙ ኀቤሁ ኵሎሙ ሳምራውያን አስተብቍዕዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ከመ ይንበር ኀቤ ሆሙ ።

፵ ሳምራውያን ሁሉ ወደርሱ መጥተው ሰን ብትልን ብለው ጌታን ማለዱት ።

፵፩ ወነበሩ ሀየ ስኑየ መዋዕለ ።

፵፩ ከዚያም ሁለት ቀን ተቀመጠ መላልሳ ችሁ አስተምሩ ለማለት አብነት ለመሆን ።
ወብዙኃን ጥቀ እምኔሆሙ እለ አምኑ ቦቱ በእን፡ ቃሉ ።
ይልቁንም ከቃሉ ሰምተው ያመኑበት ብዙ ናቸው።

፵፪ ወይቤልዋ ለዛቲ ብእሲት አኮ እንከ በነ ገረ ዚአኪ ዘአመነ ቦቱ ።

፵፪ ያችንም ሴት ያመንበት አንች በነገርሽን አይደለም አሏት የሴት ደቀ መዛሙርት እንዳይ ሉን ብለው ውዳሴ ከንቱ ሽተው ። አንድም እውነታቸው ነው ክርሷ ከሰሙ የሰሙ ናቸው አን ድም አንቺ በነገርሽን ብቻ አላመንበትም አን ችስ እንዳኢሰአመ ውእቱ ክርስቶስ ብለሽ አጠራ ጥረሽን ነበር ።
አላ ለሊነ ጠየቅነ ወሰማዕነ ከመ ዝንቱ ውእቱ ክርስቶስ በአማን መድኀነ ዓለም ።
እኛ ከቃሉ ሰምተን በውነት የዓለሙ መድኃኒት ክርስቶስ እንደሆነ ዓውቀን አምነንበታል እንጂ።

ዘከመ አሕየዎ ኢየሱስ በገሊላ ለወልደ ገብረ ንጉሥ።

፵፫ ወእምድኅረ ሰኑይ መዋዕል ወፅአ እግ ዚእ ኢየሱስ እምህየ ወሖረ ካዕበ ገሊላ ።

፵፫ ከሁለት ቀን በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክር ስቶስ ከዚያ ወጥቶ ሁለተኛ ወደገሊላ ሄደ ከተመ ችን ብላችሁ በአንድ ቦታ አትኑሩ ወጥታችሁ ወርዳችሁ አስተምሩ ለማለት አብነት ለመሆን ።

፵፬ ወለሊሁ እግዚእ ኢየሱስ ሰማዕተ ኮነ ከመ ኢይከብር ነቢይ በሀገሩ ። ማቴ፣፲፫፣፶፯ ማር፣ ፮፣፬ ሉቃ፣፬፣፳፬ ።

፵፬ አኮ እንከ በነገረ ዚአከ ዘአመነ ቦቱ ብለዋት ነበርና ካሀን በሀገሩ እንዳይከብር ጌታችን እሱ ራሱ መሰከረ።በዚያ ያልተያያዘ በሉ ቃስ የተያያዘ ።

፵፭ ወበዊአ ገሊላ ተቀበልዎ ኵሎሙ ገሊ ላውያን ። ማቴ፡፬፣፲፪ ማር፣ ፩፣፲፬ ሉቃ ፬፣፲፬ ዮሐ፣ ፪፣፲ ።

፵፭ ተራ ዋዊ አንድም ወበዊአ ገሊሳ ተቀ በልዎ ኵሎሙ ገሊላውያን ብሎ ነበርና ገሊላም በገባ ጊዜ የገሊላ ሰዎች ሁሉ አመኑበት ።
እስመ ርእዩ ኵሎሙ ተአምረ ዘገብረ በኢየሩሳ ሌም አመ በዓል ።
ለገቢረ በዓል ወጥቶ ሳለ በኢየሩሳሌም ያደረገ ውን ተአምራት ሁሉ አይተዋልና ።
እስመ እሙንቱኒ ሖሩ ለበዓል እርሳቸውም ለበ ዓል ወጥተው ነበርና ።

፵፮ ወሖረ ካዕበ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ገሊላ ኀበ ረሰየ ማየ ወይነ ።

፵፮ ጌታችንም ውኀውን ጠጅ ወዳደረገበት ወደ ቃና ሁለተኛ ሄደ ፣
ወሀሎ ሀየ አሐዱ ገብረ ንጉሥ ሰብእ አብያታዊ ።
አብያታዊ ገንዘብ ያለው ገብረ ንጉሥ እለ ማዕዜመ እገብር ቤተ ለርእስየ ወያጠርያ አብያተ እምጽድቀ ዚአሆን እለ ትበልዑ አብያተ መበ ለታት እንዲል ።
አንድም ቤተሰብነት ያለው ባሪያ ቢወልድ ፍና ጅን ፣ ፍናጅ ፣ ቅናጅን ፣ ቅናጅ አሰሰጥን ፣ አሰ ሰጥ አመለጥን ፥ አመለጥ ማን ቤቴን ማን ቤቴ ደረባ ብቴን ወይደዊ ወልዱ በቅፍርናሆም ሀሎ ይደዊ ። ልጁ በቅፍርናሆም ታሞ ነበር ።

፵፯ ወሰሚዖ ከመ መጽአ እግዚእ ኢየሱስ እምይሁዳ ውስተ ገሊሳ ሖረ ኀቤሁ ወሰአሎ ከመ ይረድ ወያሕዩ ሎቱ ወልዶ ።

፵፯ ጌታ ከይሁዳ ወደገሊላ እንደ መጣ ሰምቶ በሰማ ጊዜ ወርደህ ልጄን አድንልኝ ብሎ ለመነው ።
እስመ አልጸቀ ይሙት ።
ሊሞት ቀርቦ ነበርና ።

፵፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ እመ ተአምረ ወመንክረ ኢርኢክሙ ኢተአምኑ ።

፵፰ ጌታም ተአምራት ካላያችሁ አታምኑም አላቸው ።

፵፱ ወይቤሎ ውእቱ ገብረ ንጉሥ ስብእ እብያ ታዊ እግዚኦ ረድ ፍጡነ ዘእንበለ ይሙት ወልድየ ።

፵፱ ያም ገብረ ንጉሥ አቤቱ ልጄ ሳይሞት ፈጥነህ ወርደህ አድንልኝ አለው ድውይ መፈወስ እንጂ ሙት ማስነሣት የማይቻለው መስሎት ።

፶ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር ወልድከሰ ሐይወ ።

፶ ጌታም አንተ አላመንከም እንጂ ልጅህስ ድኖልሃል ሂድ አለው ። አንድም እመ ተአምረ ወመንከረ ኢርኢክሙ ብለህ መልስ ። ተአምራት ካላያችሁ አታምኑምን አለው ፤ ማመኑንም አምናለሁ ይልቁንም ሳይሞት ፈጥነህ ወርደህ አድንልኝ አለው ወይቤሎ ወልድከሰ ሐይወ ። አንተ በጐ አምነኸ ልጅህም ድኖልሃል አለው ።
ወአምነ ውእቱ ብእሲ በቃል ዘይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ወሖረ ።
ያም ሰው ጌታ ወልድከሰ ሐይወ ባለው ቃል አምኖ ሄደ ።

፶፩ ወእንዘ ይወርድ ተቀበልዎ አግብርቲሁ ፤
፶፩ ሲሄድ ብላቴኖቹ ተገናኙት ።

ወዜነውዎ ወይቤልዎ ወልድከሰ ሐይወ አንተ በመከራ ስንብትሃል እንጂ ልጅህስ ድኑዋል ። አንድም አንተም በጐ መጣህ ልጅህም ድኖልሃል ብለው ነገሩት ።
ወተስአሎሙ ሰዓታ እንተ ባቲ መጠነ ወይቤሎሙ ዓየ ጊዜ ሐይወ ።
የሰፈረውን ሰዓት ጠየቃቸው የዳነው ምን ጊዜ ነው አላቸው ።

፶፪ ወይቤልዎ ትማልም ጊዜ ሰብዓቱ ሰዓት ኀደጎ ፈጸንቱ ።

፶፪ እርሳቸውም ትናንት በሰባት ሰዓት ሆድ ዝማው ተወው አሉት አሕዛብ ጠንቃቆች ናቸውና ወልድከሰ ሐይወ ባለው ጊዜ ሰዓቱን ሰፍሮታል ።

፶፫ ወአእመረ አቡሁ ከመ ጊዜ ይእቲ ሰዓት እንተ ይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ወልድከሰ ሐይወ ።

፶፫ አባቱም ልጁ የዳነ ፤ ጌታ ልጅህስ ድኖልሃል ባለው ሰዓት እንደሆነ ዓወቀ ።
ወአምነ ቦቱ ውእቱ ።
እርሱም አመነ ።
ወኵሉ ሰብአ ቤቱ ።
የቤቱም ሰዎች ።

፶፬ ወዝንቱ ካዕበ ትእምርተ ለእግዚእ ኢየሱስ ዘገብረ ተአምረ መጺአ እምይሁዳ ውስተ ገሊላ ።

፶፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከይሁዳ ወደ ገሊላ መጥቶ ያደረገው ተአምራቱ ሁለተኛው ይህ ነው ፤ ለሐልዮው ፤ ለቦታው ወነውን በሐልዮ ጠጅ እንዳደረገው ፤ በሐልዮ አድኖ ነውና ወልድከሰ ሐይወ ፤ ያለው ። ለቦታው ምንም ድውዩ ያለው በቅፍርናሆም ቢሆን ወልድከስ ሐይወ ያለው በገሊላ ሆኖ ነውና ።

በእንተ ምጥማቃት ዘጽሩጸጥቄ ።

ምዕራፍ ፭ ።

፩ ወእምድኅረዝ ኮነ በበዓሎሙ ለአይሁድ ዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ። ዘሌ. ፳፱ ፭ ዘዳ. ፲፯. ፩ ።

፩ ኮነ ያለውን ዓርገ ብሎ አመጣው ዝ ሲናገረው የመጣው ነው ፤ ከዚህ በኋላ አይሁድ በዓል በሚያከብሩበት ቀን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ ኢየሩሳሌም ወጣ ። ተራ በዓል ነው ፤ አንድም ያልታወቀ በዓል አንድም ሠረቀ ወርኅ ። አንድም ሁለተኛ ፋሲካ ነው ። ያንስ ኋላ ያመጣዋል ብሎ በውስጥ በሚያመጣው ቀዳም ።

፪ ወቦ ውስተ ኢየሩሳሌም ምጥማቃት ዘጽሩጸጥቄ ቅልንብትራ ።

፪ በኢየሩሳሌም መጠመቂያ ነበር ዘጽሩጸጥቄ ዘፈውስ ዘበዓል ዘመሥዋዕት ዘጉባኤ ዘአባግዕ ቅልንብትራ ። ባንዱ ልሳን ቅልንብትራ የምትባል ፤ ወይቤልዋ ስማ በዕብራይስጥ ቤተ ሳይዳ ወይእቲ ቤተ ሣህል በዕብራይስጥ ቤተ ሳይዳ ትባላለች ፤ ዘውእቱ ቤተ ሣህል ።
ቤተ ሳይዳም ማለት ቤተ ሣህል ማለት ነው ።
ወይእቲ ቀላየ አባግዕ ።
ቀላየ ዓባግዕ ዓጸደ አባግዕ ዓዘቅተ አባግዕ ምጥማቀ አባግዕ ምሕማሰ አባግዕ ይላል ንው ነሐምስ እንዲል ትግሬ ። ያችም የበጐች መጠመቂያ ናት ወባቲ ኃምስቱ ሕዋራት ።
አምስት እርከን አምስት መደብ አላት እርከን እንደ ቍስቋም ፤ መደብ እንደ ማንኪት

፫ ወሀየ ይሰክቡ ብዙኃን ድውያን ።
፫ በእርከኑ በመደቡ ብዙ ድውያን ይተኛሉ ዕውራን ድውያን ያለውን ይተረትረዋል ።

| | |
|---|---|
| ዕውራን ። | የታወሩ ። |
| ሐንካሳን ። | አንካሶች ። |
| ወይቡሳን ። | የሰለሉ ። |
| ወጽውሳን ፤ | ልምሹ የሆኑ ። |

**ወጽቡሳን ፣**
የተድበለበሉ ። ይተኛሉ ።
**ወይጸንሁ ሁከተ ማይ ።**
የውኀውን መናወጥ ይጠብቁ ነበሩ ።

፬ እስመ መልአከ እግዚአብሔር በጊዜ ይወርድ ውስተ ምጥማቃት ይትኀወከ ማይ ።

፭ መልአኩ በወረደ ጊዜ ውኀው ይነዋወጽ ነበርና ፣
ወዘይወርድ ቀዲሙ እምድኅረ ሁከተ ማይ ወይትሐ ጸብ የሐዩ እምዙሉ ደዌ ዘቦ ።
**ወሀው** ከተናወጠ በኋላ አስቀድሞ ወርዶ የተጠመቀ ካለበት ደዌ ሁሉ ይድን ነበር ። መልአኩ ስለምን ይወርዳል ቢሉ ለቀድሶተ ማያት ለአዕርጎተ መሥዋ ዕት ። ወኀውስ ስለምን ይናወጥ ነበር ቢሉ መልእኩ እንደ ወረደ ለማጠየቅ ለፈውስ ፣ ይህም ተራ ፀኀ ነው በክረምት የሚሞላ በበጋ የሚጐድል ። አንድም ፈለገ ቄድሮስ ነው ፣ አንድም ሰሎሞን በጥበብ ያገ ባው ወኀ ነው ። አንድም ወኀበ አውፅኡ ማየ ማእ ከለ ከልኤቱ ዓረፍት እንዲል ። ሕዝቅያስና ኢሳይያስ ከስድስተኛው ቆመ ብእሲ ያወጡት ወኀ ነው ቀዳም ቀዳም አንዳንድ ድውይ ይፈወሳል አይቀርም ፣ አይ ደግምም ፣ አለመቅረቱ ተእምራት ባባቶቻችን ጊዜ ይደረጋል እንጂ በኛ ዘመንስ ቀርቷል እንዳይሉ ። እለመደገሙ በአሪት ፍጹም ድኅነት እንዳልተደረገ ለማጠየቅ እስመ አሪት መንፈቀ ፍጻሜ ወኀዳጥ መከ ፈልት እንዲል ። መልእኩ የቀሳውስት ወኀ የጥም ቀት ፭ ዕርከን ያ፭ አዕማደ ምሥጢር ። ፭ ድውያን ያ፭ቱ ጾታ ምእመናን ምሳሌ ፭ቱ ጾታ ምእመናን አዕ ሩግ ወራዙት እንስት ካህናት መነኰሳት። የአዕሩግ ጦራቸው ፍቅረ ንዋይ ነው ማን ይረዳናል ማን ያጸባ ናል እያሉ ገንዘብ ይሰበስባሉ ። ይህን ትቶ በወራዙት ጦር በዝሙት ይቃወማቸዋል በጥምቀት ባገኙት ኀይል ድል ይነሱታል የወራዙት ጦር ዝሙት ነው ይህን ትቶ በፍቅረ ንዋይ ይዋጋቸዋል በጥምቀት ባገ ኙት ኀይል ድል ይነሡባታል ። የአንስት ጦራቸው ትውዝፍት ነው የምንዝር ጌጥ ። ይህን ትቶ በሌላ ጦር ይዋጋቸዋል በጥምቀት ባገኙት ኀይል ድል ይነሡታልና ። የካህናት ጦራቸው ትዕቢት ነው አእ ምሯችን ረቂቅ መዓርጋችን ምጡቅ እያሉ ይታበያሉ ይህን ትቶ በሌላ ጦር ይቃወማቸዋል በጥምቀት ባገ ኙት ኀይል ድል ይነሡታል። የመነኰሳት ጦራቸው ስስት ነው በሹት ጊዜ እያገኙትምና ይህን ትቶ በእ ንስሐስሖ ዘበከንቱ ይቃወማቸዋል በጥምቀት ባገ ኙት ኃይል ድል ይነሡታልና ።

፮ ወሀሎ ሀየ ፩ ብእሲ ዘሠላሳ ወሰመንቱ ክረ ምቱ እምዘ ደወየ ።

፯ ከታመመ ሠላሳ ስምንት ዓመት የሆነው ድውይ ከዚያ አለ ።

፰ ወኪያሁ ርእዮ እግዚእ ኢየሱስ ይሰክብ ውስተ ዓራቱ ።

፱ ጌታ እርሱ በደዌ ዳኛ ባልጋቁራኛ እንደ ተያዘ ዐውቆ ። እእመረ ከመ ጐንደየ ውስተ ደዌሁ ።
ይህ ሰው ደዌ ጠንቶበታል ።
በዚህ ሰው ደዌ ዘግይቶበታል አለ ።
ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ትፈቅድኑ ትሕየው ።
ልትድን ትወዳለህን አለው ።

፲ ወአውሥአ ውእቱ ድውይ ።
፲፩ ያም ድውይ መለሰ ።
ወይቤሎ እወ እግዚእ ።
አወን አቤቱ አለው ። እወ እንዲለው ያውቅ የለምን ቢሉ አለዋቂ የነበረ ሥጋን እንደ ተዋሐደ ለማጠ የቀ ። አኮ ኢያእሚሮ ኀቡአተ አላ ከመ የሀብ መካነ ለጥንተ ትስብዕቱ ዘኢያአምር ኀቡአተ እንዲል አን ድም አወቅሁ ብሎ ሥራውን አይተውምና ። አን ድም አስፈቅዶ ለማድረግ በዕለተ ዓርብ በጥፊ የሚ መታው ነውና ያዳነህን ባሉት ጊዜ እርሱ የቀለብሳብ ነቱን አድኖኛል እንጂ አድነኝ ብየው አድኖኛልን እንዳይል ።
አላ ሰብእ አልብየ ከመ ሶበ ይትወሀከ ማይ ያውርደኒ ወይደየኒ ውስተ ምጥማቃት ። ወኀው በተናወጠ ጊዜ ከመጠመቂያው አውርዶ የሚጥለኝ ሰው የለ ኝም እንጂ አለው የሠላሳ ዓመት ጉልማሳ ቢሆው ነጥቆ ይጥለኛል ብሎ ። አንድም አምስት ገበያ ሰው ይከተለው ነበርና አንዱን ያዝልኛል ብሎ ።
ወሶበ እመጽእ አነ ባዕድ ይቀድመኒ ወሪዶ ።
እኔ በመጣሁ ጊዜ ሌላው ቀድሞኝ ወርዶ ይጠመቃል

፲፪ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ተንሥእ ንሣእ ዓራተከ ወሑር ።

፲፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ተነሥተህ አል ጋህን ተሸከመህ ሂድ አለው ። ሐተታ እንደ ማቴዎስ መምህር ኤስድሮስ ግን አልጋው ቅሉ የብረት አልጋ ነው ብለዋል ጽንዓ ተእምራቱን ለማጠየቅ ።

፲፬ ወሐይወ ሶቤሃ ውእቱ ብእሲ ወነሥአ ዓራቶ ወሖረ ።

፲፭ ያም ሰው ፈጥኖ ተነሥቶ አልጋውን ተሸከሞ ሄደ ።
ወሰንበት እሜሃ ውእቱ ዕለት መፃጉዕ የተፈወሰበት ቀኑ ቅዳሜ ነው ። አንድም እስመ ሰንበት እሜሃ ቅዳሜ ነበርና ።

ዘከመ አስተዋደይዎ አይሁድ ለኢየሱስ ።

፲፮ ወይቤልዎ አይሁድ ለውእቱ ብእሲ ዘሐይወ ሰንበት ውእቱ ዮም ። ዘፀ ፳ ፣ ፲፭ ኤር. ፲፯ ፳፩ ።

፲ ያን የዳነውን ሰው አይሁድ ዛሬ ቅዳሜ ነውና ወኢይከውነከ ትጹር ዓራተከ ፡፡ አልጋህን ተሸከመህ ልትሄድ አይገባህም አሉት ወኢታብኡ ጾረ ከቡደ ውስተ ኆዋሕዊሃ ለኢየሩሳሌም በዕለተ ሰንበት ፡፡ ያለውን የኤርምያስን ቃል ይዘው ትዝ ብሏቸው ብትል ፡፡
ወአውሥአ ውእቱ ብእሲ ፡፡ እሱም መለሰ ፡፡

፲፩ ወይቤሎሙ ዘአሕየወኒ ውእቱ ይቤለኒ ተንሥእ ንሣእ ዓራተከ ወሑር ፡፡

፲፩ ያዳነኝ እሱ አልጋህን ተሸከመህ ሂድ አለኝ አላቸው ፡፡

፲፪ ወተስእልዎ አይሁድ ወይቤልዎ መኑ ውእቱ ብእሲሁ ዘይቤለከ ጹር ዓራተከ ወሑር ፡፡

፲፪ ተነሥተህ አልጋህን ተሸከመህ ሂድ ያለህ ማነው ብለው አይሁድ ጠየቁት ፡፡

፲፫ ወውእቱሰ ዘሐይወ ኢያእመረ መኑ ወእቱ ዘአሕየዎ ፡፡

፲፫ የዳነው እርሱ ግን ያዳነውን ማንም እንደ ሆነ አላወቀም ነበር ፡፡ እስመ ተሰወረ እግዚእ ኢየሱስ ማእከለ ብዙኃን ሰብእ እለ ሀለዉ በውእቱ መካን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዚያ ቦታ ባሉ በብዙ ሰዎች መካከል ተሰውሮ ነበርና ይህ ቅሉ ከሰንፍና አያወጣውም እንኳን ይህን ያህል ሥራ የሠራለትን ጥቂት ሥራ የሠራለትን ስንኳን ጠይቆ ማወቅ ይገባ ነበር ፡፡

፲፬ ወእምዝ በሳኒታ ረከቦ ካዕበ እግዚእ ኢየሱሰ ለውእቱ ዘሐይወ በምኵራብ ፡፡

፲፬ ከዚህ በኋላ ጌታ ያን ያዳነውን ሰው በምኵራብ አገኘው ፡፡ ወይቤሎ ናሁኬ ሐየውከ ፡፡
እነሆ ከደዌህ ድነሃል ፡፡
ዑቅ ኢተአብሰ ዳግመ እንከ ከመ ዘየአኪ ኢይርከብከ ፡፡
እንግዲህ ከዚህ የጠና እንዳያገኝህ ሁለተኛ እንዳትበድል አስተውል አለው ፡፡ ከዚህ የጠና ምን አለ ቢሉ የቀድሞው ደዌ ሥጋ ነበር ፡፡ ዛሬ ግን ደዌ ነፍስ ነው ይህም አልቀረ በዕለተ ዓርብ ጌታን በጥፊ ቢመታው የመታበት እጁ ስሎ ደርቆ ቀርቷል ፡፡ ሐተታ ደዌ ዘንጽሕ ደዌ ዘዕሤት ደዌ ዘመቅሠፍት ደዌ ዘኃጢአት አለ ፡፡ ደዌ በንጽሕ እንደ ጢሞቴዎስ ፡፡ ደዌ ዘዕሤት እንደ ኢዮብ ደዌ ዘመቅሠፍት እንደ ሳኦል እንደሄሮድስ ደዌ ዘኃጢአት እንደዚህ ሰው ፡፡

፲፭ ወሖረ ውእቱ ብእሲ ወነገሮሙ ለአይሁድ ከመ እግዚእ ኢየሱስ ውእቱ ዘአሕየዎ ፡፡

፲፭ ያም ሰው ሄዶ ያዳነው ጌታ እንደሆነ ለአይሁድ ነገራቸው ፡፡

፲፮ ወበእንተ ዝንቱ ያስተዋድይዎ አይሁድ ለእግዚእ ኢየሱስ ፡፡

፲፮ ስለዚህም አይሁድ ጌታን ያጣሉት ያሳጡት ያካስሱት ነበር ወየኀሥሥዎ ይቅትልዎ ፡፡
ሊገሉት ይፈልጉ ነበር ፤
እስመ ከመዝ ይገብር በሰንበት ፡፡
ቅዳሜ ድውይ ይፈውስ ነበርና ፡፡

፲፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፡፡
፲፯ ጌታም መለሰ ፡፡
ወይቤሎሙ አቡየሂ እስከ ይእዜ ይገብር ፤
አባቴ እስካሁን ድረስ ሥራ ይሠራል አለ ፤ ሥነ ፍጥረትን ማመላለስ ነው ፡፡
ወአነሂ ካዕበ ከማሁ እገብር ፤
እኔም እሠራለሁ ፡፡ ሥነ ፍጥረትን አመላልሳለሁ ፤ ይህስ ያልያዘው ነው ብሎ ፤ አባቴ ቅዳሜ ቅዳሜ አንዳንድ ድውይ ይፈውስ ነበር ፡፡ ወአነሂ ፤ እኔም ጉሕቁትን መፃጉዕን ፈወስኩ ፡፡

፲፰ ወበእንተ ዝንቱ ፈድፋደ የኃሥሥዎ አይሁድ ይቅትልዎ ፡፡

፲፰ ይልቁንም አቡየ ስላለባቸው አይሁድ ሊገድሉት ይሹ ነበር ፡፡ እስመ አኮ ከመ ሰንበተ ባሕቲቶ ዘይሥእር ፤
የሚሹት ሰንበትን ሻረ ብለው ብቻ አይደለም ፡፡
ዳዕሙ ዓዲ አባሁ ይሬስዮ ለእግዚአብሔር ፡፡
የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ ብሏል ወያዔሪ ርእሶ ምስለ እግዚአብሔር ፡፡ እግዚአብሔር ነኝ ብሏልና ስለዚህም ነው እንጂ ወእምዝ አውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ፡፡
ከዚህ በኋላም ጌታ መለሰ ፡፡

፲፱ ወይቤሎሙ አማን እብለክሙ ኢይክል ወልድ ገቢረ ዘእምኀቤሁ ወኢምንተኒ ፡፡

፲፱ ወልድ ከራሱ ብቻ አንቅቶ ምንም ምን ሥራ አይሠራም ፡፡
ዘእንበለ ዘርእዮ ለአብ ይገብር ከአብ በህልውና ያየውን በህልውና ያገኘውን ይሠራዋል እንጂ ፡፡ እስመ ግብረ ዘይገብር አብ ወልድኒ ኪያሁ ይገብር በአምሳሉ አብ የሚሠራውን ሥራ ወልድም ይሠራዋልና ፡፡

፳ እስመ አብ ያፈቅር ወልዶ ወኵሎ ያሬእዮ ዘውእቱ ይገብር ፡፡

፳ አብ ልጁን ይወደዋልና በህልውና የሚሠራውን ያሳየዋል ፡፡
ወዘየዓቢ እምዝ ያሬእዮ ግብረ ያበላልጣል ፡፡ ድውይ ከመፈወስ ሙት ማንሣት እንዲበልጥ ከዚህም የበለጠ ሥራ ያሳየዋል ፣ ከመ ፣ አንትሙ ታእምሩ ወታንክሩ ፡፡ እናንተ ታምኑ ዘንድ ወአንክረቶ ኵላ ምድር እንዲል

፳፩ ወበከመ አብ ያነሥኦሙ ለምውታን ወያ
ሐይዎሙ ።

፳፩ አብ ሙታንን እንዲያሥነሣቸው እንዲያድ
ናቸው ።
ከማሁ ወልድኒ ለዘፈቀደ ያሐዩ ወልድም ሊያድነው
የወደደውን ያድነዋል ፈቀደ ለሁለቱም ነው ።

፳፪ እስመ አብሰ ኢይኴንን ወኢመነሂ ።
፳፪ አብ ታይቶ ማንንም ማንን አይገዛም ።
ታይቶ በማንም በማን አይፈርድም ።
አላ ኵሎ ኵነኔሁ አወፈዮ ለወልዱ ።
ታይቶ መግዛትን ታይቶ መፍረድን ለልጁ ሰጠው
እንጂ ።

፳፫ ከመ ኵሉ ሰብእ ያክብርዎ ለወልድ በከመ
ያከብርዎ ለአብ

፳፫ ሰው ሁሉ አብን ወላዲ ወልድን ተወላዲ
ይለው ዘንድ ። ወዘሰ ኢያከብሮ ለወልድ ኢያከብሮ
ለአብ ለዘፈነዎ ።

ወልድን የማያከብረው አብን አያከብረውም
ማለት ወልድን ተወላዲ የማይለው ግን አብን ወላዲ
አይለውም ። አባት አልባ ልጅ ። ልጅ አልባ አባት
የለምና ።

፳፬ አማን አማን እብለክሙ ዘይሰምዕ ቃልየ
ወየአምን በዘፈነወኒ ይረክብ ሕይወተ ዘለዓለም ።

፳፬ ያበላልጣል ። ሙት ከማንጣት ትንሣኤ
ሕሊና እንዲበልጥ ። የኔን ቃል ሰምቶ አብ በላከኝ
በኔ ። እኔን በላከኝ በአብ ያመነ የማታልፍ መንግሥተ
ሰማያትን ይወርሳል ።
ወኢየሐውር ውስተ ደይን ።
ወደገሃነም አይሄድም ።
አላ አደወ እሞት ውስተ ሕይወት ።
ከሞት ወደሕይወት ይሄዳል እንጂ ።

፳፭ አማን አማን እብለከሙ ከመ ይበጽሕ
ጊዜሁ ።

፳፭ ከትንሣኤ ሕሊና ትንሣኤ ልቡና እንዲ
በልጥ ፤ ጊዜው እንዲደርስ በውነት እነግራችኋለሁ
ወይእዜ ውእቱ ከመ ምውታን ይሰምዕዎ ቃሎ ለወ
ልደ እግዚአብሔር ።
ሙታነ ሕሊና የእግዚአብሔርን ልጅ ትምህርቱን
የሚቀበሉበት ጊዜም ዛሬ ነው ።
ወእለሰ ይሰምዕዎ የሐይዉ ።
ትምህርቱን የሚቀበሉት ትንሣኤ ልቡና ይነሣሉ ።

፳፮ ወበከመ ለአብ ቦቱ ሕይወት ኀቤሁ ።
፳፮ ለአብ ሕይወትነት የባሕርዩ እንደሆነ ሕይ
ወት እንዳለው ። ከማሁ ለወልድኒ ወሀቦ ሕይወተ
ከመ ይኩን ሕይወት ኀቤሁ ሕይወት የባሕርዩ ይሆን
ዘንድ ሕይወትን ሰጠው ።

፳፯ ወወሀቦ ሥልጣነ ከመ ይግበር ፍትሐ ወኵ
ነኔ ።

፳፯ ይፈርድ ዘንድ ፤
እስመ ወልደ እግዚአብሔር ወልደ ዕጓለ እመ ሕያው
የእግዚአብሔር ልጅ የሰው ልጅ ነውና ። ወሀቦ ሕይ
ወተ ። ቦ ዘይቤላ መጻሕፍት በእንተ ትስብእቱ እን
ዲል ። አንድም የሰው ልጅ የእግዚአብሔር ልጅ
ነውና ። ከመ ይግበር ፍትሐ ላለው ፤ ወቦ ዘይቤላ
መጻሕፍት በእንተ መለኮቱ እንዲል አንድም ወልደ
እግዚአብሔር ነውና ፤ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ነውና
ወሀቦ ሕይወተ ከመ ይግበር ፍትሐ ። ቦ ዘይቤላ መጻ
ሕፍት በእንተ ትስብእቱ ወበእንተ መለኮቱ ኀቡረ
እንዲል ።

፳፰ ወበእንተ ዝንቱሰ ኢታንክሩ ።
፳፰ ይኸንንስ አታድንቁ ።

እስመ ትመጽእ ሰዓት ወይበጽሕ ጊዜሁ በዘይሰም
ዕዎ ቃሎ ለወልደ እግዚአብሔር ኵሎሙ እለ ውስተ
መቃብር ።
ያበላልጣል ከትንሣኤ ልቡና ደገኛው ትንሣኤ ሥጋ
እንዲበልጥ ። በመቃብር ያሉ ቃሉን የሚሰሙበት
ጊዜ ይደርሳልና ።

፳፱ ወይወፅኡ እለ ሠናየ ገብሩ ውስተ ትንሣኤ
ዘለሕይወት ። ማቴ ፳፭፣ ፯ ።

፳፱ በጎ ሥራ የሠሩ ሁሉ በሕይወት በሚያ
ኖር ትንሣኤ ይነሣሉ ።
ወእለሰ እኩየ ገብሩ ይትነሥኡ ውስተ ትንሣኤ ዘለ
ደይን ። ክፉ ሥራ የሠሩ ግን በስቃይ ለመኖር በስቃይ
በሚያኖር ትንሣኤ ይነሣሉ ።

፴ ኢይክል አንሰ ገቢረ ለልየ ዘእምኅቤየ ወኢ
ምንትኒ ።

፴ እኔ ምንም ምን ከራሴ ብቻ አንቅቼ አላስተ
ምርም ። አላ በከመ ሰማዕኩ እኴንን ። በሀልወና
እንደሰማሁ የሰማሁትን አስተምራለሁ እንጂ ።
ወኵነኔየኒ ጽድቅ ውእቱ ።
ትምህርቴም እውነት ነው ።
እስመ ኢየኃሥሥ ፈቃደ ዚአየ ዘእንበለ ፈቃዱ ለዘ
ፈነወኒ የላከኝ ያባቴን ፈቃድ ሳያደርግ እወዳለሁ እንጂ
የኔ ፈቃድ ሊደረግ አልወድምና። አንድም የኔ ፈቃድ
ካባቴ ፈቃድ ልዩ ሁኖ የኔ ፈቃድ ሊደረግ አልወድም
የኔ ፈቃድ ካባቴ ፈቃድ ጋራ አንድ ነውና ያባቴ
ፈቃድ ሊደረግ እወዳለሁ እንጂ ።

፴፩ ወእመሰ ለልየ ሰምዓ ኮንኩ ለርእስየ ኢኮነ
ጽድቀ ስምዕየ ።

፴፩ እኔ ለራሴ ብመስክር ምስክርነቴ እውነት አይደለም የርሱ ሐሰት ሁኖ አይደለም ንጹሐን ነን በሚሉ ዘለፋ ሊሆንባቸው ነው እንጂ እርሱስ በሐልዮ እንዳልሠራ ለማጠየቅ ። ይመጽእ መልአኩ ለዝንቱ ዓለም ወኢይረክብ በላዕሌየ ወኢምንተኒ ብኳል በነቢብም እንዳልሠራ ለማጠየቅ ነቢይ ኢገብረ ኃጢአተ ወ ኢተረክበ ሐሰት ውስተ አፉሁ ብሎ መስክሮ ለታል በገቢርም እንዳልሠራ ለማጠየቅ ። መኑ ይዛለፈኒ በእንተ ኃጢአት ብኳል ። ንጹሐን ነን በሚሉ መፈራረጃ ሊሆንባቸው እንዲህ አለ እንጂ ።

፴፪ ወባሕቱ ካልዕ ውእቱ ስማዕትየ ማቴ፡ ፫ ፲፯ ፣ ዮሐ. ፩ ፡ ፲፭ ።

፴፪ ምስክሬ ሌላ ነው አለ ። ዮሐንስ ፣ ፩ም ተአምራት ፡ መጻሕፍት አብ ወእእምር ከመ ጽድቅ ውእቱ ስምዑ ዘስምዓ ኮነ በእንቲአየ ስለኔም የመሰከረው ምስክሩ እውነት ነው ።

፴፫ አኮኑ አንትሙ ለአክሙ ኀበ ዮሐንስ ።
፴፫ እናንተ ወደ ዮሐንስ ልካችሁ አልነበረምን

ወነገረክሙ ስምዖ በጽድቅ በእንቲአየ ።
ስለኔ ምስክርነቱንስ በውነት ነግሯችሁ አልነበረምን።

፴፬ ወአንሰ አኮ ስምዓ ሰብእ ዘእፈቅድ ።
፴፬ ነገርግን እኔ የሰውን ምስክርነት አልሻም።

ወባሕቱ ዘንተ ዘእብል ከመ አንትሙ ትእመኑ ወትድኃኑ ። ነገር ግን ይኸን የምናገር እናንተ ታምኑ ትድኑ ዘንድ ነው እናንተ ታምኑ ትድኑ ዘንድ ይህን እናገራለሁ እንጂ ፣

፴፭ ወዝንቱ ውእቱ ማኅቶት ዘያሐቱ ወያበርህ
፴፭ የሚያበራ ፋና ይህ ነው ። ከዚያ ወለሊሁስ ኢኮነ ብርሃን አለ ፣ ከዚህ እንዲህ አለ እንደምን ነው ቢሉ ፀሐይ በወጣ ጊዜ የፋናን ብርሃን የሚሻው እንደሌለ ጌታም ባስተማረ ጊዜ የዮሐንስን ትምህርት የሚሻው የለምና የዮሐንስንትምህርት በፋና የጌታን ትምህርት በፀሐይ መስሎ ተናገረ ። አንድም ፋና ለመጣለት ነው የሚያበራ ፀሐይ ግን ለሁሉ ነው ። እንደዚህም ሁሉ ዮሐንስ ያስተማረ ለመጣለት ነው ጌታ ያስተማረ ለሁሉ ነውና የዮሐንስን ትምህርት በፋና የጌታን ትምህርት በፀሐይ መስሎ ተናገረ ።

፴፭ ወአንትሙ ፈቀድክሙ ትትፈሥሑ፡ በብርሃኑ እሐተ ሰዓተ ።

፴፮ እናንተ በትምህርቱ መንፈቅ ደስ ሊላችሁ ወደዳችሁ ።
ወአንሰ ብየ ስማዕት ዘየዓቢ እምስምዓ ዮሐንስ ።
እኔ ግን ከዮሐንስ ምስክርነት የሚበልጥ ምስክር አለኝ ።
እስመ ዝንቱ ግብር ዘወሀበኒ አቡየ እግበር ወእፈጽም ውእቱ ግብር ዘእገብር ሰማዕትየ ከመ አብ ፈነወኒ ።
በአብ ፈቃድ ሰው እንደሆንኩ ልሠራው ልፈጽመው አባቴ ገንዘብ ያደረገልኝ ተአምራት ምስክሬ ነው ።

፴፯ ወአቡየ ዘፈነወኒ ውእቱ ሰማዕትየ፥ ማቴ ፫፥ ፲፯ ዘዳ፥ ፩፥፲፱ ።

፴፯ የላከኝ አባቴም ምስክሬ ነው ።
ወእም አመ ኮንክሙ ቃሎ ኢሰማዕክሙ ።
ከሆነ ጀምሮ ማለት ወልድየ ዘበሁርየ ከተባላችሁ ጀምሮ ቃሉን በደብረ ሲና አልሰማችሁም ።
ወራእዮሂ ኢርኢክሙ ።
መልኩን አላያችሁም ።

፴፰ ወቃሉሂ አልብክሙ ወኢይነብር ኀቤክሙ
፴፰ ዓሥርቱ ቃላትን አልተቀበላችሁም ።አንድም ወእምአመ ኮንክሙ እያልክ መልስ ። ወልድየ ዘበሁርየ ከተባላችሁ ጀምሮ ቃሉን በደብረ ታቦር አልሰማችሁም ወራእዮሂ ። መልክአ መለኮቱን አላያችሁምን ። ወቃሉሂ ፣ ወንጌልን አልተቀበላችሁም ። አንድም ወልድየ ዘበሁርየ ከተባላችሁ ጀምሮ ወንጌልን አልተቀበላችሁም ። ወራእዮሂ ፣ መልክአ መለኮቱን አላያችሁም ወቃሉሂ ። አካላዊ ቃል አላደረባችሁም ። እንድም ስለሥጋዌ የተነገረውን ትንቢት አልተቀበላችሁም ።

እስመ ዘውእቱ ፈነወ ኪያሁ ኢአመንክሙ ።
እሱ በላከው አላመናችሁምና ።

፴፱ ኅሡ ትርአዩ ውስተ መጻሕፍት እንተ ቦቶን ይመስለክሙ ትረክቡ ሕይወተ ዘለዓለም ።

፴፱ በንባባቸው ብቻ የዘላለም ድኅነትን የምታገኙባቸው የሚመስሏችሁ መጻሕፍትን ሹ መርምሩ ።
አንድም እስመ ቦቶን ።
በንባባቸው ብቻ የዘላለም ድኅነት የምታገኙባቸው ይመስላችኋልና ። አንድም የዘላለም ድኅነት የምታገኙበት ሃይማኖትን የምትረዱባቸውን አንድም የዘላለም ድኅነትን የምታገኙበት ሃይማኖትን ትረዱባቸዋላችሁና መጻሕፍትን ሹ መርምሩ ወእማንቱ ሰማዕትየ ። መጻሕፍት ምስክሮቼ ናቸው ።

፵ ወኢትፈቅዱ ትምጽኡ ኀቤየ ከመ ትርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም ።

፵ ድኅነትን ታገኙ ዘንድ በኔ ልታምኑ አትሹም

፵፩ አንሰ ኢይፈቅድ ያድሉ ሊተ ሰብእ ።
፵፩ እኔ ግን የሌለኝን እምላክነት ሰው አምላክ ነህ ሊለኝ አልሻም ።

፵፪ ወባሕቱ አመርኩክሙ ከመ አልብክሙ ፍቀረ እግዚአብሔር ላዕሌክሙ ።

፵፪ ነገር ግን ፍቅረ እግዚአብሔር እንዳላደረባ ችሁ ነገርኳችሁ። አጠየቁከሙ ይላል አስረዳኋችሁ።

፵፫ አነ መጻእኩ በስመ አቡየ ወኢተወከፍክ ሙኒ ።

፵፫ እኔ ባባቴ ስም ፡ አባቴ ባወጣልኝ ስም ።
በስምዓ አቡየ ፡ አባቴ መስክሮልኝ መጣሁ ።
ወኢተወክፍክሙኒ ።
አላመናችሁብኝም ።
ወእመ መጽአ ካልዕ በስመ ነፍሱ ኪያሁ ትትዌከፉ
ሐሳዌ መሲሕ ግን ራሱ ባወጣው ስም ፤ አንድም
ራሱ በመሰከረው ምስክር በመጣ ጊዜ ታምኑበታላ
ችሁ ።

፵፬ እፎ ትክሉ አንትሙ አሚነ ዘተጋሥሡ ክብረ እምቢጽከሙ ወኢተኃሥሡ ክብረ እምኀበ እግዚአብሔር ባሕቲቱ ዋሕድ ፩ ቀሮ ፩፫ ።

፵፬ ከእግዚአብሔር ክብርን የማትሹ እንደና ናንተ ካለ ከዕሩቅ ብእሲ ክብርን የምትሹ እናንተ በኔ ማመን እንደምን ይቻላችኋል ። እፎ ትክሉ አን ትሙ አሚነ ዘታበድሩ አድልዎ ለቢጽከሙ እምታደ ልው ለዘባሕቲቱ እግዚአብሔር ዋሕድ ይላል ። ተዋ ርዳችሁ ተምራችሁ እግዚአብሔርን ብቻ አክብረን ብትሉት ይልቅ ለባልጀሮቻችሁ መስሎ መታየትን የምትወዱ እናንተ በኔ ማመን እንደምን ይቻላችኋል

፵፭ ኢይምሰልከሙ ዘአነ አስተዋድየክሙ ኀበ አብ ።

፵፭ እኔ ወደአብ የማጣላችሁ የማካስሳችሁ አይ ምስላችሁ ። አላ ሀሎ ሙሴ ዘያስተዋድየክሙ ዘኪ ያሁ ትትዌከሉ ወትሴፈው ።
እናንተ ተስፋ የምታደርጉት የሚያጣላችሁ የሚያ ሳጣችሁ ሙሴ አለ እንጂ ።

፵፮ ሶበሰ አመንክምዎ ለሙሴ ኪያየኒ እምአመ ንክሙኒ ። ዘፍ ፫ ፲፭ ዘዳ. ፲፰ ፲፭ ።

፵፮ ሙሴንስ ተቀብላችሁት ቢሆን እኔንም በተ ቀበላችሁኝ ነበር ፤ እስመ በእንቲአየ ጸሐፈ ውእቱ ። እርሱ ስለኔ ጽፏልና ።

፵፯ ወእመሰ ዘጸሐፈ ሙሴ ኢተአምኑ እፎ ቃልየ ተአምኑ ።

፵፯ ሙሴ የጻፈውን ካልተቀበላችሁ ትምህርቴን እንደምን ትቀበሉኛላችሁ ።

ምዕራፍ ፮ ።

፩ ወእምድኅረ ዝንቱ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ ማዕዶተ ባሕረ ገሊላ ኀበ ጥብርያዶስ ። ማቴ ፲፬ ፲፫ ማር ፮ ፴ ሉቃ. ፱፥ ፱-፲ ።

፩ ዝ ሲናገረው የመጣ ነው ከዚህ በኋላ ጌታ ችን በገሊላ ባሕር ማዶ ወደጥብርያዶስ ሄደ አንድም የገሊላ ባሕር ማዶ ወደሚሆን ወደጥብርያዶስ ሄደ ።

፪ ወተለውዎ ብዙኃን አሕዛብ ።
፪ ብዙ ሰዎች ተከተሉት ።
እስመ ርእዩ ተአምረ ዘገብረ በላዕለ ድውያን ።
ድውይ ሲፈውስ አይተዋልና ።

፫ ወዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ደብር ወህየ ነበረ ምስለ አርዳኢሁ ።

፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከተራራ ላይ ወጥቶ ከዚያ ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ተቀመጠ ።

፬ ወቀርበ በዓለ ፋሲካሆ ሙ ለአይሁድ ።
፬ አይሁድ በዓል የሚያከብሩበት ቀን ደረሰ ።
፭ ወአንሥአ እግዚእ ኢየሱስ አዕይንቲሁ ወር
እየ ብዙኃነ ሰብአ እንዘ ይመጽኡ ኀቤሁ ።

፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዓይኑን አራምዶ ብዙ ሰዎች ወደሱ ሲመጡ አየ ። ርእየን ቢያዩ ብዙ ኃነ ሰብአ ይመጽኡን ቢያዩ ብዙኃን ሰብእ
ወይቤሎ ለፊልጶስ እምአይቴ ንሣየጥ ኅብስተ ዘናበ ልዮሙ ለእሉ ።
ፊልጶስን ለኔህ ሰዎች የምንመግባቸውን ኅብስት ከወ ዴት እንገዛለን ከየት እንግዛ አለው ።

፮ ወዘንተ ዘይቤ እንዘ ያሜክሮ
፮ እንዲህ ያለው ሊፈትነው ነው ወዘንተ ይቤ ሊፈትነው እንዲህ አለው ። የሚያመጣውን ቢናገር ሕጸጹን ለመግለጥ ። አንተ ኅብስት አበርክተህ ትመግባቸው የለምን ቢለው ብፅዓን ለመስጠት ነው ።
ወውእቱሰ የአምር ዘሀለዎ ይግበር ።
እርሱ ግን ሊያደርገው ዘንድ ያለውን ያውቅ ነበር ማለት ። ኅብስት አበርክቶ እንዲመግባቸው ።

፯ ወአውሥአ ፊልጶስ ።
፯ ፊልጶስም መለሰ ።
ዘክልኤ ምእት ዲናር ኅብስት ኢየአክሎሙ
ከመ ይንሥኡ በበሕቅ ለለ ፩ እምኔሆሙ ፤
በሁለት መቶ ወቄት በሁለት ድሪም የተገዛ ኅብስት ክርሳቸው ወገን ጥቂት ጥቂት ማለት አንዳንድ ጉርሻ አይደርሳቸውም አለው ።

፰ ወይቤሎ አሐዱ እምአርዳኢሁ ዘውእቱ እን ድርያስ እኁሁ ለስምዖን ጴጥሮስ ሀሎ ዝየ ወልድ ዘቦቱ ኃምስ ኅብስተ ሰገም ወክልኤቲ ዓሣት ።

፰ የስምዖን ጴጥሮስ ወንድም ከደቀ መዛ ሙርቱ አንዱ እንድርያስ አምስት የገብስ እንጀራ ሁለት ዓሣ የያዘ ብላቴና ከዚህ አለ አለው ። ሁሉም ሕጸጻቸውን ለመግለጥ ነው ።

፰ ወባሕቱ ምንተ ይበቍዓ እማንቱ ለዘመጠ ነዝ ሰብእ ።

፱ ነገር ግን እሊህ ለዚህን ያህል ሰው ምን ይበቃሉ ።

፲ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ግበሩ ምርፋቃተ ለሰብእ ።

፲ ጌታም ይህስ ካለ መቀመጫውን አሰናዱ አላቸው ።
ወብዙኅ ማዕሩ ለውእቱ መካን መስኩ በዚያ ሥፍራ እጅግ ምቹ ነበረ ። ግበሩ ያለው ምኑን ነው ቢሉ ዕንጨቱን ድንጊያውን አንሱላቸው ሲል ።
ወረፈቁ ዲበ ማዕር አደዊሆሙ። ወንዶችም ከመስኩ ተቀመጡ ወየአክሉ ፶፻ ብእሲ ።
አምስት ሺህ ሰው ያህል ናቸው ።

፲፩ ወነሥአ እግዚእ ኢየሱስ ውእተ ኅብስተ ።
፲፩ ጌታም እንጀሮችን አንሥቶ ያዘ ።
ወአእኰተ ።
አመስገነ ።
ባረከ ወፈተተ ። ገመሰ ቈረሰ ወወሀቦሙ ለአርዳኢሁ ስጡ ብሎ ለደቀ መዛሙርቱ ሰጣቸው ።
ወአርዳኢሁኒ አቅረቡ ለሰብእ እለ ይረፍቁ ።
ደቀመዛሙርቶቹም ለተቀመጡት ሰዎች አቀረቡ ።
ወእምዓሣሁኒ ከማሁ መጠነ ፈቀዱ ።
ከዓሣውም የሚሹትን ያህል ሰጧቸው ፤

፲፪ ወእምድኅረ በልዑ ወጸግቡ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ አስተጋብኡ ዘተርፈ ፍተታተ ከመ ኢይትገደፍ ወኢምንተኒ እምኔሆን ።

፲፪ በልተው ከጠገቡ በኋላ ደቀመዛሙርቱን አንሡ ከርሳቸው ምንም ምን እንዳይቀር አላቸው ።

፲፫ ወአስተጋብኡ ። ሰበሰቡ ።
፲፫ ወመልኡ ዓሠርተ ወክልኤተ መሳይምተ እምኃምስቱ ኅብስተ ሰገም ዘተርፈ እምዘ በልዑ ወጸግቡ ።
በልተው ከጠገቡ በኋላ ከተረፈው ከቀረው የተረፈው የቀረው ቍርስራሽ ዐሥራ ሁለት መሶብ ዐሥራ ሁለት ቅርጫት መላ ። ወትትሐነጺ ፣ ምዘነሠቱኪ ወእምዘረወዩ አግማሊሁ ነሥአ ኢያውብር አዕኑገ ዘወርቅ እንዲል ። የበረከተ ኅብስት መገናኛ እንደ ምን ነው ቢሉ እንደ ዮሐንስ ። ወአንሥአ እግዚእ ኢየሱስ አዕይንቲሁ ወርእየ ብዙኃነ ሰብአ እንዘ ይመጽኡ ኀቤሁ ወይቤሎ ለፊልጶስ እምአይቴ ንሣየጥ ኅብስተ ዘናበልዖሙ ለእሉ አላቸው ፣ ወምሴተ ከዊኖ እንደ ማቴዎስ ። ወእምድኅረ ብዙኅ ሰዓት እንደ ማርቆስ ፣ ወተቀልቀለ ፀሐይ እንደ ሉቃስ ፤ መገናኛ ዮሐንስ ፣ በተገናኝ ፣ ሲመሽ ማለት ነው ። ፈንዎሙ ማቴዎስ ፣ ሠዓር ሰብአ ማርቆስ ፣ ፍትሖሙ ሉቃስ ፣ መገናኛው ዮሐንስ በተገናኝ አሰናብት አሉት አሰናብት ቢሉት እንደ ፫ቱ አኮ መፍትው ይሑሩ ርኁባኒሆሙ አላ ሀብዎሙ አንትሙ ዘይበልዑ አላቸው እንደ ማርቆስ ፣ ንሑርኑ ንሣየጥ በ፪፻ ዲናር ኅብስተ ዘናበልዖሙ ለእሉ ይሉታል ። እንደ ዮሐንስ ፣ ዘ፪፻ ዲናር ኅብስት ኢየአክሎሙ ከመ ይንሥኡ በበሕቅ ለለ ፩ዱ እምኔሆሙ አሉት ፣ እንደ ማርቆስ ፣ ሑሩ ወርእዩ ሚመጠን ኅባውዝ ብከሙ ይላቸዋል ። እንደ ሦስቱ አልብነ ዝየ ዘእንበለ ኃምስ ኅብስት ወክልኤቲ ዓሣት እንደ ዮሐንስ ፣ ሀሎ ዝየ ወልድ ዘቦ ኃምስ ኅብስት ሰገም ወክልኤቲ ዓሣት ፣ እንደ ሉቃስ ፣ ለእመ ኢሖርነ ንሣየጥ ይሉታል ። ይህንስ ተታችሁ ግበሩ ምርፋቃተ ይላቸዋል ፣ ይኸንስ ለምን ይሻዋል ቢሉ ከውንድሞቹ ለማያያዝ ስማያዊ ኅብስትን የሚያመጣ ነውና ከርሱ ለማነጻጸር ።

፲፬ ወርእዮሙ ሕዝብ ዘገብረ ተአምረ እግዚእ ኢየሱስ ይቤሉ አማን ነቢይ ውእቱ ዝንቱ ዘመጽአ ውስተ ዓለም ።

፲፬ ሕዝቡ ጌታ ያደረገውን ተአምራት አይተው ነቢየ ያንሥኢ ተብሎ የተነገረለት በውነት ወደዚህ ዓለም የመጣው የአብ የባሕርይ ልጅ ነው አሉ ።

ዘከመ ሖረ ኢየሱስ ዲበ ማይ

፲፭ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ይመጽኡ ይምስጥዎ ወያንግሥዎ ተግኅሠ ውስተ ደብር ባሕቲቶ ።

፲፭ ቢራቡ ያመስል ። ቢታመሙ ይፈውሳል ። ቢሞቱ ያሥነሣል እንዲህ ያለውን ቢያነግሡት ምን ይብሳል ብለው ይዘው ሊያነግሡት እንደመደዱ አውቆባቸው ለብቻው ወደ ተራራ ሄደ እንሹማችሁ ባሏችሁ ጊዜ ሽሹ አትገኙ ለማለት አብነት ለመሆን መውጣቱ ግን ሰው የማያነግሠኝ ልዑለ ባሕርይ ነኝ ሲል ።

፲፮ ወመስዮ ወረዱ አርዳኢሁ ውስተ ባሕር ።
፲፮ ሲመሽ በመሸ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ወደ ባሕር ወረዱ ።

፲፯ ወዐርጉ ሐመረ ወሖሩ ማዕዶተ ባሕር ኀበ ቅፍርናሆም ።
፲፯ በመርከብም ሁነው በባሕር ማዶ ወደቅፍርናሆም ሄዱ ።
ወናሁ ኮነ ጽልመት ወድአ ።
ፈጽሞ ጨልሞ ነበር ።
ወዓዲሁ ኢመጽአ እግዚእ ኢየሱስ ኀቤሆሙ ።
ጌታ ግን ገና አልመጣም ነበር ።

፲፰ ወባሕርስ ይትሀወክ ።
፲፰ ባሕሩም ይነዋወጥ ነበር ።
እስመ ዓቢይ ነፋስ ይነፍሕ ውስቴቱ ።
ጽኑ ነፋስ ተነሥቷልና ይነፍሳልና ።
፲፱ ወቀዘፉሙ መጠነ ፳ወ፭ቱ ምዕራብ ።
፲፱ ሀያ አምስት ምዕራፍ ከሄዱ በኋላ ።
አው ሠላሳ ።
ወይም ፴ ምዕራፍ ከሄዱ በኋላ ፤
ርእይዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እንዘ የሐውር ዲበ ባሕር ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን በባሕር ላይ ሲሄድ አዩት
ማጠራጠሩ ስለምን ነው ቢሉ የባሕር ነገር በዓይነ
ገመድ ነው እንጂ ለሥፍር አይመችምና ግብርም እን
ዳይገባለት ነገሩ ተራ ቢሆንበት ። አንድም በዓቢይ
፳፭ በንኡስ ፴ ምዕራፍ።ወሶበ ቀርበ ኀበ ሐመሮሙ።
ወደ መርከቡ በቀረበ ጊዜ ።
ወፈርኁ ወደንገፁ ፈሩ ።

፳ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ወኢ
ትፍርኁ ።

፳ ጌታም እኔ ነኝ አይዟችሁ አትፍሩ አላቸው ።
፳፩ ወእንዘ ይፈቅዱ ያዕርግዎ ውስተ ሐመር በጽ
ሐት ሐመር ሶቤሃ ውስተ ምድር ኀበ ፈቀዱ ይሑሩ ።

፳፩ ወደመርከብ እናወጣዋለን ሲሉ መርከቢቱ
ሊሄዱባት ወደ ወደዱባት ወደብ ደረሰች ፡ ማቴዎስ
ወዓረገ አለ ፡ ከዚህ እንዲህ አለ ። እንደምን ነው አይ
ጣላም ቢሉ አይጣላም ፡ ነገር እንደ ማቴዎስ ነው ።
ምድር ቤትና ደርብ ነው ከምድር ቤቱ ወጥቷል
ከደርቡ አልወጣምና ዮሐንስ አልወጣም አለ አንድም
ነገር እንደ ዮሐንስ ነው ። አልወጣም ማቴዎስ ወዐ
ረገ ማለቱ ነፋሱ ማዕበሉን በመርከቡ ልክ ያወጣው
ነበር ጌታም ማዕበሉን እየተረገጠ በመርከቡ ልክ
ይታይ ነበርና ።

፳፪ ወበሳኒታ ሰብእ ብዙኅ እለ ይቀውሙ ማዕ
ዶተ ባሕር ርእዮሙ ከመ አልቦ ህየ ካልዕ ሐመር
ዘእንበለ አሐቲ ሐመር ።

፳፪ ሳኒታን አቆየው ። ሁለት መርከብ ነበር
ባንዱ ሐዋርያት ሄደውበታል ። ከባሕሩ ማዶ ያሉ
ሰዎች ካንዲት መርከብ በቀር ሌላ መርከብ እንደሌለ
ባዩ ጊዜ ፤
ወከመ ኢዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ምስለ አርዳኢሁ
ውስተ ሐመር ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም በመርከብ ተጭኖ ከደቀ
መዛሙርቱ ጋራ እንዳልሄደ ባዩ ጊዜ ።
አላ አርዳኢሁ ባሕቲቶሙ ሖሩ
ደቀ መዛሙርቱ ብቻቸውን ሄደዋል እንጂ ።

፳፫ ወመጽአ ካልዓትኒ አሕማር እምጥብርያ
ዶስ ቅሩብ ብሔር ኀበ በልዑ ኅብስተ ዘባረከ እግዚእ፤።

፳፫ ሌሎችም መርከቦች ጌታችን ኢየሱስ ክር
ስቶስ ኅብስት አበርክቶ ካበላበት ቦታ አቅራቢያ
ከሚሆን ከጥብርያዶስ መጡ ።

፳፬ ወሶበ ርእዩ እሙንቱ ሰብእ ከመ ኢሀሎ
እግዚእ ኢየሱስ ህየ ።

፳፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ከዚያም እን
ደሌለ ባዩ ጊዜ ።
ወኢአርዳኢሁ ።
ደቀ መዛሙርቱም እንደሌሉ ባዩ ጊዜ ።
ዓርጉ ውስተ ውእቶን አሕማር ።
በሳኒታ ዓርጉ ባለ ፤ በነጋው በቀረው መርከብ ከጥ
ብርያዶስም በመጡት መርከቦች ተጭነው ።
ወሖሩ ወበጽሑ ቅፍርናሆም ይኅሥሥዎ ለእግዚእ
ኢየሱስ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን እየፈለጉት ሄዱ ። ቅፍ
ርናሆም ደረሱ ። አንድም ወበሳኒታ ብለህ መልስ ።
የሕሊና አስተያየት ነው ። አንድ መርከብ ነበር በር
ሱም ሐዋርያት ሄደውበታል ፡ አንድ መርከብ እንደ
ነበረ ያውም እንደሌለ ባዩ ጊዜ ፤ ወከመ ኢዓርገ
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ
በመርከብ እንዳልሄደ ፤ አላ አርዳኢሁ ደቀ መዛ
ሙርቱ ብቻ ሄደዋል እንጂ ወመጽአ ካልዓትኒ አሕ
ማር ፤ እምጥብርያዶስ ሌሎች መርከቦችም ከጥብ
ርያዶስ መጡ ።
ወሶበ ርእዩ ። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ከዚያ
እንደሌለ ወኢአርዳኢሁ ፤ ደቀ መዛሙርቱም እንደ
ሌሉ ባዩ ጊዜ ዓርጉ ውስተ ውእቶን አሕማር ።
ከጥብርያዶስ በመጡት መርከቦች ተጭነው ጌታ
ችንን እየፈለጉት ቅፍርናሆም ደረሱ ።

፳፭ ወሶበ ረከብዎ በማዕዶተ ባሕር ይቤልዎ
ረቢ ማእዜ መጻእከ ወበጻሕከ ዝየ ።

፳፭ ባሕሩን ተሻግሮ ባዩት ጊዜ መምህር ሆይ
ከዚህ ምን ጊዜ መጣህ ምን ጊዜ ደረስህ አሉት ።

፳፮ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳፮ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎሙ አማን አማን እብለክሙ ከመ አኮ አን
ትሙ ዘተኃሥሡኒ በእንተ ዘርኢክሙ ተአምራተ ።
እናንተ የምትሹኝ ተአምራት ስላያችሁ እንዳይደለ
በውነት እነግራችኋለሁ ።
አላ በእንተ ዘበላዕክሙ ኅብስተ ወጸገብክሙ ።
ኅብስት አበርክቼ ስለአበላኋችሁ ነው እንጂ ።

፳፯ ተገበሩ እንከሰ ። ማቴ፫ ፤ ፲፫ ዮሐ ፩ ፡ ፴፪
፳፯ ከእንግዲህስ ወዲህ ጻሩ ።
አኮ ለመብልዕ ኃላፊ ።
መጣራችሁም ለኃላፊው መብል አይደለም ።

አላ ለመብልዕ ዘይነብር ለሕይወት ዘለዓለም ዘይ ሁበክሙ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
የዘላለም ሕይወት ሊሆን የሰው ልጅ ክርስቶስ ለሚ ሰጣችሁ ለማያልፈው ምግብ ነው እንጂ ።
እስመ ለዝሰ እግዚአብሔር ሐተሞ ።
ይኸነን ሥጋዊውን ምግብ እግዚአብሔር አብ አሳ ልፎታልና ።
አኮ ለመብልዕ ኃላፊ ፤ ወገጸ ከዋክብት የሐትም እን ዲል አንድም ሥጋን ራሱን አስመስሎታልና ።
አላ ለመብልዕ ዘይነብር ለሕይወት ዘለዓለም በከመ የሐትሙ እለ የሐትሙ መዓረ ግራ በማኅተመ ወርቅ እንዲል ።
የኔን አምላክነት ሰውሮታል እኮን የኔን አምላክ ነትስ ሰወረው ኅትም ወኢትጽሐፍ እንዲል ።

፳፰ ወይቤልዎ ምንተ ንሬሲ ከመ ንግበር ግብረ እግዚአብሔር ፤

፳፰ እግዚአብሔር የሚወደውን ሥራ እንሠራ ዘንድ ምን እናድርግ ንሬሲ ምን እናደርጋለን አሉት።

፳፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ። ፩ ዮሐ፡ ፫፡ ፳፫
፳፱ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ዝንቱ ውእቱ ግብረ እግዚአብሔር ከመ ትእመኑ በዘፈነዎ ውእቱ ።
እግዚአብሔር የሚወደው ሥራ እርሱ በላከኝ በኔ እንድታምኑ መሆን ነው ።

፴ ወይቤልዎ ምንተ ተአምረ ትገብር ከመ ንርአይ ወንእመን ብከ በዘገበርከ ።

፴ የሠራኸውን ሥራ አይተን በሠራኸው ሥራ እናምንብህ ዘንድ ምን ሥራ ትሠራለህ አሉት ።

፴፩ አበዊነሰ መና በልዑ በገዳም ዘፀ፡ ፲፮ ፡ ፲፬ ዘኍ፡ ፲፩ ፡ ፯ መዝ፡ ፸፰ ፡ ፯-፳፭ ዮሐ፡ ፲፯ ፡ ፳ ።

፴፩ ኅብስት አበርክቼ መግቤያችሁ የለምን ትላለን እንደሆን እንዲህ ያለስ ቀድሞ አባቶቻችን መናውን ተመግበዋል ።
በከመ ጽሑፍ ኅብስተ እምሰማይ ወሀቦሙ ይብልዑ። ሰማይን አይሻውም ሊመገቡት መናውን ሰጣቸው ተብሎ ተጽፎ እንዳለ ፤

፴፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን አማን እብለክሙ አኮ ሙሴ ዘወሀበክሙ ውእተ ኅብስተ እምሰማይ ።
መናውን ሙሴ አልሰጣችሁም ።
አላ አቡየ ወሀበክሙ ኅብስተ ጽድቅ እምሰማይ ።

፴፪ ነገር ግን አባቴ እውነተኛ እንጀራ ከሰማይ ሰጣችሁ መናውንስ ኅብስተ ጽድቅ አይለውም ብሎ ኅብስተ ጽድቅ እኔን ሙሴ አልሰጣችሁም አባቴ ሰጣችሁ እንጂ ፤ አንድም ከመ እምላዕሉ አውረድከ ሥጋ ይለዋል በሊቁ ብሎ ከሰማይ ሥጋ ይዘህ እንደ መጣህ ምን ምልክት አለህ አሉት ፤
አበዊነሰ ፤ ኅብስት አበርክቼ መግቤያችሁ የለም ትለን እንደሆነ ይህስ ያለውን ማበርከት ነው የሌለ ውንስ አባቶቻችን መናውን ተመግበዋል ። በከመ ጽሑፍ ኅብስተ እምሰማይ ወሀቦሙ ይብልዑ ፤ ሊመገቡት ከሰማይ ሰጣቸው ተብሎ ተጽፎ እንዳለ ፤ ወይቤሎሙ አኮ ሙሴ ዘወሀበክሙ እምሰማይ ሙሴ መናውን ከሰማይ አልሰጣችሁም የፍ በበረረ ዘንግ በተወረወረ ከሰማይ ወረደልን ይባላልን ፤ ልብስህ አላለቀ ጫማህ አልወለቀ በትርህ አልወደቀ እንዲሉ፤ ከውቅያኖስ በደመና አይበት ተቋጥሮ በነፋስ ወደ ልጋዝ ተጭኖ መልኩ በረድ መስሎ መጠኑ ድንብ ላል አህሎ ወእንዘ የኃድግ ሀቦ ይላል፤የውርጭ ገበታ እየተነጸፈ አርባ ዘመን እያዘነበላቸው እስራኤል መናውን ተመግበዋልና ፤ አንድም ኅብስተ ጽድቅ እኔን ሙሴ አልሰጣችሁም አባቴ ከሰማይ አውርዶ ሰጣችሁ እንጂ ።

፴፫ እስመ ኅብስቱ ለእግዚአብሔር ውእቱ ዘወ ረደ እምሰማይ ።

፴፫ የእግዚአብሔር ኅብስቱ ከሰማይ የወረደ ነውና ።
ወይሁብ ሕይወተ ዘለዓለም ።
የዘለዓለም ድኅነትንም ለሰው ይሰጣልና ።

፴፬ ወይቤልዎ እግዚኦ ሀበነ በኵሉ ጊዜ እም ውእቱ ኅብስት ።

፴፬ አቤቱ ዘወትር ከዚያ ኅብስት ስጠን አሉት።
፴፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ኅብስተ ሕይወት ።

፴፭ ጌታም የሕይወት እንጀራ እኔ ነኝአላቸው።
ዘመጽአ ኀቤየ ኢይርኅብ ።
ወደኔ የመጣ ማለት በኔ ያመነ አይራብም ።
ወዘሂ የአምን ብየ ኢይጸምዕ ለዝሉፉ ።
በኔ ያመነም ለዘላለም አይጸማም ። አንድም በኔ ያመነ ረኃበ ነፍስ ጽምዓ ነፍስ የለበትም ።

፴፮ ወእቤለክሙ ባሕቱ ርኢክሙኒሂ ወኢአ መንክሙኒ ።

፴፮ ነገር ግን አይታችሁኝ አልተቀበላችሁ ኝም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፴፯ ወኵሉ ዘወሀበኒ አቡየ ይመጽእ ኀቤየ ።
፴፯ አባቴ በሀብት ስቦ በረድኤት አቅርቦ የሰጠኝ ሁሉ በኔ ያምናል ።
ወለዘሂ መጽአ ኀቤየ ኢይሰድዶ ወኢያወፅኦ አፍአ ።
በኔ ያመነውንም ከመንግሥተ ሰማይ አፍአ ወደ

ገሃነም አላወጣውም ፤ ከቀደመው ሀገረ ምስካይ ሲለይ ከገባ በኋላ ኃጢአቱ ተመርምሮ ወጥቶ ይደ በደባል ። መንግሥተ ሰማይ ግን ከገቡ መውጣት ካገኙ ማጣት የለምና ።

፴፰ እስመ ወረድኩ እምሰማይ አኮ ከመ እግበር ፈቃድየ ።

፴፰ ከሰማይ የወረድኩ የኔን ፈቃድ ላደርግ አይደለም ።
ዘእንበለ ፈቃዱ ለዘፈነወኒ ።
የላከኝ ያባቴን ፈቃድ ላደርግ ነው እንጂ ። አንድም የኔ ፈቃድ ካባቴ ፈቃድ ልዩ ሁኖ የኔን ፈቃድ ላደ ርግ ሰው አልሆንኩም አልወረድኩም የኔ ፈቃድ ካባቴ ፈቃድ ጋራ አንድ ነውና ያባቴን ፈቃድ ላደ ርግ ነው እንጂ ፤

፴፱ ወዝንቱ ውእቱ ፈቃዱ ለዘፈነወኒ አብ ።
፴፱ የላከኝ ያባቴም ፈቃድ ይህ ነው ።
ከመ ኵሉ ዘወሀበኒ ኢይትኀጐል እምኔሆሙ ወኢ አሐዱሂ ።
በኔ ካመኑ አንዱ ስንኳን እንዳይጐዳ መሆን ነው ።
አላ አነ አነሥኦ በደኃሪት ዕለት ።
በዕለተ ዓርብ አሥነሣዋለሁ ።

፵ ወዝንቱ ውእቱ ፈቃዱ ለዘፈነወኒ አብ ።
፵ የላከኝም ያባቴ ፈቃድ ይህ ነው ።
ከመ ኵሉ ዘርእዮ ለወልድ ወአምነ ቦቱ ይረክብ ሕይወተ ዘለዓለም ።
ወልድን አይቶ ያመነበት ሁሉ የዘላለም ድኅነትን ያገኝ ዘንድ ነው ።
ወአነ አነሥኦ በደኃሪት ዕለት ።
በዕለተ ትንሣኤ አድነዋለሁ ።

፵፩ ወአንጐርጐሩ አይሁድ በእንቲአሁ እስመ ይቤሎሙ አነ ውእቱ ኅብስተ ሕይወት ዘወረደ እም ሰማይ ።

፵፩ ከሰማይ የወረደ የሕይወት እንጀራ እኔ ነኝ ስላላቸው አይሁድ በርሱ ምክንያት ታወኩ ።
፵፪ ወይቤሉ አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ኢየሱስ።

ወልደ ዮሴፍ ዘለሊነ ነአምር አባሁ ወእሞ ። ማቴ፡ ፲፫ ፡ ፶፭ ማር፡ ፮ ፡ ፫ ።

፵፪ እኛ አባት እናቱን የምናውቅ የዮሴፍ ልጅ አይደለምን ።
ወእፎ እንከ ይእዜ ይብለነ እምሰማይ ወረድኩ ።
አወይ ውሸት አወይ ማታለል እንደምን ከሰማይ ወረድኩ ይለናል አሉት ።
፵፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፵፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ኢታንጐርጕሩ በበይናቲክሙ ።
እናንት በናንት አትታወኩ አላቸው ።

፵፬ አልቦ ዘይክል መጺአ ኀቤየ እመ ኢስ ሐቦ አብ ዘፈነወኒ ።

፵፬ የላከኝ አባቴ በሀብት ስቦ በረድኤት አቅ ርቦ ካልሰጠኝ በኔ ማመን የሚቻለው የለም ።
ወአነ አነሥኦ በደኀሪት ዕለት በዕለተ ዕርገት አድ ነዋለሁ ፤ አንድም በጰራቅሊጦስ ።

፵፭ ወሀሎ ጽሑፍ ውስተ መጽሐፈ ነቢያት ከመ ይከውኑ ኵሎሙ ምሁራነ እምኀበ እግዚአ ብሔር ። ኢሳ ፶፬ ፡ ፲፫

፵፭ ሁሉ ከእግዚአብሔር ተምረው አዋቆች ይሆናሉ የሚል በመጽሐፈ ነቢያት አለ ። ኢሳይያስ ደቂቅኪ ይከውኑ ምሁራነ በኀበ እግዚአብሔር ያለውን ፤ ኤርምያስ ወኢይምህር እኁ እኁዋሁ እንዘ ይብል አእምርዎ ለእግዚአብሔር እስመ ኵሎሙ የአምሩኒ ንኡሶሙ ወዓቢዮሙ ያለውን ዕንባቆም ትመልእ ምድር እምአእምሮ ስብሐተ እግዚአብሔር ከመ ማይ ዘይደፍን ባሕረ ያለውን ለውጦ አነበበው ። መጽሐፈ ነቢይ ያለ እንደሆነ ኢሳይያስን ብቻ ።

፵፮ ወኵሉ እንከ ዘሰምዓ እምኀበ አቡየ ተም ሒሮ ይመጽእ ኀቤየ ። ማቴ ፲፩ ፡ ፳፯

፵፮ ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ብሎ ሲመሰክር ልኝ የሰማ ሁሉ ዐውቆ በኔ ያምናል ።
ወአልቦ ዘርእዮ ለአብ ዘእንበለ ዘእምኀቤሁ ለእግ ዚአብሔር ውእቱ ።
ከርሱ አካል ዘእም አካል ባሕርይ ዘእምባሕርይ ከተወለደ ከልጁ በቀር አብን በባሕርዩ ያየው የለም።
ወውእቱኬ ርእዮ ለአብ ።
እሱን አባቱን አየው እንጂ ።
አንድም ከነቢያት ወገን ልጅ ሁኖ ያየው የለም ልጁ ልጅ ሁኖ አየው እንጂ ።

፵፯ አማን አማን እብለክሙ ዘየአምን ብየ ቦ ሕይወት ዘለዓለም ።

፵፯ በኔ ያመነ መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል ብኖ በውነት እነግራችኋለሁ ።
፵፰ አነ ውእቱ ኅብስተ ሕይወት ።
፵፰ የሕይወት እንጀራ እኔ ነኝ ።
፵፱ አበዊክሙሰ መና በልዑ በገዳም ወሞቱ ፡ ዘፀ፡ ፲፮ ፡ ፲፭ ።

፵፱ አባቶቻችሁ መናውን በሉ በምድረ በዳ ክሞት አላዳናቸውም ።

፶ ዝንቱ ውእቱ ኅብስት ዘእምሰማይ ወረደ ከመ ኵሉ ዘበልዓ እምኔሁ ኢይመውት ዘለዓለም ።

፶ ከርሱ የበላ ሁሉ በሥጋ ቢሞት በነፍስ እንዳይሞት ፈርሶ በሰብሶ እንዳይቀር ትንሣኤ ዘለ ክብር እንዲነሣ ከሰማይ የወረደ ኅብስት ይህ ነው ።

፶፩ አነ ውእቱ ኅብስተ ሕይወት ዘወረደ እም ሰማይ ።

፶፩ ከሰማይ የወረደ ኅብስት እኔ ነኝ ።
ወዘበልዐ እምዝንቱ ኅብስት የሐዩ ለዓለም ።
ከዚህ ኅብስት የበላም ለዘላለም ሕያው ሆኖ ይኖራል።
ወዝኒ ኅብስት ዘአነ እሁቦ ሥጋየ ውእቱ በእንተ ሕይወት ዘለዓለም ።
ሥጋየ በእንተ ሕይወት እሁቦ በእንተ ሕይወት ብለህ ግጠም የዘለዓለም ሕይወት ሊሆንእኔ የምሰ ጠው ኅብስት ሥጋዬ ነውእንድም እኔ የምሰጠው ኅብስት ሥጋዬ ነው ።
በእንተ ሕይወት ዘለዓለም ።
የዘለዓለም ሕይወት ሊሆነው ።

፶፪ ወተገአዙ አይሁድ በበይናቲሆሙ እንዘ ይብሉ እፎ ይክል ዝንቱ የሀበነ ሥጋሁ ንብላዕ ።

፶፪ ሥጋውን እንበላ ዘንድ ሥጋውን መስጠት ይህ እንደምን ይቻለዋል ብለው እርስ በርሳቸው ተከራከሩ ። እሁበከሙ ቢላቸው እአላፈ እስራኤል ብዙ ነን ፤ አንዳንድ ጉርሻ ስንኳን ይደርስናል ብለው፤ ትብልዑ ቢላቸው ማን እገድልሃለሁ ብሎታል ታን ቆን ይሞታል ብለው ፤ ሥጋየ በእንተ ሕይወት ቢላ ቸው የዕሩቅ ብእሲ ሥጋ ቢበሉት ደሙን ቢጠጡት ደዌ ይሆናል እንጂ ሕይወት ይሆናልን ብለው ።

፶፫ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን እብለ ክሙ እመ ኢበላዕክሙ ሥጋሁ ለወልደ ዕጓለ እመ ሕያው ወኢሰተይክሙ ደሞ አልብክሙ ሕይ ወት ላእሌክሙ ።

፶፫ ጌታም የሰውን ልጅ ሥጋውን ካልበላችሁ ደሙንም ካልጠጣችሁ ለናንተ ሕይወት የላችሁም ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ።

፶፬ ዘበልዐ ሥጋየ ወስተየ ደምየ ቦ ሕይወት ዘለዓለም ።

፶፬ ሥጋዬን የበላ ደሜን የጠጣ የማታልፍ መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል ። ፈረንጆች ደም የሌለው ሥጋ የለም ብለው ሥጋውን ብቻ ያቈርባሉ ይህ ይመሰክርባቸዋል ።
ወአነ አነሥኦ በደኀሪት ዕለት ።
በዕለተ ምጽአት አድነዋለሁ ።

፶፭ እስመ ሥጋየኒ መብልዓ ጽድቅ ዘበአማን ውእቱ ።

፶፭ ሥጋዬ እውነተኛ መብል ነውና ።
ወደምየኒ ስቴ ሕይወት ውእቱ ።
ደሜም እውነተኛ መጠጥ ነውና ።

፶፮ ዘበልዐ ሥጋየ ወስተየ ደምየ ይሄሉ ምስሌየ።
፶፮ ሥጋዬን የበላ ደሜን የጠጣ ከኔ ጋራ ተዋ ሕዶ ይኖራል ።
ወአነሂ እሄሉ ምስሌሁ ፤
እኔም አድሬበት እኖራለሁ እንደ ብረትና እንደ እሳት የጸጋ ተዋሕዶ ።

፶፯ ወበከመ ፈነወኒ አብ ሕያው ።
፶፯ የላከኝ አብ ሕያው እንደሆነ ።
ወአነሂ ሕያው በእንተ አብ ።
እኔም ከአብ አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእምባሕ ርይ ስለተወለድኩ ሕያው ነኝ ።

፶፰ ወዘበልዐ ሥጋየ የሐዩ በእንቲአየ ።
፶፰ ሥጋዬን የበላ ሥጋዬን ስለበላ ሕያው ሆኖ ይኖራል ።

፶፱ ዝኬ ውእቱ ኅብስት ዘእምሰማይ ወረደ ።
፶፱ የሚገባ ኬ ፤ ከዚያ ሁሉ ቅዱስ ጳውሎስ የብሉዩንና የሐዲሱን ሊቀ ካህናት እያነጻጸረ የሐ ዲሱን ሊቀ ካህናት እያበለጠ መጥቶ ። ዘከመ ዝኬ ሊቀ ካህናት ይደልወነ እንዳለ ፤ ከዚህም ምድራዊ ውንኅብስትና የሰማያዊው ን ኅብስት እያነጻጸረ ሰማያ ዊውን ኅብስት እያበለጠ መጥቶ ከሰማይ የወረደ ኅብስት ይህ ነዋ ይህ ነው አለ ።
ወአኮ በከመ በልዑ አበዊክሙ መና በገዳም ወሞቱ ።
አባቶቻችሁ መናውን በገዳም በልተውት ከሞት እንዳላዳናቸው ያለ አይደለም ።
ወዘበልዖስ ለዝንቱ ኅብስት የሐዩ ለዓለም ።
ከዚህ ኅብስት የበላ ግን ለዘለዓለሙ ሕያው ሆኖ ይኖራል ።
በእንተ ዕቅፍት ወእልወት ዘእምአርድዕተ ኢየሱስ ።

፷ ወከመዝ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ በም ኵራብ በቅፍርናሆም እንዘ ይሜህሮሙ ።

፷ በቅፍርናሆም ባለ ምኵራብ ሲያስተም ራቸው ጌታ ይኸን ነገራቸው ።

፷፩ ወብዙኃን እምአርዳኢሁ እለ ሰምዑ ወይ ቤሉ ዕፁብ ዝንቱ ነገር ።

፷፩ ከደቀ መዛሙርቱ ወገን ይኸን ሰምተው ይኸን ነገር ድንቅ ነው ያሉ አሉ ።
ወመኑ ይክል ሰሚዖቶ ።
መስማት ለማን ይቻለዋል አሉ መስማትማ ጆሮ መብረቅስ ይስማ የለምን ፤ ለብዎቶ ሲል ነው ማወቁ ለማን ይቻለዋል አሉ ።
፷፪ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ በመንፈሱ ከመ አን ጐርጐሩ አርዳኢሁ በእንተ ዝንቱ ።

፷፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ሕዝቡ በዚህ ምክንያት እንደታወኩ በአእምሮው ዐውቆ ፡፡
ወይቤሎሙ ዝኑ የአቅፈክሙ ፡፡
ይኽ ይደንቃችኋልን ፡፡
እፎ እንከ እመ ርኢክምዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው እንዘ የዓርግ ኀበ ሀሎ ቀዲሙ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ክርስቶስ ቀድሞ ወደነበረበት ሲወጣ ብታዩ እንደምን በደነቃችሁ ነበር አላቸው ፡፡ ምነው ከርደቱ ዕርገቱን አብልጦት ነውን ሁሉስ የአምላክነት ሥራ አይደለምን ቢሉ መሆኑስ ሁሉም የአምላክነት ሥራ ነው ሲወርድ ያየው የለም ሲያርግ ግን ሁሉ ያየዋልና ፤ ስውም ካላየው ያየውን ማድነቅ ልማድ ነውና ስው በሚያደንቀው ተናገረ እንጂ አንድም ዝኑ የዐቅፈክሙ እያልክ መልስ ፡፡ ይህ ይደንቃችኋል ኋላ እዋሕጀ አሥነሥቼ በመንግሥተ ሰማይ መንፈሳዊ ምግብ ስመግባችሁ ብታዩ እንደምን ባደነቃችሁ ነበር ፡፡ ይኽን በምን ያውቁታል ቢሉ ኅብስት አበርክቶ በመመገቡ ፤ አንድም ይህን ይደንቃችኋል ወእፎ እንከ ይህን ዓለም እምኀበ ቦ ኀበ አልቦ ከመኖር ወዳለመኖር ሳሳልፈው ብታዩ እንደምን በደነቃችሁ ነበር ፡፡ ይኽን በምን ያውቁታል ቢሉ በደረቅ ግምባር ዓይን በመፍጠሩ፡፡

፷፫ መንፈስ ውእቱ ዘያሐዩ ፡፡ ዮሐ፥ ፫ ፣ ፲፫፡፡
፷፫ የሚያድን መለኮት ነው ፡፡
ወሥጋስ አልቦ ዘይበቍዕ ወኢምንትኒ ፡፡
ሥጋ ግን አንዳች አይጠቅምም ፡፡
ወዝኒ ቃል ዘአነ ነገርኩክሙ መንፈስ ውእቱ ወሕይወት ውእቱ ፡፡

ይኽም የምነግራችሁ ነገር መለኮት ነው ሕይወት ነው ፡፡ አንድም መንፈስ ውእቱ እያልክ መልስ ፡፡ የሚያድን መለኮት ነው ፡፡ ወሥጋስ ሥጋ ግን አያድንም ፡፡ ኅብስትስ መብልዕ ይእቲ አላ ኃይል እንተ ኃደረት ላዕሌሁ ይእቲ ትገብሮ እንዲል ፡፡ መብላት የሰውነት ማደን የመለኮት ነውና ፡፡ አንድም የሚያነፃ መለኮት ነው ፡፡ ወሥጋስ ፡፡ ሥጋ ግን ተነሽ ነው ፡፡

ወኢየንሥእ እመንገለ ሥጋሁ ድኩም አላ በኃይለ እግዚአብሔርእንዲል ፡፡ አንድም ዘየሐዩ ብለህ ሦስት ሌሊት ሦስት መዓልት በከርሠ መቃብር ኑሮ የሚነሣ መለኮት የተዋሐደው ሥጋ ነው ፡፡ የሩቅ ብእሲ ሥጋ ግን በሦስት ቀን አይነሣም ትንሣኤ ዘጉባኤን ይጠብቃል ፡፡ አንድም ዘያሐዩ የሚያድን መንፈሳዊ ትምህርት ነው ወሥጋስ ፡፡ ሥጋዊ ትምህርት ግን ምንም ምን አይረባም አይጠቅምም ፡፡ ይህም የምነግራችሁ ነገር ረቂቅ ነው ሕይወት ነው፡፡

፷፬ ወባሕቱ ቦ እምውስቴትክሙ እለ ኢየአምኑ ፡፡

፷፬ ነገር ግን ከናንተ ወገን የማያምኑ አሉ ፡፡
እስመ የአምር እግዚእ ኢየሱስ እምትካት ከመ መኑ እሙንቱ እለ ኢየአምኑ ቦቱ ፡፡
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከጥንት ጀምሮ የማያምኑበት እነማንም እንደሆኑ ያውቅ ነበርና አይሁድ እንደሆኑ ፡፡
ወመኑ ውእቱ ዘየኀብእ ፡፡
የሚያሲዘውም ማንም እንደሆነ ያውቅ ነበር ይሁዳ እንደሆነ ፡፡

፷፭ ወእምዝ ይቤሎሙ በእንተ ዝንቱ እብለክሙ አልቦ ዘይክል መጺአ ኀቤየ ለእመ ኢተውህበ ሎቱ እምኀበ አቡየ ፡፡

፷፭ ዕውቀቱ ካባቴ ካልተሰጠው ስለዚህ ነገር በኔ ማመን የሚቻለው የለም ብዬ እነግራችኋለሁ ፡፡

፷፮ ወበእንተ ዝንቱ ነገር ብዙኃን እምአርዳኢሁ አለ ገብኡ ድኅሬሆሙ ወኢሖሩ እንከ ምስሌሁ ፡፡

፷፮ ስለዚህ ማለት እንዲህ ስላላቸው ከሕዝቡ ወገን ከርሱ ጋራ ያልሄዱ ወደኋላቸው የተመለሱ ብዙ ናቸው የተናገረው አይቀርም እያደርገውን አይናገር ብለው ፡፡

፷፯ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለ፲ ወ፪ቱ አርዳኢሁ አንትሙኒ ትፈቅዱኑ ትሑሩ ፡፡

፷፯ ዐሥራ ሁለቱን እናንተም ልትሄዱ ትወዳላችሁን አላቸው ፡፡ አኒያስ ወደው ተከትለውታል በኃቻ ይነዳቸዋል እንጂ እንዳይሉት አስፈቅዶ ለማስከተል ፡፡

፷፰ ወአውሥአ ስምዖን ጴጥሮስ ፡፡
፷፰ ስምዖን ጴጥሮስም መለሰ ፡፡
ወይቤሎ እግዚኦ ኀበ መኑ ነሐውር እንዘ ቃለ ሕይወት ዘለዓለም ብከ ፡፡
ጌታዬ የዘለዓለም ደኅንነት የሚገኝበት ትምህርት ካንተ ዘንድ እያለ የት እንሄዳለን አለው ፡፡

፷፱ ወንሕነሰ አመነ ወአእመርነ ከመ አንተ ውእቱ ክርስቶስ ወልዱ ለእግዚአብሔር ሕያው ፡፡

፷፱ እኛስ አስከ ክርስቶስ ንጉሥ ተብሎ የተነገረልህ የሕያው እግዚአብሔር የባሕርይ ልጁ እንደሆንኽ ዐውቀን አምነናል ፡፡

፸ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ አኮኑ አነ ኀረይኩክሙ ለ፲ወ፪ቱ ፡፡ ማቴ፥፲፮ ፣ ፲፯ ማር፥፰ ፣ ፳፱ ሉቃ፥፬ ፣ ፳

፸ ጌታም ዐሥራ ሁለታችሁንማ እኔ መርጫችሁ የለምን ፡፡
ወባሕቱ አሐዱ እምኔክሙ ሰይጣን ውእቱ ፡፡

ነገር ግን ከናንተ አንዱ ሰይጣን ነው ባላጋራዬ ነው
አላቸው ፤ ወኀቀመ አዴርሃ ሰይጣን ላዕለ ስሎሞን
እንዲል ።

፸፩ ወዘንተሰ ዘይቤ እንበይነ ይሁዳ ስምዖን
አስቆሮታዊ ይቤ ።

፸፪ ይኸን ነገር የተናገረ የአስቆሮት ሰው
ስለሚሆን ስለ ይሁዳ ነው ።
እስመ ውእቱ ሀለዎ ያግብኦ ኢሐዱ እም፲ቱ ወ፪ቱ ።
ካሥራ ሁለቱ አንዱ ይሁዳ ያሲዘው ዘንድ አለውና ።

ዘከመ ሖረ ኢየሱስ ኀበ በዓለ መጸለት ።

ምዕራፍ ፯ ።

፩ ወእምድኅረ ዝንቱ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ
ውስተ ገሊላ ።

፩ ከዚህ በኋላ ጌታ ወደ ገሊላ ሄደ ።
ወኢፈቀደ ይሑር ምድረ ይሁዳ ።
ወደ ይሁዳ ሊሄድ አልወደደም ።
እስመ የኃሥሡ አይሁድ ከመ ይቅትልዎ ።
አይሁድ ሊገሉት ይሹታልና ።

፪ ወቀርበ በዓለ መጸለቶሙ ለአይሁድ ።
ዘሌ፡ ፳፫ ፣ ፴፬ ።

፪ አይሁድ ፋሲካቸውን የሚያከብሩበት ቀን
ደረሰ ፤ ስለምን መጸለት አለው ቢሉ የተደራረበ
በዓል ነው መጸለትን እናከብራለን ሲሉ ቈማር በግ
ብር ምክንያት አስጠርቶ ሮም ወስዷቸዋል ከዚያ
ተመልሰው መጸለትን ሳያከብሩ ፋሲካን አያከብሩምና
ደራርበው አክብረውታል ። አንድም በግብር ስለ
መሰለው ሰው ከበዛ ዘንድ ድንኳን ተከለው ጃንጥላ
ጥለው ያከብሩታልና ። አንድም በዓለ ናዕት ሲል
ነው ጸልቲዮ ይላል ትግሬ ። አንድም በጸያፍ የገባ
ነው ።

፫ ወይቤልዎ አኃዊሁ ለእግዚእ ኢየሱስ
ፍልስ እምዝየ ወሑር ምድረ ይሁዳ ።

፫ አኃዊሁ ያቂቀ ዮሴፍ ናቸው ከዚህ ተን
ሥተህ ወደ ይሁዳ ሂድ አሉት ።
ከመ አርዳኢከኒ ይርአዩ ግብረከ ዘትገብር ወይእመኑ
የምትሠራውን ተአምራት አይተው ሕዝቡ ያምኑ
ብህ ዘንድ ከጉባኤው ከዋለ ደቀ መዝሙር ማለት
ልማድ ነው ።

፬ እስመ አልቦ ዘይገብር ምንተኒ ጽሚተ
ወይፈቅድ ክሡተ ይኩኖ ።

፬ እንዘ ይፈቅድ በል ሥራው ሊገለጥ ወዶ
ሳለ ሥራውን ሰውሮ ምንም ምን የሚሠራ የለምና ።
አንተም ሥራህ ሊገለጽልህ ትወዳለህና ። አንድም
እስመ አልቦ ዘይገብር ወኢምንተኒ ጽሚተ
ወኢይፈቅድ ክሡተ ይኩኖ ። ሥራውን ምንም
ምን ሰውሮ የሚሠራ የለምና ሊገለጽለትም የማ
ይወድ የለምና ፥ አንተም ሥራህ ሊገለጽልህ ትወ
ዳለህና ። አንድም እስመ አልቦ ዘኢይገብር ፤ ሥራ
ውን ምንም ምን ሰውሮ የማይሠራ የለምና ፤ ወይ
ፈቅድ ሊገለጽበትም የሚወድ የለምና አንተ ግን
ሊገለጽልህ ትወዳለህና ። አንድም እስመ አልቦ
ዘኢይገብር ወኢይፈቅድ ፤ ሥራውን ምንም ምን
ሰውሮ የማይሠራ ሊገለጽለትም የማይወድ የለምና
አንተም ሊገለጽልህ ትወዳለህና ።
ወእመሰ ዘንተ ምግባረ ትገብር አርኢ ርእሰከ
ለዓለም ።
ይህን የምታደርግ ከሆነ አምላክነትህን ለሁሉ ግለጽ።

፭ እስመ አኃዊሁኒ ኢአምኑ ቦቱ ።
፭ ወንድሞቹ ደቂቀ ዮሴፍ አላመኑምና እን
ዲህ አሉ ።

፮ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ጊዜየ ዓዲ
እስከ ይእዜ ኢበጽሐ ።

፮ ጌታም እኔ የምወጣበት ጊዜ አልደረሰም ።
ወጊዜ ዚአክሙሰ ዘልፈ ድልው ውእቱ ።
የናንተ ጊዜ ዘወትር የተዘጋጀ ነው ማለት እናንተ
ግን የምትወጡበት ጊዜ ደርሷል የተደራረበ በዓል
ነው ቢሉ ጌታ የሚወጣ ለበዓለ ፋሲካ ነው እንጂ
ለበዓለ መጸለት አይደለምና ። በዓለ ፋሲካ ነው ቢሉ
ጌታ የሚወጣ ለማስተማር ነው እንጂ ለገቢረ በዓል
አይደለምና ። አንድም በኔ ሳላውቀው ሞት አይመ
ጣብኝም በናንተ ግን ሞት ሳታውቁት ሞት ይመጣ
ባችኋል ።

፯ ለክሙሰ ኢይክል ዓለም ጸሊኦተክሙ ።
፯ እናንተን ሰው አይጠላችሁም ።
ወሊተሰ ይጸልኡኒ ።
እኔን ግን ይጠሉኛል ።
እስመ ስምዕ ላዕሌሆሙ ።
እኔ እመሰክርባቸዋለሁና ።
ወእዛለፎሙ በከመ እከየ ምግባሮሙ ።
እንደ ሥራቸው ክፋት ፤ አንድም በክፉ ሥራቸው
እዛለፋቸዋለሁና እሌ ለክሙ ጸሐፍት ፈሪሳው
ያን እያልኩ ።

፰ አንትሙሰ ዕርጉ ውስተ ዝንቱ በዓል ።

፰ እናንተ ወደዚህ በዓል ውጡ ።
ወአንሰ ኢየዓርግ ይእዜ ውስተ ዝንቱ በዓል ።
እኔ ግን ወደዚህ በዓል ዛሬ አልወጣም ።

**እስመ ዓዲ ኢበጽሐ ጊዜየ ።**
**የምመጣበት ጊዜ ገና አልደረሰምና ።**

፱ ወከመዝ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ነበረ ውስተ ገሊላ ።

፱ ተርፈ ሲል ነው ወነበረ ውስተ ኢየሩሳሌም እንዲል ። ይኽን ነግሯቸው በገሊላ ቀረ ።

፲ ወዓረጉሙ አኃዊሁ ለበዓል ውእተ አሚረ ዓርገ ውእቱኒ ጽሚተ ወአኮ ገሃደ ።

፲ ደቂቀ ዮሴፍ ከወጡ በኋላ እርሱም ተገ ልጦ ያይደለ ተሰውሮ ወጣ ።

፲፩ ወኀሠሥዎ አይሁድ ይኅሥሥዎ በበዓል ።

፲፩ አይሁድ በበዓል ይሹት ጀመር።
ወይቤሉ አይቴ ውእቱ ዝኩ ።
ያ የት ነው ያለ አሉ ፤ ዝኩ ቃለ ጸብዕ ነው ዝኩ ወልደ ሰሴይ እንዲል ።

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ ገሃደ በእንተ
ተፈንዎቱ መለኮታዊ ።

፲፪ ወብዙኃን እንጐርጐሩ ሕዝብ በእንቲአሁ።
፲፪ ሕዝቡም በርሱ ምክንያት ፈጽመው ታወኩ
ወቦ እለ ይቤሉ በእንቲአሁ ኄር ውእቱ ።
ደግ ነው ያሉ አሉ ።
ወካልዓን ይቤሉ አልቦ ።
ደግም አይደለ ያሉም አሉ ።
አላ ያስሕቶሙ ለሕዝብ ።
ሕዝቡን ያስታቸዋል እንጂ ሊያስታቸው ነው እንጂ።

፲፫ ወባሕቱ ከሡትስ አልቦ ዘተናገረ በእን ቲአሁ በእንተ ፍርሃቶሙ ለአይሁድ ።

፲፫ ነገር ግን አይሁድን ስለፈሩ ኄር ውእቱ ማለትን ገልጦ የተናገረ የለም ።

፲፬ ወበማእከለ በዓል ዓርገ እግዚእ ኢየሱስ ምኵራብ ወአኃዘ ይምሐር ።

፲፬ የተደራረበ በዓልነው ቢሉ በዓለ መጸለት አልቆ በዓለ ፋሲካ ሲጀመር በዓለ ፋሲካ ነው ቢሉ በአራተኛው ቀን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከምኵራብ ገብቶ ያስተምር ጀመር ።
፲፭ ወአንከሩ አይሁድ ምህሮቶ እንዘ ይብሉ ዝንቱ እፎ የአምር መጽሐፈ ዘኢመሀሮ መኑሂ ።
፲፭ የበጐ እንከሮ ፤ ማንም ማን ያላስተማረው

ይህ መጽሐፍን እንደምን ያውቃል ብለው አደነቁ ።

አንድም ማንም ማን መጽሐፍን ያስተማረው የሌለ ይህ እንደምን ዓውቃለሁ ይላል ብለው አደነቁ ይህ ሠራርቼ አሉት ።

፲፮ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ትምህርትየሰ ኢኮነት እንቲአየ አላ እንቲአሁ ለዘፈነወኒ ።

፲፮ ትምህርቴ የኔ አይደለችም የላከኝ ያባቴ ናት እንጂ ። አንድም የኔ ብቻ አይደለችም የላከኝ ያባቴም ናት እንጂ ።

፲፯ ወዘሰ ይፈቅድ ይግበር ሥምረቶ ውእቱ ይቅድም ወያእምር ከመ እምኀበ እግዚአብሔር ውእቱ ትምህርትየ ።

፲፯ ያባቱን ፈቃድ ሊያደርግ የወደደ ትምህ ርቱ ከእግዚአብሔር እንደ ተገኘች ያውቃል ።
ወአኮ ዘእምኀቤየ እነግር ።
ከኔ እንዳልተገኘ ። አንድም ከኔ ብቻ እንዳልተገኘ ከእግዚአብሔርም እንደ ተገኘ ያውቃል ።
፲፰ ወዘሰ ለሊሁ ዘእምኀቤሁ ይነግር ተድላ ርእሱ የኃሥሥ
፲፰ ከራሱ አንቅቶ የሚያስተምር ግን ራሱን

ደስ ሊያሰኝ ይወዳል ። ለልየኑ እነግር ለርእሰየ ዘሰ

ለርእሱ ይነግር ተድላ ርእሱ የኃሥሥ ይላል ።

ወዘሰ ይፈቅድ ያድሉ ለዘፈነዎ ጻድቅ ውእቱ ።

ላኪውን ደስ ሊያሰኝ የሚወድ ግን እውነተኛ ነው ።

ወአልቦ ዓመፃ በኀቤሁ ።

በርሱም ሐሰት የለበትም ፤ አንድም ላኪየን ደስ ላሰኝ የምወድ እኔ የባሕርይ አምላክ ነኝ ብዬ ባስ ተምር ሐሰት አላስተምርም ።

፲፱ አኮኑ ሙሴ ወሀበክሙ ኦሪተ ።
ዘፀ ፳፬ ፡ ፫ ።

፲፱ ሙሴ ኦሪትን ሠርቶላችሁ የለምን ።
ወኢ፩ሂ እምኔክሙ ኢትገብርዋ ለኦሪት ።
ከናንተ አንዱ ስንኳ ኦሪትን አይሠራትም አንድም አንዳችሁ ስንኳ ኦሪትን አትሠሩዋትም ። አንድም አልቦ ዘይገብራ ። የሚሠራት የለም ።

፳ ለምንት እንከ ተኃሥሡ ወትፈቅዱ ትቅ ትሉኒ ።

፳ ኦሪትን የማንሠራት እንደምን ነው ትሉኝ እንደሆን ኦሪት ኢትቅትል ጻድቀ ትላለች ጻድቅ እኔን ልትገድሉኝ ለምን ትሻላችሁ ።

፳፩ ወአውሥኡ ሕዝብ ወይቤልዎ ጋኔንኑ ብከ
፳፩ ሕዝቡም መለሱ ሎቱ ስብሐት ጋኔን አድ ሮብሃልን ።
መኑ የኃሥሥ ይቅትልከ ።
ማን ሊገድልህ ይሻሃል አሉት ።
ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎሙ ፩ደ ግብረ ገበርኩ ።
አንድ ሥራ ሠራሁ ጕሕቁትን መጻጕዕን ፈወስኩ ።
ወዅልክሙ እንክርክሙኒ ።
ለጊዜው ሁላችሁ አደነቃችሁኝ ።

፳፪ በእንተ ዝንቱ ወሀበክሙ ግዝረተ ።
ዘሌ፡፲፪ ፣ ፫ ዘፍ፡፲፯ ፣ ፲ ።

፳፪ ስለዚህ ማለት ጥንቃቄ አይሁድስ እንዳ ይሆን ሙሴ ግዝረትን ሠርቶላችኋል ።
ወኢኮነት እምኀበ ሙሴ ፤
እፎ የአምር ዝንቱ መጽሐፈ ዘኢመሐሮ መኑሂ ብለውት ነበርና ታሪክ አያውቅም እንዳይሉት ነገር ግን በሙሴ አልተጀመረችም ።
አላ እምአበው ይእቲ ፤
በነአብርሃም ነው እንጂ ።
ወበሰንበት ትገዝርዎ ለሰብእ ።
ቅዳሜ የተወለደውን ቅዳሜ ትገዝሩታላችሁ ።

፳፫ ወእመሰ በሰንበት ግዝረተ ይነሥእ ብእሲ ከመ ኢይሠዓር ሕጉ ለሙሴ ፤

፳፫ ዘኢተገዝረ ክተማ ነፍስቱ እመ ሳምንት ዕለት ብላ አሪት ።
የተናገረችው እንዳይፈርስ ቅዳሜ የምትገዝሩት ከሆነ ለምንት እንከ ሊተ ትግዕዘኒ ለእመ አሕየውክዎ ለብእሲ ዅለንታሁ በሰንበት ።
የሰውን ሁለንታ ሥጋውን በተአምራት ሁለንታ ነፍሱን በትምህርት ቅዳሜ ባድነው ለምን ትነቅፉኛላችሁ ።

፳፬ ኢትፍትሑ በአድልዎ ።
፳፬ በግብዝነት በሐሰት አትፍረዱ ። ዘዳ፡ ፩ ፣ ፲፮

አላ ፍትሐ ጽድቅ ፍትሑ ።
በሚገባ በውነት ፍረዱ እንጂ ሰንበትን መሻር ይሆታ
ምላጩ ሲለመጥ ሥጋው ሲቆረጥ ደሙ ሲፈስ ፤

፳፭ ወቦ እለ ይቤሉ እምሰብአ ኢየሩሳሌም አኮኑ ዝንቱ ዘየኃሥሡ አይሁድ ይቅትልዎ ።

፳፭ በኢየሩሳሌም ካሉ ሰዎች ወገን አይሁድ ሊገድሉት የሚሹት ይኸ አይደለምን ።

፳፮ ወናሁ ገሃደ ይትናገሮሙ ።
፳፮ እነሆ ቃል ለቃል ይነጋገራቸዋል ።
ወአልቦ ዘይቤልዎ ምንተኒ ።
ምንም የመለሱለት ምላሽ የለም ያሉ አሉ ።
አእመሩኑ እንጋ መላእክት ወሊቃውንት ከመ ዝንቱ ውእቱ ክርስቶስ በአማን ።
ሊገሉት የሚሹት እርሱ እንደሆነ አለቆቹ አውቀው ንቀው ትተውታልና አሉ ። አንድም እስከ ክርስቶስ ንጉሥ ተብሎ የተነገረለት እርሱ እንደሆነ በውነት አውቀው እምነውበታልን አሉ ።

፳፯ ወባሕቱ ለዝንቱሰ ነአምሮ እምአይቴ ውእቱ ።

፳፯ ነገር ግን ይኸን ከወዴትም እንደመጣ እናውቃለን ።
ወክርስቶስሰ አመ ይመጽእ አልቦ ዘየአምሮ እምኀበ ይመጽእ ።
ክርስቶስ ግን በመጣ ጊዜ የመጣበትን የሚያውቅ የለም የዕዝራ ነገር ትዝ ብሏቸው ፤
ወርእኩ ዓቢይ ነፋስ ይወፅእ እምባሕር እንዲል ።
ከባሕር ጥቅል ነፋስ ሲወጣ አይቷል ወዲያው መል
አኩ ይህ የመጣበት እንዳይመረመር ክርስቶስበመጣ
ጊዜ የሚመረምረው የለም ብሎታል ።

፳፰ ወአልዓለ ቃሎ እግዚእ ኢየሱስ በምኵራብ እንዘ ይሜህሮሙ ።

፳፰ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በምኵራብ ሲያስተምር ቃሉን አሰምቶ ተናገረ ።
ወይቤሎሙ ኪያየኒ ተአምሩ ።
እኔን ታውቁኛላችሁን ።
ወተአምሩኑ እምአይቴ መጻእኩ አነ ።
ከወዴትም እንደመጣሁስ ታውቃላችሁን ።
ወአኮ ለልየ ኢመጻእኩ ።
በኔ ፈቃድ ብቻ ሰው ልሆን አልመጣሁም ።
አላ ሀሎ ጻድቅ ዘፈነወኒ ።
በላከኝ ባባቴ ፈቃድ ነው እንጂ ፤
ዘኢተአምርዎ አንትሙ ።
እናንተ የማታውቁት ።

፳፱ ወአንሰ አአምሮ ።
፳፱ እኔ ግን አውቀዋለሁ ።
እስመ እምኀቤሁ አነ ፤
ከርሱ እካል ዘእምአካል ተወልጃለሁና ።
ወውእቱ ፈነወኒ ።
በርሱ ፈቃድ ሰው ሁኛለሁና ።

፴ ወፈቀዱ የአኃዝዎ ።
፴ ሊይዙት ወደዱ ።
ወባሕቱ አልቦ ዘአንሥአ እዴሁ ላዕሌሁ ።
ነገር ግን በጠላትነት እጁን ያነሣበት የለም ።
እስመ ዓዲሁ ኢበጽሐ ጊዜሁ ።
የሚሞትበት ጊዜ ገና አልደረሰምና ።

፴፩ ወእምውእቶሙ ሰብእ ብዙኃን እለ አምኑ ቦቱ ።

፴፩ በዚያ ካሉ ሰዎች ያመኑበት ብዙ ናቸው ብዙ ሰዎች አመኑበት ።
ወይቤሉ እመ ይመጽእ ክርስቶስ ቦኑ ፈድፋደ ተአ

ምረ ዘይገብር እምዘገብረ ዝንቱ ።
በውኑ ክርስቶስ በመጣ ጊዜ ይህ ሰው ካደረገው ተአምራት የሚበልጥ የሚያደርገው ተአምራት አለን አንድም የበለጠ ተአምራት ያደርጋል አሉ ።

፴፪ ወሰሚዖሙ ፈሪሳውያን ከመ እንጐርጐሩ ሕዝብ በእንቲአሁ ።

፴፪ ፈሪሳውያን ሕዝቡ በርሱ ምክንያት እን ዳዘኑ ሰምተው ።
ፈነወ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን ወአልያኒሆሙ ከመ የአኃዝዎ ።
ይህ ሁሉ እኛ ዝም ብንል አይደለም ብለው ፈሪሳ ውያንና የካህናት አለቆች ያዙ ብለው ብላቴኖቻ ቻውን ላኩ ።

፴፫ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ዓዲ ኅዳጠ መዋዕለ ሀሎኩ ምስሌክሙ ።

፴፫ ጌታም ገና ጥቂት ቀን ከናንተ ጋራ እኖ ራለሁ ።
ወእምዝ እሐውር ኀበ አብ ዘፈነወኒ ።
ከዚህ በኋላ ወደላከኝ ወዳባቴም እሄዳለሁ ።

፴፬ ተኀሥሡኒ ወኢትረክቡኒ ። ዮሐ፣፲፫ ፣ ፴፫
፴፬ ትሹኛላችሁ አታገኙኝም ።
ወኀበ እነ እሐውር አንትሙ ኢትክሉ መጺአ ።
እኔ ወደምሄድበት መምጣት አይቻላችሁምና ።
አንድም ተኃሥሡኒ እያልክ መልስ ። በፈቃዱ የምሞተውን ሞት በግድ እንገድለዋለን ብላችሁ ትሹኛላችሁ ። ወኢትረክቡኒ አታገኙኝም በፈቃድ የምሞተውን ሞት በግድ መግደል አይቻላችሁምና። አንድም በጽድቀ አብርሃም ያጸድቀናል ብላችሁ ትሹኛላችሁ አታገኙኝም ፣ እኔ በተሰቀልኩበት መስቀል ተሰቅላችሁ እኔ በሞትኩበት ሞት ሞታ ችሁ እኔ ከገባሁበት ውሣጤ መንጦላዕት ገብቶ መኖር አይቻላችሁምና ። አንድም ዓመተ ቃይናንን ፍቃችሁ እንደገና ይወርዳል ይወለዳል ብላችሁ ትሹኛላችሁ ፣ አታገኙኝም ከዚህ ቀድሞ የተወለደው እርሱ አይደለም ብሎ ማመን አይቻላ ችሁምና ፤ አንድም በጥጦስ ጊዜ አግኝተነው ተአ ምራት አድርጎልን ብላችሁ ትሹኛላችሁ አታገኙ ኝም ፣ ዛሬም ብናምንበት ይሆን የለም ብሎ ማመን አይቻላችሁም ።

፴፭ ወይቤሉ አይሁድ በበይናቲሆሙ አይቴኑ ሀለዎ ለዝንቱ ይሑር ዘኢንክል ረኪቦቶ ንሕነ ።

፴፭ አይሁድ እርስ በርሳቸው እኛ የማናገ ኘው ለዚህ ወዴት ይሄድ ዘንድ አለው አሉ ።
ውስተ ብሔረ አረሚኑ የሐውር እንጋ ወይሜህሮሙ ለአረሚ ።

እንዳች ግዙፍ ሥርዓት አፍርሶ ወደ አረማውያን ሄዶ አረማውያንን ያስተምር ዘንድ አለውን ።

፴፮ ምንትኑ ዝንቱ ነገር ዘይብለነ ተኀሥሡኒ ወኢትረክቡኒ ።

፴፮ ትሹኛላችሁ አታገኙኝም ።
ወኀቤ እነ እሐውር አንትሙ ኢትክሉ መጺአ ።
እኔ ወደምሄድበት መምጣት አይቻላችሁም የሚ ለን ነገር ምንድር ነው ።

ዘከመ ከሠተ ኢየሱስ መንፈስ ቅዱስ ።

፴፯ ወበደኃሪት ዕለት ዘበዓል ዓባይ ቆመ እግዚእ ኢየሱስ ከልሐ ወይቤ ዘጸምዓ ይምጻእ ኀቤየ ወይስተይ ። ዘሌ፣፳፫ ፣ ፳፯ ።

፴፯ እስመ ይእቲ ዘዐአት ይላታል ።
በአራት ዘመድ ከዘመዱ ወዳጅ ከወዳጁ የተረፉቸ ውን ስንቃቸውን በልተው የሚለያዩበት ናት በየ ሀገራቸው ለመሄድ በዚህ ቀን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሻ በኔ ይመን ልጅነትንም ያግኝ ብሎ አሰምቶ ተናገረ ።

፴፰ ወዘሂ የአምን ብየ በከመ ይቤሉ መጻሕፍት አፍላገ ማየ ሕይወት ዘይውኅዝ እምከርሡ ኢሳ፣፶፩፣፫

፴፰ መጻሕፍት ጻድቅኢ በአሚን የሐዩ ወዙሉ ዘጸውዓ ስመ እግዚአብሔር ይድኀን ብለው መጻሕ ፍት እንደ ተናገሩ በኔ ካመነ ሀብታት ምሥጢራት ከሱ ይገኛሉ ። አንድም ዘጸምዓ ብለህ መልስ የሻ በኔ ይመን ልጅነትንም ያግኝ ። ወዘሂ የአምን ብየ ዝርዝሩን ለጌታ ስጥ ኢሳይያስ እነ አነቅዕ አፍላገ በውስተ በድው ወይውኅዝ ማይ በውስተ በድው ወይረውዩ ጽሙዓን ወይከውን ብሔርከሙ አፍላገ ማይ ወይውሕዝ ማይ ርጊብ ወስፉሕ ወእለ ጸምዑ ይሑሩ ኀበ ማይ ወይስተዩ ዘእንበለ ወርቅ ። ኤርም ያስ ኀደጉኒ ሊተ ነቅዓ ማየ ሕይወት ወከረዩ ሎሙ ዓዘቅተ ዘኢይትረከብ ማዩ ። ዘካርያስ ማየ ሕይወት ዘይውኅዝ እምኢየሩሳሌም መንፈቁ መንገለ ባሕር ቀዳሚት ፣ ወመንፈቁ መንገለ ባሕር ደኀሪት ። ሆሴዕ በጥሬው ወልድ ጠቢብ ዘኢያጠብዕ በሞተ ውሉድ ዕሤተ አብ አፍላገ ማየ ሕይወት ይውኅዝ እምከርሡ ብለው መጻሕፍት እንደተናገሩ ሀብታትም ሥጢራት ከኔ ይገኛሉና የሻ በኔ ይመን ልጅነትን ያግኝ ።

፴፱ ወዘንተ ዘይቤ በእንተ መንፈስ ቅዱስ ዘሀሰዎሙ ይንሥኡ እለ የአምኑ ቦቱ ። ኢዩ፣፪፣ ፳፰ ግብ፣፪ ፣ ፲፯ ።
፴፱ በርሱ ያመኑ ምእመናን ይቀበሉት ዘንድ ስላላቸው ስለመንፈስ ቅዱስ ይኸን ተናገረ ።
እስመ ዓዲ ኢወረደ መንፈስ ቅዱስ በእንተ ዘኢተሰ ብሐ ዓዲሁ እግዚእ ኢየሱስ ።

ጌታ ገና ስላልተሰቀለ መንፈስ ቅዱስ ገና አልተሰጠ ምና ፡

ዘከመ ሐለዩ አይሁድ ላዕለ ኢየሱስ ዘዘዚአሆሙ ሐልዮታተ ።

፵ ወብዙኃን እምሕዝብ ሰሚዖሙ ዘንተ ነገረ ይቤሉ አማን ነቢይ ውእቱ ዝንቱ ።

፵ ከሕዝቡ ወገን ብዙዎቹ ይህን ሰምተው ነቢይ ነው አሉ ።

፵፩ ወቦ ይቤሉ ክርስቶስ ውእቱ ።
፵፩ ተሻልን ያሉት ልዩ ልዩ መስሏቸው ክር ስቶስ ነው ያሉም አሉ ።
ወመንፈቆሙ ይቤሉቦኑ እምገሊላ ይመጽእ ክርስቶስ። ዓወቅን ጠነቀቅን ያሉ ጸሐፍት ፡ ፈሪሳውያን ግን በውኑ ክርስቶስ ከገሊላ ይነሣልን አሉ ።

፵፪ አኮኑ ይብል መጽሐፍ ከመ እምዘርዐ ዳዊት ወእምነ ቤተ ልሔም ሀገሩ ለዳዊት ይመጽእ ክርስቶስ ፡ ሚክ. ፭፡፪ ማቴ፡ ፪፡፮ ።

፵፪ ከዳዊት ወገን ከዳዊት አገር ከቤተልሔም ክርስቶስ እንዲወለድ መጽሐፍ ተናግሮ የለም አሉ ። መካህ ይወፅእ እምኤዶም ያለውን መተርጉም ወይ እቲ ኤዶም እምአድያማተ ገሊላ ብሎ እንደ ተረጐመው ባያውቁ ።

፵፫ ወተገዓዙ ወተናፈቁ ሕዝብ በበይናቲሆሙ በእንቲአሁ ።

፵፫ ሕዝቡ በርሱ ምክንያት እርስ በርሳቸው ተለያዩ ተከራከሩ ።

፵፬ ወቦ እለ ፈቀዱ የአኃዝዎ ።
፵፬ ሊይዙት የወደዱም አሉ ።
ወባሕቱ አልቦ ዘአንሥአ እዴሁ ፡
ነገር ግን ማንም እጁን አላነሣበትም ።

፵፭ ወተሠውጡ እልክቱ ወዓሊያኒሆሙ ኀበ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን ።

፵፭ ብላቴኖቻቸው ወደሊቃነ ካህናትና ወደ ፈሪሳውያን ተመለሱ ።
ወይቤልዎሙ እሙንቱ እፎኑመ ዘኢያምጻእክምዎ ።
እርስ በርሳቸውም ምነው ያላመጣችሁት አሏቸው ።

፵፮ ወአውሥኡ ወዓልያኒሆሙ ።
፵፮ ብላቴኖቻቸውም መለሱ ።
ወይቤልዎ ግሙራ ኢተናገረ ሰብእ ዘከመ ተናገረ ውእቱ ብእሲ ።
ያሰው እንደተናገረው ፡ ያለ ነገር ከቶ ሰው ተናግሮት አያውቅም አሏቸው ።

፵፯ ወአውሥኡ ፈሪሳውያን ።
፵፯ ፈሪሳውያንም መለሱ ።
ወይቤልዎሙ ትጌግዩኑ አንትሙኒ ።
እናንተም ታስታላችሁን አሏቸው ዋዌው ለሐዋርያት ነው ።

፵፰ ቦኑ እመላእክት ወእምፈሪሳውያን ዘአምነ ቦቱ ።

፵፰ ወይስ ካለቆች ከፈሪሳውያንም ወገን ያመነበት አለ ።

፵፱ ዘእንበለ እሉ ጊጉያን ሕዝብ እለ ኢያአምሩ ኦሪተ ።

፵፱ ኦሪትን ከማያውቁ ከኒህ ስሁታን በቀር ። ወእሙንቱሰ ርጉማን ፤ እነሱ ግን የተረገሙ ናቸው ።

፶ ወይቤሎሙ ኒቆዲሞስ ዘሖረ ኀቤሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ቀዲሙ ሌሊተ አሐዱ እምኔሆሙ ዮሐ ፫ ፪ ።

፶ አስቀድሞ በሌሊት ወደ ጌታ የሄደ ከርሳቸው አንዱ ኒቆዲሞስ አላቸው ።

፶፩ ኦሪትክሙኑ ትኴንኖ ለሰብእ ዘእንበለ ይሕ ትትዎ ቅድመ ወያእምሩ ምግባሮ ዘገብረ ዘዳ፡፲፱፡፲፮ ።

፶፩ ኦሪትነኑ ሲል ነው በእንተ ክብርከሙ እን ዲል ። ከርሳቸው ወገን የሚሆን አስቀድሞ በሌሊት ወደ ጌታ የሄደ ኒቆዲሞስ ኦሪታችን ሥራውን አስቀ ድሞ መርምሮ ሳያውቁ ፍረዱበት ትላለችን አላቸው። አንድም እርሱ አምኑዋልና ። ኦሪትክሙኑ ይላል ።

፶፪ ወአውሥእዎ ወይቤልዎ አንተኒ እምገሊ ላኑ ትብል አንተ ።

፶፪ አንተም ዐዋቂው እንዳላዋቂ ትሆናለህ አሉት ።
ኀሥሥ መጽሐፈ ወትርአይ ከመ እምገሊላ ኢይትነ ሣእ ነቢይ ፤
ነቢይ ከገሊላ እንዳይነሣ ከመጽሐፍ ሻ መርምር ።

፶፫ ወገብኡ ኵሉ ለለ አሐዱ ውስተ ቤቶሙ ።
፶፫ ሁሉም እያንዳንዳቸው ወደቤታቸው ተመ ለሱ ። ሻ መርምር ብለውታልና ሊሹ ሊመረምሩ ፣ አንድም እርስ በርሳቸው ተጃመሩ ይሉናል ብለው። አንድም ነገራቸው ቢፈርስባቸው ብላቴኖቻቸው ግሙራ ኢተናገረ ሰብእ ዘከመ ተናገረ ውእቱ ብእሲ አሉ ፣ ኒቆዲሞስ ኦሪትክሙኑ ትኴንኖ ለሰብእ አለ።

በእንተ ዘማዊት ብእሲት ።

ምዕራፍ ፰ ።

፩ ወኢየሱስኒ ሖረ ውስተ ደብረ ዘይት ።
፩ ጌታ በምሥራብ ሲያስተምር ውሎ አዳሩን

ደ ደብረ ዘይት ሄደ ።

፪ ወአንግሀ በጽባሕ ወቦአ ካዕበ ምኵራበ ፣
፪ ወኮነ መዓልተ ይሜህር በምኵራብ ወሌሊተ ይበይት ውስተ ደብረ ዘይት እንዲል ፣ ሌሊት በደብረ ዘይት ሲጸልይ ያድራል ፣ ቀን በምኵራብ ሲያስተምር ይውል ነበርና ማለዳ ገሥግሦ ወደምኵራብ ሄደ ።
ወተጋብኡ ኵሉ ሕዝብ ኀቤሁ ።
ሕዝቡ ሁሉ ወደርሱ መጡ ።
ወነበረ ይምሀሮሙ ።
በትምህርት ተገኘላቸው ። ወአኃዘ ይምሀሮሙ ይላል ያስተምራቸው ጀመር ፣ ትምህርቱ ብፁዓን ነው ፣ አንድም ሌላ ።

፫ ወአምጽኡ ኀቤሁ ጸሐፍት ወፈሪሳውያን ብእሲተ እስርተ እንተ ተረከበት በዝሙት ።

፫ ጸሐፎችም ፈሪሳውያንም በሴሰኝነት ተይዛ የታሰረች ሴት ወደርሱ አመጡ ።
ወአብእዋ ውስጠ ወአቀምዋ ቅድመ እግዚእ ኢየሱስ ።
ከውስጥ አግብተው ጌታ ካለበት አቀረቧት ። ዕለቱን ነው ቢሉ አንዱን ቅጥር አግብተው በሦስተኛው ቀን ነው ቢሉ ሁለቱን ቅጥር አግብተው።

፬ ወይቤልዎ ኦሊቅ ረከብናሃ ለዛቲ ብእሲት በዝሙት እንዘ ትጌብስ ።

፬ መምህር ሆይ ይህች ሴት በሴሰኝነት አግኝተናታል ።

፭ ወበሕግነሰ ሠርዓ ሙሴ ከመ ትትወገር በእብን ፣ ዘሌ. ፳፥፲ ።

፭ እንደኛ ሥርዓት ሙሴ በደንጊያ ተወግራ ትሙት ብሏል ።
ወአንተ እንከ ምንተ ትብል በእንቲአሃ ።
አንተስ የእርሷን ነገር ምን ትፈርዳለህ አሉት ።
እስመ ናሁ ተረከበት በዝሙት ።
በሴሰኝነት ተገኝታለችና ፣

፮ ወዘንተ ይቤሉ እንዘ ያሜክርዎ ።
፮ ሲፈትኑት እንዲህ አሉት ።
ከመ ይርከቡ በላዕሌሁ ምክንያተ ።
ምክንያት ያገኙበት ዘንድ ትምህርቱ ብፁዓን ነው ቢሉ አትሙት ቢል ወሀሉ ዘይድኅር ብእሲቶ ዘእንበለ ትዘሙ በላዕሌሁ ለሊሁ ረስያ ዘማ ይላል። አንድ ጊዜ እንዲህ ይላል ነገሩ ቀዋሚ አይደለ ምሳ ለማለት ። ትወገር ቢል የእግዚአብሔር ወገን ነኝ ይላል የሰው ጥፋት እያሳዝነውም ለማለት ትምህርቱ ሌላ ነው ቢሉ ትወገር ቢል። አንሰ ኢመጻእኩ ለኰንኖ ዝንቱ ዓለም ይላል ፣ አንድ ጊዜ እንዲህ ይላል ነገሩ ቀዋሚ አይደለምሳ ለማለት ። አትወገር ቢል የሙሴን ሥርዓት አፈ ረሰ ብለው እንማላቸዋለን ብለው ።
ወአትሐተ እግዚእ ኢየሱስ አዕይንቲሁ ውስተ ምድር ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ኖራ ኖራውን ተመለከተ።
ወጸሐፈ በአፅባዕቱ ።
ቀረጸውም ።

፯ ወሶበ ቆሙ ብዙኃን ወአጕንደዩ ተስእሎቶ አንሥአ አዕይንቲሁ ዘዳ፥ ፲፯፥፯ ።

፯ ቁመው መላልሰው በጠየቁት ጊዜ ዐይኑን አቀና ።
ወይቤሎሙ ዘአልቦ ኃጢአት እምኔከሙ ቀዲሙ ለይገራ በእብን ።
ከናንተ ወገን እርሷ የሠራችውን ኃጢአት ያልሠራ ሰው ደንጊያ ይጣልባትና ከዚያ በኋላ ግደሏት አላቸው ። ኖራውን በቀረጸው ጊዜ ኃጢአታቸው በየግንባራቸው እየተጻፈ ታይቷል ይህስ እንዳይሆን ከባቴ አበሳ ነው ያንዱን ኃጢአት አንዱ ይይበት ብሎ እንዲህ አያደርግም የአንዱ ኃጢአት ባንዱ ግንባር የአንዱ ኃጢአት ባንዱ ግንባር እየተጻፈ ታይቷል ።

፰ ወካዕበ ደነነ ዲበ ምድር ።
፰ ሁለተኛም ወደ ምድር አየ ።
ወጸሐፈ በአፅባዕቱ ፣
ቀረጸው ። የነቢቡን የገቢሩን የሐልዮውን ለማለት ደገመው ።

፱ ወሰሚዖሙ እሙንቱ ዘንተ ዘለፋ በለብዎ አኃዙ ይሑሩ በበአሐዱ እስከ ወፅኡ ሊቃውንቲሆሙ እምቀዳሚ እስከ ደኃሪ ።

፱ ዘአልቦ ኃጢአት ያለውን ሰምተው የሰው ኃጢአት እንገልጣለን ብለን ኃጢአታችንን ገለጠብን ብለው ፊት ከገቡት በኋላ እስከ ገቡት በውስጥ ካሉት በአፍአ እስካሉት እምሊቅ እስከ ደቂቅ እንዲሉ ወጥተው ሄዱ ።

ወተርፈ እግዚእ ኢየሱስ ባሕቲቱ ።
ጌታ ብቻውን ቀረ ። ንጹሐ ባሕርይ ነውና ።
ወይእቲኒ ብእሲት ትቀውም ውስጠ ።
እርሷም ቁማ ቀረች ፣ ለጊዜው ።
ተኃድገ ለኪ ኃጢአትኪ የሚላት ነውና ።

፲ ወአንሥአ ኢየሱስ አዕይንቲሁ ወነጸረ ኀቤሃ ።

፲ ኢየሱስም ዓይኑን አቅንቶ ወደርሷ አየ።
ወይቤላ ኦ ብእሲቶ አይቴ ሀለዉ እለ ይኴንኑኪ ።
አንቺ ሴት እንፈርድብሻለን ያሉ ሰዎች የታሉ አላት ።

፲፩ ወአውሥአት ወትቤሎ አልቦ ዘእሬኢ እግዚኦ ።

፲፩ እርሷም አለች አቤቱ የማየው የለም ።
ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ አነሂ አልቦ ዘእኴንነኪ
ሑሪ እትዊ በሰላም ።
እኒያ ካልፈረዱብሽ እኔም አልፈርድብሽም ሂጂ
አላት ። አንድም ወይቤላ ብለህ መልስ አንች
ሴት ሆይ እንፈርድብሻለን ያሉ ሰዎች በምን ህል
ዎት አሉ ። ትያለሽ በጽድቅን ነው በኃጢአት አላት ።
ወአውሥአት ወትቤሎ አላውቅም አለች ። አንች
በሰው ካልፈረድሽእኔም አልፈድብሽም በፍቅር ሂጂ
አላት ። ወእምዝ ዳግመ ኢተአብሲ ።
ሁለተኛ እትበድይ አላት ፡ ይህም አልቀረ ።
ጌታ በዕለተ ዐርብ ሠለስት ሲሆን ለጸሎት ተሰ
ውሯቸው ካታክልት ቦታ ገባ ረቂቅ መለኮት
እንደሆነ ክረቂቅ መለኮት ጋር እንደ ተዋሐደ ለማ
ጠየቅ ። እርሷ አየችው አትናገሪ ብሏት ሄደ ወዲ
ያው መጥተው ጠየቋት የተናገርኩ እንደሆነ ይሰ
ማኛል ብላ ባይኑዋ ጠቅሳ አሳየቻቸው ድንጊያ
ሁና ቀርታለች ፡

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ በእንተ ተፈንዎቱ
መለኮታዊት ።

፲፪ ወካዕበ ነበቦሙ እግዚእ ኢየሱስ ዮሐ፡
፩፡፭ ።

፲፪ ደግሞም ተናገራቸው ኢየሱስ እንዲህ ሲል
አስተማራቸው ትምህርቱም ብፁዓን ነው ቢሉ ሄደው
የለም ቢሉ ተመልሰው ይሰማሉ ።
አንድም ፈጽመው አልራቁምና በአጠገቡ ሁነው ይሰ
ማሉ ትምህርቱም ሌላ ነው ያሉ እንደሆነ የተመቸ ።
ወይቤሎሙ አነ ውእቱ ብርሃኑ ለዓለም ።
የዓለም ብርሃን እኔ ነኝ ፤ ማለት
አንድነትን ሦስትነትን እንዲያውቅ የማደርገው እኔነኝ
ዘተለወኒ ኢየሐውር ውስተ ጽልመት ።
የተከተለኝ ማለት በኔ ያመነ ወደ ክሕደት አይ
ሄድም ።
አላ ይረክብ ብርሃነ ሕይወት ።
የሕይወት ብርሃንን ያገኛል እንጂ በኔ አምኖ ይኖራል
እንጂ ። አንድም አነ ውእቱ ብለህ መልስ ።
ሰውን ኃጢአቱን እንዲመረምር በራሱ እንዲፈርድ
የማደርገው እኔ ነኝ ዘተለወኒ ፡ እኔን አብነት
ያደረገ ወደ ገሃነም አይሄድም አላ ይረክብ ፡መንግሥተ
ሰማይን ይወርሳል እንጂ ።

፲፫ ወይቤልዎ ፈሪሳውያን ለሊከ ትንዕድ
ርእሰከ ።

፲፫ ፈሪሳውያንም መጽሐፍ ይወድስከ አፈ
ነኪር ይላል ፡ አንተ ራስህን ታመሰግናለህን ።
ኢኮነ ጽድቀ ስምዕከ ።
እንዲህስ ከሆነ ራስከን የምታመሰግን ያንተ ምስ
ክርነትህ እውነት አይደለም ።

፲፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ እመኒ ለልየ ስምዓ ኮንኩ ለርእስየ
ጽድቅ ውእቱ ስምዕየ ።
እኔ ለራሴ ብመሰክር ምስክርነቴ እውነት ነው ።
እስመ አአምር እምኀበ መጻእኩ ።
የመጣሁበትን አውቃለሁና ።
ወኀበሂ እሐውር ።
የምሄድበትንም አውቃለሁና ።
ወአንትሙሰ ኢትአምሩ እምኀበ መጻእኩ ወኀበሂ
እኃውር ።
እናንተ ግን የመጣሁበትን የምሄድበትንም አታ
ውቁም ።
አንትሙሰ ሕገ ዘሥጋ ትኴንኑ እናንተስ ጠበሕ
ግነሰ ሠርዓ ሙሴ ከመ ትትወገር በእብን ብሏል
ብላችሁ ትፈርዳላችሁ ።

፲፭ ወአንሰ ኢይኴንን ወኢመነሂ ።
፲፭ እኔ ግን በማንም በማን እንዲህ ብዬ
አልፈርድም ፡

፲፮ ወእመሂ ኰነንኩ አንሰ እስመ ጽድቅ
እኴንን ።

፲፮ ብፈርድም እውነት እፈርዳለሁ ተኃድገ
ለከ ኃጢአትከ ተኃድገ ለኪ ኃጢአትኪ እያልኩ
እፈርዳለሁ ፡ አንድም አንትሙስ እያልክ መልስ
እናንተ ካነጋገር ይፈረዳል ካያያዝ ይቀደዳል ብላ
ችሁ ትፈርዳላችሁ ፡
ወአንሰ ኢይኴንን እኔ ግን በማንም በማን አልፈ
ርድም ወእመሂ ኰነንኩ ብፈርድም ኩላሊት ያጤ
ሰውን ልብ የመረመረውን መርምሬ እፈርዳለሁ ።
አንድም አንትሙስ እናንተስ ከዮሴፍ ቤት ስበላ
ስጠጣ አይታችሁ እሩቅ ብእሲ ወልደ ዮሴፍ ትሉ
ኛላችሁ እኔ ግን የሌለኝን አምላክነት ለማንም
ለማን አላስተምርም ። ወእመሂ ኰነንኩ ባስተም
ርም ያለኝን አምላክነት አስተምራለሁ እንጂ ።
እስመ ኢኮንኩ አነ ባሕቲትየ እኔ ብቻዬን
አይደለሁምና ።
አላ አነ ወአብ ዘፈነወኒ ፡
እኔ የላከኝ አብም እንጂ ።

፲፯ አኮኑ ጽሑፍ ውስተ ኦሪትክሙ ስምዓ
፪ቱ ሰብእ እሙን ውእቱ ። ዘዳ፡፲፯፡፮ ፲፱ቆር፡ ፲፱፡፲፭
ማቴ፡፲፰፡፲፮ ዕብ፡ ፲፡፳፰ ።

፲፯ በኦሪታችሁ ሁለት ሰዎች የመስከሩት
ምስክር እውነት ነው የሚል ጽሑፍ ያለ አይደ
ለም ።

፲፰ ወአነሂ ስማዕት ለርእስየ ።
፲፰ እኔ ለራሴ ምስክር ነኝ ።
አብ ወስማዕትየ ዘፈነወኒ ።
የላከኝ አባቴም ምስክሬ ነው ።

፲፱ ወይቤልዎ አይቴ ውእቱ አቡከ ።
፲፱ አባትህ የት አለ አሉት ።
ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ኢኪየየ ተአምሩ ።
እኔንም አታውቁ ።
ወኢአቡየ ።
አባቴንም አታውቁም እንድም እኔን ሳታውቁ አባ
ቴን አታውቁ አላቸው ።
ሶበሰ ኪያየ አእመርክሙ አምአእመርክምዎ
ለአቡየኒ ።
እኔንስ አውቃችሁኝ ቢሆን አባቴንም ባወቃችሁት
ነበር ።

፳ ወዘንተ ነገረ ተናገሮሙ እግዚእ ኢየሱስ
በኀበ ሙዳየ ምጽዋት እንዘ ይሜህሮሙ ።

፳ በምኵራብ ሲያስተምራቸው መባውን የሚ
ያኖሩበት ሣጥን ካለበት ቦታ ይኽንን ነገራቸው።
እስራኤል ከቤተ እግዚአብሔር እጅ ሳይነሱ አይ
ውሉም ባዶ እጃቸውንም አይሄዱም ድቀት ያገ
ኘው አንዱን ቅጽር ገብቶ ከዚያ ትቶ ይሄዳል
ድቀት ያላገኘው ከውስጥ ገብቶ ሰጥቶ ይሄዳል
ካህናት እያነሱ የሚያበላሹት ሆነ ፤ንጉሡ ኢዮአስ
ሊቀ ካህናቱ ዮዳሄ ይባላሉ መክረው ብር የሚ
ያስገባ እጅ የማያስገባ ሣጥን አኖሩ ሲመላ ዕቃቤት
እያገቡ ያኖሩታል ሁለት ሦስት ሁነው እንሥተው
እንዳይወስዱት ጠባቂም አለው ይህ ባለበት ።
ወኢአኀዝዎ ።
አልያዙትም እስመ ዓዲ ኢበጽሐ ጊዜሁ ።
የሚያዝበት ጊዜ ገና አልደረሰምና ።

፳፩ ወካዕበ ይቤልዎ እግዚእ ኢየሱስ
አንሰ አሐውር ።

፳፩ ጌታም ደግሞ እሄዳለሁ አላቸው ።
ተኀሥሡኒ ። ትሹኛላችሁ ።
ወኢትረክቡኒ ። አታገኙኝም ።
ወትመውቱ በኃጢአትክሙ ።
በኃጢአታችሁም ትሞታላችሁ ።
ወኀበ አነ አሐውር አንትሙ ኢትክሉ መጺአ
እኔ ወደምሄድበት መምጣት አይቻላችሁም ።
ወትመውቱ በኃጢአትክሙ ።
በኃጢአታችሁ ሳላችሁ በኃጢአታችሁ ፍዳ ተፈር
ዶባችሁ በነፍስ ትሞታላችሁ

፳፪ ወይቤሉ አይሁድ ይቀትልኑ እንጋ ርእሶ
ለሊሁ ዘይብለነ ኀበ አነ አሐውር አንትሙ ኢት
ክሉ መጺአ ፣

፳፪ አይሁድም እኔ ወደምሄድበት እናንተ
መምጣት አይቻላችሁም የሚለን ታንቆን ይሞታል
አሉ ።

፳፫ ወይቤሎሙ አንትሙሰ እምታሕቱ
አንትሙ ።

፳፫ እናንተስ በግብርም በባሕርይም ባናኑዋ
ርም ከዚህ ዓለም የተገኛችሁ ናችሁ ፡
ወአንሰ እምላዕሉ አነ ፣
እኔ ግን ባናኑዋርም በባሕርይም ከሰማይ የተገ
ኘሁ ነኝ ።
አንትሙሰ እምዝንቱ ዓለም አንትሙ ።
እናንተስ ባናኑዋርም በባሕርይም ከዚህ ዓለም የተ
ገኛችሁ ናችሁ ።
ወአንሰ ኢኮንኩ እም ዝንቱ ዓለም ።
እኔ ግን ከዚህ ዓለም አይደለሁም ።

፳፬ ወናሁ እቤለክሙ ከመ ትመውቱ በኃ
ጢአትክሙ

፳፬ በኃጢአት ሳላችሁ ንስሐ ሳትገቡ ፡አን
ድም ብኃጢአታችሁ በመጣ ፍዳ በነፍስ እንድ
ትሞቱ እነሆ ነግሬያችኋለሁ ለእመ ኢአመን
ክሙ ከመ አነ ውእቱ ትመውቱ በኃጢአት
ክሙ ፣
እኔ እንደሆንኩ ባታምኑ ማለት የባሕርይ አም
ላክ እንደሆንኩ ካላመናችሁ በኃጢአት ትሞታ
ላችሁ ።

፳፭ ወይቤልዎ አንተ መኑ አንተ
፳፭ አንተ ማነህ አሉት ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ቀዳሚኒ ነገርኩክሙ ።
ጌታም ቀድሞ ነግሬያችሁ ነበር ።

፳፮ ወብዙኅ ብየ ዘእብል በእንቲአክሙ ።
፳፮ ለናንተም የምነግራችሁ ብዙ ነገር ነበረኝ።
ወእኪንን ቦቱ ።
ኪያሁ ሲል ነው ያኑ የማስተምረው ።
ወባሕቱ ዘፈነወኒ ጻድቅ ውእቱ ።
ነገር ግን የላከኝ አባቴ የባሕርይ አምላክ ነው ።
ወአንሰ ዘሰማዕኩ በኀቤሁ እነግር ለዓለም ።
እኔም በርሱ በህልውና የሰማሁትን ለዓለም አስተ
ምራለሁ ።

፳፯ ወኢያእመሩ ከመ በእንተ አብ ይቤሎሙ።
፳፯ ጻድቅ ውእቱ ያለው ስለ አብ እንደሆነ
አላወቁም ።

፳፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አመ ተለዓለ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ይእተ አሚረ ተአምሩ ከመ አነ ውእቱ ።

፳፰ የሰው ልጅ ክርስቶስ ከፍ ባለ ጊዜ ማለት በተሰቀልኩ ጊዜ የባሕርይ አምላክ እንደሆንኩ ታውቃላችሁ ።
ወአኮ ዘእምኅቤየ ዘእነግር ።
የማስተምረውም ከራሴ አንቅቼ እንዳይደለ ።
አላ በከመ መሐረኒ አቡየ ከማሁ እነግር ።
አባቴ በሀልውና የነገረን እንደነገረኝ አስተምራለሁ እንጂ ።

፳፱ ወዘፈነወኒ ሀሎ ምስሌየ ።
፳፱ የላከኝ አባቴ በኔ ሀልው ነው ።
ወኢየኃድገኒ አብ ባሕቲትየ ።
አብ ብቻየን አይተወኝም ማለት አይለየኝም ።
እስመ አነ እገብር ሥምረቶ ዘልፈ በኵሉ ጊዜ ።
በፈቃድ አንድ ነንና ። አንድም ዘወትር ፈቃዱን እፈጽማለሁና ።

፴ ወዘንተ ብሂሎ ብዙኃን እለ አምኑ ቦቱ ።
፴ ይህን በተናገረ ጊዜ ብዙ ሰዎች አመኑበት ያመኑበት ብዙ ሰዎች ናቸው ።

፴፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ለእለ የአምኑ ቦቱ አይሁድ አንትሙሂ ለእመ ነበርክሙ በቃልየ አማን አርዳእየ አንትሙ ።

፴፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያመኑበትን አይሁድን እናንተም ባስተማርኳችሁ ትምህርት ብትጸኑ በውነት የኔ ደቀመዛሙርት ናችሁ አላቸው ።

፴፪ ወተአምርዋ ለጽድቅ ።
ጽድቅንም ታውቋታላችሁ ።
ወጽድቅኒ ታግዕዘክሙ ።
ጽድቅም ነጻ ታወጣችኋለች ።

ዘከመ ገሠጾ ኢየሱስ ትዝኅርቶሙ ለአይሁድ ።

፴፫ ወአውሥኡ አይሁድ ወይቤልዎ ዘርዓ አብርሃም ንሕነ ።

፴፫ እኛስ የአብርሃም ልጆች ነን ።
ወእም አመኮነ ኢተቀነይነ ግሙራ ወኢለመኑሂ ።
ከሆነ ጀምሮ ለማንም ለማን ተገዝተን አናውቅም ።
እፎ እንከ ትብለነ አንተ ትግዕዙ ።
እንደምን አንተ አርነት ትወጣላችሁ ትለናለህ አሉት ይኸም ሐሰታቸው ነው ። በግብጽ ሁለት መቶ ዐሥራ አምስት ። በባቢሎን ሰባ ዘመን ተገዝተዋል ።

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ። ሮሜ፡፮፡ ፲፮ ፪ ጴጥ፡፪፡ ፲፱ ።

፴፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ አማን አማን እብለክሙ ኵሉ ዘይገብራ ለኃጢአት ገብራ ውእቱ ለኃጢአት ።
ኃጢአት የሚሠራ ሁሉ የኃጢአት ተገዥ ነው ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፴፭ ወገብርሰ ኢይነብር ውስተ ቤት ለዝሉፉ
፴፭ የኃጢአት ተገዥ ማለት ኃጥእ በመንግሥተ ሰማይ አይኖርም ። ወወልድስ ይነብር ለዓለም ። ምእመን ግን በመንግሥተ ሰማይ ይኖራል ። ፩ም ወገብርሰ እያልክ መልስ ። ገብር ሙቤ በምእመን አድሮ አይመግብም ። ወወልድስ እኔ ግን አድሬ እመግባለሁ ። አንድም ባሪያ በጌታው ቤት አይኖርም ይሸጠው ይለውጠው ማጫ ጥሎት አሳልፎ ይሰጠውም እንደሆነ አያውቅምና ። ወወልድስ ልጅ ግን ለዘለዓለም በቤት ይኖራል ይህ ሁሉ የለበትምና ።

፴፮ ወእም ከመስ ወልድ አግዐዘክሙ አማን ግዑዛን አንትሙ ።

፴፮ እኔ ነጻ ካወጣኋችሁ በውነት ነጻ ናችሁ ።
፴፯ ወአእምር ከመ ዘርዓ አብርሃም አንትሙ ።
፴፯ የአብርሃም ልጆች ነን እንድትሉስ አውቃለሁ ።
ወባሕቱ ተሐሥሡ ትቅትሉኒ ።
የአብርሃም ልጅ ባትሆኑ ልትገሉኝ ትሻላችሁ እንጂ ።
እስመ ኢይነብር ቃልየ ኀቤክሙ ።
ትምህርቴን አትቀበሉኝምና ።

፴፰ ወአንሰ ዘርኢኩ በኀበ አቡየ እነግር ።
፴፰ እኔ ካባቴ በሀልውና ያየሁትን አስተምራለሁ ።
ወአንትሙሰ ዘርእክሙ በኀበ አቡክሙ ትገብሩ ።
እናንተ ግን ካባታችሁ ከሰይጣን የሰማችሁትን ትሠራላችሁ ።

፴፱ ወአውሥኡ ወይቤልዎ ለነሰ አብርሃም አቡነ ።

፴፱ እኛስ የአብርሃም ልጆች ነን አሉት ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሶበሰ ውሉደ አብርሃም አንትሙ ግብረ አብርሃም እምገበርክሙ ።
የአብርሃም ልጆችስ ብትሆኑ የአብርሃምን ሥራ በሠራችሁ ነበር አላቸው ።
ወቃሎሂ እምዓቀብክሙ ወኪያየሂ እምአፍቀርክሙኒ ።
ሕጉን በጠበቃችሁ እኔንም በወደዳችሁ ነበር ።

፵ ወይእዜሰ ተኀሥሡ ትቅትሉኒ ብእሴ ጻድቀ ዘጽድቀ እነግረክሙ ዘሰማዕኩ በኀበ እግዚ አብሔር ።

፵ ነገር ግን ዛሬ ከእግዚአብሔር ዘንድ የሰማ ሁትን እውነተኛ ትምህርት የማስተምራችሁን እውነተኛ መምህር እኔን ልትገሉኝ ትሻላችሁ ።
ወአብርሃምሰ ኢገብረ ከመዝ ።
አብርሃምስ እንዲህ ያለ ሥራ አልሠራም ፤ አስተም ረውት አላምንም ማለቱ ይቅርና ያስተማረው ሳይ ኖር በእእምሮ ጠባይዕ ዐውቆ በሥነ ፍጥረት ተመራ ምሮ አመነ እንጂ ። አንድም አብርሃምስ እንዲህ አላደረገም ሰው ልግደል ማለቱስ ቀርቶ ከተመሳ ቀለ መንገድ አራት ደጅ ያላት ቤት ሠርቶ የቴራበ እያበላ የተጠማ እያጠጣ የታረዘ እያለበሰ ነፍስ ያድን ነበር እንጂ ።

፵፩ አንትሙሰ ትገብሩ ግብረ አቡክሙ ።
፵፩ እናንተስ ያባታችሁን የሰይጣንን ሥራ ትሠራላችሁ ።
ወይቤልዎ ንሕነሰ ኢተወለድነ እምዝሙት ።
እኛስ ከሰይጣንም አልተወለድንም ።
አላ አሐዱ አብ ብነ ።
ከአብርሃም ተወልደናል እንጂ አንድ አባት አለን እንጂ ።
ወውእቱ እግዚአብሔር ።
ያውም እግዚአብሔር ነው ።
አንድም አብርሃም በአምልኮተ ጣዖት ሳለ የወለደው ልጅ ኑሮት ከርሱ አልተወለድንም አለ አሐዱ አብ ብነ ። በአምልኮተ እግዚአብሔር ሳለ ከወለደው ከይስሐቅ ተወልደናልና አንድ አባት አለን ያውም እግዚአብሔር ነው እንጂ ። አንድም ንሕነሰ ኢተወ ለድነ ፤ በሴሰኝነት ከተወለደው ከኤስማኤል አልተ ወለድንም በሩካቤ ዘበሕግ ከተወለደው ከይስሐቅ ተወልደናልና አንድ አባት አለን እንጂ ያውም እግ ዚአብሔር ነው ።

፵፪ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሶበሰ እግዚ አብሔር አቡክሙ እምአፍቀርክሙኒ ኪያየ ።

፵፪ እግዚአብሔርስ አባታችሁ ቢሆን እኔን በወደዳችሁኝ ነበር ።
ወቃልየኒ እምዓቀብክሙ ።
ሕጌንም በጠበቃችሁ ነበር ።
እስመ አነ እምኀበ እግዚአብሔር ወፃእኩ ወመ ጻእኩ ።
እኔ ከእግዚአብሔር አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእ ምባሕርይ ተወልጄ መጥቻለሁና ።
ወአኮ ለልየ ዘመጻእኩ ።
በኔ ፈቃድ ብቻ ሰው አልሆንኩም ።
አላ ውእቱ ዘፈነወኒ ።
በላከኝ ባባቴም ፈቃድ ነው እንጂ ።

፵፫ አፎ እንከ ተአምኑ ቃልየ ።
፵፫ በኔ ማመን እንደ ምን ይቻላችኋል ።

እስመ ትከሉ ሰሚዓ ነገረ ዚአየ ።
ትምህርቴን አትቀበሉኝምና ።

፵፬ አንትሙሰ እምአቡክሙ ሰይጣን አንትሙ፤ ፩ ዮሐ፫ ፡ ፰ ።

፵፬ እናንተስ ካባታችሁ ከሰይጣን ወገን ናችሁ። ወፍትወቶ ለአቡክሙ ትፈቅዱ ትግበሩ ።
ያባታችሁ የሰይጣንን ፈቃድ ልትሠሩ ትወዳላችሁ ።
ወውእቱ ቀታሌ ነፍስ ሰብእ ውእቱ እምጥንቱ ።
እርሱ ከጥንት ጀምሮ ነፍስ ገዳይ ነው ፤ በቃየል አድሮ አቤልን ሲያስገድል ማን ነገረው ።
ወኢይቀውም በጽድቅ ።
በውነት ጸንቶ አይኖርም ፤ እምላክነትን ሲሻ ማን አስተማረው ።
እስመ አልቦ ጽድቅ በኀቤሁ ።
በርሱ ዘንድ እውነት የለምና ።
ወሶበሂ ይነብብ ሐሰተ እምዚአሁ ይነብብ ።
ሐሰትን በተናገረ ጊዜ ከራሱ አንቅቶ ይናገራል ።
አንድም በተናገረ ጊዜ ሐሰትን ከራሱ አንቅቶ ይና ገራል ።
እስመ ሐሳዊ ውእቱ ።
ሐሰተኛ ነውና ።
ወአቡሃ ለሐሰት ።
የሐሰት ነቋ መገኛዋ ነውና ዓመፃ ወዕአት እመዛ ግብቷሃ እንዲል ።

፵፭ ወአንሰ እስመ ጽድቀ እነግር ወኢተአ ምኑኒ ።

፵፭ እኔ እውነት ባስተምር አትቀበሉኝም ፤ መኑ ማንሻ ። አንድም እኔ እውነት ባስተምር ባት ቀበሉኝ ።

፵፮ መኑ እምኔክሙ ዘይዛለፈኒ በእንተ ኃጢ አት ።

፵፮ ከእናንተ ወገን ስለ ኃጢአት የሚወቅሰኝ ማለት ኃጢአት ሠርተሃል ብለው አልሠራሁም የሚለኝ ማነው ። አንድም ኃጥእ ነህ ብለው መልሶ ኃጥእ ነህ የሚለኝ ማነው ። በገቢርም እንዳልሠራ ለማጠየቅ እንዲህ አለ ። በነቢብም እንዳልሠራ ለማጠየቅ ነቢይ ኢገብረ ኃጢአተ ወኢተረከበ ሐሰተ ውስተ አፉሁ ብሎ መስክሮለታል በሐልዮም እንዳ ልሠራ ለማጠየቅ ይመጽእ መልአኩ ለዝንቱ ዓለም ወኢይረከብ በላዕሌየ ወኢምንተኒ ብሏል ። ፍጹማን ነን በሚሉ ሰዎች ዘለፋ ሊሆንባቸው እን ዲህ አለ ።

ወእመሰ አነ ጽድቀ እነግር ለምንት ኢተአምኑኒ ።
እኔ እውነትን የማስተምር ከሆነ የማትቀበሉኝስ ለምን
ነው ።

፵፯ ዘሰ እምእግዚአብሔር ውእቱ ቃለ እግ
ዚአብሔር ይሰምዕ ።

፵፯ ከእግዚአብሔር የተገኘ የእግዚአብሔር
ወገን የእግዚአብሔርን ነገር ይሰማል ይቀበላልም ።
ወበእንተ ዝንቱ አንትሙሰ ኢትሰምዑኒ እስመ
ኢኮንክሙ እምእግዚአብሔር ።
እናንተ ግን የእግዚአብሔር ወገን አይደላችሁምና
ስለዚህ አትቀበሉኝም ።

፵፰ ወተሰጥውዎ አይሁድ ።
፵፰ አይሁድም መለሱለት ።
ወይቤልዎ አኮኑ ሠናየ ንቤለከ ከመ ሳምራዊ አንተ ፤
ሳምራዊ እንደሆንከ ።
ወጋኔን ብከ ።
ሎቱ ስብሐት ፤ ጋኔን አድሮብሀ እንዳለ በውነት
ነግረንሀ የለምን አሉት ። ሳምራዊ ያይወልደው
ያዕቆብን ያዕቆብ አቡነ እንዲል ፤ አንተም ያይወ
ልድሀ እግዚአብሔርን አባቴ ትላለሀ ለማለት ።

፵፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ
አንሰ ጋኔን አልብየ ፤

፵፱ ጌታም መለሰ ሳምራዊ ላሉት አይመል
ስላቸውም በስመ ትዕይርቱ ተጠቅመንበታልና ፤
እኔስ ጋኔን የለብኝም አላቸው ።
ወባሕቱ አከብር አባየ ፤
ነገር ግን አባቴን አከብራለሁ ፤
አከብር ።
አከብር ዘንድ ነው እንጂ ፤
ወአንትሙሰ ታስተሐቅሩኒ ።
ትንቁኛላችሁ ማለት እናንተ ግን ዕሩቅ ብእሲ ትሉ
ኛላችሁ ።

፶ አንሰ ኢየኃሥሥ ተድላ ለርእስየ ።

፶ እኔ ራሴን ደስላለኝ አልሻም ማለት የሌ
ለኝን አምላክነት አምላክ ነኝ ብዬ አላስተምርም።
ሀሎ ዘየኃሥሥ ሊተ ፤
የሚመሰክርልኝ አባቴ አለ ።
ወዘሂ ይኴንን ።
የሚያስተምርልኝ፥ አንድም ባታምኑ የሚፈርድልኝ።

፶፩ አማን አማን እብለክሙ ዘዓቀበ ቃልየ
ኢይጥዕም ለሞት ለዓለም ።

፶፩ ሕጌን የጠበቀ ለዘለዓለም ሞት የለበትም
ብዬ በውነት እንግራችኋለሁ በሥጋ ቢሞት በነፍስ
አይሞትም ፈርሶ በስብሶ አይቀርም ትንሣኤ ዘለ
ክብር ይነሣል ።

፶፪ ወይቤልዎ አይሁድ ይእዜሰኬ አእመርናከ
ከመ ጋኔን ብከ ።

፶፪ ሎቱ ስብሐት ፤ ጋኔን አድሮብሀ እንዳለ
ገና ዛሬ ዐወቅን ።
አብርሃም ጥቀ ሞተ ።
አብርሃም ስንኳ ሞተ
ወነቢያትኒ ሞቱ ፤
ነቢያትም ሞቱ ።
ወአንተሰ ትብል ዘዓቀበ ቃልየ ኢይጥዕም ለሞት
ለዓለም ።
አንተ ግን ሕጌን የጠበቀ ሞት የለበትም ትላለሀ ።

፶፫ አንተኑ ተዓቢ እምአብርሃም አቡነ ዘሞተ ።
፶፫ ከሞተ አባታችን ከአብርሃም አንተ ትበ
ልጣለሀን ።
ወእምነቢያትኒ እለ ሞቱ ።
ከሞቱ ከነቢያት ትበልጣለሀን ፤
መነ ትረሲ ርእሰከ ።
ማንኛ ትላለሀ መጽላት ምቀኝነት ፈራሽ ነገር አና
ገራቸው ለልማዱ ጠባቂውን ከጠባቂ አስጠባቂውን
ካስጠባቂ አነጻጽሮ መናገር ይገባ ነበር እርሳቸው
ግን አስጠባቂውን ከጠባቆች አነጻጽረው ተናገሩ ።

፶፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፶፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ እመሰ ለልየ ሰባሕኩ ርእስየ አይበ
ቍዓኒ ስብሐትየ ወኢምንተኒ ።
እኔ ራሴን ባከብር ምስጋናዬ አይረባኝም አይጠ
ቅመኝም ።
ሀሎ አቡየ ዘይሴብሐኒ ።
የሚያከብረኝ አባቴ አለ ፤ አንድም እኔ ራሴን ባመ
ሰግን ምስጋናዬ ባይረባኝ ባይጠቅመኝ የሚያከብ
ረኝ አባቴ አለ ።
ዘአንትሙ ትብልዎ አምላክነ ውእቱ ።
እናንተ አምላካችን የምትሉት ፤

፶፭ ወኢተአምርዎ
፶፭ የማታውቁት ፤

ወአንሰ አአምሮ ፤
እኔ ግን አውቀዋለሁ ።
ወእመሰ እቤ ኢየአምሮ እከውን ከማከሙ ሐሳዌ
ወአንሰ አአምሮሂ ።
እኔ ግን አውቀዋለሁ አላውቀውም ብል እንደናንተ
ሐሰተኛ ሆንኩ ።
ወቃሎሂ አዓቅብ ።
ሕጉንም እጠብቃለሁ ፤

፶፮ አብርሃም አቡክሙ ተመነየ ከመ ይርአይ
ዕለትየ ።
አንተኑ ተዓቢ እምአብርሃም ።

፶፮ እቡን ብለውት ነበርና ፤ አባታችሁ አብ ርሃም የምወለድበትን ቀን ሊያይ ተመኘ ። ተነበየ ጸለየ ፈተወ ይሳል ወደደ አመለከተ በል ።
ወርእየኒ ወተፈሥሐ ።
አይቶም ደስ አለው ።

፶፯ ወይቤልዎ አይሁድ ኀምሳ ዓመት አል ብከ በእፎ አብርሃምሃ ርኢከ ፤

፶፯ ኀምሳ ዓመት ያልሞላህ አብርሃምን እን ደምን አየህ አሉት ። ምን ይዘው እንዲህ አሉት ቢሉ በሃያ ዓመት ደግ ሹመት ይሾማሉ ሃያ አምስት ዓመት አገልግለው ዝቅ ያለ ሹመት ይሾማሉና ።

፶፰ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን አማን እብለከሙ እምቅድመ ይትወለድ አብርሃም ሀሎኩ አነ ።

፶፰ አብርሃም ሳይፈጠር ነበርኩ ብዬ እንደ ነበርኩ በውነት እነግራችኋለሁ አላቸው ፤
አሪት ዘልደት እንዲል ፤ ከአብርሃም አስቀድሞ ታራስ አልነበረምን ቢሉ በአብርሃም መላውን መናገር ነው

፶፱ ወነሥኡ አይሁድ እብነ ከመ ይውግርዎ ።
፶፱ ሊጣሉት አይሁድ ደንጊያ አነሱ ። ብእሴ ጻድቅ ያሰው ማኅደር ፤ እምቅድመ ይትወለድ ያለ ውን ኀዳሪ ነው ይላል ፈረንጅ ነሥኡ እብነ ከመ ይውግርዎ ባለው ይረታል ።
ወተኀብኦሙ እግዚእ ኢየሱስ ወወፅአ እምኵራብ ወኃለፈ እንተ ማእከሎሙ ።
ከምኵራብ ወጥቶ በመካከላቸው አልፎ ሄደ ፤ ረቂቅ መለኮት እንደሆነ ከረቂቅ መለኮት ጋራ እንደ ተዋ ሐደ ለማጠየቅ ።

ዘከመ ፈወሶ ለዘዕውሩ ተወልደ ።
ምዕራፍ ፱ ።

፩ ወእንዘ የኃልፍ እምህየ ርእየ ብእሴ ዘዕ ውሩ ተወልደ እምከርሠ እሙ ።

፩ እምቅድመ ይትወለድ አብርሃም ሀሎኩ አነ ብሎ ነበርና ።
እስመ ሰምዓ ቃላቲሁ ምግባሩ ውእቱ እንዲል ነገ ሩን በሥራው ለማስረዳት ያመጣዋል ከዚያ አልፎ ሲሄድ ከናቱ ማኅፀን ጀምሮ ዕውር ሁኖ የተወለደ ሰው አገኘ ። ዕውር ሁኖ ተወልዷል ቢሉ የተመቸ አንድም ልሙጽ ሁኖ ተወልዷል ።

፪ ወተስእልዎ አርዳኢሁ ወይቤልዎ ረቢ በኃጢአተ መኑ ተወልደ ዝንቱ ዕውር ።

፪ መምህር ሆይ ይህ ሰው ዕውር ሁኖ የተ ወለደ በማን ዕዳ ነው ብለው ደቀ መዛሙርቱ ጠየቁት።

በዘርእሱኑ ፤ በራሱ ዕዳ ነውን ፤ ተነክሩ ኃጥአን እማኅፀን ያለውን ይዘው ።
ወሚመ በዘአዝማዲሁ ። ወይም ባባት በናቱ ዕዳ ነውን ዕውር ሆኖ ይወለድ ዘንድ ። ሕፃናት አብዕልት ይመውቱ በጌጋየ ወላድያኒሆሙ ያለውን ይዘው ፤

፫ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ኢውእቱ አበሰ ።
፫ በርሱም ዕዳ አይደል ። ወኢአዝማዲሁ ባባት በናቱም ዕዳ አይደል ።
ዳዕሙ ከመ ያስተርኢ ግብረ እግዚአብሔርበላዕሌሁ።
የእግዚአብሔር ሥራ በርሱ ይገለጥበት ዘንድ ነው እንጂ ማለት አምጻኤ ዓለማትነቱ ከሃሊነቱ ጌትነቱ ተአምራቱ መግቦቱ ዓይን ነሥቶ ዓይን ለሌለው ዓይን ሰጥቶ መመገቡ ይታወቅ ዘንድ ነው እንጂ አላቸው ።

፬ ወባሕቱ ርቱዕ ሊተ እግበር ግብሮ ለዘፈ ነወኒ እንዘ መዓልት ውእቱ ።
፬ ነገር ግን መዓልት ዕድሜዩ ሳለ ያባቴን ሥራ ሠርቼ እናንተን ማሳመን ይገባኛል ።
እስመ ትመጽእ ሌሊት ዘኢይክል ቦቱ አሐዱ ሂገቢረ።
አንዱ ስንኳ ሥራ ሊሠራበት የማይችልበት ሞት አለብኝና ከፍዳ የነጻንበትን ልጅነት ያገኘንበትን ሞቱን ስለምን በሌሊት መሰለው ቢሉ ሰው በመ ዓልት የሚሠራውን በሌሊት እንዳይሠራው እር ሱም በሕይወተ ሥጋ ሳለ የሚሠራውን ከሞተ በኋላ አይሠራውምና አንድም ፤
ዘኢትክሉ ቦቱ ገቢረ አሐዱሂ እምዘ ሀሎ ውስተ ዓለም ።
በዚህ ዓለም ካለው ሥራ አንዱን ስንኳ ልትሠሩበት የማትችሉበት ሞት አለባችሁና መዓልት ዕድሜያችሁ ሳለ ያባቴን ሥራ ሠርቼ እናንተን ማሳመን ይገባኛል።

፭ እንዘ ሀሎኩ ውስተ ዓለም አነ ውእቱ ብርሃኑ ለዓለም ።

፭ በዚህ ዓለም ሣለሁ የሰው ዕውቀቱ እኔ ነኝ።
፮ ወዘንተ ብሂሎ ወረቀ ውስተ ምድር ።
፮ ይኸን ተናግሮ ምራቁን ትፍ አለ ።
ወገብረ ጽቡረ በምራቁ ።
በምራቁም ጭቃን ለወሰ ።
ወቀብዖ አዕይንቲሁ ለውእቱ ዕውር ።
የዚያን ዕውር ዓይኑን ቀባው ።

፯ ወይቤሎ ሑር ተሐፀብ በምጥማቃተ ሰሊ ሆም ።

፯ ሂደህ በፈሳሽ ውኃ ተጠመቅ አለው ።
ዘበትርጓሜሁ ሐዋርያ ።
ፈላሽ ማለት ነው ፤ ሑር ማለቱ አራቱ ባሕርያት እንዲተካከሉለት ሦስቱ ከዜህ አሉ ነፋስ ሲሄድና ሲመለስ እንዲተካከልለት ። አንድም እየተመራ ሂዶ እያየ ቢመለስ ተአምራቱ ድንቅ ይባላልና

ወሖረ ወተሐፀበ ።
ሂዶ ተጠመቀ ።
ወገብአ እንዘ ይሬኢ ።
እያየ ተመለሰ ።

፰ ወአግዋሪሁሰ ወእለሂ የአምርዎ ትካት ወይሬእይዎ እንዘ ይስእል ይቤሉ ።

፰ ጐረቤቶቹ ቀድሞ ሲለምን እንደነበረ የሚያውቁት ዕውር እንደሆነ ።
አኮኑ ዝንቱ ውእቱ ዘይነብር ውስተ ፍኖት ወይስእል ይህ በመንገድ ተቀምጦ ይለምን የነበረው አይደለምን አሉ ።

፱ ወቦ እለ ይቤሉ ውእቱ ዝንቱ ፤
፱ ነው ያሉም አሉ ።
ወካልዓን ይቤሉ አልቦ ።
ሌሎቹም እርሱ አይደለም ፤
አላ ይመስሎ ፤
ይመስለዋል እንጂ አሉ ፤
ወለሊሁሰ ይቤ አነ ውእቱ ።
እርሱ ግን እኔ ነኝ አለ ።

፲ ወይቤልዎ እፎ ተከሥታ አዕይንቲከ ።
፲ ዓይንህ እንደምን በራልህ አሉት ።

፲፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ብእሲሁ ዘስሙ ኢየሱስ ጽቡረ ገብረ በምራቁ ወቀብዓኒ አዕይንትየ።
ኢየሱስ የሚባል ሰው በምራቁ ጭቃ ለውሶ ዓይኔን ቀባኝ ።
ወይቤለኒ ሑር ተሐፀብ በምጥምቃተ ሰሊሆም ።
ሂደህ በፈሳሽ ውኃ ተጠመቅ አለኝ ።
ወሖርኩ ወተሐፀብኩ ፤
ሄጄ ተጠመቅሁ ፤
ወርኢኩ ፤ አየሁ አላቸው ።

፲፪ ወይቤልዎ አይሁድ አይቴ ውእቱ ብእሲሁ
፲፪ ያሰው የት አለ አሉት ።
ወይቤሎሙ ኢየአምር ።
አላውቅም አላቸው ።

፲፫ ወወሰድዎ ኀበ ፈሪሳውያን ለውእቱ ዘዕውሩ ተወልደ ።

፲፫ ለኛ ብትነግረን አለቆች በጢጢ በሳንባ ጠለፍ ገርፈው ያናግሩህ የለምን ብለው ወደ ፈሪሳውያን ይዘውት ሄዱ ።

፲፬ እስመ ሰንበት አሚሁ አመ ገብረ እግዚእ ኢየሱስ ጽቡረ በምራቁ ወከሠቶ አዕይንቲሁ ።

፲፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በምራቁ ጭቃ ለውሶ ዓይኑን ያዳነበት ቀኑ ቅዳሚ ነበርና ። ወሰንበት አሚሁ ቀኑ ቅዳሚ ነበር ።

፲፭ ወተስእልዎ ካዕበ ፈሪሳውያን ዘከመ እፎ ርእየ ።

፲፭ ለብላቴኖቻቸው ካዕበ አለ ። አንድም እንደ ዳን ፈሪሳውያን ሁለተኛ ጠየቁት ።
ወይቤልዎ እፎ ርኢከ ።
እንደምን ዳንህ አሉት ።
ወይቤሎሙ ጽቡረ ገብረ በምራቁ ወወደየ ውስተ አዕይንትየ ።
በምራቁ ጭቃ ለውሶ ካይኔ አገባልኝ ።
ወሖርኩ ወተሐፀብኩ ወርኢኩ ።
ሔጄ ተጠምቄ ዳንኩ አላቸው ። ቢጋሩ ያለ ነው ቢሉ እንደእንዝርት ራስ ቀርጾ ያገባለታል ይህስ እንዳይሆን አዳም በዠር ያልሆነበት ሥጋ አይፈጥርም ብሎ እንደ ሥዕል ማይ ይነድፍለታል ፤ ጽጌያት ከአዕጹቃቸው እንዲፈነዱ ከባሕርዩ ያነቃለታል።
፲፮ ወቦ እለ ይቤሉ እምፈሪሳውያን ። ዝንቱ ብእሲ ኢኮነ እምእግዚአብሔር ዘኢየዓቅብ ሰንበተ ።
፲፮ ከፈሪሳውያን ወገን የሚሆኑ ሰዎች ቅዳሜን የማያከብር ይህ ሰው ደግም አይደለም ያሉም አሉ ።
ወቦ እለ ይቤሉ በአይቴ ይክል ብእሲ ኃጥእ ገቢረ ዘከመዝ ተአምረ ።
ኃጥእ ሰው በደረቅ ግንባር ዓይን መፍጠር እንደምን ይቻለዋል ያሉም አሉ ።
ወተናፈቁ በበይናቲሆሙ በእንተ ዝንቱ ነገር ። ኃጥእ ነው አይደለም በማለት እርስ በርሳቸው ጸብ ሆነ ተለያዩ ።

፲፯ ወይቤልዎ ካዕበ ለውእቱ ዕውር ምንተ ትብል አንተ በእንቲአሁ እስመ ከሠተከ አዕይንቲከ።

፲፯ ሁለተኛ ያነን ዕውር ዓይንህን አብርቶል ሃልና አንተ የርሱን ነገር ምን ትፈርዳለህ አሉት ።
ወይቤሎሙ ነቢይ ውእቱ ፤
እርሱም መለሰ ዓለም ። ነቢየ ያነሥእ ለክሙ ተብሎ የተነገረለት ነቢይ ነው ።

፲፰ ወኢአምንዎ አይሁድ ከመ ዕውሩ ተወልደ ወርእየ ።

፲፰ ዕውር ሁኖ ተወልዶ ኋላ እንደዳነ አይሁድ አላመኑም ።

፲፱ እስከ ጸውዑ አዝማዲሁ ለዘርእየ ።
ዘመዶቹን ጠርተው እስቲጠይቁ ድረስ ።
ወተስእልዎሙ ወይቤልዎሙ ዝኑ ውእቱ ወልድክሙ ዘትብሉ ዕውሩ ተወልደ ።

፲፱ ጠየቋቸውም እንዲህ ሲሉ ዕውር ሁኖ የተወለደ የምትሉት ይህ ልጃችሁ ነውን ።
ወበእፎ እንከ ይእዜ ይሬኢ ።

ዛሬስ እንደምን ዳነ ብለው ጠየቋቸው ።

፳ ወአውሥኡ አዝማዲሁ ።
፳ እናት አባቱም መለሱ ።
ወይቤሉ ነአምር ከመ ዝንቱ ውእቱ ወልድነ ።
ልጃችን ይህ እንደሆነ ።
ወከመሂ ዕውሩ ተወልደ ።
ዕውር ሁኖም እንደተወለደ እናውቃለን አሉ ።

፳፩ ወይእዜሰ ዘከመ እፎ ይሬኢ ።
፳፩ ዛሬ ግን እንደምን እንደዳነ ።
አው መኑ ከሠቶ አዕይንቲሁ ኢነአምር ።
ማንም ዓይኑን እንዳዳነው አናውቅም ።
ኪያሁ ተሰአልዎ ።
እርሱን ጠይቁት ።
እስመ ልሂቅ ውእቱ ።
ዐዋቂ ነውና ።

ወይክል ተናግሮ ለርእሱ ።
ለመናገር በቅቷል ፤

፳፪ ወዘንተ ይቤሉ አዝማዲሁ እስመ ይፈርህዎሙ ለአይሁድ ።

፳፪ አባት እናቱ አይሁድን ስለ ፈሩ ይህን ተናገሩ ።
እስመ አዘዙ አይሁድ ለእመ በ ዘአምነ ቦቱ ከመ ውእቱ ክርስቶስ ይሰደድ እምኵራብ ክርስቶስ እን ደሆነ ያመነበት ሰው ቢኖር ከምኵራብ ይለይ ብለው ዐዋጅ ነግረው ነበርና ።

፳፫ ወበእንተ ዝንቱ ይቤሉ አዝማዲሁ ልሒቅ ውእቱ ሎቱ ተሰአልዎ ።

፳፫ ስለዚህ አባት እናቱ ዐዋቂ ነው ለመናገር በቅቷል እርሱን ጠይቁት አሉ ።

፳፬ ወጸውዕዎ ዳግመ ለውእቱ ብእሲ ዕውር ።
፳፬ ሁለተኛም ያነን ዕውር የነበረውን ሰው ጠሩት ።
ሀቡ ስብሐተ ለእግዚአብሔር ።
ይህ ሰው አላዳነህም እግዚአብሔር ነውና ያዳነህ ሂደህ እግዚአብሔርን አመስግን ።
ንሕነሰ ነአምር ከመ ኃጥእ ውእቱ ዝብእሲ ።
ይህ ሰው ግን ኃጥእ እንደሆነ እኛ እናውቃለን ።

፳፭ ወአውሥአ ውእቱ ብእሲ ዕውር ።
፳፭ ያም ሰው መለሰ ።
ወይቤሎሙ አንሰ ኢየአምር ከመ ኃጥእ ውእቱ ።
እኔ ኃጥእ መሆኑን አላውቅም ።
ወዘንተ ባሕቱ አአምር ከመ ዕውር አነ ።
ዕውር ሁኜ እንደተወለድሁ ።
ወይእዜኒ እሬኢ ።
ዛሬ እንደ ዳንሁ ይህን ብቻ አውቃለሁ እንጂ ።

፳፮ ወይቤልዎ ካዕበ ምንተ ገብረ ለከ ።
፳፮ ለቀረበው ካዕበ አለ ፤ ሁለተኛ ምን አደረገልህ ።
ወእፎ ከሠተከ አዕይንቲከ ።
ዓይንህንስ እንደምን አዳነህ አሉት ።

፳፯ ወአውሥአ ወይቤሎሙ ነገርኩክሙሂ ዳዕሙ ወኢትሰምዑ ወኢተአምኑኒ ።

፳፯ አትሰሙኝም አታምኑኝም እንጂ እኔስ ነገርኋችሁ ።
ምንተ እንከ ትፈቅዱ ካዕበ ትስምዑ ።
ሁለተኛ ምን ልትሰሙ ትወዳላችሁ ።
አንትሙኒ አርዳኢሁኑ ትኩኑ ትፈቅዱ ።
እናንተም የሱ ደቀ መዛሙርት ልትሆኑ ትወዳላችሁን አላቸው ።

፳፰ ወጸአልዎ ፤
፳፰ የዕውር ስድብ ሰደቡት ጠንባሳ ዕውር ብለው ። እንድም ሌላ ስድብ ሰደቡት ።
ወይቤልዎ አንተ ኩን ረድአ ሎቱ ።
አንተ ለርሱ ደቀ መዝሙር ሁነው ።
ወንሕነ አርዳኢሁ ለሙሴ ንሕነ ።
እኛስ የሙሴ ደቀ መዛሙርት ነን ።

፳፱ ወንሕነ ነአምር ከመ ለሙሴ ተናገሮ እግዚአብሔር ገጸ በገጽ ።

፳፱ ሙሴን ቃል ለቃል እንደተነጋገረው እናውቃለን ።
ወለዝንቱሰ ኢነአምሮ እምአይቴ ውእቱ ።
ይኸን ግን ከወዴትም እንደመጣ አናውቀውም አሉ ።

፴ ወአውሥአ ውእቱ ብእሲ ።

፴ ያም ሰው መለሰ ።

ወይቤሎሙ ዓዲ በዝንቱ ጥቀ መንከር ውእቱ ዘኢተአምርዎ አንትሙ እምአይቴ ውእቱ ወከሠተኒ አዕይንትየ ።
ቢሆን ተአምራቱን አይቶ ማመን ይገባ ነበር ።
በዝንቱ ፤

ተአምራቱን አይታችሁ ባለማመናችሁ ላይ ዓይኔን ያዳነኝን ከየትም እንደመጣ የማታውቁትን ኃጥእ ነው ማለታችሁ እጅግ ድንቅ ነው ። አንድም ተመራምሮ ዐውቆ ማመን ይገባ ነበር ፤ ተመራምራችሁ ባለማመናችሁ ላይ እኔን ያዳነኝን ከወዴትም እንደመጣ የማታውቁትን ኃጥእ ነው ማለታችሁ እጅግ ድንቅ ነው ።

፴፩ ወንሕነስ ነአምር ባሕቱ ከመ ለኃጥአን ኢይሰምዖሙ እግዚአብሔር ።

፴፩ እኛ ኃጥአንን እግዚአብሔር እንዳይቀበላቸው እናውቃለን ።
እመኒ አብዛኅከሙ ምህላከሙ ኢይሰምዓከሙ እግዚአብሔር እስመ ደም ምሉእ ውስተ እደዊክሙ እንዲል ።
ዘእንበለ ዘያፈርሆ ለፈራሂ ወለዘይገብር ፈቃዶ ሎቱ ይሰምዖ ።
የሚፈራውን ፈቃዱን የሚሠራውን ይሰማዋል እንጂ።
ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ጻድቅ ወፈራሄ እግዚአብሔር ወረከብክዎ ለዳዊት ገብርየ ብእሴ ምእመነ ዘከመ ልብየ እንዲል ።

፴፪ ግሙራ ኢተሰምዓ እምአመ ተፈጥረ ዓለም ከመ ቦ ዘዕውሩ ተወልደ ወተከሥተ አዕይንቲሁ ።

፴፪ ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ዕውር ሁኖ የተወለደ ኋላ ዓይኑ ያየ ከቶ ተሰምቶም አያውቅም ይህ ሰው ትውልዱ ከእስራኤል ነው ያሉ እንደሆነ ተወልደን ከአሕዛብ ነው ቢሉ ተክሥተን ይሻል ፤ ከብዛት አንድ አንድ አይታጣምና ።

፴፫ ሶበሰ ኢኮነ እምኀበ እግዚአብሔር ዝንቱ ብእሲ እምኢክህለ ገቢረ ወኢምንተኒ ።

፴፫ ይህ ሰው ደግ ባይሆንስ ተአምራት ማድረግ ባልተቻለውም ነበር ።

፴፬ ወአውሥኡ አይሁድ ወይቤልዎ ዘለሊከ በኃጢአትከ ተወለድከ አንተሁ ትሜህረነ ለነ ።

፴፬ ዘዘኍኔ ቀድሞ ባዮች ናቸውና የኋላ ኃጢአትክን ፀውቆ ዕውር አድርጎ ቢፈጥርህ አንተ ለኛ ታስተምራለህ አሉት ።
ወሰደድዎ ወአውፅእዎ አፍአ ከምኵራብ አወጡት ከሰው ለዩት ።

፴፭ ወሰምዓ እግዚእ ኢየሱስ ከመ አውፅእዎ አፍአ ።

፴፭ ከምኵራብ እንዳወጡት ከሰው እንደ ለዩት ጌታ ሰምቶ ።
ወረከቦ ።
አገኘው አኒያ ቢለዩዋችሁ እኔ አልለያችሁም ሲል ።
ወይቤሎ ተአምንሁ አንተ በወልደ እግዚአብሔር ።
አንተ በእግዚአብሔር ልጅ ታምናለህን አለው ።

፴፮ ወአውሥአ ወእቱ ብእሲ ።
፴፮ ያም ሰው መለሰ ።
ወይቤሎ መኑ ውእቱ ወልደ እግዚአብሔር ከመ እእመን ቦቱ ።
እምንበት ዘንድ ወልደ እግዚአብሔር ማነው አለው ።

፴፯ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዘትሬእዮ ወዘ ይትናገር ምስሌከ ውእቱ ዝንቱ ።

፴፯ የምታየው ካንተ ጋራ የሚነጋገረው ነው ማለት እኔ ነኝ አለው ።

፴፰ ወይቤ ከሊሆ አመንኩ እግዚኦ ።
፴፰ አምናለሁ ብሎ አሰምቶ ተናገረ ።
ወሰገደ ሎቱ ፤ ሰገደለት ።

፴፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አንሰኬ መጻእኩ ለኰነኔ ዝንቱ ዓለም ።

፴፱ እኔ በሰው መፈራረጃ ልሆን መጥቻለሁ ላመነብኝ ልፈርድለት ባላመነብኝ ልፈርድበት ።
ከመ እለ ኢይሬእዩ ይርአዩ የማያዩ ያዩ ዘንድ ማለት ዐላዋቆች ነን የሚሉ ሐዋርያት ዐዋቆች ይሆኑ ዘንድ ልፈርድለት ላለው ።
ወእለኒ ይሬእዩ ይዑሩ ።
ዐዋቆች ነን የሚሉ ጸሐፍት ፈሪሳውያንም ዐላዋቆች ይሆኑ ዘንድ ልፈርድበት ላለው ።

፵ ወቦ እምፈሪሳውያን እለ ሀለዉ ምስሌሁ እለ ሰምዑ ዘንተ ወይቤልዎ ዕውራንኑ ንሕነኬ ።

፵ ከርሱ ጋራ ያለ ከፈሪሳውያን ወገን ይኸን ሰምተው ዕውራን የምትለው እኛን ነውን አሉት ።

፵፩ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ሶበሰ ዕውራን አንትሙ እምኢኮንክሙ ጌጋየ ።

፵፩ ጌታም ዕውራንስ ብትሆኑ ዕዳ ባልሆነ ባችሁም ነበር አላቸው ነውረ ሥጋ ከመንግሥተ ሰማይ አያወጣምና ።

ወይእዜሰ ንቡር ጌጋይክሙ ።
ጽሑፍ ሲል ነው ዛሬ በደላችሁ ታውቋል ።
እስመ ትብሉ ንሬኢ ወኢትሬእዩ ።
እናውቃለን ትላላችሁ አታውቁምና ።
ወበእንተ ዝንቱ ኢይትኃደግ ለክሙ ጌጋይክሙ ።
ስለዚህ ኃጢአታችሁ አይሰረይላችሁም ።

በእንተ ኖላዊ ኄር ።

ምዕራፍ ፲ ።

፩ አማን አማን እብለክሙ ዘኢቦአ እንተ አንቀጽ ውስተ ዓጸደ አባግዕ ወዓርገ እንተ ካልዕ ገጽ ሠራቂ ወፈያት ውእቱ ።
ስለ ሦስት ነገር ያመጣዋል አንሰ መጻእኩ ለኰነኔ ዝንቱ ዓለም ብሎ ነበርና ለምሕረትም እንደመጣ ለማጠየቅ ፤ ለዝንቱሰ ኢነአምሮ ብለውት ነበር ከየትም እንደመጣ ለማጠየቅ ኄር ኖላዊ አይደለም ብለውታልና ኄር ኖላዊ እንደሆነ ።

፩ ለማጠየቅ ።
እባግዕ ወዳሉበት ቦታ በበር ያልገባ እጥር ጥሶ፥ቅጥር እፍርሶ የገባ ሌባ ወንበዴ ነው ።

፪ ወዘሰ እንተ አንቀጽ ይበውእ ኖላዌ አባግዕ ውእቱ ።

፪ በበር የገባ ግን ባለቤት ነው ።
፫ ወሎቱ ሰዓፃዊኒ ያርኅዎ ፤

፫ ለርሱ በረኛውም ይከፍትለታል ።
ወአባግዕኒ ይሰምዓሁ ቃሎ ።
በጎችም ቃሉን ይሰሙታል ።
ወይጼውዖን ለአባግዒሁ በበአስማቲሆን ።
በጎችንም በየስማቸው ይጠራቸዋል ፤ ሶሪት ቆሪት ቀንዲት እያለ ።
ወያወፅኦን ወያወፍሮን ።
ያወጣቸዋል ያሠማራቸዋል ።

፬ ወሶበ እውፅአን ወአውፈሮን የሐውር ቅድሜሆን ።

፬ ካወጣቸው ካሠማራቸው በኋላም በፊት በፊት ይሄድላቸዋል ።
ወይተልዉሁ አባግዒሁ ።
በጎችም ይከተሉታል ።
እስመ የእምራ ቃሎ ።
ቃሉን ያውቁታልና ።
፭ ወለነኪርሰ ኢይተልዉሁ ።
፭ ሌላውን ግን አይከተሉትም ።
ጹጋ እላ ይጎይያ እምኔሁ ።
ይሸሹታል እንጂ ።
እስመ ኢየእምራ ቃሎ ፤
ቃሉን እያውቁትምና ፤ የእምራ ቢል የባለቤቱን ባልሆነ ምሳሌ እያስተምርም ብሎ እንደ ሙሴ እባግዕ እማን እማን እያልከ መልስ ፤ ትንቢት ተነግሮለት እግዚአብሔር እብ መስክሮለት ምእመናን ወዳሉ በት ወደዚህ ዓለም ያልመጣ ፤ ይህስ እንዳይሆን ወብየ ካልዓትኒ አባግዕ እለ ኢኮና እምዝንቱ ዓጸድ ብሎ ያመጣዋል ። ዓጸድ የተባለች ኢየሩሳሌም ናት ፤ ትንቢት ተነግሮለት እግዚአብሔር እብ መስክሮለት ምእመናን ወዳሉባት ወደ ኢየሩሳሌም በመምህርነት ያልመጣ ወዓርገ ትንቢት ሳይነገርለት እግዚእብ ሔር እብ ሳይመሰክርለት የመጣ የመምህርነት ሌባ ወንበዴ ነው ። እንደ ይሁዳ ዘገሊላ እንደ ቴዎዳስ ዘግብጽ ። ወዘሰ እንተ አንቀጽ ። ትንቢት ተነግሮ ለት እግዚአብሔር እብ መስክሮለት የመጣ ግን የመምህርነት ባለቤት ነው ። ወሎቱስ ። እባቱ ይመሰክርለታል ። እንድም መጻሕፍት ዮሐንስ ተአምራት ይመሰክሩለታል ። እንድም እማን ብለሀ መልስ ዓሠርቱ ቃላትን ይዘው በወንጌል ያላመኑ ዓሠርቱ ቃላትን ሳይዙ በወንጌል እናምና ለን የሚሉ ጸሐፍት ፈሪሳውያን ናቸው ። ወዘሰ ። ዓሠርቱ ቃላትን ይዘው እናምናለን የሚሉ ግን ሐዋርያት ናቸው ። ዓጸዊኒ ። እኔ እቀበላቸዋለሁ። እንድም ዘኢቦእ ብለህ መልስ ። ሕዋሳቱን በስበሰበ ዓሠርቱ ቃላትን በያዘ በሰቂለ ሕሊና በንቂሃ ልቡና በሆነ የማያድር ሕዋሳቱን ባልሰበሰበ ዓሠርቱ ቃላትን ባልያዘ በሰቂለ ሕሊና በንቂሐ ልቡና ሁኖ በሚኖር የማያድር ሰይጣን ነው ። ወዘሰ እንተ እንቀጽ። ሕዋሳቱን ባሰባሰበ ዓሠርቱ ቃላትን በያዘ በስቂለ ሕሊና በነቂሃ ልቡና በሆነ የሚያድር ግን መንፈስ ቅዱስ ነው ። እጸዊኒ። አእምሮ ይመሰክርለታል እንድም ዘኢቦእ ። በምክረ ካህን የማይኖር በምክረ ርእሱ በፈቃደ ርእሱ የሚኖር ኃጥእ ነው ። ወዘሰ በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን የሚኖር ግን ጻድቅ ነው ። ዓፃዊኒ ። አፃዊ እኔ በፅለተ ምጽእት እቀበለዋለሁ ወዓባግዕኒ ። ሐዋ ርያት ትምህርቱን ይቀበሉታል ። ወይጼውዖን ። ሐዋርያት ሰብዓ አርድዕት እያለ። አንድም ስምዖንን ጴጥሮስ ልብድዮስን ታዴዎስ ዲዲሞስን ቶማስ እያለ ይጸራቸዋል ። ያወፅኦን ወያወፍሮን ዘኢጾረ መስቀለ ሞትየ ባኡ እንተ ጸባብ እንቀጽ እያለ ያስ ተምራቸዋል ወሶበ አውፈሮን ካስተማራቸው በኋ ላም ይስቀልላቸዋል ። ወይተልዉሁ ። እርሱን አብነት አድርገው መከራ ይቀበላሉ በመከራ ይመ ስሉታል ። እስመ የእምራ ትምህርቱን ተቀብለው ታልና። ወለነኪርስ የመምህርነት ሌባ ወንበዴውን ግን አብነት እያደርጉትም እይመስሉትም እላ ይጐይያ ። ይነቅፉታል እንጂ። እስመ ኢየእምራ ። ትምህርቱን አይቀበሉትምና ። የእምራ ቢል ለላይኛው ።

፮ ወዘንተ ምሳሌ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ።
፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ይኽነን ምሳሌ ነገራቸው ።
ወእሙንቱሰ ኢያእመሩ ዘይቤሎሙ ።
እርሳቸው ግን ኖላዊ የተባለ እርሱ ። እባግዕ የተባሉ እርሳቸው እንደሆኑ ዐላወቁም ።

፯ ወካዕበ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አማን አማን እብለክሙ እነ ውእቱ አንቀጸ አባግዕ ።

፯ ዳግመኛ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የበ ጎች ደጅ እኔ ነኝ አላቸው ።

፰ ኵሎሙ እለ መጽኡ እምቅድሜየ ሠረ ቅት ወጦሕልያ እሙንቱ ።

፰ ከኔ አስቀድሞ የመጡ ሁሉ የመምህርነት ሌባ ወንበዴ ናቸው እንደ ይሁዳ ዘገሊላ እንደ ቴዎ

ዳስ ዘግብጽ ።
ወባሕቱ ኢይሰምዕዎሙ አባግዕ ።
ነገር ግን አባግዕ ምእመናን አይቀበሏቸውም ።

፯ እነ ውእቱ አንቀጸ አባግዕ ዘበእማን ።
፯ ዘበእማን ለማለት ደገመው እውነተኛ ደጅ እኔ ነኝ ።
ዘቦአ ብእሲ እንተ ኆቤየ ይድኅን ።
በኔ በኩል የገባ ማለት በኔ ያመነ ሰው ከክህደት ይድናል ።
ወይበውእ ፤
ወደ ሃይማኖት ይገባል ።
ወይወፅእ ፤
ሥራ ለመሥራት ይወጣል ።
ወይረክብ ምርአየ ፤
መሰማርያም ያገኛል ማለት እሳቱን ስለቱን መስቀሉን ያገኛል ፤ እንድም እኔን አብነት ያደረገ ፤ ይድኅን ከፍዳ ፤ ወይበውእ ወደወንጌል ፤ ወይወፅእ ። ለማስተማር ፤ ወይረክብ ምርዓየ ። ጕባኤን ፤ አንድም መራዕየ ምእመናንን አንድም እኔን በዢር ያደረገ ይድኅን ፤ ከፍዳ ፤ ወይወፅእ ከፈቃደ ሥጋ ወይበውእ ፤ ወደፈቃደ ነፍስ ።
ወይረክብ ክብረ ሥጋን ክብረ ነፍስን ያገኛል መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል ።

፲ ወሰራቂሰ ኢይመጽእ ዘእንበለ ከመ ይሰርቅ ወይጥባሕ ወያኅጕል ።

፲ ሌባ ግን ሊጐዳ ነው እንጂ ሊጠቅም ሊያጠፋ ነው እንጂ ሊያለማ አይመጣም ፤ እንድም የመምህርነት ሌባ ወንበዴ ግን ሊጐዳ ነው እንጂ ሊጠቅም ሊያጠፋ ነው እንጂ ሊያለማ አይመጣም ።
ወእንሰኬ መጻእኩ ከመ ይርከቡ ሕይወተ ዘለዓለም ።
እኔ ግን የዘለዓለም ድኅነትን ያገኙ ዘንድ ሰው ሆንኩ በመምህርነት መጣሁ ።
ወፈድፋደ ይርከቡ ።
በነፍስ በሥጋ ለማለት ደገመው ይበዛላቸው ዘንድ ።

፲፩ እነ ውእቱ ኖላዊ ኄር ። ኢሳ፡፵ ፤ ፲፩ ሕዝ፡፴፬ ፣ ፳፫ ።

፲፩ ቸር ጠባቂ እኔ ነኝ ።
ወኖላዊሰ ኄር ይሜጡ ነፍሶ ቤዛ አባግዒሁ ።
ባለቤት ለበጎቹ ቤዛ ሰውነቱን አሳልፎ ይሰጣል ።

፲፪ ወአሳብስ ዘኢኮነ ኖላዌ ወዘኢኮና አባግዕ ዘዚአሁ ሶበ ይሬኢ ተኵላ እንዘ ይመጽእ ይጕይይ ወየኃድጎን ለአባግዒሁ ።

፲፪ ዓባግዕ ገንዘቦቹ ያይደሉ ጠባቂ ያይደለ ምንደኛ ግን ተኵላ ሲመጣ ባየ ጊዜ አባግዕን ጥሏቸው ይሸሻል ።
ወእምዝ ይመጽእ ወይመስጠን ተኵላ ።
ከዚህ በኋላ ተኵላ መጥቶ ይነጥቃቸዋል ።
ወይዘርዎን ለአባግዕ ።
በጎችን ይበትናቸዋል ።

፲፫ ወአሳብስ ይጕይይ ።
፲፫ ምንደኛ ግን ይሸሻል ።
እስመ አሳብ ውእቱ ።
ምንደኛ ነውና ።
ወኢያኃዝኖ በእንተ አባግዕ ።
የበጎቹም ጥፋት አያሳዝነውም ፤ አንድም ወኖላዊሰ ኄር ብለህ መልስ ። እውነተኛ መምህር የምሆን እኔ ለምእመናን ቤዛ ራሴን ለሕማም ለሞት አሳልፌ እሰጣለሁ ፤ ወአሳብስ ምእመናን ወገኖቹ ያይደሉ ሐሰተኛ መምህር ግን መናፍቅ ጳጳስ አላዊ ንጉሥ በተነሣ ጊዜ ይከዳል ። ወየኃድግ ፤ ምእመናንን አሳልፎ ይሰጣቸዋል ። እንደ ፎላቀሲስ ። ወይመሥጠን ይጣላቸዋል ። ወይዘርዎን አገር አስጥሎ ይሰዳቸዋል ፤ ወአሳብስ ፤ ሐሰተኛው መምህር ግን ይከዳል እስመ ሐሳዊ ውእቱ ። ሐሰተኛ ነውና ። ወኢያኀዝኖ ፤ የምእመናን ጥፋት አያሳዝነውምና ።

፲፬ እነ ውእቱ ኖላዊ ኄር ።
፲፬ ቸር ጠባቂ እውነተኛ መምህር እኔ ነኝ ።
ወአአምር ዘዚአየ መርዔትየ ።
በጎቼን አውቃቸዋለሁ ለምእመናን እሞትላቸዋለሁ ።
ወየአምራኒ መራዕይየ ፤
ያውቁኛል ማለት እኔን አብነት አድርገው ምእመናን መከራ ይቀበላሉ ።

፲፭ ወበከመ የአምረኒ አብ ። ማቴ፡ ፲፩ ፣ ፳፯ ሉቃ፡፲ ፣ ፳፪ ።

፲፭ አብ ሙት ተሰቀል እንዳለኝ ።
አነኒ አእምሮ ለአብ ።
እኔም ልሞት ልሰቀል እንደመጣሁ ።
እሜጡ ነፍስየ ቤዛ አባግዕየ ።
ለምእመናን ቤዛ ለሕማም ለሞት አሳልፌ ሰውነቴን እሰጣለሁ ።

፲፮ ወብየ ካልዓትኒ ዓባግዕ እለ ኢኮና እምዝንቱ ዓጸድ ።

፲፮ በዚህ ቦታ የሌሉ ሌሎች በጎች አሉኝ በኢየሩሳሌም የሌሉ ባራቱ ማዕዘን ያሉ ሌሎች አሉኝ ወኪያሆንሂ ህለወኒ እምጽአን ዝየ ።
ወደዚህ አመጣቸው ዘንድ ማለት እርሳቸውንም በሃይማኖት አንድ አደርጋቸው ዘንድ አለኝ ፤ አጽምዖን ይላል አስተምራቸው ዘንድ ፤
ወይሰምዓኒ ቃልየ ።
ትምህርቴን ይቀበሉኛል ።
ወይከውና አሐደ መርዔተ ለአሐዱ ኖላዊ ።
ላንድ ጠባቂ መንጎች ይሆናሉ ላንድ ለክርስቶስ

አካል ብልት ላንድ ኤጲስቆጶስ ማኅበር ቤተ ሰብእ ይሆናሉ ።

፲፯ ወበእንተዝ ያፈቅረኒ አብ እስመ አነ እሜጡ ነፍስየ ቤዛ አባግዕየ ከመ ካዕበ እንሥኣ ። ኢሳ፡፶፫ ፡ ፮ ።

፲፯ ዳግመኛ አሥነሣት ዘንድ ሰውነቴን ለሕማም ለሞት አሳልፌ እሰጣለሁና ስለዚህ አብ ይወደኛል ፤ ያልተካከለ ። ትንሣኤውን ለሞቱ ካዕበ አለ ፤ አንድም የተካከለ ነው ፤ በሕይወት ለመኖሩ ትንሣኤውን ካዕበ አለ ።

፲፰ ወአልቦ ዘየሐይደንያ ፤
፲፰ ያለኔ ፈቃድ ነፍሴን ከሥጋዬ የሚለያት የለም ።

አላ ስልየ እሜጥዋ በፈቃድየ ።
እኔ ወድጄ እለያታለሁ እንጂ ።
እስመ ብውሕ ሊተ እመጥዋ ።
ነፍሴን ከሥጋዬ እለያት ዘንድ ይገባኛልና ።
እንብራሂ ፤
ነፍሴን ከሥጋዬ ለይቼ በገነት ።
ወእሚማ ።
ሥጋዬን ከነፍሴ ለይቼ በመቃብር አኖራት ዘንድ ፤
ወብውሕ ሊተ ካዕበ እንሥኣ ።
ደግሞም አሥነሣት ዘንድ ይቻለኛል ። አንድም አንብራ ሥጋዬን በመስቀል እሚማ በመቃብር አንሥእ በትንሣኤ ። አንድም ሥጋዬን ከነፍሴ ለይቼ ሥጋዬን በመቃብር ነፍሴን በገነት አንሥእ በትንሣኤ ። አንድም እንብራሂ ነፍሴን ከሥጋዬ ለይቼ በገነት ሥጋዬን ከነፍሴ ለይቼ በመቃብር ። ወአንሥእ በትንሣኤ ፣ ወእሚማ ፣ በዕርገት በየማነ አብ በዘባነ ኪሩብ ። ወዘንተ ትእዛዘ ነሣእኩ እምኀበ አቡየ ።
አዋሕዶ ማሥነሣትን ካባቴ ገንዘብ አደረግሁ ።

፲፱ ወተናፈቁ እንከ ካዕበ አይሁድ በበይናቲሆሙ በእንተ ዝንቱ ነገር ።

፲፱ ስለዚህ ነገር አይሁድ ዳግመኛ ተለያዩ ኃጥእ ነው ጻድቅ ነው በማለት ተለያይተው ነበርና ፤

፳ ወይቤሉ ብዙኃን እምኔሆሙ ጋኔን አኃዞ ወየኢብድ ምንትኑ ታጸምዕዎ ።
ሎቱ ስብሐት ከርሳቸው ወገን ብዙዎቹ ጋኔን አድሮበት አእምሮውን ይነሣዋል ለምን ትሰሙታላችሁ አሉ ።

፳፩ ወቦ እለ ይቤሉ ዝንቱ ነገር ኢኮነ ዘጋኔን
፳፩ ይህ ነገር ጋኔን ያደረበትም አይደለ ። ዘጋኔንኑ ይክል አሕይዎ ከሚተ እዕይንቲሆሙ ። ለዕውራን ።

የዕውራንን ዓይን ይከፍት ዘንድ ይችላልን ያሉምአሉ።

ዘከመ ሀሎ ኢየሱስ በበዓለ ሐድሶ ሕንጸት ።

፳፪ ወኮነ በውእቱ መዋዕል ሐድሶ ሕንጸታ ለኢየሩሳሌም ።

፳፪ የኢየሩሳሌም ሕንጻ መታደሻ በዚያ ወራት ነበር ።
ወከረምት ውእቱ ።
ማንሻ ፤ አንድም የኢየሩሳሌም ሕንጻ መታደሻ ወራት ክረምት ነበረ ። አንድም አመ መድቅሕ ይላል ፤ የኢየሩሳሌም ሕንጻ መታደሻ ጊዜ ክረምት ነበር ደቅሖሙ በመድቅሑ እንዲል ፣ ከሀነት ከምስፍና አንድ አድርጎ ይዞ የሚኖር አልዓዛር የሚባል አንድ ሰው ነበር የእኅቶቹ ልጆች ስምዖን አልፍሞስ መባልስ ይባላሉ ሹመት በተራ ሥጋ በገበታ እንዲሉ ፤ ፈንታችንን ሹመን አሉት ። እኔ ከእግዚአብሔር አግኝቼ በእግዚአብሔር ፈቃድ ነው የተሾምኩት ሕዝቡን አስፈቅዳችሁ ተሾሙት አላቸው ሕዝቡን ቢያማክሩዋቸው አባታችን ምንብሎን አኗቸው ጽርእ ወርደው ከአንጥያኮስ ዘንድ ነገሩ የዳዊት የሰሎሞን አገር መንግሥት ጠፍቶባቸዋል መጥተህ አትገዛንም አሉት ። ለጊዜው ፈጣሪያችሁ ኃያል ነው እምባችሁ ጽኑ ነው አይሆንልኝም አላቸው ይህስ አይቸግርህም እንደ አባቴ እንደ እስክንድር በእሪት አምናለሁ መሥዋዕት በግዕ እሠዋለሁ ለሥዕለ ኪሩብ እሰግዳለሁ አነጥፋለሁ እጋርዳለሁ ብለህ ግባ ከዚህ በኋላ የወደድከውን ታደርጋለህ ብለው መከረው መጥተው እናንተ ሹመት ብትነሡን ከፉ አናደርግም ብለን ጽርእ ወርደን አንጥያኮስን ያህል ሰው አሳምነን እንደ እስክንድር በእሪት እንዲያምን መሥዋዕት በግዕ እንዲሠዋ ለሥዕለ ኪሩብ እንዲሰግድ አድርገን መጣን አሉ ።
አመስ አማን ጽድቀ ትነቡ እኳቸው የእስራኤልን በዓል ሁሉ ያውቀዋልና መጥቶ ስፈረአግቡኝ አለ ። ሕጋችን ኢይባእ ሞዓባዊ ወአሞናዊ ትላለች አይሆንም አሉት ። አያችሁ በእግዚአብሔር አማኒ ሲክለከሉበት አንጥያኮስን ያህል ሰው እንዲህ ሲል እያሉ እየዞሩ ይለፉ ፎመሩ ። ይግባ ባዩ በዛ አንተ ብቻህን ግባ አሉት የጾር ነገር ዓይነተኛው ከገባ አይቀርምና ፊታውራሪ ቀኛዝማች ግራዝማች እያለ አጸፋቸው እስራኤል ዐሥራ ሁለት አልፍ ነበሩ ። እኒያ ፳፪ እልፍ ሆኑ አልዓዛርን አንተ በግ ሠውተህ ብላ ለሕዝቡ እሪያ ሠውተህ አብላልኝ ። አንተ ለሥዕለ ኪሩብ ስገድ ሕዝቡን ለሥዕለ ፀሐይ አስግድልኝ አለው ፈጣሪዬ ለጥብዓት አብነት ቢያደርገኝ ለፍርሃት ለሃይማኖት አብነት ቢያደርገኝ ለክህደት አብነት አልሆንም

አለው ። ፺ ለክህነት የበቁ ልጆች ነበሩት ከፊቱ በሰይፍ አስመትቷቸዋል ሚስቱን በጡቶችዋ አሰ ቅሏታል እሱንም ሻሽ በሰም ጠምቶ ከራሱ እስከ እግሩ ሸፍኖ የብረት ምጣድ አግሎ በራሱ ደፋበት ሙቷል በዚህ ጊዜ አራቱ አልፍ ሞቱ አራቱ አልፍ ተማረኩ አራቱን አልፍ ያሁዳ መቃብያዊ ቅጽር አፍርሶ ይዟቸው ወጥቷል ሦስት ዓመት ከመንፈቅ ኑረው ቢመለሱ የምሥራቁ ከምዕራብ የምዕራቡ ከምሥራቅ ዙሮ የቀኙን ወደግራ የግራውን ወደቀኝ አድርጎ በግዕ በሠውበት አሪያሠውቶበት ሥዕለ ኪሩብ ባቆሙበት ሥዕለ ፀሐይ አቁሞበት አገኙት ኀልዳና የምትባል ነቢይት ነበረች ሂደው እንዲህ ሁኖ አገ ኘነው እንደምን እናድርግ አሏት ጠርጋችሁ ጥላችሁ ያን ደልድላችሁ አሪያ በሠውበት በግ ሠውበት ሥዕለ ፀሐይ ባቆሙበት ሥዕለ ኪሩብ አቁ ሙበት ብላቸዋለች ይህ ሲያያዝ ከጌታችን ከኢየሱስ ክርስቶስ ደርሷል ።

፳፫ ወእንሶሰወ እግዚእ ኢየሱስ በቤተ መቅ ደስ በሕዋረ ሰሎሞን ።

፳፫ ሰሎሞን በሠራው በብረት መመደብ በቤተ መቅደሰ ተመላለሰ አንድም ። በእምስቱ በስድስቱ በሰባቱ ቆመ ብእሲ ተመላለሰ ።

፳፬ ወዓገትዎ አይሁድ ወይቤልዎ እስከ ማእዜኑ ታመነድበነ ነፍሰነ ።

፳፬ አይሁድ ከበው ይዘው እስከመቼ ሰው ነታችነን ታስጨንቃለህ ትነሥእነ ይላል እስከ መቼ ድረስ ስታሰቅቀን ትኖራለህ ።
ለእመ አንተሁ ክርስቶስ ንግረነ ገሃደ ።
ክርስቶስ አንተ እንደሆንክ ገልጠህ ንገረን ።

፳፭ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ነገርኩክሙ ።
እኔስ ነገርኳችሁ ።
ወኢተአምኑኒ ወኢትሰምዑኒ አትቀበሉኝም እንጂ ።
ግብር ዘእገብር አነ በሰመ አቡየ ውእቱ ሰማዕትየ ።
ግብር ማንሻ ። አንድም እኔ ብነግራችሁ ባትቀበ ሉኝ ። ባባቴ ስም የምሠራው ሥራ ምስክሬ ነው ።

፳፮ ወአንትሙሰ ኢተአምኑኒ ።
፳፮ እናንተ ግን አትቀበሉኝም ፡
እስመ ኢኮንክሙ እምነ አባግዕየ ።
ከምእመናን ወገን አይደላችሁምና ፤ በከመ እቤለ ክሙ ፥ ክምእመናን ወገን አይደላችሁም ብዬ እንደ ነገርኳችሁ ። አንድም ወአንትሙሰ ፥ ከምእመናን ወገን አይደላችሁምና ትምህርቴን አትቀበሉኝም ።

፳፯ አባግዕየሰ እሊአየ ይሰምዓኒ ቃልየ ።
፳፯ ወገኖቼ ምእመናን ትምህርቴን ይቀበሉ ኛል ብዬ እንደ ነገርኳችሁ ፡ ይሰምዓኒ ብለህ አስር ።
ወአነሂ ። እአምሮን ።
እኔም ዐውቃቸዋለሁ ማለት እሞትላቸዋለሁ ።
ወይተልዉኒ እማንቱ ድኅሬየ ።
እርሳቸውም እኔን አብነት አድርገው መከራ ይቀ በላሉ ።

፳፰ ወአነሂ እሁቦን ሕይወተ ዘለዓለም ።
፳፰ እኔም የዘለዓለም ሕይወትን እሰጣቸዋለሁ የማታልፍ መንግሥተ ሰማያትን አወርሳቸዋለሁ ።
ወኢይትኀጐላ ለዓለም ።
ለዘለዓለም ጉዳት አያገኛቸውም
ወአልቦ ዘየሐይደንዮን እምእዴየ ።
ከኔ አንድነት የሚለያቸው የለም ።

፳፱ እስመ አቡየ ዘወሀበኒዮ ውእቱ የዓቢ እምኵሉ ።

፳፱ እርሳቸውን የሰጠኝ አባቴ ከሁሉ ይበል ጣል ማለት የባሕርይ አምላክ ነው ።
ወአልቦ ዘይክል ሐይደ ወመሢጠ እምእዴሁ ለአቡየ ካባቴ እጅ ይነጥቃቸው ዘንድ ማለት እዱ መዝ ራዕቱ ከተባልሁ ከኔ አንድነት የሚለያቸው የለም ።

፴ አነ ወአብ ፩ዱ ንሕነ ።
፴ እኔና አባቴ ፩ ነን በሥልጣን በብርሃን በቅዳሴ ፥ እስመ ስብሐተ አብ ስብሐተ ወልድ ወስ ብሐተ መንፈስ ቅዱስ እንዲል ።

በእንተ ጽልዕ ዘአይሁድ ላዕለ ኢየሱስ ።

፴፩ ወነሥኡ እብነ ካዕበ አይሁድ ከመ ይወ ግርዎ ።

፴፩ ዳግመኛ ሊጣሉት ደንጊያ አነሡ ። ፈረ ንጅ አነ ወአብ አሐዱ ንሕነ ያለው ኃዳሪ ። አብ የአብየኒ ያለው ማኅደር ነው ይላል ወነሥኡ እብነ ከመ ይወግርዎ ባለው ይረታል ።

፴፪ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፪ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ብዙኃ ግብረ ሠናየ አርአይኩክሙ ዘእምኀበ አቡየ ።
ካባቴ በህልውና ያገኘሁትን ብዙ ትምህርት አስ ተማርኋችሁ ብዙ ትሩፋት ሠራሁላችሁ ብዙ ተአ ምራት አደረግሁላችሁ ።
በአይ ግብር እምኔሆሙ ትዌግሩኒ ።
ከሦስቱ በማናቸው ልትጣሉኝ ትወዳላችሁ አላቸው ።

፴፫ ወአውሥኡ አይሁድ ።
፴፫ አይሁድም መለሱ ።
ወይቤልዎ በእንተ ሠናይስ ግብርከ ኢንዌግረከ ።
በትሩፋትህስ በተአምራትህስ አንጣላህም ።
ወባሕቱ በእንተ ጽርፈትከ ።
በትምህርትህ ነው እንጂ ።
እስመ ሽንዘ ሰብእ አንተ እግዚአብሔርሃ ትሬሲ
ርእሰከ ።
ሰው ስትሆን አምላክ ነኝ ብለህ ታስተምራለህና ።

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰ ።
መዝ ፹፩ ፡ ፮ ።
ወይቤሎሙ አኮኑ ጽሑፍ ውስተ ኦሪትክሙ አንሰ
እቤ አማልክት አንትሙ ።
እኔ አማልክት ናችሁ አልኩ የሚል በኦሪታችሁ
ተጽፎ የለምን አላቸው ፤ ይህንማ ዳዊት አይደለም
የተናገረው ስለምን ኦሪት አለው ቢሉ ፤ መጻሕፍተ
ሐዲሳትን በመከብባቸው ወንጌል እንዲላቸው መጻ
ሕፍተ ብሉያትንም በመከብባቸው ኦሪት ይላቸ
ዋልና ፤ ሰማዕነ በውስተ ኦሪት ከመ ለዓለም ይነብር
ክርስቶስ እንዳለ ዳንኤልን ኦሪት ብሎ ወበውስተ
ኦሪትኒ ይብል በካልዕ ልሳን ወበካልዕ ከናፍር እት
ናገሮሙ ለዝ ሕዝብ እንዳለ ኢሳይያስን ኦሪት ብሎ ፤

፴፭ ወሶበ ለእልክቱ አማልክት ይቤሎሙ እለ
እስተርአየ ወኮነ ቃለ እግዚአብሔር ኀቤሆሙ ።

፴፭ ቃለ እግዚአብሔር ያደረባቸውን ቃለ እግ
ዚአብሔር የተገለጸላቸውን እኒያን አማልክት ናቸው
ካሏቸው አማልክት እንደሆኑ ከተናገሩላቸው ።
ወኢይትከሃል ይትነሠት ወይትሔሰው ቃለ መጻ
ሕፍት ።
መጽሐፍ የተናገረው አይፈርስ አይታበል ።

፴፮ ዘቀደሶ አብ ወፈነዎ ውስተ ዓለም እፎ
እንከ ትብሉኒ ትጸርፍ ለእመ እቤለክሙ ወልደ
እግዚአብሔር አነ ።

፴፮ ልኮ ያዋሐደኝ እኔ አምላክ ነኝ ብላችሁ
ትሳደባለህ ለምን ትሉኛላችሁ ።

፴፯ ወእመሰ ኢይገብር ግብሮ ለአቡየ ኢት
አመኑ ብየ ።

፴፯ ያባቴን ሥራ ካልሠራሁ ልትቀበሉኝ አይ
ገባም ።

፴፰ ወእመሰ እገብር ግብሮ ለእመ ኢያየ ኢአመ
ንክሙ ለግብርየ እመኑ ።
፴፰ ያባቴን ሥራ ግን ከሠራሁ ሰውነቴን አይታ
ችሁ ባታምኑ ሥራዬን አይታችሁ እመኑ ፤ ይህን ሥራ
አምላክ ሰው ሁኖ ቢሠራው ነው እንጂ ዕሩቅ ብእሲ
ይህን አይሠራውም ብላችሁ ።

ከመ ታእምሩ ወትጠይቁ ከመ አነ በአብ ወአብ ብየ
እኔ በአባቴ አባቴ በኔ ህልው እንደሆነ ታውቁ ትረዱ
ዘንድ ።

፴፱ ወፈቀዱ አይሁድ ካዕበ ከመ የአኃዝዎ ።
፴፱ ዳግመኛ አይሁድ ሊይዙት ወደዱ ።
ወአምሠጠ እምእደዊሆሙ ።
አልተያዘም ፤ ወአምሠጠ ዳዊት ውስተ እደ ኢሎ
ፍሊ እንዲል ።

፵ ወሖረ ካዕበ ማዕዶተ ዮርዳኖስ ብሔረ ኀበ
አጥመቀ ዮሐንስ ቀዲሙ ።

፵ ዮሐንስ ቀድሞ ያጠምቅበት ወደነበረ ወደ
ዮርዳኖስ ዳር ዳግመኛ ሄደ ።
ወነበረ ህየ ።
ከዚያም ተቀመጠ ።

፵፩ ወብዙኃን እለ ሖሩ ኀቤሁ ።
፵፩ ብዙ ሰዎችም ወደርሱ ሄዱ ።
ወይቤሉ ዮሐንስ አልቦ ዘገብረ ለነ ተአምር ወኢ
ምንተኒ ።
ዮሐንስ ምንም ምን የሠራልን ተአምራት የለም ።

፵፪ ወባሕቱ ኵሉ ዘይቤ ዮሐንስ በእንተዝ
ብእሲ ኦሙነ ኮነ ።

፵፪ ዮሐንስ ስለዚህ ሰው የተናገረው ነገር
እውነት ሆነ እንጂ ቦታውን ቢያዩ ትዝ ብሏቸው ።
አንድም ከራሳቸው ኦንቅተው ።
ወብዙኃን እለ አምኑ ቦቱ በህየ ።
በዚያም ያመኑበት ብዙ ናቸው ።

ዘከመ አንሥአ ኢየሱስ ለአልዓዛር ።

ምዕራፍ ፲፩ ።

፩ ወሀሎ አሐዱ ብእሲ ዘይደዊ ዘስሙ አልዓ
ዛር በቤታንያ ዘሀገረ ማርያ ወማርታ ።
አነ ወአብ አሐዱ ብሎ ነበርና ነገሩን በሥራው ለማ
ስረዳት ያመጣዋል ። እስመ ሰምዓ ቃላቲሁ ምግ
ባሩ ውእቱ እንዲል ።

፩ የማርያ የማርታ አገር በምትሆን በቤታንያ
የታመመ አልዓዛር የሚባል ሰው ታሞ ነበር ። ከሞተ
ብሎ ለሙት የለው መብት እንዲሉ ። አንድም አባ
ታቸው ለሙቅ ለመቀነት ይሁናችሁ ብሎ ለያቶ
ሰጥቷቸው ነበርና አንድም ባባት አይገናኙምና ዘሀ
ገረ ማርያ ወማርታ አለ ።

፪ ወማርያሰ ይእቲ እንተ ቀብዓቶ ዕፍረተ
ለእግዚእነ ። ማቴ ፳፮ ፯ ሉቃ ፯ ፴፯ ዮሐ ፲፪ ፡ ፫ ፡
፪ ማርያ ግን ጌታን ሽቱ የቀባችው ናት ።
ወመዝመዘት እገሪሁ በሥእርታ ።
እግሩን በጸጉሯ ያበሰችው ናት ።

ወእኁሁ ላቲ አልዓዛር ይደዊ ።
ወንድሟ አልዓዛር ታሞ ነበር ።

፫ ወለእካ አኃቲሁ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ይብላ እግዚኦ ናሁ ዘታፈቅር ይደዊ ።

፫ ጌታ ሆይ ወዳጅህ ታሟል ብለው ወደ ጌታ ላኩ

፬ ወሰሚዖ እግዚእ ኢየሱስ ይቤ ዝንቱ ደዌ ኢኮነ ለሞት ።

፬ ጌታም እንደታመመ ሰምቶ በሰማ ጊዜ ይህ ደዌ ለሞት የሚያበቃ አይደለም ፣ አንድም ሙቶ ሊቀር አይደለም ።

አላ በእንተ ሰብሐተ እግዚአብሔር ።
በልጁ ሀልው ሁኖ እርሱን አሥነሥቶ የእግዚአብሔር አብ ጌትነቱ ይገለጥ ዘንድ ነው እንጂ ።
ወከመ ይሰባሕ ወልደ እግዚአብሔር በእንቲኡሁ ።
የእግዚአብሔር ልጅ እርሱን አሥነሥቶ በጌትነት ይገለጥ ዘንድ ነው እንጂ ።

፭ ወያፈቅሮን እግዚእ ኢየሱስ ለማርያ ወለማርታ እኅታ ወለአልዓዛር ።

፭ ማርያና ማርታን አልዓዛርንም ጌታ የፍጹማን ፍቅር ይወዳቸው ነበር ።

፮ ወሶበ ሰምዓ ከመ ይደዊ ነበረ ህየ ኀበ ሀለወ ብሔረ ሰኑየ መዋዕለ ።

፮ እንደ ታመመ ሰምቶ ካለበት ቦታ ሁለት ቀን ተቀመጠ ።
ሐተታ ረቡዕ ይሞታል ገሥግሠው ገብተው ይነግሩታል ረቡዕ አንድ ሐሙስ ሁለት ዓርብ ቀርቦ አድሮ ቅዳሜ ገብቶ ያሥነሣዋል ። አንድም ረቡዕ ተሸኝተው አድረው ሐሙስ ገቡ ሐሙስ አንድ ዓርብ ሁለት ቅዳሜ ካለበት ገሥግሦ ገብቶ ያሥነሣዋል ።

፯ ወእምዝ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ንሑ ንሑር ብሔረ ይሁዳ ካዕበ ።

፯ ከዚህ በኋላ ደቀ መዛሙርቱን ወደ ይሁዳ እንሂድ አላቸው

፰ ወይቤልዎ አርዳኢሁ ረቢ ይእዜ የኃሥሡ አይሁድ ይውግሩከ ።

፰ ደቀ መዛሙርቱም አሉት አይሁድ ሊወግሩህ ይሹህ ነበሩ ።
ወካዕበ ትፈቅድ ሐዊረ ህየ ።
ዳግመኛ ልትሄድ እንደምን ትወዳለህ እንደምን ልሂድ ትላለህ አሉት አዝነውለት ። አንድም ፅራሳቸው ፈርተው ።

፱ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ እኮኑ ፲ ወ፪ ሰዓቱ ለዕለት ።

፱ ጌታም ሰዓተ መዓልቱ ፲፪ አይደለምን ፲፪ ነውና ።

ብእሲ ዘየሐውር መዓልተ ኢይትዓቀፍ ።
ማንም በቀን የሚሄድ መሰናክል የለበትም ።
እስመ ይሬኢ ብርሃና ለዝንቱ ዓለም ።
የዚህን ዓለም ብርሃን ያያልና ።

፲ ወዘሰ የሐውር ሌሊተ ይትዓቀፍ ።
፲ በሌሊት የሚሄድ ግን መሰናክል አለበት ።
እስመ አልቦ ውስቴቱ ብርሃን ዘይሬኢ ።
የሚያየው ብርሃን የለምና ። ጨረቃ ያለች አይደለምን ቢሉ እንደ ፀሐይ አትሆንምና አንድም የጠፋን መናገር ነው ። አንድም ብእሲ ዘየሐውር መዓልተ አያልክ መልስ ። በኔ ባመነ እኔን አብነት ባደረገ ዕቅፍተ ነፍስ የለበትም ። እስመ ይሬኢ ብርሃና ፣ በኔ አምኑዋል እኔን አብነት አድርጓልና ። ወዘሰ የሐውር ሌሊተ በኔ ባላመነ እኔን አብነት ላደረገ ግን ዕቅፍተ ነፍስ አለበት ። እስመ አልቦ ውስቴቱ ብርሃን ፣ በኔ አላመነም እኔን አብነት አላደረገምና ። አንድም ለእርሱ አዝነውለት ላለው ፲፪ ሰዓተ መዓልት ሳይፈጸም ሰዓተ ሌሊት እንዳይመጣ የምሞትበት ጊዜ ሳይደርስ አይጣሉኝም ። እስመ ይሬኢ ። የምሞትበት ጊዜ ገና ነውና ። ወዘሰ የሐውር ። የምሞትበት ጊዜ የደረሰ እንደሆነ ይጣሉኛል ። እስመ አልቦ ። የምሞትበት ጊዜ ደርሷልና ልጅነት ያገኘንበትን ከፍዳ የነጻንበትን ሞቱን ስለምን በዕቅፍት መሰለውቢሉ ዕንቅፋት የመታው ሰው ለጊዜው ተግ ይላል ኋላ ግን ይሄዳል ። እርሱም ፫ ሌሊት ፫ መዓልት በከርሠ መቃብር ኑሮ ፈጥኖ ተነሥቷልና ። ወአሕጸረ ዕድሜ ለርእሱ እንዲል ። አንድም ለራሳቸው ፈርተው ላለው ፲፪ ሰዓተ መዓልት ሳይፈጸም ሰዓተ ሌሊት እንዳይመጣ እኔ ሳለሁ አይጣሏችሁም ። እስመ ይሬኢ ፤ እኔ አለሁና ፤ ወዘሰ የሐውር ፤ እኔ የሞትኩ እንደ ሆነ ግን ይጣሏችኋል ። እስመ አልቦ ፤ እኔን አያዩምና ፤ አንድም በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን የሚኖር ዕቅፍተ ነፍስ የለበትም በምክረ ካህን ይኖራልና ። ወዘሰ የሐውር ሌሊተ በምክረ ርእሱ በፈቃደ ርእሱ በሚኖር ግን ዕቅፍተ ነፍስ አለበት እስመ አልቦ ። በምክረ ካህን በፈቃደ ካህን አይኖርምና ።
ወዘንተ ነገረ ይቤሎሙ ለአርዳኢሁ ።
ለደቀ መዛሙርቱ ይህን ነገራቸው ።

፲፩ ወእምዝ ይቤሎሙ አልዓዛር ዓርክነ ኖመ ።
፲፩ ወዳጃችን አልዓዛር ተኝቷል ወባሕቱ አሐውር አንቅሖ ።
ነገር ግን ላሥነሣው እሄዳለሁ አላቸው ።

፲፪ ወይቤልዎ አርዳኢሁ እግዚኦ እመሰ ኖመ ይነቅሕ ወይጥዒ ።

፲፪ ደቀ መዛሙርቱም ከተኛስ ዕንቅልፉን ፈጅቶ ጤና ገዝቶ ይነሣል አሉት የታመመ ሰው የተኛ እንደሆነ ጤና ገዝቶ ይነሣል ይባላልና ።

፲፫ ወእግዚእ ኢየሱስ ይቤ በእንተ ንዋመ ሞቱ ።

፲፫ ጌታ ግን ሞት ስለሚባል ዕረፍቱ ነገራቸው ።
ወሎሙሰ መሰሎሙ በእንተ ንዋመ ድቃስ ዘይቤሎሙ ።
ለርሳቸው ግን ዕንቅልፍ ስለሚባል ዕረፍቱ የነገራቸው መስሏቸው ነበር ።

፲፬ ወእምዝ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ገሃደ አልዓዛር ዓርክነ ሞተ ።

፲፬ ከዚህ በኋላ ገልጦ አልዓዛር ወዳጃችን ሞተ አላቸው ።

፲፭ ወእንሰ እትፌሣሕ በእንቲአከሙ ።
፲፭ እኔ ግን ስለእናንተ ደስ ይለኛል ።
እስመ ኢሀሎኩ ህየ ።
እኔ ከዚያ የለሁምና ።
ከመ ትእመኑ አንትሙ ።
እናንተ ታምኑ ዘንድ አስቀድሞ ዐውቆ የነገረን የባሕርይ አምላክ ቢሆን እንጂ ነው ብላችሁ ።
ወባሕቱ ንዑ ንሑር ኀቤሁ ።
ነገር ግን ኑ ወደርሱ እንሂድ ።

፲፮ ወይቤሎሙ ቶማስ ዘይብልዎ ዲዲሞስ ለቢጹ ለአርዳእ ንሑርኬ ንሕነኒ ከመ ንሙት ምስሌሁ ።

፲፮ ንሑር ምስሌሁ ከመ ንሙት ምስሌሁ ።
ዲዲሞስ የተባለ ቶማስ ወንድሞቹን ሐዋርያትን እኛም ከርሱ ጋራ እንደርሱ እንሞት ዘንድ እንሂድ አላቸው ፤ ሹመት ሽልማት እናገኛለን ብለን ተከት ለነው ነበር ሹመቱን ሽልማቱን ሳናገኝ እንሙት ፤ የቆላ በሬ ጤፉን ሳይበሉ ጣፊያውን እንዲሉ ።

፲፯ ወሖረ እግዚእ ኢየሱስ ቢታንያ ።
፲፯ ጌታ ወደ ቢታንያ ሄደ ።
ወበጺሖ ህየ ረከበ በዘወድአ ረቡዓ መዋዕለ እምዘ ተቀብረ ።
ከዚያም በደረሰ ጊዜ ከተቀበረ አራት ቀን ሆኖት አገኘ ።

፲፰ ወቢታንያሰ ቅርብት ይእቲ ለኢየሩሳሌም መጠነ ፲ወ፭ቱ ምዕራፍ ።
፲፰ ቢታንያ ግን ከኢየሩሳሌም ዓሥራ አም ስት ምዕራፍ ትቀርብ ነበረች ።

፲፱ ወብዙኃን እምነ አይሁድ አለ ሖሩ ኀበ ማርያ ወማርታ ከመ ያላቅስዎን በእንተ እኁኆን ።

፲፱ ወንድማቸው አልዓዛር ስለሞተ ሲያለቅ ሱለት ወደማርያና ወደማርታ የመጡ አይሁድ ብዙ ናቸው ።

፳ ወሰበ ሰምዓት ማርታ ከመ መጽአ እግ ዚእ ኢየሱስ ወፅአት ወተቀበለቶ ።

፳ ማርታም ጌታ እንደመጣ በሰማች ጊዜ ወጥታ ተቀበለችው ።
ወማርያሰ ነበረት ቤተ ።
ተርፈት ሲል ነው ወነበረት ውስተ ኢየሩሳሌም እንዲል ማርያ ግን ከቤት ቀረች ፤ ሰው ከቤት አስ ቀምጦ መውጣት አይገባምና ።

፳፩ ወትቤሎ ማርታ ለእግዚእ ኢየሱስ ሶበሰ ሀሎከ ዝየ እምኢሞተ እኁየ ።

፳፩ ማርታም ጌታዬ ከዚህ ኑረህ ቢሆን ወን ድሜ ባልሞተም ነበር ።

፳፪ ወይእዜኒ አአምር ከመ ዘሰአልኮ ለእግ ዚአብሔር ይሁበከ እግዚአብሔር ።

፳፪ እግዚአብሔር የለመንከውን እንዲያደርግ ልህ አውቃለሁና ። ድውይ መፈወስ እንጂ ሙት ማንሣት የማይቻለው መስሏት ።

፳፫ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ እኁኪሰ ይት ነሣእ ።

፳፫ አንች አላመንሽም እንጂ ወንድምሽስ ይነ ሣል አላት ።

፳፬ ወትቤሎ ማርታ አአምር ከመ ይትነሣእ አመ ትንሣኤ ሙታን በደኃሪት ዕለት ። ሉቃ፣፲፬ ፤ ፲፭ ዮሐ፣ ፭ ፤ ፳፱ ።

፳፬ የኋላውን የነገራት መስሏት በዕለተ ምጽ አት ሙታን በሚነሡበት ጊዜ እንዲነሣ ዐውቃለሁ ። ትውልዷ ከፈሪሳዊ ነው ቢሉ የተመቸ ፤ ከሰዱቃ ውያን ነው ቢሉ ሲሉ ሰምታ ።

፳፭ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ትን ሣኤ ወሕይወት ዘየአምን ብየ እመኒ ሞተ የሐዩ ። ዮሐ፣፯ ፤ ፯ ።

፳፭ ትንሣኤ ሕይወት እኔ ነኝ ያመነብኝ ቢሞ ትም ይድናል ማለት ትንሣኤ ዘጉባኤን የማልጠብቅ ባልኩ ጊዜ የማሥነሣ እንድም ሶበሰ ሀሎከ ዝየ ብለህ መልስ ፤ አምናለችና ብሎ አንተ ከዚህስ ኑረህ ቢሆን ወንድሜ ባልሞተም ነበር ። ወይእዜኒ አአምር ። አሁንም የለመንከውን እንዲያደርግልህ ዐውቃለሁ ፤ ወይቤላ እኁኪሰ ፤ አንችም አምነሻል ወንድምሽም

ይነሣል አላት ። ወትቤሎ አአምር ፤ ሙታን እንደ ሚነሡት ያለ ትንሣኤ እንዲነሣ ዓውቃለሁ ፤ ወይቤላ አነ ውእቱ አይለውጥም ፤ ዘየእምን ብየ እመኒ ሞተ የሐዩ ፤ በኔ ያመነ አይሞትም በሥጋ ቢሞት በነፍስ ይድናል ፈርሶ በስብሶ እይቀርም ትንሣኤ ዘለክብር ይነሣል ።

፳፮ ወኵሉ ዘሕያው ወየአምን ብየ ኢይመውት ለዓለም ።

፳፮ በሕይወተ ሥጋ ሳለ በኔ ባመነ ሞተ ነፍስ ሙቶ መቅረት የለበትም ።
ተአምኒኑ ዘንተ ።
ሙት ማሥነሣት እንዲቻለኝ ታምኛለሽን አላት ።

፳፯ ወትቤሎ እወ እግዚእ አንሰ እአምን ከመ አንተ ውእቱ ክርስቶስ ወልደ እግዚአብሔር ዘመጽአ ውስተ ዓለም ።

፳፯ አወን አቤቱ እኔስ እስከ ክርስቶስ ተብሎ የተነገረልህ የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ አንተ እንደሆንክ አምናለሁ አለችው ።

፳፰ ወዘንተ ብሂላ ጸውዓታ ለማርያ እኅታ ጽሚተ ።

፳፰ ይህን ተናግራ ማርያን እኅቷን ሰውራ ጠራቻት በደግ ሰው ልማድ ።
ወትቤላ ናሁ መጽአ ሊቅነ ወይጼውዓኪ ።
እነሆ መምህራችን መጥቶ ይጠራሻል አለቻት ።

፳፱ ወሶበ ሰምዓት ማርያ ተንሥአት ፍጡነ ወሖረት ኀቤሁ ።

፳፱ እርሷም ማርያ ይህነን በሰማች ጊዜ ፈጥና ተነሣች ወደርሱም ሄደች እኅቷን ተከታ ።

፴ ወዓዲሁ ኢቦአ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ሀገር ።

፴ ጌታም ገና ከከተማው አልገባም ነበር ።
እላ ህሎ ውስተ መካን ኀበ ተቀበለቶ ማርታ ።
ማርታ ካገኘችው ቦታ ነበር እንጂ ፤ በብዙ ጻዕር እንጂ አሥነሣው እንዳይሉት ።

፴፩ ወሶበ ርእይዎ ለማርያ አይሁድ እለ ሀለዉ ምስሌሃ ውስተ ቤት እለ ያላቅስዋ ከመ ተንሥእት ፍጡነ ወወፅአት ተለወዋ ።

፴፩ ሊያለቅሱለት የመጡ ከርሷ ጋራ ያሉ አያሁድ ፈጥና ተነሥታ እንደሄደች ባዩ ጊዜ ተከተሏት ።
ወመሰሎሙ ዘተሐውር ኀበ መቃብሩ ትብክዮ በህየ ።
ልታለቅስለት ወደ መቃብር የምትሄድ መስሏቸው ነበር በሦስተኛው ቀን መቃብር ከፍተው መግነዝ ፈትተው ሽቱ እየቀቡ ያለቅሳሉና ።

፴፪ ወሶበ በጽሐት ማርያ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወርእየቶ ወሰገደት ሎቱ ታሕተ እገሪሁ ።

፴፪ ማርያም ጌታም ካለበት ደርሳ ባየችው ጊዜ ከእግሩ በታች ሰገደች ።
ወትቤሎ እግዚእየ ሶበሰ ህሎከ ዝየ እምኢሞተ እኁየ ።
ጌታዬ ከዚህስ ኑረህ ቢሆን ወንድሜ ባልሞተም ነበር አለችው እሷም እንደ እኅቷ ።

፴፫ ወሶበ ርእያ እግዚእ ኢየሱስ እንዘ ትበኪ ።
፴፫ ጌታም ስታለቅስ ባያት ጊዜ ።
ወአይሁድኒ እለ መጽኡ ምስሌሃ ከመ ይበክዩ ።
ከርሷም ጋራ ያሉ ሲያለቅሱ ባየ ጊዜ ገዓረ በመንፈሱ ።
በልቡናው አዘነ ።
ወሆሰ ርእሶ ።
ራሱንም ነቀነቀ ፤ መፍቀሬ ሰብእ ነውና ፤ አንድም ሕጸጻቸውን ዓውቆ ፤

፴፬ ወይቤ አይቴ ቀበርክምዎ ።
፴፬ የት ቀበራችሁት አላቸው ፤ ሐዲስ መቃብር አይደለምን ይታወቅ የለም ቢሉ የሀገራቸው መቃብር ሕንጻ ነው ዕለት እይቆፈርም አይታወቅምና ፤ ያስ ቢሆን ያታወቅ የለም ቢሉ ዐላዋቂ ሥጋን እንደተዋሐደ ለማጠየቅ ።
አኮ ኢያእሚሮ ኅቡአተ እላ ከመ የሀብ መካነ ለጥንተ ትስብእቱ ዘኢየእምር ኅቡአተ እንዲል ። እንድም ሳይጠይቅ አሥነሥቶት ቢሆን ምትሐት ነው ባሉት ነበርና ፤ አንድም አይቴ ቀበርክምዎ ለአልዓዛር የሚል ሥጋን ተዋሕጄ አድንጋለሁ ሲል አይቴ ሀሎከ እዳም ብሎት ነበርና ያ እንደ ተፈጸመለት ለማጠየቅ ፤ አንድም ለምንት ሲል ነው ።
ከሱማናይት ትብሱ ይች ስንኳ ልጅዋ ቢሞትባት ዐፅባ አጐናጽፋ አልጋ አስተኝታ ኤልሣዕን ልትጠራ ሄደች ።
ወይቤልዎ እግዚኦ ነዓ ትርአይ ።
አቤቱ መጥተህ እይ አሉት ።

፴፭ ወአንብአ ካዕበ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፭ ጌታም ዕንባውን አፈሰሰ ።

፴፮ ወይቤሉ አይሁድ ርእዩ መጠነ ያፈቅሮ ።
፴፮ አይሁድም እንዲወደው መጠን ታያላችሁን አሉ ።

፴፯ ወቦ እምውስቴቶሙ እለ ይቤሉ እምኢክህሎኑ ዝንቱ ዘከሠተ አዕይንቲሁ ለዘዕውሩ ተወልደ ከመ ይግበር በዘኢይመውት ዝንቱኒ ። ዮሐ፡ ፱ ፡ ፮ ።
፴፯ ዕውር ሆኖ የተወለደውን የዚያን ዓይን ያበራ ይህ ከዚህ ኖሮ ቢሆን ይህንስ እንዳይሞት ማድረግ ባልተቻለውም ነበር ዳሩ ምን ይሆናል

ሞተና አሉ ድውይ መፈወስ እንጂ ሙት ማንሣት
የማይቻለው መስሏቸው ።

፴፰ ወካዕበ ተከዘ በመንፈሱ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፰ ጌታም ሁለተኛ በልቡ አዘነ ።
ወሖረ ኀበ መቃብሩ እንዘ ያንብዕ ፤
ወደ መቃብሩም እያለቀሰ ሄደ ።
ወበዓት ውእቱ ።
መቃብሩ ሕንጻ ነበር ፤
ወከዱን በእብን ዓቢይ ።
ታላቅ ደንጊያም ተገጥሞ ነበር ።

፴፱ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አዕትትዋ
ለእብን እምአፈ መቃብር ።

፴፱ ደንጊያውን አንሡት አላቸው ።
ወትቤሎ ማርታ እኅቱ ለዘሞተ እግዚእየ ናሁ ወዕአ
ጼዓ ።
የሞተው እኅት ማርታ ጌታዬ እነሆ ፈጽሞ ተለቷል
አለችው ።
እስመ ረቡዓ ኮነ ዮም ።
ዛሬ አራት ቀን ሆኖታልና ።

፵ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ኢይቤለኪኑ
ከመ እመ ተአመንኪ ትሬእዪ ስብሐተ እግዚእ
ብሔር ።

፵ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ብታምኚ
ወንድምሽ እንዲነሣ ነግሬሽ አልነበረምን አላት ።
ወአዕተትዋ ለይእቲ እብን እምአፈ መቃብር ።
ደንጊያይቱን አነሡ ።

፵፩ ወአንሥአ እግዚእ ኢየሱስ አዕይንቲሁ
ላዕለ ።

፵፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዓይኑን ወደ
ሰማይ አቀና ፤ ይህን የማሥነሣበት ሥልጣን ካንተ
ጋር አንድ ነው ሲል ፤ አንድም ተአምራት ይደረ
ግልን ባላችሁ ጊዜ ወደ እግዚአብሔር አመልከቱ
ለማለት እብነት ለመሆን ።
ወይቤ አአኰተከ አባ ።
አባቴ አለምንሃለሁ ።
እስመ ሰማዕከኒ ።
ከዚህ አስቀድሞ ልመናዬን ሰምተኸኛልና ።

፵፪ ወአእምር ከመ ዘልፈ ትሰምዓኒ ።
፵፪ አሁንም እንድትሰማኝ ዐውቃለሁና ።
ወባሕቱ በእንተ እለ ይቀውሙ ሰብእ እብል ዘንተ
ከመ ይእመኑ ከመ አንተ ፈነውከኒ ።
ነገር ግን ከዚህ ቆመው ስላሉ ሰዎች ይህን እናገራ
ለሁ ፤ ባንተ ፈቃድ ሰው እንደሆንኩ ያውቁ ዘንድ ።

፵፫ ወዘንተ ብሂል ከልሐ በዓቢይ ቃል ።
፵፫ ይህን ተናግሮ አሰምቶ ተናገረ ።
ወይቤ አልዓዛር አልዓዛር ንዓ ፃእ አፍአ ።
አልዓዛር አልዓዛር ና ውጣ አለው ፡ ለዕብራው
ያን ደጊመ ቃል ልማድ ነውና ። አብርሃም አብ
ርሃም ፡ ስምዖን ፡ ስምዖን ፡ ማርታ ማርታ እንዲል ።
አንድም የሥጋ የነፍስ ፈጣሪ ነኝ ሲል ። አንድም
ሥጋን ከመቃብር ነፍስን ከገሃነም ሲጠራ ።

፵፬ ወወፅአ ውእቱ ምውት እንዘ ግኑዝ ወእ
ሱር እደዊሁ ወእገሪሁ ።

፵፬ እጁን እግሩን እንደታሰረ ።
ወገጹኒ ጥብሉል በሰበን ።
ሻሹን እንደጠመጠመ ወጣ ።
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ፍትሕዎኬ እንከሰ
ወኅድግዎ ይሑር ።
ምትሐት መስሏቸው ነበርና ምትሐት አለመሆ
ኑን ካወቃችሁስ ፈትታችሁ ተውት ይሂድ አን
ድም እልጸናም መስሏቸው ደግፈውት ነበርና መጽ
ናቱን ካወቃችሁ ፈትታችሁ ተውት ይሂድ አላ
ቸው ።

፵፭ ወብዙኃን እምአይሁድ እለ መጽኡ ኀበ
ማርያ ወማርታ ርእዮሙ ዘንተ ተአምረ ዘገብረ
እግዚእ ኢየሱስ አምኑ ቦቱ ።
፵፭ ወደማርያና ወደማርታ የመጡ አይሁ
ሁድ ወገን የሚሆኑ ብዙ ሰዎች ጌታችን ኢየሱስ
ክርስቶስ ያደረገውን ይኸን ተአምራት አይተው
አመኑበት ። ።

፵፮ ወቦ እምውስቴቶሙ እለ ሖሩ ኀበ ፈሪ
ሳውያን ወአስተዋደይዎ ።

፵፮ ከርሳቸው ወገን ወደፈሪሳውያን ሂደው
ያሳጡትም አሉ ።
ወነገርዎሙ ኵሎ ተአምረ ዘገብረ እግዚእ
ኢየሱስ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ያደረገውንም ተአም
ራት ሁሉ ነገሯቸው ። ሙት አሥነሣ ብለው ።

ዘከመ ተማከሩ አይሁድ ይቅትልዎ ለኢየሱስ ።

፵፯ ወአስተጋብእዎሙ ሊቃነ ካህናት ወፈ
ሪሳውያን ለሕዝብ ።
፵፯ ሊቃነ ካህናት ፈሪሳውያን ሕዝቡን ሰበ
ሰቧቸው ፤
ወይቤልዎሙ ምንተ ንሬሲ ።
ምን እናያደርጋለን ምን እናድርግ ።
ናሁ ዝንቱ ብእሲ ብዙኃ ተአምረ ይገብር ።
እነሆ ይህ ሰው ብዙ ተአምራት ያደርግ ጀመር።
፵፰ ወእመኒ ኀድግናሁ ከመዝ ኵሉ የአምን
ቦቱ ።
፵፰ እንዲያውም ዝም ብለን ብንተወው ሁሉ
ያምንበታል ።

ወይመጽኡ ሰብአ ሮሜ ወይነሥኡ ብሔረነ ወኪ
ያነኒ ወሕዝበነኒ ፡
የሮም ሰዎች ተአምራቱን ሲሹ መጥተው ። አን
ድም ወሬኛ ንጉሥ አነገሣችሁ ብለው ወገናችንን
ወገን አገራችንን አገር ያደርጉብናል ።

፵፱ ወይቤሎሙ ፩ዱ እምኔሆሙ ዘስሙ ቀያፋ
ሊቀ ካህናት ዘዕብሬቱ ይእቲ ዓመት አንትሙሰ
ኢተአምሩ ወኢምንተኒ ። ዮሐ፡ ፲፰፥፲፬ ።

፵፱ ሹመቱ በዚያ ወራት የሚሆን የካህናቱ
አለቃ ከነሱ አንዱ ስሙን ቀያፋ የሚሉት እናንተ
ምንም ምክር አታውቁም ።

፶ ወኢኂ ትመክሩ ።
፶ አታስቡም ።
ይኄይሰነ ፩ደ ብእሲ ንቅትል ።
አንድ ሰው ብንገድል ይሻለናል ።
ወይሙት ህየንተ ኵሉ እምይትኃጐል ኵሉ ሕዝብ።
ስለ ሕዝቡ ቤዛ ። ሕዝብም ሁሉ በርሱ ምክ
ንያት ከሚጠፋ ።

፶፩ ወዘንተሰ አኮ እምልቡ ዘይቤ ።
፶፩ ይህን የተናገረ ከልቡ አይደለም ማለት
በመንፈስ ቅዱስ በታደሰ አእምሮው አይደለም ።
አላ እስመ ሊቀ ካህናት ውእቱ ።
ሊቀ ካህናት ነውና ።
ወዕብሬቱ ይእቲ ዓመት ተነበየ ዘንተ ።
ሹመቱም በዚያ ዓመት ነውና በተአምራት እና
ገረው እንጂ ዕድሜተ በለዓምን እብነ ሆሣዕናን
እንዳናገረ ። አንድም አኮ እምልቡ ። በአእምሮ
ጠባይዕ ዐውቆ አይደለም በሹመቱ አድሮ ያለ
ሀብት አናገረው እንጂ በሳኦል አድሮ ሠላሳ ስም
ንት ዘመን የመንግሥት ሥራ እንደ ሠራ በኃ
ጥእ ቄስ አድሮ ሥጋውን ደሙን እንዲለውጥ።
እስመ ሀለዎ ለእግዚእ እየሱስ ይሙት በእንተ
ኵሉ ሕዝብ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስሕዝቡ
ሁሉ ቤዛ ሁኖ ይሞት ዘንድ አለውና ።

፶፪ ወአኮ በእንተ ሕዝብ ባሕቲቶሙ ።
፶፪ ቤዛነቱ ለሕዝብ ብቻ አይደለም ።
አላ ከመ ያስተጋብኦሙ ለውሉደ እግዚአብሔር እለ
ተዘርዉ አሕተኔ ።
በኃጢአት በጣዖት የተበተኑ አሕዛብንም አንድ
ያደርጋቸው ዘንድ ነው እንጂ ። ምነው
አንድ የሆኑማ በሃይማኖት አይደለምን ቢሉ ሞቱ
ያለ ሃይማኖቱ ሃይማኖቱ ያለ ሞቱ አይሆ
ንምና እንዲህ አለ እንጂ አንድ የሆኑስ በሃይማ
ኖት ነው ።

፶፫ ወእምይእቲ ዕለት ተማከሩ ሊቃነ ካህ
ናት ከመ ይቅትልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፶፫ ከዚያ ቀን ጀምሮ ከዚያ ቀን ወዲህ ሊቃነ
ካህናት ጌታችንን ሊገሉት መከሩ ።

ዘከመ ተግኅሠ ኢየሱስ እም ኢየሩሳሌም ።

፶፬ ወኢያንሶሰወ እንከ እግዚእ ኢየሱስ ገሃደ
ማእከለ አይሁድ

፶፬ ከዚያ ወዲያ ጌታችን ኢየሱስ በአይሁድ
ዘንድ ታይቶ አልኖረም ፡
አላ ሖረ ኀበ ሀገር እንተ ትሰመይ ሀገረ ኤፍሬም
ቅርብት ለበድው ።
ለምድረ በዳ አቅራቢያ ወደምትሆን የኤፍሬም
አገር ወደምትባል ሄደ እንጂ ።
ወነበረ ህየ ምስለ አርዳኢሁ ።
ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ እዚያ ኖረ ፡ ለስቅለት እስ
ኪወጣ ድረስ ከዚያ ይኖራል ።

፶፭ ወቀርበ በዓለ ፋሲካሆሙ ለአይሁድ።

፶፭ አራተኛ ፋሲካ ነው ፡ አይሁድ ፋሲ
ካን የሚያከብሩበት ቀን ደረሰ ።

ወዓርጉ ብዙኃን ሕዝብ ለኢየሩሳሌም እምበሐው
ርት እምቅድመ በዓለ ፋሲካ ያንጽሑ ርእሶሙ።
ከበዓለ ፋሲካ አስቀድሞ በዓለ አንጽሖን ያደርጉ
ዘንድ ብዙ ሰዎች ከየሀገሩ ወደ ኢየሩሳሌም
ወጡ ብፅዓት ያለበት ሰው ሰባት ቀን ከሰው ተለ
ይቶ መሥዋዕት ሠውቶ ማየ ምንዛሕ ተረጭቶ
ነውና በዓለ ፋሲካውን የሚያከብር ።

፶፮ ወአኃዙ አይሁድ ይኅሥሥዎ ለእግዚእ
ኢየሱስ ።

፶፮ አይሁድ ጌታን ይሹት ጀመር ።
ወይቤሉ በበይናቲሆሙ እንዘ ይቀውሙ ውስተ
ቤተ መቅደስ ምንተ ትብሉ ።
በቤተ መቅደስ ሁነው እርስ በርሳቸው እንዲህ
አሉ ።
ናሁ ኢመጽአ ለበዓል ።
ለበዓል ሲመጣ እንይዘዋለን ብለው ነበር ፡
እነሆ ለበዓል አልመጣምሳ ። አንድም በምን ዕዳ
በምን ነውር እንይዘዋለን ብለን ነበር ከዚህ
የበለጠ ነውር አለ እነሆ ለበዓል አልመጣምሳ
አንድም ደግ ነው ትሉት ነበር ደግማ ከሆን
ለበዓል ይመጣ አልነበረምን ለበዓል አልመጣምሳ።
ወአዘዙ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን እምከመቦ
ዘአእመረ ብእሲ ኀበ ሀሎ ይቅጽብዎሙ ከመ የአ
ኃዝዎ ።

ያለበትን ያወቀ ሰው ቢኖር ጠቅሶ ያሲ
ይዛቸው ዘንድ ፈሪሳውያንና ሊቃነ ካህናት
ውስጥ ለውስጥ ዐዋጅ ነገሩ ።

በእንተ ድራር ዘቢታንያ ።

ምዕራፍ ፲፪ ።

፩ ወእምዝ ሖረ እግዚእ ኢየሱስ እምቅድመ ሰዱስ መዋዕል ዘፋሲካ ። ማቴ ፳፮ ፮ ማር፡ ፲፬ ፡ ፫ ።

፩ ከዚህ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከበዓለ ፋሲካ ስድስት ቀን አስቀድሞ ሄደ ቅዳሜ አንድም ፋሲካው ከሚውልበት ከስድስተኛው ቀን አስቀድሞ ሄደ ሐሙስ ፡ ሰዱስ ለፍጥረት ወበጽሐ ቢታንያ ኀበ ሀሎ አልዓዛር ዘአንሥአ እምነ ምውታን ።
ከሙታን ለይቶ ያሥነሣው አልዓዛር ካለበት ቢታንያ ደረሰ ።

፪ ወገብሩ ሎቱ ምሳሐ በሀየ ።
፪ ከዚያም ግብር አገቡለት ።
ወማርታ ትሜጥዎሙ ።
መፈትፈት ማሳለፍ አይደለም ማርታ እያዘጋጀች አቀረበችላቸው ።
ወአልዓዛር አሐዱ እምእለ ይረፍቁ ምስሌሁ ።
ከጌታ ጋር ተቀምጠው ከሚበሉት አንዱ አልዓዛር ነበር ምትሐት እንዳይደለ ለማጠየቅ ።

፫ ወማርያስ ነሥአት ዕፍረተ ልጥረ ዘናርዱ ጵስጥቂስ ዘዕጹብ ሤጡ ወቀብዓቶ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
፫ ማርያ ግን የደቀቀ የጣፈጠ ሽቱ አምጥታ የጌታን እግሩን ቀባችው ።
ወመዝመዞቶ በሥእርታ ።
በጠጕሯም አደፈችው ።
ወመልአ ቤተ መዓዛሁ ለውእቱ ዕፍረት ።
የሽቱው መዓዛ ቤቱን መላው ሽቱ ሲነካኩት እየተገለጠ ነውና የሚሄድ ፡ አንድም ከመዓዛ መለኮት ጋራ ቢዋሐድ ።
፬ ወያቤ ይሁዳ ስምዖን አስቆሮታዊ ፩ዱ እም ፲ቱ ወ፪ቱ አርዳኢሁ ዘሀለዎ ያግብእ ።
፬ ያሲዘው ዘንድ ያለው ከደቀ መዛሙርቱ አንዱ የአስቆሮት ሰው የሚሆን ይሁዳ እንዲህ አለ ።

፭ ለምንት ኢሤጥዎ ለዝንቱ ዕፍረት ለ፫፻ ዲናር የሀብዎ ለነዳያን ።
፭ ይህን ሽቱ ሰድኖች ይመጸውቱት ዘንድ ይትወሀብ ይላል ለነዳያን ይመጸወት ዘንድ ለሦስት መቶ ወቄት ወርቅ ምነው አልሸጡት አለ ።

፮ ወዘንተ ዘይቤ አኮ ዘያጽሕቅዎ ነዳያን ።
፮ ይህን የተናገረ ነዳያን አሳዝነውት አይደለም ምሒረ ነዳያን ይላል የነዳያን ምጽዋት አሳዝኖት አይደለም ።

አላ እስመ ሠራቂ ውእቱ ።
የሰውን ገንዘብ ያነሣሣ ነበርና ወየዓቅብ አስከሬን ጥራን ጠባቂ ነበርና ።
ወቀምጠራ ዘሙዳየ ምጽዋት ሀሎ ውስተ እዴሁ ።
የሣጥኑ መክፈቻ በእጁ ነበር ።
ወይነሥእ እምዘይትወደይ ውስቴቱ ።
ከገባውም ሁሉ ካሥር አንድ ይወስድ ነበርና ስለ ዚህ ነው እንጂ ።

፯ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ኅድጋ እስመ ፡ ተዓቅቦ ለዕለተ ቀበርየ ።

፯ ጌታም ለምቀበርበት ቀን አስጠብቃዋለችና ተዋት አለው ። ዕለቱን እንዳትቀባው አይሁድ አያስደርሷትም ። በልማዳቸው በሦስተኛው ቀን እንዳትቀባው ፈጥኖ ይነሣባታልና ።

፰ ወነዳያንሰ በኵሉ ጊዜ ሀለዉ ምስሌክሙ ወዘልፈ ትረከብዎሙ ።

፰ ድኖችስ ዘወትር ከናንተ ጋራ ይኖራሉ ፡ ዘወትር ታገኙዋቸዋላችሁ
ወጊዜ ፈቀድክሙ ታሤንዩ ሎሙ ።
በወደዳችሁ ጊዜ ትሰጧቸዋላችሁ ።
ወኪያየሰ አኮ በኵሉ ጊዜ ዘትረክቡኒ ።
እኔን ግን ዘወትር አታገኙኝም ።

፱ ወብዙኃን እምነ አይሁድ እለ አእመሩ ከመ ሀሎ እግዚእ ኢየሱስ ሀየ ወሖሩ ኀቤሁ ።

፱ ከአይሁድም ወገን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚያ እንዳለ ዐውቀው ወደዚያ የሄዱ ብዙ ናቸው ።
ወአኮ በእንተ ኢየሱስ ባሕቲቱ ዘሖረ ።
የሄዱ ጌታችን ኢየሱስን እናያለን ብለው ብቻ አይደለም ።
ዳዕሙ ከመ ይርአይዎ ለአልዓዛርሂ ዘአንሥአ እምውታን ።
ከሙታን ለይቶ ያሥነሣውን አልዓዛርንም ያዩት ዘንድ ነው እንጂ ።

፲ ወተማከሩ ሊቃነ ካህናት ከመ ይቅትልዎ ለአልዓዛር ።
፲ የካህናት አለቆች አልዓዛርን እንግደለው ብለው መከሩ ።
፲፩ እስመ ብዙኃን እምውስተ አይሁድ የሐውሩ በእንቲአሁ ወየአምኑ በእግዚእ ኢየሱስ ።
፲፩ ከአይሁድ ወገኖች አልዓዛርን እናያለን ብለው ሄደው በጌታ የሚያምኑ ብዙ ናቸውና ቢገድሉት ያስነሣባቸው እንጂ የለምን ። ሐተታ ማቴዎስ ረቡዕ ቀባችው ይላል ። ዮሐንስ ቅዳሜ ቀባችው አለ አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። ነገር እንደ ዮሐንስ ነው ። ቅዳሚት ቀብታዋለች ማቴዎስ የአይሁዳን ሲጽፍ አልፎት ነበርና ከረቡዕ አደረገው

እንጂ ቀቢዪቱም አንዲት ናት ኃጥእት ይላታልሳ ቢሉ ኋላ ተመልሳለች ። ማቴዎስ ራሱን ይላል ዮሐንስ እግሩን አለሳ ቢሉ ከራስ የፈሰሰ እስከ እግር ደረሰ እንዲሉ ። ይህ ፀምን ይታወቃል ቢሉ ተግሣጹን ባለመግደፋቸው ። አንድም እንደ ማቴዎስ በጥንተ ስብከት የፈያታይ ዘየማን እኅት የበላዔ ሰብእ ወገን የምትሆን ማርያም ኃጥእት ይላታል ረቡዕ ራሱን ቀብታዋለች። እንደ ዮሐንስ እኅተ አልዓዛር ቀዳሚት እግሩን ቀብታዋለች ። ተግሣጹንም እንደገደፋት በበረከተ ኅብስት ይታወቃል ።

ዘከመ ገብአ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ።

፲፪ ወበሳኒታ ሰብእ ብዙኃን እለ መጽኡ ለበዓል ሶበ ሰምዑ ከመ ይመጽእ እግዚእ ኢየሱስ ኢየሩሳሌም ።

፲፪ በነጋው ምእሑድ ለበዓል የመጡ ሰዎች ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመጣ በሰሙ ጊዜ ።

፲፫ ነሥኡ ፀበርተ ተመርት ዘበቀልት አም ኢየሩሳሌም ወወፅኡ ፍጡነ ሶበ ሃ ።

፲፫ የሰሌን ዛፍ ዝንጣፊ ይዘው ከኢየሩሳሌም ፈጥነው መጡ ።
ወተቀበልዎ እንዘ ይጸርሑ ወይብሉ ሆሣዕና በአርያም ቡሩክ ዘይመጽእ በስመ እግዚአብሔር ወንጉሦሙ ለእስራኤል ።
በእግዚአብሔር ስም የሚመጣ ሆሣዕና የእስራኤል ንጉሥ የተባረከ ነው እያሉ እየጮሁ ተቀበሉት ። በኢየሩሳሌም ሰሌን የለም ወደግብጽ ሲወርድ ከመ ንገድ አግኝቷት ሂደሽ ደብረ ዘይት ተተከዪ ብሎ አዟት ተነቅላ ሂዳ ተተከላለች ከዚያ ይዘው መጥተዋል ።

፲፬ ወረከበ እግዚእ ኢየሱስ ዕዋለ አድግ ። ዘካ. ፱፥፱ ማቴ፥፳፩ ፲፥፴፭ ።

፲፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም አህያ አገኘ። ወተጽእነ ዲቤሃ በከመ ጽሑፍ ተቀመጠባት እንደ ተጻፈ እንዲህ ሲል ።

፲፭ ኢትፍርሂ ወለተ ጽዮን ነዋ ንጉሥኪ ይመጽእ እንዘ ይጼዓን ዲበ ዕዋለ አድግ ።

፲፭ አትፍሪ የጽዮን ልጅ እነሆ ንጉሥሽ ይመጣል ባህያ ግልገል ተቀምጦ ።

፲፮ ወቀዲሙስ ኢያእመሩ አርዳኢሁ ዘንተ ነገረ።
፲፮ አስቀድሞ ግን ደቀ መዛሙርቱ ይህን ነገር አላወቁትም ነበር ።

ዘእንበለ አመ ተሰብሐ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታ ሳይሰቀል ።
አሜሃ ተዘከሩ ከመ ጽሑፍ ዝንቱ በእንቲአሁ፣
ጌታ በተሰቀለ ጊዜ ይህ የተጻፈ ስለ እርሱ እንደሆነ ዐወቁት እንጂ ።
ወከመዝ ገብሩ ሎቱ ።
እንዲህ አደረጉለት ።

፲፯ ወሰማዕተ ኮንዎ እሙንቱ ሕዝብ እለ ሀለዉ ህየ ምስሌሁ ከመ ጸውዖ ለአልዓዛር እመቃብር ወአንሥኦ እምነ ሙታን ።

፲፯ አልዓዛር አልዓዛር ብሎ ከሙታን ለይቶ እንዳስነሣው ባስነሣው ጊዜ ከርሱ ጋራ የነበሩ ሰዎች መሰከሩለት ።

፲፰ ወበእንተ ዝንቱ ወፅኡ ኵሉ ሕዝብ ወተቀበልዎ ።

፲፰ ስለዚህም ሕዝቡ አመኑበት ።
እስመ ሰምዑ ተአምረ ዘገብረ ።
ያደረገውን ተአምራት ሰምተዋልና ።
ወዘንተኒ መንክረ ።
የሕፃናቱንም ምስጋና አንድም አስመ ሰምዑ ።
ሦስት ዓመት ከሦስት ወር ያደረገውን ተአምራት ።
ወዘንተኒ መንከረ አልዓዛርን ማስነሣቱን ሰምተዋልና

፲፱ ወይቤሉ ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን በበይናቲሆሙ ትሬእዩኑ ከመ አልቦ ዘትበቍዑ ወኢምንተኒ ።

፲፱ ፈሪሳውያን ግን እርስ በርሳቸው የምታገኙት ረብሕ ጥቅም ዘንበቍዕ የምናገኘው ረብሕ ጥቅም እንደሌለ አታውቁምን ።
ናሁ ኵሉ ዓለም ተለዎ ድኅሬሁ ።
እነሆ ሰው ሁሉ አመነበት አሉ ።

በአንተ አምነቶሙ ለአረሚ ወበእንተ ኢአሚኖቶሙ ለአይሁድ ።

፳ ወቦ እምስብእ ጽርእ አምውስተ አረሚ እለ ዓርጉ ይስግዱ ለበዓል ።
፳ እምሰብአ ጽርእና እምውስተ አረሚ አንድ ወገን በጽርእ ካሉ ካረማውያን ተለይተው ለገቢረ በዓል የወጡ አሉ እስራኤል ከሚጠት በኋላ በየወደዱት አገር ይኖራሉ በሕጋቸው ሁነው ለገቢረ በዓል ይወጣሉ ። አንድም በጽርእ ካሉ ከአረማውያን አምነው ለገቢረ በዓል የመጡ አሉ ። አንድም በልማድ ይወጡ አሉ የእሥራኤልን በዓል ባያከብሩ በእሥራኤል የታዘዘ መቅሠፍት ያገኛቸው ነበርና ። ሰብአ ጽርእኒ እመ ኢዓርጉ ለበዓል ይግበሩ በዓለ መጸለቶሙ እሙንቱኒ ይትቄሰኩ ዲበ ድቀቶሙ ለእሉ እንዲል ። አንድም ሥነ በዓል ለማየት የወጡ አሉ። ይስግዱ ሲል ያውካል ።

፳፩ ወሐሩ እሙንቱሂ ኀበ ፊልጶስ ዘቤተ ሳይዳ ዘገሊላ ።

፳፩ እርሳቸውም የገሊላ ዕፃ የምትሆን የሳይዳ ሰው ከሚሆን ፊልጶስ ዘንድ ሂደው ።
ወሰአልዎ ወይቤልዎ ንፈቅድ ።
ንርአዮ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ኢየሱስን ልናይ ማለት ልናድርሰት እንወዳለን አሉት

፳፪ ወሐረ ፊልጶስ ወነገሮ ለእንድርያስ ።
፳፪ ፊልጶስም ሂዶ ለእንድርያስ ነገረው ካንድ ሁለት ይሻላል ብሎ አንድም ሰው ማሳደር ለምዷል ብሎ ወሐሩ እንድርያስ ወፊልጶስ ወነገርዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
እንድርያስና ፊልጶስም ሂደው ለጌታ ነገሩት ።

፳፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ናሁ በጽሐ ጊዜሁ ከመ ይሰባሕ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
የሰው ልጅ የሚመሰገንበት ጊዜ ማለት የምሞት በት ጊዜ ደረሰ እሞታለሁ እሰቀላለሁ ብላችሁ ሰው እናሳድርልህ ትሉኛላችሁን የሹም ልጅ ኃዘን ቢነግሩት አደን እንዲሉ አንድም ወልደ ዕጓለ እመ ሕያው እኔም በእምነቱ የምገለጥበት ጊዜ ደረሰ እንግዲህማ ምን እኒህ ብቻ ሁሉ ያምኑብኛል እንጂ ለማለት እንዲህ አለ ።

፳፬ አማን አማን እብለክሙ እመኢወድቀት ኀጠተ ሥርናይ ውስተ ምድር ባሕቲታ ትነብር ።

፳፬ የሥንዴ ቅንጣት ካልተዘራች ካልፈረሰች ካልበሰበሰች ብቻዋን ትኖራለች ።
ወእመሰ ሞተት ብዙኀ ፍሬ ትፈሪ ።
የተዘራች የፈረሰች የበሰበሰች እንደሆነ ግን ብዙ ፍሬ ታፈራለች የ፳፬ ። አንድም ኀጠተ ሥርናይ እኔ ካልሞትሁ ብቻዬን በተሐድሶ ጸንቼ እኖራለሁ ። ወእመሰ ሞተት የሞትኩ እንደሆነ ግን ብዙ ምእ መናን በተሐድሶ ይኖራሉ ፤ በሚያመጣው ፤ ደሙን በወይን እንደ ሰጠን ለማጠየቅ ራሱን በሐረገ ወይን መስሎ እንደተናገረ ከዚህም ሥጋውን በሥንዴ እንደሰጠን ለማጠየቅ ራሱን በኀጠተ ሥርናይ መስሎ ተናገረ ።

፳፭ ወዘሰ ያፈቅራ ለነፍሱ ለይግድፋ፡ ማቴ፡፲፡ ፴፱ ማር፡፰ ፴፭ ሉቃ፡ ፱፡ ፳፬ ።
፳፭ ሰውነቱን ሊያድናት የወደደ በገራኅተ ጥም ቀት በገራኅተ መስቀል ይጣላት ።
ወዘሰ ጸልአ ለነፍሱ በዝንቱ ዓለም ።
ነፍሱን የጠላ ማለት ሰውነቱን ለመከራ አሳልፎ የሰጠ ። የዓቅባ ለሕይወት ዘለዓለም ። መንግሥተ ሰማይን ይወርሳል አንድም በሕይወት ዘለዓለም በክብር ይከባከባታል ።

፳፮ ወእመበ ዘይትለእከኒ ሊተ ለይትልወኒ ።
፳፮ በሃይማኖት የሚያገለግለኝ ሰው ቢኖር በምግባር ይምሰለኝ ።
እስመ ኀበ ሀሎኩ አነ ሀየ ይሄሉ ዘይትለእከኒ ።
በሃይማኖት የሚያገለግለኝ እኔ ከገባሁበት ገብቶ ይኖራልና ። አንድም በሃይማኖት በምግባር የሚ ገለግለኝ ሰው ቢኖር እኔ በተሰቀልኩባት መስቀል ተሰቅሎ እኔ በሞትኩበት ሞት ሞቶ በመከራ ይምሰለኝ ።
እስመ ኀበ ሀሎኩ በሃይማኖት በምግባር የሚያገለ ግለኝ እኔ በተሰቀልኩባት መስቀል ተሰቅሎ እኔ በሞትኩባት ሞት ሙቶ እኔ ከገባሁበት ውሳጤ መንጦላዕት ገብቶ ይኖራልና ።
ወዘሊተ ተልእከኒ ያከብሮ አቡየ ።
እኔን ያገለገለኝን አባቴ ያከብረዋል ማለት እኔን ባገለገለኝ አባቴ ያድርበታል ።

፳፯ ወይእዜሰ ተሀወከተኒ ነፍስየ ።
፳፯ ዛሬስ ሰውነቴ ሁከት ሥጋዊ ታወከችብኝ ወምንተ እብል ።
ምን እላለሁ ።
አባ አድኅና ለፍስየ እምዛቲ ሰዓት ።
አባቴ ከዚህች ሰዓት ሰውነቴን አድናት እላለሁ እንጂ ሌላ ምን እላለሁ ።
ወባሕቱ በእንተ ዝንቱ መጻእኩ ።
ነገር ግን ስለዚህ ሰው ሁኛለሁ ፤
ወበጻሕክዋ ለዛቲ ሰዓት ።
ከጊዜውም ደርሻለሁ ። አንድም ወይእዜሰ ብለህ መልስ ። ሰውነቴ ሁከት መንፈሳዊ ታወከችብኝ አድርጋት እትተዋት የሚል ሁከት ተነሣሣችብኝ ወምንተ እብል አባቴ ሰውነቴን ከዚህ ሰዓት አድ ናት እላለሁን አልልም ። ወባሕቱ አድናትስ እንዳ ልል አድናትም እንዳልል ስለዚህ ሰው ሁኛለሁ ከጊዜውም ደርሻለሁ ።

፳፰ አባ ሰብሖ ለወልድከ ።
፳፰ አባቴ ሆይ ልጅህን ግለጸው ።
ወመጽአ ቃል እምሰማይ ዘይብል ሰባሕኩከኒ ።
በዮርዳኖስ በደብረ ታቦር ገለጽኩህ ።
ወዓዲ እሴብሐከ ።
ዳግመኛም ሁለተኛ በመስቀል በተአምራት እገል ጽሃለሁ የሚል ቃል ተሰማ ።

፳፱ ወሕዝብሰ እለ ይቀውሙ ወይሰምዑ ይቤሉ ነጐድጓድ ውእቱ ።
፳፱ ርቀው ቆመው የሚሰሙት ሕዝብ ግን ነጐድጓድ ነው አሉ ።
ወቦ እለ ይቤሉ መልአክ ተናገሮ ።
ቀርበው የነበሩ መልአክ ተናገረው ያሉም አሉ ። አንድም ፍሬ ነገሩን ያልሰሙት ነጐድጓድ ነው አሉ ። ፍሬ ነገሩን የሰሙት መልአክ ነው አሉ ።

፴ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎሙ አኮ በእንቲአየ ዘመጽአ ዝቃል ።

፴ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ይህ ቃል የተሰማ ስለኔ አይደለም ።
አላ በእንቲአክሙ ።
ስለናንተ ነው እንጂ ብሎ መለሰላቸው ።

፴፩ ወናሁ አብለክሙ ይእዜ በጽሐ ኵነኔሁ ለዝንቱ ዓለም ።

፴፩ የዚህ ዓለም ፍርድ ደረሰ ማለት የዚህ ዓለም አበጋዝ ዲያብሎስ ድል የሚነሣበት ጊዜ ደረሰ ብዬ እነግራችኋለሁ ።
ወ እምይእዜሰ ይሰድድዎ ለመለአኬ ዝንቱ ዓለም።
እንግዲህ ወዲህስ የዚህ ዓለም አበጋዝ የሚሆን ዲያብሎስን ድል ይነሡታል ።
ወያወፅእዎ አፍአ ።
ከማደሪያው ከሰው ልቡና አስወጥተው ይሰዱታል ቦታውን መልቀቁ ድል መነሣቱ ነውና አንድም በጽሐ ኵነኔሁ ብለህ መልስ ሰው ሁሉ አንድ ወገን ሁኖ የሚገዛበት ጊዜ ደረሰ ያወፅእዎ አፍአ አይለወጥም

፴፪ ወአነኒ አምከመ ተለዓልኩ እምድር እስ ሕዝብ ኵሉ ኀቤየ።

፴፪ እኔም ከምድር ከፍ ብዬ የተሰቀልኩ እን ደሆነ ሰውን ሁሉ በግብርም በክብርም ወደኔ እቀ ርበዋለሁ ።

፴፫ ወዘንተ ዘይቤ እንዘ ይሀምሮሙ በአይ ሞት ሀለዎ ይሙት

፴፫ ይህን የተናገረ በምን ሞት ይሞት ዘንድ እንዳለው ሲያስረዳ ነው ። አንድም በምን ሞት ይሞት ዘንድ እለው ቢሉ በመሰቀል ተሰቅሎ ይሞት ዘንድ እንዳለው ሲያስረዳ ።
ይህን ተናገረ ። እምከመ ተለዓልኩ አለ ።

፴፬ ወአውሥእዎ ሕዝብ ።

፴፬ ሕዝቡም መለሱ ። መዝ፡፻፱፡፬ ኢሳ፡ ፬፡፯ ሕዝ፡፴፯፡፳፭ ።
ወይቤልዎ ንሕነሰ ሰማዕነ በውስተ ኦሪት ከመ ለዓለም ይነብር ክርስቶስ ።
እኛስ በክርስቶስ ሞት እንደሌለበት በኦሪት ሰም ተን ነበር ስምተናል ።
ወእፎ እንከ ትብለነ አንተ ሀለዎ ለወልደ ዕጓለ እመሕያው ይትለዓል ።
አንተ የሰው ልጅ ክርስቶስ ይሰቀል ዘንድ አለው እንደምን ትላለህ አሉት ። ወርኢኩ በራእየ ሌሊት ወመጽአ ከመ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ወበ ጽሐ ኀበ ብሉየ መዋዕል ወተውህበ ሎቱ መን ግሥት ወምኵናን መንግሥቱኒ መንግሥት ዘለ ዓለም ወምኵናኑኒ ለትውልደ ትውልድ ወአልቦ ማሕለቅት ለመንግሥቱ ። ያለውን ለውጦ አነበ በው ፡ ይህንማ የተናገረ ዳንኤል አይደለምን ስለ ምን ኦሪት አለው ቢሉ መጻሕፍተ ሐዲሳትን በመ ከብባቸው ወንጌል እንዳላቸው መጻሕፍተ ብሉ ያትንም በመከብባቸው ኦሪት ይላቸዋልና ። እኮኑ ውስተ ኦሪትክሙ ጽሑፍ አንሰ እቤ አማልክት አንትሙ እንዳለ ዳዊትን ኦሪት ብሎ ። ወበውስተ ኦሪትኒ ይብል በካልዕ ልሳን ወበካልዕ ከናፍር እትናገሮሙ ለሕዝብ እንዳለ ኢሳይያስን ኦሪት ብሎ ከዚህም ዳንኤልን ኦሪት ብሎ እንዲህ አለ ።
መኑ እንከ ዝንቱ ወልደ ዕጓለ እመሕያው ።
ይህ የሰው ልጅ ክርስቶስ ማነው አሉት ።

፴፭ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ዓዲ ኅዳጠ መዋዕለ ሀሎኩ ምስሌክሙ ብርሃን ።

፴፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ብርሃን እኔ ጥቂት ቀን ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ።
እንሶሱዉ እንዘ ብከሙ ብርሃን ዘእንበለ ይርከብ ክሙ ጽልመት ።
ብርሃን ሳለ ሳይጨልም ተመላለሱ ማለት እኔ ሳለሁ በኔ እመኑ ።
እስመ ዘየሐውር ውስተ ጽልመት ኢየአምር ኀበ የሐውር ።
በጨለማ የሚሄድ የሚሄድበትን አያውቀውምና ማለት እኔ ከሞትኩ በኋላ እኔ የምሠራውን ሥራ ሠርቶ በኔ ማሳመን የሚቻለው የለምና ።

፴፮ እምጣነ አንዘ ብከሙ ብርሃን እመኑ በብ ርሃን ።
ብርሃን ሳለሁ በኔ እመኑ ።
ከመ ትኩኑ ውሉደ ብርሃን ።

፴፮ ዕውቀት ያላችሁ ልጆች ትባሉ ዘንድ አንድም እምጣነ እንዘ ብከሙ ብለህ መልስ ። ብርሃን ዕድሜያችሁ ሳለ በኔ እመኑ ከመ ትኩኑ ውሉደ ብርሃን ዕውቀት ያላችሁ ልጆች ትሆኑ ዘንድ አንድም የእኔ ልጆች ትባሉ ዘንድ ።
ወዘንተ ብሂሎ እግዚእ ኢየሱስ ሖረ ወተኀብእሙ።
ይህን ተናግሮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ተሰውሯ ቸው ሄደ ጊዜው የተከሠቶ ሲሆን ረቂቅ መለኮት እንደሆነ ረቂቅ መለኮትን እንደ ተዋሐደ ለማጠየቅ።

፴፯ ወእንዘ መጠነዝ ተአምረ ይገብር በቅ ድሜሆሙ ኢአምኑ ቦቱ ።

፴፯ በፊታቸው ይህነን ያህል ተአምራት ሲያ ደርግ አላመኑበትም ።

፴፰ ከመ ይብጻሕ ቃለ ኢሳይያስ ነቢይ ዘይቤ እግዚኦ መኑ የአምነነ ሰምዐነ ።

፴፰ አቤቱ ትምህርታችንን ማን ይቀበለናል ።
ወለመኑ ተከሥተ መዝራዕቱ ለእግዚአብሔር ።

እግዚአብሔር እብ ቢሉ መዝራዕቱ ወልድ እግዚአብ ሔር ወልድ ቢሉ መዝዕራቱ ሥልጣኑ ለማን ተገለጠ ብሎ ኢሳይያስ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።

፴፱ ወበእንተ ዝንቱ ስእኑ አሚነ ።
፴፱ ስለዚህ ማመን ተሳናቸው ።
እስመ ካዕበ ይቤ ኢሳይያስ ዳግመኛ ኢሳይያስ እንዲህ ብሏልና ።

፵ ዖራ አዕይንቲሆሙ ።
፵ ዓይናቸው ታውሯል ።
ወገዘፋ አልባቢሆሙ ልባቸው ደንድኑዋልና ።
ከመ ኢይርአዩ በአዕይንቲሆሙ ።
ባይናቸው እንዳያዩ ።
ወኢይለብው በአልባቢሆሙ ።
በልቦናቸውም እንዳያውቁ ።
ከመ ኢይትመየጡ ኅቤየ ።
ወደኔ እንዳይመለሱ ፡
ወኢይሣሃሎሙ ።
ይቅር እንዳልላቸው ።

፵፩ ወዘንተ ይቤ ኢሳይያስ እስመ ርእየ ስብሐተ እግዚአብሔር ወነገረ በእንቲአሁ ፡

፵፩ ኢሳይያስ የእግዚአብሔር ጌትነቱን እውቋልና ከሰው ሹመት ሽልማት ሳይሻ ዖራ ገዘፋ ብሎ ደፍሮ ተናገረ ። አንድም እግዚአብሔር የሚያወርሰውን ክብር ዐውቋልና በመስቀል ይሰቀሉኝ በመጋዝ ይተርትሩኝ ብሎ ሳይፈር ሳያፍር ደፍሮ እንዲህ ብሎ የርሱን ነገር ተናገረ ።

፵፪ ወብዙኃን እመላእክተ ሕዝብ እለ አምኑ ቦቱ ።

፵፪ ከሕዝብም አለቆች ወገን ያመኑበት ብዙ ናቸው ።
ወባሕቱ ኢያግሐዱ በእንተ ፍርሃቶሙ ለፈሪሳውያን።
ነገር ግን ፈሪሳውያንን ስለ ፈሩ እምነታቸውን እልገለጡትም ።

ከመ ኢይስድድዎሙ እምኩራብ ።
ከምኩራብ እስወጥተው እንዳይሰዷቸው ።

፵፫ እስመ አብደሩ ስብሐተ ሰብእ እምስብሐተ እግዚአብሔር

፵፫ እግዚአብሔር ከሚያወርሳቸው ክብር ይልቅ ውዳሴ ከንቱን ከመንግሥተ ሰማይ ምኩራብን ከወንጌል አሪትን ወደዋልና ።

፵፬ ወጸርሐ እግዚእ ኢየሱስ በዓቢይ ቃል።
፵፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ጮሆ እስምቶ ተናገረ ።
ወይቤ ዘየአምን ብየ አኮ ብየ ኪያየ ባሕቲቶ ዘየአምን ።
በኔ ያመነ በኔ ብቻ አላመነም ።

ዘእንበለ በአብ ዘፈነወኒ ፡
በላከኝ በአባቴ አመነ እንጂ ።

፵፭ ወዘርእየ ኪያየ ርእዮ ለዘፈነወኒ ።
፵፭ እኔን ያየ አባቴን አየ ።

፵፮ ወአንስ ብርሃን መጻእኩ ውስተ ዓለም ።
፵፮ ብርሃን እኔ በመምህርነት ወደዚህ ዓለም መጣሁ ሰው ሆንሁ ።

ከመ ኵሉ ዘየአምን ብየ ኢይንበር ውስተጽልመት ።
በኔ ያመነ ሁሉ በክሕደት በገሃነም እንዳይኖር።

፵፯ ወዘኒ ሰምዓ ቃልየ ወኢዓቀቦ አኮ አነ ዘእኴንኖ ።

፵፯ የኔን ቃል ሰምቶ በኔ ባላመነ እኔ አልፈርድበትም ።
እስመ ኢመጻእኩ ከመ እኴንኖ ለዓለም ።
አድነው ዘንድ ነው እንጂ ልፈርድበት አልመጣሁምና ።

፵፰ ወዘሰ ክሕደኒ ።
፵፰ እኔን በካደ ።
ወኢተወክፈ ቃልየ ።
ትምህርቴን ባልተቀበለኝ ግን ።
ሀሎ ዘይኴንኖ ።
የሚፈርድበት አለ ።
ቃል ዘአነ ነበብኩ ውእቱ ይኴንኖ በደኀሪት ዕለት።
አሁን የምናገረው ነገር በኋለኛዪቱ ቀን ይፈርድበታል ።

፵፱ እስመ አኮ ዘእምኅቤየ ነበብኩ ።
፵፱ የማስተምር ከራሴ አንቅቼ አንድም ከራሴ ብቻ አንቅቼ አይደለምና ።
አላ እብ ዘፈነወኒ ውእቱ ትእዛዘ ወሀበኒ ዘከመ እነብብ ወዘከመ ዕብል ።
የምናገረውን የማስተምረውን እንደምናገር እንደ ማስተማር የላከኝ አባቴ ትእዛዙን ነገረኝ እንጂ ።

፶ ወአአምር ከመ ትእዛዙ ሕይወት ውእቱ ዘለዓለም ።

፶ ትእዛዙም የዘለዓለም ሕይወት እንደሆነች ዐውቃለሁ ።
ወዘሂ እነግር አነ በከመ ይቤለኒ አብ ከማሁ እነግር ።

የማስተምረውንም ከአብ በሀልውና ያገኘሁትን አስተምራለሁ ። አባቴ ሙት ተሰቀል እንዳለኝ ሙቱ ተሰቀሉ እላለሁ ።

በእንተ ተፍጻሜ ድራር ወኅፅበተ
እገሪሆሙ ለሐዋርያት ።

ምዕራፍ ፲፫ ።

፩ ወእምቅድመ በዓለ ፋሲካ ኮነ የአምር እግ
ዚእ ኢየሱስ ከመ በጽሐ ጊዜሁ ከመ ይፍልስ
እምዝንቱ ዓለም ወየሐውር ኀበ አብ ዘፈነዎ ።
ማቴ፡፳፮፡፪ ፡ ማር፡፲፬፡፩ ። ሉቃ፥ ፳፪፡፩ ።

፩ ከበዓለ ፋሲካ አስቀድሞ ጌታችን ኢየሱስ
ክርስቶስ ከዚህ ዓለም በሞት ተለይቶ ወደ
አብ እንዲሄድ ጊዜው እንደደረሰ ያውቅ
ነበር ። አፍቀሮሙ ማንሻ ።
አንድም ሶበ ኮነ የአምር ከመ ይፍልስ ፡ ከበዓለ
ፋሲካ አስቀድሞ ጌታችን ኢየሱስ ክር
ስቶስ ከዚህ ዓለም በሞት ተለይቶ ወደ አብ ይሄድ
ዘንድ ጊዜው እንደ ደረሰ ያውቅ በነበረ ጊዜ ።
አፍቀሮሙ ለእሊኣሁ እለ ውስተ ዓለም ።
ወገኖቹን በዓለም ያሉትን ወደዳቸው ፡ ደቀ መዛ
ሙርቱን እግራቸውን አጠባቸው ።
ወለዝሉፉ አፍቀሮሙ ።
ፈጽሞ ወደዳቸው ማለት ሥጋውን ደሙን ሰጣ
ቸው ። አንድም አፍቀሮሙ እሰቀልላችኋለሁ አላ
ቸው ። ወለዝሉፉ አፍቀሮሙ ልጅነትን እሰጣ
ችኋለሁ አላቸው ።

፪ ወእንዘ ይዴረሩ ቦአ ሰይጣን ውስተ ልቡ
ለይሁዳ ስምዖን አስቆሮታዊ ከመ ያግብኦ ።

፪ ሲበሉ ያሲዘው ዘንድ የአስቆሮት ሰው
በሚሆን በይሁዳ ሰይጣን አደረበት ። ተለይቶትን
ያውቃል አስፈጸመው ለማለት ነው እንጂ ።

፫ ወሶበ ኮነ የእምር እግዚእ ኢየሱስ ከመ
ኵሉ ተውህቦ እምኀበ አብ ወከመ አወፈዮ
አብ ኵሎ ውስተ እዴሁ ።

፫ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ አብ ሁሉን በእጁ
ጭብጥ በእግሩ እርግጥ አድርጎ እንዳስገዛለት ያውቅ
ነበር ፡ ያውቅ በነበረ ጊዜ ።
ወከመ እምኀበ እግዚአብሔር ወፅአ ።
ከእግዚአብሔር ዘንድ እንደ መጣ ፡
ወኀበ እግዚአብሔር የሐውር ።
ወደ እግዚአብሔርም እንዲሄድ ያውቅ ነበር ያውቅ
በነበረ ጊዜ ።

፬ ወተንሥአ እምኀበ ይዴረሩ ወአንበረ አል
ባሲሁ ።

፬ እያሡሩ የመጡ እንደሆነ ወተንሥአ በን
ይዞ የመጡ እንደሆነ ከሚመገቡበት ተነሥቶ ልብ
ሱን አኖረ ። ወነሥአ መክፈ ዘለንጽ ወቀነተ
ሐቌሁ ። ዘርፍ ያላት ዝናር አንሥቶ ወገቡን
ታጠቀ ሥራ የምታሠራ የምታስጌጥ ናት ። ኢዮ
አብ ወደ ሠልፍ ሲገባ እየለበሳት ይገባ እንደ
ነበረች ያለች ናት ብሰ መንድያ ይላታል በሺህ
ዘሐ የተሠራች ናት አንቀልባፊዶ ማጠቆ ገልድ
ጕለሻ ይላታል ።

፭ ወወደየ ማየ ውስተ ንብቲራ ።
፭ ውኃ በኵስኵት ቀዳ ።
ወአኀዘ ይሕፅብ እገሪሆሙ ለአርዳኢሁ ።
የደቀ መዛሙርቱን እግር ያጥብ ጀመር ።
ወመዝመዘ በውእቱ መክፈ ዘቀነተ ።
በታጠቀበት ዘርፍ ባለው ዝናር እያበሰ ያደርቅ
ጀመር ።

፮ ወበጽሐ ኀበ ስምዖን ጴጥሮስ
፮ ከጴጥሮስ ደረሰ ።
ወይቤሎ አንተኑ እግዚኦ ተሐፅበኒ እገርየ ።
አቤቱ አንተ እግሬን ታጥበኛለህን ፣ ዘተሐፅበኒ
እግሬን የምታጥበኝ አንተን ነህ አለው ።
፯ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፯ ጌታም መለሰ ።

ወይቤሎ ዘእገብር አነ አንተ ኢተአምር ይእዜ ።
እኔ ዛሬ የምሠራውን አንተ አታውቅም አለው ።
ወባሕቱ ድኅረሰ ተአምሮ ።
ኋላ ግን ታውቀዋለህ ነገር ግን ኋላ ታውቀዋለህ ።

፰ ወይቤሎ ስምዖን ጴጥሮስ ኢተሐፅበኒ እገ
ርየ ለዓለም ።

፰ ቀርጽ አድርጎ አንተ እግሬን አታፅበኝም
ኢትሕፅበኒ አትፅበኝ አለው ። ሕፅበት በይሁዳ
ይጀመራል ልቡ በፍቅረ ንዋይ ተታኋልና ዝም ብሎ
ይታፀባል ፣ ከጴጥሮስ ይደርሳል ይከራከራል ይረ
ታል ይታፀባል ፡ አንድም በጴጥሮስ ይጀምራል
ይከራከራል ይረታል ይታፀባል ዓሥራ አንዱ ኋር
ሱን አብነት አድርገው ይታፀባሉ ወአውሥአ እግ
ዚእ ኢየሱስ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ አማን አማን እብለከ ከመ ኢሐፀብኩከ
እገሪከ አልብከ ክፍል ምስሌየ ።
እኔ ካላፀብኩህ ከኔ ጋራ አንድነት የለህም ብዬ
እንደሌለህ በውነት እነግርሃለሁ ።

፱ ወይቤሎ ጴጥሮስ አኮ እገርየ ባሕቲቶ ዘተ
ሐፅበኒ ።

፱ ካንተ ጋራ አንድነትስ ከሚቀርብኝ እግ
ሬን ብቻ አታፅበኝም የምታፅበኝ እግሬን ብቻ
አይደለም ።
ወዓዲ እደውየኒ ወርእስየኒ ።
እጄንም ራሴንም ነው እንጂ አለው ።

፲ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዘሰ ወፅአ ተሐ
ፅበ ኢይፈቅድ ይትሐፀብ ዘእንበለ እገሪሁ ዳዕሙ ።

፲ ፈጽሞ የታጠበ እግሩን ብቻ ነው እንጂ ሌላ
ውን አካሉን ሊታጠብ አይሻም ።
እስመ ንጹሕ ኵለንታሁ ።
ሌላው አካሉ ንጹሕ ነውና ።
ወአንትሙሰ ንጹሐን አንትሙ
እናንተ ግን ንጹሐን ናችሁ ።
ወባሕቱ አኮ ኵልክሙ ንጹሐን ።
ነገር ግን ንጹሐን ማለቴ ሰሁላችሁ አይደለም ።

፲፩ እስመ የአምር እግዚእ ኢየሱስ ዘያገብአ
ወበእንተ ዝንቱ ይቤ አኮ ኵልክሙ ንጹሐን ።

፲፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሚያሲዘው
ይሁዳ እንደሆነ ያውቃልና ስለዚህ ሁላችሁ ንጹ
ሐን አይደሳችሁም አለ ።

፲፪ ወሶበ ሐፀቦሙ እገሪሆሙ ነሥአ አልባሲሁ
ወረፈቀ ካዕበ ምስሌሆሙ ።

፲፪ እግራቸውን ካጠባቸው በኋላ ልብሱን አን
ሥቶ ሁለተኛ ከርሳቸው ጋራ ተቀመጠ ክዚህ
በፊት ነቢብን ኦስቀድሞ ገቢርን ያስከትልላቸው
ነበር ዛሬ ግን ገቢርን አስቀድሞ በነቢብ ለማስተማር
ተቀመጠ የታጠቀበትን ለዮሐንስ ወንጌላዊ ሰጥቶ
ታል ጌታ በታጠቀበት ቢታጠቅ ሕገ ሥጋ ጠፍ
ቶለታል ፍቁረ እግዚእ ያሰኘውም ይህ ነው ።
ወይቤሎሙ እእመርክሙኑ ዘገበርኩ ለክሙ እነ ።
ያደረግሁላችሁን ዐወቃችሁትን አላቸው ።

፲፫ አንትሙሰ ትብሉኒ ሊቅነ ወእግዚእነ ።

፲፫ እናንተ መምህራችን ጌታችን ትሉኛላችሁ።
ወሠናየ ትብሉ ።
መልካም ተናግራችኋል ።
እስመ ከማሁ እነ ሊቅክሙ ወእግዚእክሙ ።
መምህራችን ጌታችን እንዳላችሁኝ መምህራችሁ
ጌታችሁ ነኝና ።

፲፬ ወሶበ እነ እንዘ ሊቅክሙ ወእግዚእክሙ
ሐፀብኩክሙ እገሪክሙ ።

፲፬ እኔ መምህራችሁ ጌታችሁ ስሆን እግራች
ሁን ካጠበኳችሁ ።
አንትሙኒ ይደልወክሙ ትሕፅቡ እግረ ቢጽክሙ ።
እናንተም የወንድማችሁን እግር ልታጥቡ ይገባ
ችኋል ።

፲፭ እስመ እርአያየ ወሀብኩክሙ
፲፭ አብነት ሁኛችኋለሁና ።
ከመ ትግበሩ አንትሙኒ ለቢጽክሙ በከመ ገበርኩ
ለክሙ እነ ።
እናንተም እኔ እንዳደረግሁላችሁ ታደርጉ ዘንድ
ይህንም መጻሕፍት ትሕትና ብለው ወስደውታል
ትርጓሜ ወንጌል እዘርዕ ፍቅረ ወትሕትና ውስተ
አልባቢክሙ ብሎ ሊቁም ከመ ያርትዕ እእጋረ
ሕዝብ በፍቅረ ትሕትና ብሎ ፡ ሠለስቱ ምእትም
በሕንጻ መነኮሳት ኢትትሐከይ ሐፂበ እግረ እኀው
ሶበ መጽኡ ኀቤከ እስመ በእንተ ዛቲ ግብር ይትኃሠ
ሥዎሙ ለእለ ያጸርእዋ እመኒ ኮኑ ኤጲስቆጶሳተ
እስመ እግዚእነ ሐፀበ እግረ አርዳኢሁ ፡ ወይቤሎሙ
በከመ ገበርኩ ለክሙ እነ ከማሁ አንትሙኒ ይደ
ልወክሙ ትሕፅቡ እግረ ቢጽክሙ እስመ አርአያየ
ወሀብኩክሙ ብለዋል ፊልክስዩስም ወሕፅበተ ፋሲካ
ትትሜሰል በምሥጢረ ትሕትና ፍጽምት ብሏል ።

፲፮ አማን አማን እብለክሙ አልቦ ገብር ዘየ
ዓቢ እምእግዚኡ ወአልቦ ሐዋርያ ዘየዓቢ እምዘፈ
ነዎ ። ማቴ.፲፣ ፳፬ ሉቃ. ፯፣ ፵ ዮሐ፡፲፭፡ ፳ ።

፲፮ በዚያውም ላይ ከጌታው የሚበልጥ ባሪያ
ከላኪው የሚበልጥ መላክተኛ የለም ።

፲፯ ወእመሰ ዘንተ ተአምሩ ብፁዓን አንትሙ
እመ ገበርክምዎ ።

፲፯ ይኸን ዐውቃችሁ ብትሠሩት ንዑዳን ክቡ
ራን ናችሁ ። ዓሥረኛውን ብፁዓን በዮሐንስ ያመጣ
ዋል ያልነው ይህ ነው ።

፲፰ ወኢኮ በእንተ ኵልክሙ ዘእብል ዘንተ።
፲፰ ይህን የምናገር ስለ ሁላችሁ አይደለም።
እስመ እነ እእምር መኑ እሙንቱ እለ ኃረይኩ ።
የመረጥኳችሁ እነማንም እንደሆናችሁ ዓውቃለሁና።
ወባሕቱ ከመ ይብጻሕ ቃለ መጽሐፍ ዘይቤ ዘይሴ
ሰይ እክልየ እንሥአ ሰኰናሁ ላዕሌየ ።
ባሕቱ ዋዌ ነው ። መጽሐፍ እንዲህ ብሎ የተናገረው
ይደርስ ይፈጸም ዘንድ የመረጥኳችሁ እነማንም እን
ደሆናችሁ ዐውቃለሁና ። አንድም መጽሐፍ እንዲህ
ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ እህሌን የሚመገብ
አንድም እህል ትምህርቴን የሚመገብ ይሁዳ ሰኰ
ናውን እነሣብኝ ወፅአ በሌሊት የሚል ነው ።

፲፱ ወይእዜሰ እነግረክሙ ዘእንበለ ይኩን ።
፲፱ ዛሬ ግን አስቀድሞ ነገርኳችሁ ።
ከመ እመ ኮነ ትእመኑ አንትሙ ከመ እነ ውእቱ ።
እኔ እንደሆንኩ ማለት በተደረገ ጊዜ የባሕርይ
አምላክ እንደሆንኩ ታምኑ ዘንድ አስቀድሞ ዐውቆ
እንጂ ነው የነገረን የባሕርይ አምላክ እንጂ ቢሆን
ብላችሁ ። ማቴ፤፲፥ ፵ ሉቃ፥ ፲፮ ።

፳ አማን አማን እብለክሙ ዘተወክፎ ዘፈ
ነውኩ እነ ኪያየ ተወክፈ ።

፳ የላክሁትን የተቀበለ እኔን ተቀበለ እኔን
በተቀበለ ማለት የላክሁትን በተቀበለ እድርበታለሁ
ወዘኪያየ ተወክፈ ተወክፎ ለዘፈነወኒ ።

እኔን የተቀበለ አባቴን ተቀበለ እኔ ባደርኩበት እባቴ ያድርበታል ።

ዘከመ አእመረ እግዚእ ኢየሱስ ዘያገብእ ።

፳፩ ወዘንተ ብሂሎ እግዚእ ኢየሱስ ተሀውከ በመንፈሱ። ማቴ፡፳፮፡፳፩ ማር፡፲፬፡፲፰ ሉቃ፡፳፪፡፳፩።

፳፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ይህን ተናግሮ በልቡ አዘነ ።
ወስምዓ ኮነ ወይቤ እማን እማን እብለክሙ ከመ አሐዱ እምኔክሙ ያገብእኒ ።
ከናንተ አንዱ እንዲያስይዘኝ ያስይዘኛል ብዬ በውነት እነግራችኋለሁ ብሎ መሰከረ ።

፳፪ ወተናጸሩ አርዳኢሁ በበይናቲሆሙ ።
፳፪ ደቀ መዛሙርቱም እርስ በርሳቸው ተጠቃቀሱ ።
እስመ ኢያእመሩ ወኃጥኡ እንበይነ መኑ ይብል ዘንተ ።
ይህን የተናገረ ስለማንም እንደሆነ ዐላወቁምና ።

፳፫ ወሀሎ አሐዱ እምአርዳኢሁ ዘይረፍቅ ውስተ ሕፅኑ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፫ የጌታ ባለሟል የሚሆን ከደቀ መዛሙርቱ አንድ ሰው ነበር ።
ወያፈቅሮ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም ይወደዋል ።

፳፬ ወቀጸቦ ስምዖን ጴጥሮስ ሎቱ ወይቤሎ ተሰአል በበይነ መኑ ይብል ዘንተ ።

፳፬ ይህን የተናገረ ስለ ማንም እንደሆነ ቀርበህ ጠይቀው አለው ።

፳፭ ወረፈቀ ውእቱ ረድእ ዲበ እንግድአሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፳፭ ያም ባለሟሉ በጌታችን እጠገብ ተቀመጠ።
ወይቤሎ እግዚእ መኑ ውእቱ ዘያገብእከ ።
እቤቱ የሚያሲዝህ ማነው አለው ።

፳፮ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ዝውእቱ ዘእነ እጸብሕ ሎቱ ኅብስተ ወእሜጥዎ ውእቱ ዘያገብእኒ ።

፳፮ እንጀራ በወጥ ጠልቄ የምሰጠው እሱ ያሲዘኛል አለው ።
ወጸብሐ ኅብስተ ወመጠዎ ለይሁዳ ስምዖን አስቆሮታዊ ።
እንጀራ በወጥ ጠልቆ የአስቆሮት ሰው ለሚሆን ለይሁዳ ሰጠው ።

፳፯ ወእምድኅረ ውእቱ ኅብስት ወሀበ ኅብስተ

፳፯ ለሐዋርያት ሥጋውን ከሰጣቸው በኋላ ወደ ኅብስትነት ለውጦ ሰጠው ፤ ፍትሐተ ማይ እን ዳለ ፍትሐተ ማይስ በሀገራችን ነው እንጂ በሀገራቸው የለም ። ማየ ኀቦን ከሆነ በኋላ ማየ መቍረርን አይሆንም እርሱስ ዳቦ ቢበላ ፍዳ ያመጣበታልን ብሎ በግዓ ፋሲካውን ከበሉ በኋላ ሥጋውን ሰጠው ወምስለ ውእቱ ኅብስት ቦአ ሰይጣን ውስተ ልቡ ለይሁዳ በሥጋው ምክንያት ሰይጣን አደረበት ፤ ሥጋው ደሙ ሰይጣን ያርቃል እንጂ ሰይጣን ያሳድራልን ቢሉ ፍዳ የሚያመጣበት ነውና ፤ ሆድ ቁርጠት ታማሚ ነው በመረቅ በበላ ጊዜ ደዌው እንዲቀሰቀስበት ።
ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ዘትገብር እንከ ፍጡነ ግበር ።
የምትሠራውን ፈጥነህ ሥራ አለው ።

፳፰ ወኢያእመሩ እለ ይረፍቁ ምስሌሁ ከመ በእንተ ምንት ይቤሎ ዘንተ ።

፳፰ ተቀምጠው ያሉት ይህን ያለው ስለምንም እንደሆነ ዐላወቁም ።

፳፱ ወቦ እለ መሰሎሙ ከመ በእንተ እስ ከሬን ዘሙዳየ ምጽዋት ዘሀሎ በኀበ ይሁዳ ዘይ ቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ሑር ተሣየጥ ዘንገብር ለበዓል።

፳፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በይሁዳ ዘንድ ስላለው ጥሬን ለበዓል የምናደርገው ።
እው ዘንሁብ ለነዳያን ።
ወይም የምንመጸውተው ዋጋ እድርግ ያለው የመሰላቸው አሉ ።
እስመ ውእቱ የዓቅብ እስከሬነ ቀምጠራ ዘሙዳየ ምጽዋት ።

መከፈቻ ያለው ሳጥን ጠባቂ ነበርና ።
ወቀምጠራ ዘሙዳየ ምጽዋት ሀሎ ውስተ እዴሁ ።
የሳጥን መከፈቻም በጁ ነበርና ።

፴ ወተመጢዎ ይሁዳ ውእተ ኅብስተ ወፅአ በሌሊት ።

፴ ይሁዳም ሥጋውን ደሙን ተቀብሎ እንደ ጽኑ ጠላት በሌሊት ወጥቶ ሄደ ።

ዘከመ ተናገረ ኢየሱስ እምድኅረ ድራር ወዘ ከመ ተነበየ ኅዲገተ ዘሐዋርያት ።

፴፩ ወወፂአ ውስተ ጊዜ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ይእዜኬ እንከ ተሰብሐ ወልደ ዕጓለ እመሕያው

፴፩ እርሱ ወጥቶ ከሄደ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሰው ልጅ ተመስገነ ተገለጠ እላ

ቸው በዮርዳኖስ ።
ወእግ ዚአብሔርኒ ተሰብሐ ቦቱ ።
እግዚአብሐርም ተመሰገነበት ተገለጸበት ፤ በደብረ ታቦር ።

፴፪ ወእመሰ እግዚአብሔር ተሰብሐ ቦቱ ።
፴፪ እጸፋውን ተናገረ እግዚአብሔርም ክተመሰ ገነበት ክተገለጸበት ።
እግዚአብሔርኒ ይሴብሖ ።
እግዚአብሔርም ያመሰግነዋል
ይገልጸዋል በመስቀል ።
ወሶቤሃ ይሴብሖ ።
ያን ጊዜ ያመሰግነዋል ይገልጸዋል በተእምራት ።
ወዓዲ ካዕበ ይሴብሖ ።
ዳግመኛ ያመሰግነዋል ይገልጸዋል በትንሣኤ የሕፅበተ እግር መገናኛ እንደምን ነው ቢሉ እንደ ሉቃስ ሑሩ ወእስተዳልው ለነ ዘንበልዐ ፍሥሐ ይላቸዋል እንደ ማቴዎስ በአይቴ ትፈቅድ ናስተዳሉ ለከ ፍሥሐ ትብላዕ ይሉታል እንደ ማርቆስ ምልክት ነግሮ ይሰዳቸዋል ሑሩ ሀገረ ዘቅድሜክሙ ወበ ህየ ትረክቡ ዘይጸውር ፃሕበ ማይ ወትልወዎ ኀበ ቦአ ቤት ወበልዎ ለበዓለ ውእቱ ቤት ይቤለከ ሊቅ ጊዜየ ቀርበ በኀቤከ እገብር ፋሲካ ምስለ አር ዳእየ ወውእቱ ያርእየክሙ ጽርሐ ንጡፈ ርቡየ ወስርግወ ወበህየ እስተዳልዉ ለነ ይላቸዋል ወሐዊሮሙ እርዳኢሁ ገብሩ በከመ አዘዞሙ እንዲል በጉን የሚያርዱበት ወቅለምት ደሙን የሚቀበሉበት ብርት ሥጋውን የሚቀቅሉበት ድስት አዘጋጅተዋል ።
ወምሴተ ከዊኖ እንደ ማቴዎስ ።
ወሶበ ኮነ ጊዜሁ ለድራር እንደ ሉቃስ ።
ወእንዘ ይዴረሩ እንደ ዮሐንስ ሲገቡ እንደ ሦስቱ አማን አማን እብለክሙ ከመ ፩ዱ እምኔክሙ ያገብአኒ ይላቸዋል ። እንደ ሁለቱ ወአኃዙ ይተክዙ አርድዕት ወይቤሉ በበ፩ዱ አነኑ እንጋ እግዚእ ይሉታል ፤ ይሁዳም ተለይቼ ብቀር ያውቅብኛል ብሎ አነኑ እንጋ ረቢ አለው ። ለሊከ ትቤ አለው እንድም እንደ ዮሐንስ ወሀሎ ፩ዱ እምእርዳኢሁ ዘይረፍቅ ውስተ ሕፅኑ ለእግዚዚእ ኢየሱስ ወያፈቅሮ እግዚእ ኢየሱስ ወቀጸቦ ስምዖን ጴጥሮስ ሎቱ ተሰአል እንበይነ መኑ ይብል ዘንተ ወረፈቀ ውእቱ ረድዕ ዲበ እንግድአሁ ወይቤሎ መኑ ውእቱ ያገብአከ ይለዋል ። እንደ ማቴዎስ ዘያወርድ እዴሁ ውስተ መጽብሕየ ። እንደ ሉቃስ እዴሁ ምስሌየ እንደ ዮሐንስ ዘእነ እጸብሕ ሎቱ ኅብስተ ወእሜጥዎ እንደ ዮሐንስ ምልክት ነግሮ እንኞራ በወጥ ጠልቆ ለይሁዳ ሰጠው ፤ ጴጥሮስና ዮሐንስ ይሁዳ እንደሆነ ዐውቀው ተጠቃቀሱ ። ወተዋከሁ አርድ ዕት ይላል ፤እንደ ሉቃስ ፲ሩ እኛን እኑረውን ሹመት ይካሰሱብናልን ብለዋቸዋል ። ጌታ ኢተእምሩኑ ከመ ነገሥቶሙ ለአሕዛብ ይኬንንዎሙ ወዓበይቶሙ ይቀንይዎሙ ወለክሙሰ እኮ ከማሁ እላ ዘይፈቅድ እምኔክሙ ይኩን ሊቀ ይኩንክሙ ገብረ ይላቸዋል ።

፴፫ ደቂቅየ ኅዳጠ መዋዕለ ሀሎኩ ምስሌክሙ።
፴፫ ልጆቼ ጥቂት ወራት ከናንተ ጋራ እኖራለሁ ።
ተኃሥሡኒ ። ትሹኛላችሁ ።
ወበከመ እቤሎሙ ለአይሁድ ኀበ አነ አሐውር እንትሙ ኢትክሉ መጺአ ።
ለአይሁድ እናንተ ወደኔ መምጣት አይቻላችሁም ብዬ እንደ ነገርኳቸው ።
ወለክሙኒ ይእዜ እነግረክሙ ።
ለናንተም ዛሬ እነግራችኋለሁ ።

፴፬ ወእሁበክሙ ሐዳሰ ትእዛዘ ።
፴፬ እንግዳ ሥርዓትን እሰጣችኋለሁ ።
ከመ ትትፋቀሩ በበይናቲክሙ
ትፋቀሩ ዘንድ ማለት አንዱ ላንዱ ይሞትለት ዘንድ ።
በከመ አነ አፍቀርኩክሙ ከማሁ እንትሙኒ ተፋቀሩ በበይናቲክሙ ።
እኔ እንደ ወደድኳችሁ እናንተም ደግሞ እርስ በርሳችሁ ትዋደዱ ዘንድ እንደ ሞትኩላችሁ እናንተም አንዱ ላንዱ ይሙትለት ።

፴፭ ወበዝንቱ የአምረክሙ ኵሉ ከመ አማን እርዳእየ እንትሙ ፤

፴፭ አንዱ ላንዱ የሞተለት እንደሆነ በዚህ በውነት የኔ ደቀ መዛሙርት እንደ ሆናችሁ ሁሉ ያውቃችኋል ።
እምከመ ተፋቀርክሙ በበይናቲክሙ ።
እርስ በርሳችሁ የተዋደዳችሁ እንደሆነ አንዱ ላንዱ የሞተ እንደሆነ ።

፴፮ ወይቤሎ ስምዖን ጴጥሮስ እግዚእ አይቴኑ ተሐውር ።

፴፮ ስምዖን ጴጥሮስም አቤቱ ወዴት ትሄዳለህ አለው ።
ወእውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ወይቤሎ ኀበስ አነ አሐውር ኢትክል ተሊወትየ ይእዜ ።
እኔን መከተል እኔ ወደምሄድበት ዛሬ መሄድ አይቻልህም ።
ወባሕቱ ድኅረሰ ትተልወኒ ።
ኋላ ግን ትከተለኛለህ ።

፴፯ ወይቤሎ ጴጥሮስ እግዚእ በእንተ ምንት ኢይክል ተሊዎተከ ይእዜ ።

፴፯ ጴጥሮስም አቤቱ ዛሬ አንተን መከተል የማይቻለኝ ስለምን ነው ።
ወእነ ነፍስየ እሜጡ በእንቲአከ ።
እኔ ስላንተ ሰውነቴን ስንኳ አሳልፌ እሰጣለሁ አለው ።

፴፰ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ማቴ፡ ፳፮ ፴፫ ማር፡ ፲፬ ፡ ፴ ሉቃ፡ ፳፪ ፡ ፴፫ ።

፴፰ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ነፍሰከኑ ትሜጡ በእንቲአየ እ ስምዖን ።
ስምዖን ሆይ ስለኔ ብለህ ሰውነትከን ለሕማም ለሞት አሳልፈህ ትሰጣለህን ።
አማን አማን እብለከ ዘእንበለ ይንቁ ዶርሆ ሠልሰ ትክሕደኒ ።
ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ብዬ እንድ ትክደኝ በውነት እነግርሃለሁ አለው ።
የክሕደተ ጴጥሮስ
መገናኛ እንደምን ነው ቢሉ ፡ ደቂቀየ ዓዲ ኅዳጠ መዋዕለ ሀሎኩ ምስሌክሙ በእንተ ምንት ኢይክል ተልወተከ ይእዜ እስኪል አንብ ። እንደ ማቴዎስ ፡ አማን አማን እብለክሙ ኵልክሙ ትክሕዱኒ በዛቲ ሌሊት እስመ ይብል መጽሐፍ እቀትሎ ለኖላዊ ወይዘረዉ አባግዓ መርዔቱ እንደ ሉቃስ ስምዖን ናሁ ሰአለ ስኢለ ሰይጣን የሐንጽጽክሙ ወየሐን ፍጽክሙ ከመ ስርናይ ። አንተሰ ተመይጠከ ጸን ዖሙ ለአኃዊከ ይለዋል ። እንደ ማቴዎስ እመኒ ኵሎሙ ክሕዱከ አንሰ ኢይክሕደከ ። እንደ ሉቃስ አንሰ ጥቡዕ ለሐዊር ምስሌከ ውስተ ኢየሩሳሌም እመኒ ለመዊት ወእመኒ ለተሞቅሖ ። እንደ ዮሐንስ ነፍስየ ጥቀ እሜጡ በእንቲአከ ይለዋል ። ጌታም እንደ ዮሐንስ ነፍስከኑ ትሜጡ በእንቲአየ እ ስምዖን ብሎ እንደ አራቱ አማን አማን እብለከ ዘእንበለ ይንቁ ደርሆ ሠልሰ ትክሕደኒ ይለዋል ። እንደ ማቴ ዎስ እመ ውትሂ ምስሌከ ወኢይክሕደከ ይለዋል ፡ ወከማሁ ይቤሎ ኵሎሙ ንመውትሂ ምስሌከ ወኢ ንክሕደከ ይሉታል እንደ ማርቆስ ወአፈድፈደ ጴጥ ሮስ ትሕልፍት ወትምክሕተ እንዘ ይብል እመው ትሂ ምስሌከ ወኢይክሕደክ ተመክቶ ያስመካቸዋል ። ወከማሁ ይቤሉ ኵሎሙ ንመውትሂ ምስሌክ ወኢ ንክሕደከ ይሉታል ።

በእንተ ፍሬያት ዘድኅነት ።

ምዕራፍ ፲፬ ።

፩ ኢይደንግፅክሙ ልብክሙ ።
፩ ሹመት ሽልማት ቀረብን ብላችሁ ልቡና ችሁ አይሸበርባችሁ ።
እመኑ በእግዚአብሔር ወእመኑ ብየ ።
ባባቴም በእኔም እመኑ እንጂ ።
፪ እስመ ውስተ ቤተ አቡየ ብዙኅ ማኅደር ወምዕራፍ ቦቱ ።

፪ ባባቴ ቤት በመንግሥተ ሰማይ ብዙ ማዕ ርገ ሀብታት አለና ። አንድም ኢይደንግፅክሙ እያልከ መልስ ። ፍቅር ክታዘዘ እኛ ካላደረግነው ብላችሁ ልቡናችሁ አይሸበርባችሁ ። እመኑ በእግዚ አብሔር ባባቴም በኔም እመኑ እንጂ ። እስመ ውስተ ቤተ አቡየ ባባቴ ቤት በዚህ ዓለም ብዙ ትሩፋት ሥጋ ትሩፋተ ነፍስ አለና ። አንድም ኢይደንግፅክሙ ። መስቀል ክታዘዘ እኛ ካላደረግነው ብላችሁ ልቡና ችሁ ኢይሸበርባችሁ ባባቴም በኔም እመኑ እንጂ ። ባባቴ ቤት በወንጌል ብዙ ተዋልጦተ ገድል አለና ። ወናሁ ነገርኩክሙ ከመ አሐው ር ወአስተዳሉ ለክሙ መካነ ።
እንድሄድ ልጅነትንም እንዳዘጋጅላችሁ ነገርኳችሁ ።
ወእመ አኮሰ እምኢይቤለክሙ ከመ አሐውር ወእ ስተዳሉ ለክሙ ማኅደረ ።
ያለዚያ ግን ባልነገርኳችሁም ነበር ።

፫ ወእምከመ ሖርኩ ወአስተዳሎኩ ለክሙ መካነ ።
ከሄድኩ ልጅነትንም ፡
፫ ወማኅደረ
መንግሥተ ሰማያትን ።
ወምዕራፈ መስቀልን ፡
ካዘጋጀሁላችሁ በኋላ ።
እመጽእ ካዕበ ወእነሥአክሙ ኀቤየ ።
ሁለተኛ መጥቼ እኔ ወዳለሁበት እወስዳችኋለሁ ፡
እመጽእ በረድኤት እነሥእክሙ በሞት ።
በረድኤት መምጣቱን በኩት ለመምጣቱ ካዕበ አለው ።
ከመ ተሀልዉ አንትሙኒ ኀበ ሀሎኩ አነ ።
እናንተም እኔ ከምኖርበት ትኖሩ ዘንድ ።

፬ ወለሊክሙ ተአምሩ ኀበ አሐውር ።
፬ እኔ የምሄድበትን አገር ታውቁታላችሁ።
ወተአምሩ ፍኖቶ ።
መንገዱንም ታውቁታላችሁ ።

፭ ወይቤሎ ቶማስ እግዚኦ ዘኢነአምር ኀበ ተሐውር በአፎ እንከ ነአምር ፍኖቶ ።

፭ ቶማስ እንዲህ አለው አቤቱ የምትሄድበትን አገር የማናውቅ መንገዱን እንደምን እናውቃለን አለው ። አገሩ የታወቀ እንደሆነ የገሌ አገር መንገድ ብየት በኩል ነው ተብሎ ተጠይቆ ይኬዳል ።

፮ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ፍኖተ ጽድቅ ወሕይወት ።
፮ የሕይወትና የጽድቅ መንገድ እኔ ነኝ ማለት ያንድነት የሦስትነት ባለቤት እኔ ነኝ ።
ወአልቦ ዘይመጽእ ኀበ አብ ዘእንበለ እንተ ኀቤየ

ያለኔ ወደ አብ የሚመጣ የለም እኔን ተወላዲ ካላለ አብን ወላዲ የሚለው የለም ።

፯ አምከመ ኪያየ አእመርክሙኒ እምአእመርክምዎ ለአቡየኒ ።

፯ እኔን ዐውቃችሁኝስ ቢሆን አባቴን ባወቃችሁት ነበር እኔን ተወላዲ ብላችሁኝ ቢሆንስ አባቴንም ወላዲ ባላችሁት ነበር፣እነ ውእቱ እያልክ መልስ የትሩፋተ ሥጋ የትሩፋተ ነፍስ ጀማሪ እኔ ነኝ ፣ ወአልቦ ዘይመጽእ ኀበ እብ ፣ እኔን አብነት ካላደረገ አባቴን ሥራ አሠራኝ የሚለው የለም ፣ ሰበሰ እኔንስ አብነት እድርጋችሁኝ ቢሆን አባቴንም ሥራ አሠራን ባላችሁት ነበር እንድም የክብረ ሥጋ የክብረ ነፍስ ጀማሪ እኔ ነኝ ። እኔን በዙር ካላደረገ አባቴን አከብረኝ የሚለው የለም ። ሰበሰ እኔን በዙር አድርጋችሁኝስ ቢሆን አባቴንም አክብረን ባላችሁት ነበር ወይእዜሰ አእመርክምዎሂ ወርኢክምዎሂ ። ዛሬ ግን አውቃችሁታል አይታችሁታል ።

፰ ወይቤሎ ፊልጶስ እግዚኦ አርእየነሁ ለአብ ወየአክለነ ።

፰ ፊልጶስ አብን አሳየን መስማቱ ይበቃናል። እንድም መስማት በማየት ይፈጸምልናል እንድም ለናፍቆት ለእሜት በደጅ ጽናት ይሆንልናል አለው ።

፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ መጠንዝ መዋዕል ሀሎኩ ምስሌክሙ ።

፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ይህን ያህል ዘመን ከናንተ ጋራ ስኖር ።
ወኢያእመርከኒኑ ፊልጶስ ።
ፊልጶስ አላወቅኸኝምን አለው
ዘርእየ ኪያየ ርእዮ ለአብ ።
እኔን ያየ አብን አየ ።
ርእየሰ ዘመለኮት አኮ በሥጋ እላ በኃይል ወበስብሐት ዘድልው ለመለኮት እንዲል
እፎ አንከ ትብል እርእየነሁ ለአብ ።
እንዴትም ትላለህ አብን አሳየን ።

፲ ኢተአምንሁ ከመ አነ በአብ ወአብ ብየ
፲ እኔ ባባቴ አባቴ በኔ ህልው እንደሆነ አታውቅምን ።
ወዝኒ ቃል ዘነገርኩክሙ አኮ ዘእምኀበ ባሕቲትየ ዘነበብኩ ይህም የነገርኳችሁ ነገር ከራሴ ብቻ አንቅቼ አይደለም ።
አላ አብ ዘሀሎ ብየ ውእቱ ይገብሮ ለዝንቱ ግብር ።
በኔ ህልውና ያለ አብ ይሠራዋል እንጂ ።

፲፩ እመኑ ከመ አነ በአብ ወአብ ብየ ።
፲፩ እኔ በአብ፡ አብ በኔ ህልው እንደሆነ እመኑ ።

ወእመ አኮስ በእንተ ግብርየ እመኑኒ ።
ያም ባይሆን ሥራዬን አይታችሁ እመኑ ። ይህን ሥራ አምላክ በሠራው እንጂ ዕሩቅ ብእሲ አይሠራውም ብላችሁ ።

፲፪ እማን እማን እብለክሙ ዘየአምን ብየ ግብረ ዘአነ እገብር ውእቱኒ ይገብር ።
፲፪ በኔ ያመነ እኔ የምሠራውን ሥራ እርሱም ይሠራል ።
ወዘየዓቢ እምኔሁ ይገብር ፡ ከርሱም የበለጠ ይሠራል ብዬ እንዲሠራ በውነት እነግራችኋለሁ ። እርሱ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር ነው ተአምራት ያደረገ እነሱ ብዙ ዘመን ሲኖሩ ብዙ ተአምራት ያደርጋሉና ።
እንድም እርሱ ያሥነሣ ያ፬ ቀን ሬሳ ነው ፡ እኒያ የሰባ የሰማንያ ዘመን ሙታን ያሥነሣሉና ይህስ እንዳይሆን እርሱንም እለ አብርሃምን አሥነሣ ይለዋል በተአምረ ኢየሱስ ብሎ የርሱ አይደነቅም ሕያወ ባሕርይ ነው ፡ እኒያ ድውይ ሲሆኑ ድውይ መፈወስ ሙት ሲሆኑ ሙት ማሥነሣት ይደነቃሉና ። እንድም ወአርባዕቱ እደዊሁ ለሰብእ እንዲል ሞትን ኃጢአትን ፍዳን ሰይጣንን ድል ነሥቷልና ። እንድም ሙት ከማሥነሣት የሚበልጥ ፍቅርን ገንዘብ ያደርጋል ። ዘሰ የዓቅባ ለፍቅር ውእቱ የአቢ እምአለ ያነሥኡ ሙታነ እንዲል ። በእንተ አለ መጽኡ ይትፌውሱ የሚደረግ ተአምራት አለና ። እስመ ገቢረ ተአምራት ወመንክራት ኢይክል ያድኅን እምዘነኔ ገሃነም እንዲል ። እንድም ከራሱ የበለጠ ተራራን ያፈልሳል ።
እስመ አነ እሐውር ኀበ አብ ፡
እኔ ወደ አብ እሄዳለሁና ።

፲፫ ወዙሉ ዘሰአልክሙ በስምየ ይገብር ፡ ለክሙ ። ማቴ፣ ፯፥፯ ማር. ፲፩፥፳፬ ዮሐ. ፲፮፥፳፫ ።

፲፫ በቅንው ወልድክ በስቁል ወልዩክ ብላችሁ የለመናችሁትን ያደርግላችኋል ።
ከመ ይሰባሕ አብ በወልድ ።
አብ በወልድ ይገለጽ ዘንድ

፲፬ ወእመቦ ዘሰአልክሙ በስምየ እገብር ለክሙ ኪያሁ ።

፲፬ ብትለምኑኝም አብ ያደረገውን አደርግላችኋለሁ ።

፲፭ ወእመሰ ታፈቅሩኒ ዕቀቡ ትእዛዝየ ።
፲፭ ከወደዳችሁኝስ ትእዛዜን ጠብቁ ።

፲፮ ወአነ እስእሎ ለአብ ይፈኑ ለክሙ ጰራቅሊጦስሃ ካልዓ ዘይሄሉ ምስሌክሙ እስከ ለዓለም

፲፯ ለዘላለም ከናንተ ጋራ የሚኖር ጰራቅሊ
ጦስን ይልክላችኋል ጰራቅሊጦስ ማለት መጽንኢ
መንጽሒ ናዛዚ ከሣቲ መሥተፍሥሒ መስተስርዪ
ማለት ነው ።
ክልዓ ባለው አንድ ገጽ የሚል ሰባልዮስ ይረታል
ዘከማየ የሚል አብነት ይገኛል መንፈስ ቅዱስ
ሕጹጽ የሚል መቅዶንዮስ ይረታበታል ።

፲፯ መንፈስ ጽድቅ ።
፲፯ አካላዊ ባሕርያዊ ሕይወት አከባሬ ሕይ
ወት አንድም መንፈስ ሐሰት አለና ከዚያ ሲለይ
መንፈስ ጽድቅ አለ ።
ዘኢይክል ዓለም ነሢአቶ ።
ዓለም እኔን ለሕማም ለሞት አሳልፎ እንዲሰጠኝ
ለሕማም ለሞት አሳልፎ ሊሰጠው የማይቻለው
አንድም እንደ ግሡሥ ከብት ገንዘብ ሊያደርገው
የማይቻለው ።
እስመ ኢይሬእዮ ወኢየአምሮ እያየውም አያው
ቀውምና ፤ አንድም ዘኢይክል ብለህ መልስ ፈትለ
ሣሬት ለንፍሃተ ነፋስ መቆም መቆየት እንዳይ
ቻለው ዓለማዊ ሰውነች ማደሪያው ሊሆን የማይ
ቻለው ። እስመ ኢይሬእዮ ፤ አያየውምና አይወ
ደውምና ።
ወአንትሙሰ ተአምርዎ ።
እናንተ ግን ታውቁታላችሁ ፤
እስመ ውእቱ ኀቤክሙ ይነብር
አድሮባችሁ ይኖራልና ።
ወውስቴትክሙ ይሄሉ ፤
በነፍስ በሥጋ ለማስት ደገመው ፤ በውስጣችሁ
ይኖራል ።

፲፰ ወኢየኀድገክሙ ዕጓለ ማውታ ትኩኑ ።
፲፰ ድኆች ትሆኑ ዘንድ አልተዋችሁም ።

፲፱ እስመ አነ እመጽእ ኀቤክሙ ዓዲ
እምድኅረ ኅዳጥ መዋዕል ።

፲፱ ከጥቂት ቀን በኋላ ወደናንተ እመጣለሁና
ወኢይሬእየኒ እንከ ዓለም ።
ሌላው ሰው አያየኝም ፤
ወአንትሙሰ ትሬእዩኒ
እናንተ ግን ታዩኛላችሁ ።
እስመ አነ ሕያው ።
እኔ ሕያው ነኝና ። በትንሣኤ ።
ወአንትሙሂ ተሐይው ፤
እናንተም ሕያዋን ናችሁና ።

፳ ይእተ አሚረ ተአምሩ ከመ አነ በአብ
ወአብ ብየ ።

፳ እኔ ባባቴ ፤ አባቴ በኔ ህልዋን እንደሆን
ያን ጊዜ ታውቃላችሁ ።

ወአንትሙሂ ብየ ።
እናንተም በኔ ታምናላችሁ ።
ወአነሂ ብክሙ ፤
እኔም በናንተ አድርባችኋለሁ

፳፩ ዘቦቱ ትእዛዝየ ወየዓቅቦ ውእቱ ያፈቅ
ረኒ ።

፳፩ በሕጌ የጸና ሕጌን የጠበቀ የሚወደኝ
እርሱ ነው ።
ወለዘያፈቅረኒ ያፈቅሮ አቡየ
የሚወደኝንም አባቴ ይወደዋል ያድርበታል ።
ወአነሂ አፈቅሮ ።
እኔም እወደዋለሁ አድርበታለሁ ።
ወአርኢዮ ርእስየ ።
ራሴንም እገልጽለታለሁ ።

፳፪ ወይቤሎ ይሁዳ ወእኮ አስቆሮታዊ
፳፪ የአስቆሮት ሰው ያይደለ ይሁዳ ታዴዎስ
አለ ።

እግዚኦ ምንትኑ ዘትቤ ከመ ለነ ሀለወከ ታርኢ
ርእሰከ ወአኮ ለዓለም ፤
አቤቱ ለዓለም ያይደለ ለኛ ራስህን ትገልጽ ዘንድ
እንዳለህ የምትናገረው ምንድነው አለ ።

፳፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፳፫ ጌታም መለሰለት ።
ወይቤሎ ዘያፈቅረኒ ይዕቀብ ቃልየ ።
የሚወደኝ ሕጌን ይጠብቅ ።
ወያፈቅሮ አቡየ ።
አባቴ ይወደዋል ያድርበታል
ወእመቦ ዘዓቀበ ቃልየ አነ ወአቡየ ንመጽእ ኀቤሁ
ወንገብር ምዕራፈ ውስቴቱ ፤
ሕጌን የጠበቀ ቢኖር ወደርሱ እንመጣለን በርሱም
ዘንድ ማደሪያ እናደርጋለን ማለት ሥራ እናሠራ
ዋለን ።

፳፬ ወዘሰ ኢያፈቅረኒ ኢየዓቅብ ቃልየ ።
፳፬ የማይወደኝ ግን ሕጌን አይጠብቅም ።
ወዝኒ ቃል ዘትሰምዑ ኢኮነ ቃለ ዚአየ ።
ይህም የምነግራችሁ ነገር የኔ ብቻ አይደለም ።
አላ ቃሉ ውእቱ ለአብ ለዘፈነወኒ ።
የላከኝ ያባቴም ነው እንጂ ።

፳፭ ወዘንተ ነገርኩክሙ እንዘ ሀሎኩ ምስ
ሌክሙ ።

፳፭ ከናንተ ጋራ ሳለሁ ይህን ነገርኳችሁ ።
፳፮ ወባሕቱ ጰራቅሊጦስ መንፈስ ጽድቅ ዘይ
ፌኑ አብ በስምየ ውእቱ ይሜህረክሙ ኵሎ ።

፳፮ ነገር ግን በስሜ ብታምኑ አብ የሚል
ክላችሁ ጰራቅሊጦስ ሁሉን ይገልጽላችኋል ።

ወያዜክረክሙ ዘነገርኩክሙ አነ ፡፡
እኔ የነገርኋችሁን ሁሉ ያሳስባችኋል ፡፡

፳፯ ሰላምየ አኀድግ ለክሙ ፡፡

፳፯ ወንጌልን እሠራላችኋለሁ ፡፡
ወሰላመ አቡየ እሁበክሙ ፡፡
ልጅነትን እሰጣችኋለሁ፡፡ አንድም ሰላምየ መስቀልን እዛችኋለሁ ፡፡ ወሰላመ አቡየ ፡ መንግሥተ ሰማይን አወርሳችኋለሁ አኮ በከመ ይሁብ ዓለም ዘእሁበክሙ አነ ፡፡ እኔ የምሰጣችሁ ሰው እንደሚሰጠው ያለ አይደለም ፡፡ ሰው ቢሰጥ ያን ዱን ሳንዱ ኃላፊውን ነው እርሱ ግን የባሕርዩን ነውና ፡፡ አንድም ሰው የሚሰጠው ግዙፉን ነው ፡፡ እርሱ ግን ረቂቁን ነውና ፡ ሰው ቢሰጥ ላዝማሪ ለዘዋሪ ነው ፡ እርሱ ግን ለዚህ አይሰጥ ምና ፡፡ አንድም ሰው ቢሰጥ ማፍጀት ፡ መሰል ቸት መጸጸት መመረር ፡፡ መሰቀቅ አለበት ፡፡ በሱ ግን ይህ ሁሉ የለበትምና
ኢይደንግፅክሙ ልብክሙ ፡፡
ልቦናችሁ አይደንግፅባችሁ ፡፡
ወኢትፍርሁ ፡፡
አትፍሩ ፡፡ ኢትፍርሁ ለማለት ደገመው ፡፡

፳፰ ሰማዕክሙ ዘእቤለክሙ ከመ እነ እሐውር ወእሰውጥ ኀቤክሙ ፡፡

፳፰ እንድሄድ እንደሰማችሁ ፡፡ እንድመለስ ሰምታችኋልና ፡፡ አንድም እንድሄድ እንደሰማችሁ እንድሄድ ብትሰሙ እንድመለስም ሰማችሁ ፡፡
ሶበሰ ታፈቅሩኒ እምተፈሣሕክሙ በሐዊርትየ ኀበ አብ ብትወዱኝስ ወደአብ በመሄዴ ደስ ባላችሁ ነበር፡፡
እስመ ውእቱ አብ የዓብየኒ ፡፡
አብ ያከብረኛልና ይበልጠኛልና ፡፡ አኮ እንዘ ይን እስ እም እብ በሕላዌሁ ወበዕሪናሁ ይነግር ዘንተ በእንተ ትስብዕቱ እንዲል ፡፡

፳፱ ወይእዜኒ ናሁ ነገርኩክሙ ዘእንበለ ይኩን ከመ እመ ኮነ ትእመኑ ፡፡

፳፱ በተደረገ ጊዜ አስቀድሞ ዐውቆ የነገረን የባሕርይ አምላክ ቢሆን እንጂ ነው ብላችሁ ታም ኑኝ ዘንድ ሳይደረግ አስቀድሜ ዛሬ ነገርኳችሁ ፡፡

፴ ወኢይትናገር እንከ ብዙኀ ምስሌክሙ ፡፡

፴ ለክሙ ሲል ነው ለናንተ ብዙ ነገር አልነገራችሁም ፡፡
እስመ ይመጽእ መልእኩ ለዝንቱ ዓለም ፡፡
የዚህ ዓለም አበጋዝ ዲያብሎስ ይመጣልና ፡፡
ወኢይረክብ በላዕሌየ ወኢምንተኒ ፡፡
በኔ ምንም ምን እያገኝብኝም የሐልዮ ለንኳን ኃጢአት አያገኝብኝም ፡፡ በሐልዮ እንዳልሠራ ለማ ጠየቅ እንዲህ አለ በነቢብ እንዳልሠራ ለማጠየቅ ነቢይ ኢገብረ ኃጢአተ ወኢተረክበ ሐሰት ውስተ አፉሁ ብሏል ፡፡ በገቢርም እንዳልሠራ ለማጠየቅ መኑ እምኔክሙ ዘይዛለፈኒ በእንተ ኃጢአት ብሏል፡፡

፴፩ ወባሕቱ ከመ ያእምር ዓለም ከመ አነ አፈቅሮ ለአብ ወበከመ ወሀበኒ አብ ትእዛዞ ከማሁ እገብር ፡፡ ግብ፲፱፥፳፱ ፡፡

፴፩ ነገር ግን አብን እንድወደው ሰው ሁሉ ያውቅ ዘንድ ተሰቀል ሙት እንዳለኝ እሰ ቀላለሁ እሞታለሁ ፡፡ አንድም እኔን አብ ፡፡ ተሰቀል ሙት እንዳለኝ ተሰቀሉ ሙቱ እላለሁ፡፡ ተንሥኡ ንሑር እምዝየ ከዚህ ተነሡ እንሂድ ይሁዳ አራት ቤት ጭፍራ ይዞ የሚመጣ ነውና ምክ ንያት ሁኘ የሰው ክብት አላዘርፍም ሲል እናን ተም ምክንያት ሁናችሁ የሰው ገንዘብ አታዘር ፉ ለማለት አብነት ለመሆን አንድም ትምህርት ባይክ ተትለት ከምሥጢር ወደ ምሥጢር እንሂድ ፡፡

በእንተ ሐረገ ወይን ወበእንተ አዕጹቂሁ ፡፡

## ምዕራፍ ፲፭ ፡፡

፩ አነ ውእቱ ሐረገ ወይን ዘጽድቅ ፡፡

፩ እውነተኛ ሐረገ ወይን እኔ ነኝ አብ ጉንደ ወይን ወልድ ጉንደ ወይን መንፈስ ቅዱስ ጉንደ ወይን እንዲል ፡፡
ወአቡየ ተካሊሁ ፡፡
ተካዩ አባቴ ነው ማለት ግንድ አድራጊው ግን አባቴ ነው ፡፡ አንድም እነ ውእቱ ሐረገ ወይን እንደ በዙርነቱ በዙር እኔ ነኝ ፡፡ በዙር አድራ ጊው ግን አባቴ ነው ፡፡ ወይን በተተከለ በሦስት ዓመት ደስ ሠርተውለት ያፈራል ጌታም ማስ ተማር በጀመረ በሦስት ዓመት ተሰቅሎ ለምእ መናን ፍሬ ክብርን ያፈራላቸዋልና ፡፡ እንድም ወይን ባመት ባመት አንዳንድ ቃዳ እያከለ ይሄ ዳል እየቀደም የምትሰፋ ሕግ ሠራሁላችሁ ሲል ባለፈው ሥጋውን በኀብስት እንደሰጠን ለማጠ የቅ ራሱን በኀጠተ ሥርናይ መስሎ እንደተናገረ ከዚህም ደሙን በወይን እንደሰጠን ለማጠየቅ ራሱን በሐረገ ወይን መስሎ ተናገረ ፡፡

፪ ወለኵሉ ዐጽቅ ዘኢይፈሪ በላዕሌየ ይገ ዝምዎ ፡፡

፪ ወደ ወርቅ ሂዶ በላዕሌየ አለ የማያፈራ ውን ዕንጨት ሁሉ ይቆርጡታል ፡፡
ወያአትትዎ ፡፡
ይጥሉታል ፡፡
ወለኵሉ ዐጽቅ ዘይፈሪ ያስተናጽሕዎ ፡፡
ለሚያፈራው ዕንጨት ያርሙለታል ይኰተኩቱ ለታል ፡፡
ከመ ብዙኀ ይፍረይ ፡፡
ብዙ ፍሬን ያፈራ ዘንድ ፡፡ አንድም ወለኵሉ ዐጽቅ ዘኢይፈሪ ብሰሀ መልስ ፡፡ በኔ አምኖ በጐ ሥራ የማይሠራውን ሰው ሁሉ ሥጋዉ ነፍሱን ከሥ

ጋው ይለዩታል። ወለኵሉ ዐጽቅ ዘይፈሪ በጐ ሥራ ለሚሠራ ለምእመን ግን መናፍቁን አውግዘው ይለ ዩበታል ፫ቱ መቶ አርዮስን ፡ መቶ አምሳው መቅ ዶንዮስን ፡ ሁለት መቶ ንስጥሮስን ። እስከ ምጽ አት የሚነሡ መምህራን እስከ ምጽአት የሚነሡ መናፍቃንን ። ከመ ብዙኃ ይፍረይ ምእመናን ብዙ ፍሬትሩፋት ያፈሩ ዘንድ። ወለኵሉ ዐጽቅ ያስተ ናጽሕዎ ይላል አብነት ። በጐ ፍሬ የሚያፈራውን ዕንጨት ሁሉ ይቆርጡታል ። ከመ ብዙኃ ይፍ ረይ። በጐው ዕንጨት ብዙ ፍሬ ያፈራ ዘንድ። በጐ ሥራ ለሚሠራው መናፍቁን አውግዘው ይለዩታል ምእመንም ብዙ ፍሬ ትሩፋትን ያፈራ ብዙ ፍሬ ክብርን ያገኝ ዘንድ ።

፫ ወአንትሙሰ ወዳእክሙ ንጹሓን አንትሙ በእንተ ቃል ዘነገርኩክሙ ። ዮሐ. ፯ ፲፫ ፡ ፲ ።
፫ እናንተ ግን እኔ ባላስተማርኳችሁ ፈጽማ ችሁ ንጹሐን ናችሁ ።

፬ ንበሩ ብየ ።
፬ በትምህርቴ ጸንታችሁ በኔ እምናችሁ ኑሩ ።
ወአነሂ ብክሙ ።
እኔም በናንተ አድሬባችሁ እኖራለሁ ።

፭ ወበከመ ዐጽቅ ኢይክል ፈርየ ባሕቲቱ እመ ኢሀሎ ውስተ ጕንደ ወይኑ ።

፭ ከጕንዱ የተለየ ዐጽቅ ማፍራት እንዳይቻ ለው ።
ከማሁ አንትሙኒ ኢትክሉ ፈርየ ለእመ ኢነበርክሙ ብየ ። እናንተም በኔ ካላመናችሁ ሥራ መሥራት አይቻላችሁም ።
አነ ውእቱ ጕንደ ወይን ዘጽድቅ ።
ጕንደ ወይን እኔ ነኝ ።
ወአንትሙሂ ዐፅጺቂሁ ።
ዐጽቆቹም እናንተ ናችሁ ።
ዘነበረ ብየ በኔ ባመነ
ወአነሂ ቦቱ ።
እኔም አድሬበት እኖራለሁ ፡ ውእቱ ማንሻ አን ድም በኔ ያመነ እኔ ያደርኩበት ።
ውእቱኬ ዘይፈሪ ብዙኃ ፡
ብዙ ፍሬ ትሩፋትን የሚያፈራ ብዙ ፍሬ ክብርን የሚያገኝ እርሱ ነው ።
እስመ ዘእንበሌየሰ አልቦ ዘትክሉ ገቢረ ወኢምንተኒ በኔ ካላመናችሁ ምንም ምን ሥራ መሥራት አይ ቻላችሁምና ።

፮ ወእመቦ ዘኢነበረ ብየ ይገድፍዎ ፍእአ ከመ ዐጽቅ ይቡስ

፮ በኔ ያላመነ ሰው ቢኖር ይቡስ ዐጽቅ እንደ መሆኑ እንደ ይቡስ ፀጽቅ እንደ አቢል ነፍሱን ከሥጋው ይለዩታል ። አንድም ከመ ፀጽቅ ይየብስ ይላል ነፍሱ ከሥጋው ይለያል ፡
ወያወፅእዎ ።
ከቤት ያወጡታል ። ወይገድፍዎ በመቃብር ይጥ ሉታል ። ወያነሥእዎ ፡ በትንሣኤ ያነሡታል ።
ወያውዕይዎ በእሳት ።
በገሃነም ፍዳ ያመጡበታል ። አንድም ይገልይዎ ወይገምድዎ ያወፅእዎ ወይገድፍዎ ያስተጋብእዎ ወያነሥእዎ ወያውዕይዎ ይላል አብነት ፡ ይገልይዎ ነፍሱን ከሥጋው ፡ ይገምድዎ ሥጋውን ከነፍሱ ይለዩታል ። ያወፅእዎ ከቤት ፡ ይገድፍዎ በመቃብር ያስተጋብእዎ በትንሣኤ ዘጉባኤ ያነሥእዎ ፡ ያሥነ ሡታል ያውዕይዎ በገሃነም ፍዳ ያመጡብታል ።

፯ ወእመሰ ነበርክሙ ብየ ፡
፯ በኔ አምናችሁ ብትኖሩ ፤
ወነበረ ቃልየ ኀቤክሙ ።
ያስተማርኳችሁም ትምህርት በናንተ ጸንቶ ቢኖር ።
ኵሉ ዘፈቀድክሙ ይከውን ለክሙ ።
የሻችሁት ሁሉ ይደረግላችኋል ።

፰ ወበዝንቱ ይሴባሕ አቡየ እምከመ ብዙኃ ፍሬ ትፈርዩ ።

፰ ብዙ ፍሬ ትሩፋት እንድታፈሩ ብትሆኑ ።
ወትከውኑኒ አርዳእየ እምጸማከሙ ።
ከጻማ እሬት ተለይታችሁ የኔ ደቀ መዛሙርት እንድትሆኑ ብትሆኑ በዚህ አባቴ ይመሰገናል ። አንድም በዝንቱ ይሰባሕ ይላል ፡ በዚህ አባቴ ይመ ሰገን ዘንድ ። ከመ ትፍረዩ ፡ ፍሬ ትሩፋትን ታፈሩ ዘንድ ፡ ወትከውኑ ። የኔ ደቀ መዛሙርት ትባሉ ዘንድ ። እምጸማከሙ እምጸእኩክሙ ። ከጻማ እሬት ለይቼ አመጣኋችሁ ።

፱ ወበከመ አፍቀረኒ አብ ከማሁ አነኒ አፍ ቀርኩክሙ ።

፱ አባቴ እኔን እንደ ወደደኝ አወዳችኋለሁ ትሰቀል ሙት እንዳለኝ ተሰቀሉ ሙቱ እላችኋለሁ።
ሀልዉ በፍቅረ ዚአየ ።
በኔ ፍቅር ጸንታችሁ ኑሩ ።

፲ ወእመሰ ታፈቅሩኒ ዕቀቡ ትእዛዝየ ።
፲ ከወደዳችሁኝ ትእዛዜን ጠብቁ ።
ወሀልዉ በፍቅረ ዚአየ ።
በኔ ፍቅር ጸንታችሁ ኑሩ ።
በከመ ዓቀብኩ አነ ኵሎ ትእዛዞ ለአቡየ ።
እኔ ያባቴን ትእዛዛት እንደ ጠበቅሁ ።
ወእሄሉ በፍቅሩ ።
በፍቅሩም ጸንቼ እንዳለሁ ፡ ዕቀቡ ሀልዉ በሌ ።

፲፩ ወነገርኩክሙ ዘንተ ።
፲፩ ይህን ነገርኳችሁ ።
ከመ የሀሉ ሐብየ ወፍሥሐየ ወፍቅርየ ኀቤክሙ ።

ልብየ ትምህርት ፣ ፍሥሐየ ልጅነት ። ፍቅርየ መስ
ቀል በናንተ ዘንድ ጸንቶ ይኖር ዘንድ ፣
ከመ ፍጹመ ይኩን ፍሥሐክሙ ።
ፈጽሞ ደስ ይላችሁ ዘንድ ።

ዘከመ ይደልዎሙ ለአኃው ተፋቅሮ ።

፲፪ ወዛቲ ይእቲ ትእዛዝእንቲአየ ወዘንተ እዘ
ዝኩክሙ ከመ ትትፋቀሩ በበይናቲክሙ በከመ አነ
አፍቀርኩክሙ ። ዮሐ ፣ ፲፪፣፴፬ ኤፌ፣፭፣፪ ፩ ተሰ፣፬፣፱።

፲፪ እኔ እንደ ወደድኋችሁ እናንት በናንት
ትዋደዱ ዘንድ ማለት እኔ እንደ ሞትኩላችሁ አንዱ
ላንዱ ይሞትለት ዘንድ ይህን ነገርኋችሁ ።

፲፫ አልቦ ዘየዓቢ ወይኄይስ እምዝፍቅር ከመ
ብእሲ ዘይሜጡ ነፍሶ ቤዛ ቢጹ ።

፲፫ ሰውነቱን ለባልንጀራው ቤዛ አድርጎ ለሕ
ማም ለሞት አሳልፎ እንዲሰጥ ከመሆን ፣ እንዲሰጥ
ሁኖ ከመገኘት እንዲሰጥ ሁኖ ተገኝቶ ከዚህ የበ
ለጠ ፍቅር የለም ። ታሪክ
አበምኔቱ ሲቀድስ የሚለብሰው ክቡር ልብስ አለ
ከማኅበሩ አንዱን ሰይጣን አገብሮት እንሥቶ ሰው
ሮታል አምጡ አለ ። ቢፈልጉ አጡት ከዚያው አንድ
ደግ ሰው አለ ያ ሰው ከዚያ ሂዶ ይጫወታል ደወል
መቱ ደወሉን ሰምቶ ደነገጠ ምነው ደነገጥክ አለው
ይህን የሚፈልጉትን ዕቃ ሰይጣን አገብሮኝ ወስጄ
ሰውሬ ነበር አለው አምጥተህ አትሪኸው ሂድ አለው
አምጥቶ አኑሮት ሄደ መጥተው እጅ ጸፉ ፣ ወጥቶ
ምነው አላቸው ፣ ገንዘብ ጠፍቶን እንፈልጋለን
አባታችን አንተን ጠርጥረንህ አይደለም ከሰው
ተለይተህ እንዳትቀር ብለን ነው እንጂ አሉት ፣
ገብታችሁ ፈልጉት ምን ዐውቃችሁ አላቸው ፣
ቢገቡ አገኙት አልሰወረውምና ፣ ላየ ደህና ውከጠ
ቀጣሬ ብለው ገርፈው ወገድ ውጣልን አሉት
ሁለት ቅጣት አቀጣለሁን ቀኖናየን ስጡኝና ከዚሁ
ላድርስ እንጂ አላቸው አይሆንም ከሌባ ጋራ እን
ኖርም አሉት ልብሱን እናንሣህ ቢሉት የማይነጣ
ሆነ ። ነገሩስ ካልቀረ ብሎ የወሰድኩ እኔ ነኝ አለ።
እርሱ በኔ ኃጢአት ነው የተገረፈው ብሎ ገልጠ
ተናገረ ጌታ በወንጌል እንዲህ ያለው ይህን ነው
ብለው አድንቀዋል ። ።

፲፬ እንትሙሰኬ አእርክትየ አንትሙ እምከመ
ገበርክሙ ኵሎ ዘአዘዝኩክሙ ።

፲፬ እናንተም ያዘዝኋችሁን ሁሉ ብታደርጉ
ወዳጆቼ ናችሁ ።

፲፭ ኢይብለክሙ እንከ አግብርትየ ።
፲፭ እንግዲህ ወዲህ ባሮች አልላችሁም ።
እላ አእርክትየ አንትሙ ።

ወዳጆቼ እላችኋለሁ እንጂ ።
እስመ ገብርሰ ኢየአምር ዘይሬስዮ እግዚኡ ።
ባሪያ ጌታው የሚያደርገውን አያውቀውም ይሸጠው
ይለውጠው ማጫ ትሎት አሳልፎ ይሰጠውም
እንደሆነ አያውቀውም ።
ወለክሙሰ አእርክትየ እብለክሙ ።
እናንተንስ ወዳጆቼ እላችኋለሁ ።
እስመ ኵሎ ዘሰማዕኩ በኀበ አቡየ ነገርኩክሙ ።
ካባቴ በህልውና የሰማሁትን ነግሬያችኋለሁና ።

፲፮ አኮ አንትሙ ዘኀረይክሙኒ ወሤምክሙኒ
ማቴ፣፳፰ ፣ ፲፱ ።

፲፮ ነገር ግን ማኅበር አባቱን ፣ ጭፍራ ፣ አለ
ቃውን መርጦ እንዲሾም እናንተ መርጣችሁ የሾ
ማችሁኝ አይደለም ።
አላ አነ ኀረይኩክሙ ወሤምኩክሙ ።
እኔ መርጬ ሹሜያችኋለሁ እንጂ ።
ወአፈድፈኩሙ ከመ ትሖሩ ።
እንድትሄዱ ማለት በሃይማኖት ጸንታችሁ እንድት
ኖሩ ።
ወፍሬ ትፍረዩ ።
ፍሬ ትሩፋትን እንድታፈሩ አደረጋችኋለሁ ።
ወውእቱ ፍሬክሙ ይንብር ለዓለም ።
ፍሬ ትሩፋታችሁም ለዘለዓለም ይኖራል ።
ከመ እመ ሰአልክምዎ ለአብ በስምየ ኵሎ ይሁበክሙ
በቅንው ወልድከ በስቁል ወልድከ ብላችሁ ብት
ለምኑት አብ እንዲያደርግላችሁ መጣን ።

፲፯ ወዘንተ እኤዝዘክሙ ከመ ትትፋቀሩ በበ
ይናቲክሙ ። ፩ ዮሐ፣ ፫፣ ፲፩ ።

፲፯ እርስ በርሳችሁ ትዋደዱ ዘንድ አንዱ ላንዱ
ይሞትለት ዘንድ ይህን ነገርኋችሁ ።

በእንተ ጸልአ ዝንቱ ዓለም ።

፲፰ እመሂ ዓለም ጸልአክሙ አእምሩ ከመ
ኪያየ ተደመ ጸሊአ ።

፲፰ ሰው ቢጠላችሁም አስቀድሞ እኔን እን
ደጸላኝ ዕወቁ ።

፲፱ ሶበሰ እምዓለም አንትሙ እምአፍቀረክሙ
ዓለም ።
፲፱ ከዓለም ወገን ብትሆኑ ሰው በወደዳችሁ
ነበር ።
እስመ ዓለም እሊአሁ ያፈቅር ።
ወገን ወገኑን ይወዳልና ሌባ ሌባውን ቀጣፊ
ቀጣፊውን ።
ወባሕቱ እስመ ኢኮንክሙ እምዓለም ።
እናንት ግን ከዓለም ወገን አይደላችሁም ።
አላ አነ ኀረይኩክሙ እምውስተ ዓለም ።

እኔ ከዓለም መርጫችኋለሁ እንጂ ።
በእንተ ዝንቱ ይጸልአክሙ ዓለም ።
ስለዚህ ሰው ይጠላችኋል ።

፳ ተዘከሩ ቃልየ ዘአነ እቤለክሙ አልቦ ገብር ዘየዓቢ እምእግዚኡ ወኢሐዋርያ ማቴ፣፲፣፳፬፣ዮሐ፣ ፲፫፣፲፮ ። ማቴ፡፳፬፡፱ ።

፳ በዚያውም ላይ ከጌታው የሚበልጥ ባሪያ ከላኪው የሚበልጥ መልከተኛ የለም ያልኳችሁን አስቡ ።
እምከመ ኪያየ ሰደዱ ኪያክሙኒ ይሰድዱክሙ ።
እኔን በሞት አስወጥተው ከሰደዱኝ እናንተንም ከሀገራችሁ አስወጥተው ይሰዱዋችኋል ።
ወሶበሰ ዓቀቡ ቃልየ ቃለክሙኒ እምዓቀቡ ።
ነገሬን ተቀብለውኝስ ቢሆን እናንተንም በተቀበ ሏችሁ ነበር

፳፩ ወባሕቱ ዘንተ ኵሎ ይገብሩ ላእሌክሙ በእንተ ስምየ እስመ ኢየአምርዎ ለዘፈነወኒ ።

፳፩ ነገር ግን እባቴን አያውቁትምና በኔ ስም ስለአስተማራችሁ ይህን ሁሉ ያመጡባችኋል።
አንድም በኔ ስም ስለአስተማራችሁ ፤ ይህን ሁሉ የሚያመጡባችሁ አባቴን አያውቁትምና ስለዚህ ነው ።

፳፪ ሶበሰ ኢመጻእኩ አነ ወኢነገርክዎሙ እም ድኅኑ ወእምኢኮነሙ ጌጋየ ።

፳፪ ሰው ሁኜስ ባላስተማርኋቸው ዕዳ ባልሆ ነባቸው ነበር ከፍዳም በዳኑ ነበር ።
ወይእዜሰ ባሕቱ አልቦሙ ምክንያት ለጌጋዮሙ ።
ዛሬ ግን ለበደላቸው ምክንያት የላቸውም ። ባናውቅ ያስተምረን ባይኖር አይሉም ።

፳፫ ዘጸልዓ ኪያየ ጸልዓ ለአቡየ ።
፳፫ እኔን የጠላ አባቴን ጠላው ።
፳፬ ሶበሰ ኢገበርኩ ሎሙ ግብረ ዘባዕድ ኢገ ብሮ እምኢኮኖሙ ጌጋየ ።

፳፬ ሌላ ያልሠራው ሥራስ ባልሠራላቸው ዕዳ ባልሆነባቸውም ነባር ፤ ምነው ኤልያስ አንድ ምውት ኤልሣዕ ሁለት ምውት አሥነሥተው የለምን ቢሉ የኒያ ሕጸጽ አለበት፣የሉ ግን ሕጸጽ የለበትምና።
የኒያ የጸጋ ነው ፤ የርሱ የባሕርይ ነውና ።
ወይእዜሰ ባሕቱ ርእዩኒ ወጸልዑኒ ።
ዛሬ ግን አዩኝ ጠሉኝ ።
ኪያየኒ ወአቡየኒ ።
አንድም እኔንም አባቴንም አዩን ጠሉን ።

፳፭ ወባሕቱ ከመ ይብጻሕ ቃል ዘጽሑፍ ውስተ ኦሪቶሙ ዘይቤ ጸልዑኒ በከንቱ ፤ መዝ፡ ፲፱ ሉቃ. ፳፬ ፣ ፵፰ ።

፳፭ ነገር ግን በኦሪት ጽልዓ በዓመፃ ይጸልዑኒ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ በከንቱ ጠሉኝ ።

፳፮ ወሶበ መጽአ ጰራቅሊጦስ ዘአነ እፌኑ ለክሙ ዘይወፅእ እምአብ ውእቱ ሰማዕትየ ።

፳፮ ከአብ የሚወጣ እኔ የምልክላችሁ ጰራ ቅሊጦስ በመጣ ጊዜ ምስክሬ ነው ።

፳፯ ወአንትሙኒ ሰማዕትየ ።
፳፯ እናንተም ምስክሮቼ ናችሁ ።
እስመ እምትካት ሀለውክሙ ምስሌየ ኅሩያንየ ።
ተመርጣችሁ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር ከኔ ጋራ ነበራችሁና አንድም ዕሩይየ ይላል አብነት ከጥንት ጀምሮ መንፈስ ቅዱስ በዕሪናየ አለና ።

በእንተ ሰደታት ።

ምዕራፍ ፲፮

፩ ወዘንተ ነገርኩኩሙ ከመ ኢትትዓቀፉ
፩ እንዳትጠራጠሩ ይህን ነገርኳችሁ ።
፪ እስመ እምኵራባቲሆሙ ያወፅኡክሙ

፪ ከምኵራባቸው ያወጧችኋልና
ወባሕቱ ትመጽእ ሰዓት ወይበጽሕ ጊዜሁ ከመ ኵሉ ዘይቀትለክሙ ይመስሎ ከመ ዘመሥዋዕተ ያበውእ ለእግዚአብሔር ።
ባሕቱ ዋዌ ነው እናንተን የገደለ ሁሉ ለእግዚአብ ሔር መሥዋዕት ያቀረበ የሚመስልበት ጊዜ ይደ ርሳል ።

፫ ወዘንተኒ ዘይገብሩ ላዕሌክሙ
፫ ይህንም የሚያደርጉባችሁ ።
እስመ ኢየአምርዎ ለአብ ።
አብን አያውቁትምና ።
ወኢኪያየ ።
እኔንም አያውቁኝምና አንድም መከራ የሚያመ ጡባችሁ እኔንም አባቴንም አያውቁንምና ስለዚህ ነው ።

፬ ወባሕቱ ዘንተሰ ነገርኩክሙ ከመ ትዘከ ርዎ አመ በጽሐ ጊዜሁ

፬ ነገር ግን በተደረገ ጊዜ እኔ እንደነገርኋችሁ ታስቡት ዘንድ ይህን ነገርኋችሁ ሳይደረግ አስቀድሞ ዐውቆ የነገረን የባሕርይ አምላክ እንጂ ቢሆን ነው ብላችሁ ታስቡት ዘንድ ።
፭ ወቀዲሙሰ ኢነገርኩክሙ ዘንተ ።
፭ አስቀድሞ ግን ይህን አልነገርኋችሁም ።
እስመ ሀሎኩ ምስሌክሙ ።
ከናንተ ጋራ በሕይወት ነበርኩና ።
ወይእዜሰ ባሕቱ አሐውር ኀበ አብ ዘፈነወኒ ።
ነገር ግን ወደላከኝ ወደ አብ እሄዳለሁ ።
ወኢ፩ዱኒ እምኔክሙ ኢትብሉኒ አይቴ ተሐውር።

ከናንተ እንዳችሁ ስንኳ ወዴት ትሄዳለህ አትሉኝም አብራችሁኝ አትሞቱም ።

፮ ወባሕቱ እስመ ዘንተ ነገርኩክሙ ኀዘን መልአ ውስተ ል ብክሙ ።

፮ ባሕቱና ባሕቱ አንድ ወገን ይህንስ ስለነ ገርኋችሁ በልባችሁ ኀዘን ሰፍሮባችኋል ።

ዘከመ አሰፈዎሙ ኢየሱስ መንፈስ ቅዱስ ።

፯ ወአንሰ አማን ህልወ እብለክሙ ።
፯ እኔስ ቀዋሚ ነገር ነገርኋችሁ ።
ይኄይሰክሙ ኢሐውር አነ ኀበ አብ
ወደ አብ እኔ ብሔድ ይሻላችኋል ።
እስመ እመ ኢሖርኩ አነ ኢይመጽእ ጰራቅሊጦስ ኀቤክሙ
እኔ ካልሄድኩ መንፈስ ቅዱስ አይሰጣችሁምና ።
ወእመሰ ሖርኩ አነ ኀበ አብ እፌንዎ ለክሙ ።
እኔ ወደአብ የሄድኩ እንደሆነ ግን እልከላችኋለሁ።

፰ ወመጺኦ ውእቱ ይዛለፍ ለዓለም በእንተ ኃጢአት ።

፰ በመጣም ጊዜ በኃጢአት ምክንያት ሰውን ይዘልፈዋል ።
ወበእንተ ጽድቅ ።
በጽድቅ ምክንያት ።
ወበእንተ ኵነኔ ።
በኵነኔም ምክንያት ይዘልፈዋል ። ሦስት አርእስት ተናገረ ። ስምስቱም ያመጣል ።
በእንተ ኃጢአትስ ።
በኃጢአትም ምክንያት ይዘልፈዋል ያልኋችሁ ።

፱ እስመ ኢየአምኑ ብየ ።
፱ አላመኑብኝምና ስለዚህ ነው ።
አስተኃፈረ ኃጢአተ በዲበ ምድር ብለው ይነግሯ ቸዋል በዚህ ባያምኑ ድውይ ፈውሰው ያባዩዋቸዋል በዚያ ባያምኑ ዕዳ ይሆንባቸዋልና ።

፲ ወበእንተ ጽድቅ ።
፲ በጽድቅ ምክንያት ይዘልፈዋል ያልኩት ።
እስመ አነ እሐውር ኀበ አብ ወደአብ እሄዳለሁና ።
ወኢትሬእዩኒ እንከ ።
ከእንግዲህ ወዲህ አታዩኝምና ስለዚህ ነው ። አብ ጠለ ሞተ በውስተ ሲኦል ወነሥተ ሙስና በውስተ መቃብር ብለው ይነግሯቸዋል በዚህ ባያምኑ ሙት አሥነሥተው ያሳዩዋቸዋል በዚህ ባያምኑ ይፈረ ድባቸዋልና ።

፲፩ ወበእንተስ ኵነኔ እስመ ይትኴነን መል አኩ ለዝንቱ ዓለም ።

፲፩ በኵነኔ ምክንያት ይዘልፈዋል ያልኩት የዚህ ዓለም አበጋዝ ዲያብሎስ ድል ይነሣልና ስለ ዚህ ነው ። ወሠዓረ መርገመ በዲበ ዕፀ መስቀል ብሰው ይነግሩዋቸዋል በዚህ ባያምኑ ጋኔን አው ጥተው ያሳዩዋቸዋልና በዚያ ባያምኑ ዕዳ ይሆን ባቸዋልና ። አንድም በእንተ ኃጢአት አስተኃፈረ ኃጢአተ በዲበ ምድር ወአብጠለ ሞተ በውስተ ሲኦል ብሰው ይነግሩዋቸዋል በዚህ ባያምኑ ድውይ ፈውሰው ሙት አሥነሥተው ያሳዩዋቸዋል በዚህ ባያምኑ ይፈረድባቸዋል ። ወበእንተ ጽድቅስ እም ቅድመ ይትወለድ አብርሃም ሀሎኩ አነ ብኋል ብለው ይነግሩዋቸዋል በዚህ ባያምኑ ከራሳቸው አንቅተው ቀዳሚሁ ቃል ብሰው ይነግሩዋቸዋል፤ በዚህ ባያምኑ ዕዳ ይሆንባቸዋልና ። ወበእንተ ኵነኔ አይሰወጥም ።

፲፪ ወብየ ብዙኃ ነገረ ዘእነግረክሙ ።
፲፪ የምነግራችሁ ብዙ ነገር ነበረኝ ።
ወባሕቱ ኢትክሉ ጸዊሮቶ ይእዜ ።
ለብዎቶ ሲል ነው ። ነገር ግን ዛሬ ማወቅ አይቻላ ችሁም ።

፲፫ ወመጺኦ ውእቱ መንፈስ ጽድቅ ይመር ህክሙ ኀበ ኵሉ ጽድቅ ።

፲፫ መንፈስ ቅዱስ በመጣ ጊዜ ወደትሩፋተ ሥጋ ወደትሩፋተ ነፍስ መርቶ ያደርሳችኋል ።
እስመ ኢይነግር ዘእምኅቤሁ ፤
ከራሱ አንቅቶ አያስተምርምና ፤
ወዘሰምዐ ዳዕሙ ይነግር ።
ከኔ በሀልው የሰማውን ያስተምራል እንጂ።አንድም ከርሱ ብቻ አንቅቶ አይናገርም ከአብ ከኔም በሀ ልውና የሰማውንም ያስተምራል እንጂ ።
ወዘይመጽእኒ ይነግረክሙ ፤
ዘይመጽእ ጰራቅሊጦስ ይነግራችኋል ። አንድም ያለፈውን ብቻ አይነግራችሁም የሚመጣውንም ይነ ግራችኋል ።

፲፬ ወውእቱ ኪያየ ይሴብሕ ።
፲፬ እርሱ እኔን ይገልጻል ።
እስመ እምዚአየ ይነሥእ ወይነግረክሙ ።
እግዚአነትን መምህርነትን ቃልነትን ትንቢትን ዘመ ንን ከኔ ገንዘብ ያደርጋልና ይነግራችኋል ።
እስመ ኵሉ ዘቦ ለአቡየ ዚአየ ውእቱ ፣
ያባቴ ገንዘብ ሁሉ ገንዘቤ ነውና ።

፲፭ ወበእንተ ዝንቱ እብለክሙ እምዚአየ ይነ ሥእ ወይነግረክሙ ኵሎ ።

፲፭ ስለዚህ ከኔ ገንዘብ አድርጎ ሁሉን ይነ ግራችኋል እላችኋለሁ ።

በእንተ ተመይጦተ ኢየሱስ ውስተ ሰማይ ።

፲፮ ዓዲ ኅዳጠ ኢትሬእዩኒ ።
፲፮ ጥቂት ወራት አታዩኝም ።
ወካዕበ ኅዳጠ ትሬእዩኒ ።
ዳግመኛ ጥቂት ወራት ታዩኛላችሁ ።
እስመ አሐውር ኀበ አብ ።
ወደአብ እሄዳለሁና ።

፲፯ ወተበሀሉ አርዳኢሁ በበይናቲሆሙ ምን
ትኑ ዝንቱ ዘይብለነ ዓዲ ኅዳጠ ኢትሬእዩኒ ወካዕበ
ዓዲ ኅዳጠ ትሬእዩኒ ።

፲፯ ደቀ መዛሙርቱ እርስ በርሳቸው ጥቂት
ወራት አታዩኝም ጥቂት ወራት ታዩኛላችሁ የሚ
ለን ምንድነው ።
እስመ እሐውር ኀበ አብ ።
ወደአብ እሄዳለሁና ።

፲፰ ወይቤሉ ምንትኑ ዝንቱ ዘይብለነ ኅዳጠ።
፲፰ ጥቂት ወራት አታዩኝም የሚለን ምንድነው
ኢነአምር ዘይትናገር ቦቱ ።
የሚናገረውን አናውቀውም አሉ ።

፲፱ ወአእመሮሙ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ይፈ
ቅዱ ይሰአልዎ

፲፱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ሊጠይቁት
እንደወደዱ አውቆ ወይቤሎሙ በእንተ ዝንቱ ትት
ኃሠሡ በበይናቲክሙ እስመ እቤለክሙ ዓዲ ኅዳጠ
ኢትሬእዩኒ ወካዕበ ኅዳጠ ትሬእዩኒ ጥቂት ወራት
አታዩኝም ጥቂት ወራት ታዩኛለችሁ ብያችኋለሁና
ስለዚህ እርስ በርሳችሁ ትመራመራላችሁን አላቸው።

፳ አማን አማን እብለክሙ ከመ ትበክዩ ወት
ላህዉ አንትሙ ።

፳ እንድታለቅሱ እንድታዝኑ በውነት እነግ
ራችኋለሁ አላቸው ።
ወዓለምስ ይትፌሣሕ ።
ዓለም ግን ደስ ይለዋል ፤
ወአንትሙሰ ትቴዝኑ ፤
እናንተም ታዝናላችሁ ።
ወባሕቱ ኃዘንክሙ ፍሥሐ ይከውንክሙ ።
ነገር ግን ኃዘናችሁ ደስ ያሰኛችኋል ።

፳፩ በከመ ብእሲት ትቴክዝ ሶበ እል
ጸቀት ለወሊድ ።

፳፩ ለመውለድ የቀረበች ሴት እንድታዝን።
እስመ በጽሐ ጊዜሃ ።
የምትወልድበት ጊዜ ደርሷልና ።
ወእምከመ ወለደት ዕጓላ ኢትዜክሮ እንከ ለሕማማ
በእንተ ፍሥሓሃ።

ልጁዋን ከወለደች በኋላም ደስ ስላላት መከራ
ዋን እንዳታስበው ።
እስመ ወለደት ብእሴ ውስተ ዓለም ።
በዚህ ዓለም ወንድ ልጅ ወልዳለችና ።

፳፪ ወከማሁ አንትሙኒ ትቴክዙ ይእዜ ።
፳፪ እርሷ እንዳዘነች እናንተም ታዝናላችሁ።
ወባሕቱ ካዕበ እሬእየክሙ ወይትፌሣሕከሙ ልብ
ክሙ ።
ነገር ግን እርሷን ደስ እንዳላት እናንተም ደስ
ይላችኋል አንድም በከመ ብእሲት ብለህ መልስ።
ልወለድላቸው የቀረብኩ ነቢያት አምስት ሽህ፡
ካምስት መቶ ዘመን ያዝኑ እንደነበረ ። እስመ
በጽሐ ጊዜሃ እኔ የምወለድበት ዘመን ቀርቧልና።
ወእመከመ ወለደት ። ኑኔ ከተወለኩላቸው በኋላ
ግን አምስት ሽህ ካምስት መቶ ዘመን የነበረውን
መከራ እንዳያስቡት ። በእንተ ፍሥሐሃ ደስ ስላ
ላቸው ። እስመ ወለደት እኔ ተወልጄላቸዋለሁና።
ከማሁ አንትሙኒ። እኒያ ያዝኑ እንደነበረ እናን
ተም ታዝናላችሁ ወባሕቱ ። እኒያን ደስ እንዳላቸው
እናንተንም ደስ ይላችኋል ወፍሥሐክሙኒ አልቦ
ዘየሐይደክሙ ።
ከደስታችሁ ከኔ አንድነት የሚለያችሁ የለም ።

፳፫ ወይእተ አሚረ አልቦ ዘትሰእሉኒ ኪያየ
ወኢምንተኒ ። ማቴ፡፯፡፯ ማር፡፲፩፡፳፬ ሉቃ፡ ፲፩፡፱
ዮሐ፡፲፬፡፲፪ ያዕ፡ ፩፡፭ ።

፳፫ ያን ጊዜ እኔን የምትለምኑኝ ምንም ምን
የለም ።
አማን አማን እብለክሙ ከመ እመ ሰአልክምዎ
ለአብ በስምየ ኵሎ ይሁበክሙ ።
በቅንው ወልድክ በስቁል ወልድክ እያላችሁ አብን
ብትለምኑት የለመናችሁትን ሁሉ እንዲያደርግላ
ችሁ በውነት እነግራችኋለሁ ።

፳፬ ወእስከ ይእዜ ኢሰአልክምዎ ወኢምን
ተኒ በስምየ ።
፳፬ ነገር ግን እስካሁን ምንም ምን በስሜ
አላመናችሁትም ።
ሰአሉ ወትነሥኡ ።
ለምኑ ታገኛላችሁ ።
ከመ ፍጹመ ይኩን ፍሥሐክሙ ።
ፈጽሞ ደስ ይላችሁ ዘንድ ።

ዘከመ ተሰናአል ኢየሱስ እም አርድዕት ።

፳፭ ወይእዜሰ በምሳሌ ነገርኩክሙ
፳፭ የአብን ነገር ገልጬ ነገርኳችሁ።
ወባሕቱ ይበጽሕ ጊዜሁ አመ ኢይነግረክሙ በምሳሌ።

ነገር ግን ገልጬ የማልነግራችሁ ጊዜ ደርሷል ፡ አላ ከሡተ እየድዓክሙ በእንተ አብ ።
የአብን ነገር በልቦናችሁ እስልባችኋለሁ እቀርጽ ባችኋለሁ እንጂ ። እንዲህስ እንዳይሆን ።
ወይእዜሰ ገሃደ ተናገርከነ ወአልቦ ዘመሰልከ ብሎ ያመጣዋል ወይእዜሰ በምሳሌ ነገርኩክሙ ብለህ መልስ ዛሬ የአብን ነገር ሰውሬ ነገርኳችሁ ። ወባ ሕቱ ግን ሰውሬ የማልነግራችሁ ጊዜ ደርሷል ፡ አላ እየ ድዓክሙ ከሡተ ፡ ገልጬ እነግራችኋለሁ እንጂ ።

፳፮ ወይእተ አሚረ ትስእሉ በስምየ ።
፳፮ ያን ጊዜ በቅንው ወልድከ በዕቁል ወል ድከ ብላችሁ ትለምናላችሁ ።
ወኢይብለክሙ ከመ አነ ዘእስእሎ ለአብ በእንቲ አክሙ ።
ለናንተ አብን እንዳለምነው አልነግራችሁም ።

፳፯ ወአኮ ዘእስእሎ ለአብ በእንቲአክሙ ።
፳፯ ስለናንተ አብን አለምነውም ።
እስመ ለሊሁ አብ ያፈቅረክሙ ።
እርሱ አብ ይወዳችኋልና ።
እስመ አንትሙ አፍቅርክሙኒ ወአመንክሙኒ ብየ ከመ እምኀበ እግዚአብሔር ወፃእኩ ።
እናንት ወዳችሁኛልና አምናችሁብኛልምና እኔ ከእ ግዚአብሔር እንደ ወጣሁ ።

፳፰ ወመጻእኩ ውስተ ዓለም ።
፳፰ ከእግዚአብሔር አብ አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእምባሕርይ ተወልጄ ወደዚህ ዓለም ፡ መጣሁ ።
ወካዕበ እኀድጎ ለዓለም ወአሐውር ኀበ አብ ዳግመኛ ሰውን ተለይቼው ወደ አብ እሄዳለሁ ፡ ፀሞት መለየቱን በረድኤት ለመለየቱ ካዕበ አለ ። አን ድም በዕርገት መለየቱን በሞት ለመለየቱ ካዕበ አለ ።

፳፱ ወይቤልዎ አርዳኢሁ ይእዜሰ ገሃደ ተና ገርከነ ።

፳፱ ደቀ መዛሙርቱም ዛሬ ግን ገልጸህ ነገርከን ።
ወአልቦ ዘመሰልከ ወኢምንተኒ ።
ምንም ምን ስውረህ የነገርከን ነገር የለም ።

፴ ወይእዜሰ አእመርነ ከመ ኵሎ ተአምር አንተ ።

፴ ዛሬ ግን ሁሉን እንድታውቅ ዐወቅን ።
ወኢትፈቅድ ይንግርከ መኑሂ ።
ማንም ማን ሊነግርህ አትሻም አሉት ።
ወበእንተ ዝንቱ ነአምር ከመ እምኀበ እግዚአብ ሔር ወፃእከ ።
ከእግዚአብሔር አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእ ምባሕርይ እንደተወለድህ በዚህ እናውቃለን ።

፴፩ ወአውሥአ ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ይእዜሰኬ አእምሩ ወእመኑ ።

፴፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም መለሰላቸው አላቸውም አሁን ዕወቁ እመኑ ።

፴፪ ናሁ ከመ ይበጽሕ ጊዜሁ ።
፴፪ እነሆ ጊዜው እንደደረሰ ።
ወበጺሖሂ ከመ ተዘረውከሙ ትዘረው ለለ፩ዱ ፩ዱ ውስተ መካኑ ።
በደረሰም ጊዜ ሁላችሁ እያንዳንዳችሁ እንድት በተኑ ዕወቁ አላቸው ።
ወተኃድጉኒ ባሕቲትየ ።
ብቻየን ትተውኛላችሁ ።
ወባሕቱ ኢኮንኩ አነ ባሕቲትየ ።
እኔ ግን ብቻዬን አይደለሁም ።
እስመ አብ ምስሌየ ውእቱ ።
አብ በኔ ህልውና ነውና ።

፴፫ ወዝንቱ ውእቱ ዘነገርኩክሙ ከመ ብየ ሰላመ ትርከቡ ።

፴፫ በኔ አንድነትን ታገኙ ዘንድ የነገርኳችሁ ይህ ነው ።
ወበዓለምሰ ሕማመ ትረክቡ ።
በዓለም ግን መከራን ትቀበላላችሁ ።
ወባሕቱ ጽንኡ እስመ አነ ሞዕክዎ ለዓለም ።
ነገር ግን እኔ ድል ነሥቻለሁና ድል ንሡ ። ድል ነሥቶ ድል ንሡ አለ ድል የተነሣን ጾር ሴት ሳት ቀር ትማርከዋለችና ።

ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ ።

ምዕራፍ ፲፯ ።

፩ ወዘንተ ነገረ ተናጊሮ እግዚእ ኢየሱስ አንሥአ አዕይንቲሁ ውስተ ሰማይ ።

፩ ይህን ተናግሮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ዓይኑን ወደ ሰማይ አቀና ። ሐተታ እስካሁን ከደቀ መዛሙርቱ ጋራ ይነጋገር ነበር እንግዲህ ወዲህ ግን ከአብ ጋራ ለመነጋገር ።
ወይቤ አባ በጽሐ ጊዜሁ ከመ ትስብሖ ለወልድከ።
አባቴ ሆይ ልጅህን ትገልጸው ዘንድ ጊዜው ደረሰ ።
ወከመ ወልድከኒ ይሰብሕከ ።
ልጅህም ደግሞ ያመሰግንህ ዘንድ ።

፪ በከመ አኰነንኮ ላዕለ ኵሉ ዘሥጋ ወነ ፍስ ከመ የሀቦሙ ሕይወተ ዘለዓለም ለኵሉ ወሀ ብካሁ ። ማቴ. ፳፰፥ ፲፰ ።

፪ በሀብት ሰበህ በረድኤት አቅርበህ ለሰጠ ኸው ለምአመናን የዘለዓለም ሕይውት የሚገኝበ ትን ይሰጣቸው ዘንድ ። የዘለዓለም ሕይወት

የሚገኝበትን ሃይማኖት ያስተምራቸው ዘንድ በሥጋዊ በነፍሳዊ ሁሉ ላይ እንዳሠለጠንከው መጠን ልጅህም ይገልጽልህ ዘንድ ።

፫ ወዛቲ ይእቲ ሕይወት ዘለዓለም ከመ ያእ ምሩ ኪያከ ለኪ ዘበአማን አምላከ ጽድቅ ባሕ ቲትከ ።

፫ የዘለዓለም ሕይወት የሚገኝበት ሃይማኖትም አንተ ብቻ የባሕርይ አምላክ እንደሆንክ ።
ወዘፈነውኮ ኢየሱስ ክርስቶስ ወልድከ ።
የላከኸው ኢየሱስ ክርስቶስም የባሕርይ አምላክ እንደሆነ ያውቁ ዘንድ ነው ። እንዲያውቁ መሆን ነው ቢያውቁ በጐ ነው ቢያውቁ የዘለዓሰም ሕይወት የሚገኝባት ሃይማኖት ይህች ናት ።

፬ አንሰ ሰባሕኩከ በዲበ ምድር ፈጺምየ ግብረ ዘወሀብከኒ ከመ እግበር ።

፬ እሠራው ዘንድ ገንዘብ ያደረግህልኝን ሥራ ሥርቼ ገለጽሁህ ።

፭ ወይእዜኒ አንተ አባ ሰብሐኒ በስብሐትየ ዘሀሎ ኀቤከ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ።

፭ አባት ሆይ አሁንም አንተ ዓለም ሳይፈጠር ካንተ ዘንድ ባለ ጌትነቴ ግለጸኝ ፡ አንድም በስብሐቲከ ዘሀሎ ኀቤየ ይላል ዓለም ሳይፈጠር ከኔ ዘንድ ባለ ጌትነትህ ግለጸኝ ።

፮ ወነገርኩ ሰመከ ለሰብእ ለእለ ወሀብከኒ እምዓለም ።

፮ በሀብት ሰበህ በረድኤት አቅርበህ ለሰጠኸኝ ለምእመናን አባትነትህን ነገርኳቸው ።
እሰመ ዚአከ እሙንቱ ።
ያንተ ገንዘቦች ናቸውና ።
ወሊተ ወሀብከኒዮሙ ።
ለኔም ሰጠህቸው ።
ወዓቀቡ ቃለከ ።
ሕግህንም ጠበቁ ።

፯ ወይእዜኒ አእመሩ ከመ ኵሉ ዘወሀብከኒ እምኀቤከ ውእቱ ።

፯ የሰጠኸኝ ሁሉ ካንተ እንደሆነ የነገርኳቸው ሁሉ ካንተ እንደተገኘ ዐውቀዋልና ።
እሰመ ወሀብክዎሙ ቃለ ዘወሀብከኒ ።
የሰጠኸኝን ነገር ሰጥቻቸዋለሁና ማለት የነገርከኝን አስተምሬያቸዋለሁና ።

፰ ወእሙንቱሂ ነሥእዎ አማን አእመሩ ከመ እምኀቤከ ወፃእኩ ወአምኑ ከመ አንተ ፈነውከኒ ።

፰ እርሳቸውም የነገርኳቸውን ትምህርት ተቀብለው ከአንተ አካል ዘእምአካል ባሕርይ ዘእምባሕርይ ተወልጄ እንደመጣሁ ባንተ ፈቃድ ሰው እንደሆንሁ አውቀው አምነዋል ።

፱ ወአንሰ በእንቲአሆሙ እስእል ።

፱ እኔ ሰለርሳቸው እለምንሃለሁ ።
ወአኮ በእንተ ዓለም ዘእስእለከ አላ በእንተ እለ ወሀብከኒ ።
የምለምንህ በሀብት ሰበህ በረድኤት አቅርበህ ለሰጠኸኝ ለነዚህ ነው እንጂ ለሌላው ያይደል ፤
እስመ እሊአከ እሙንቱ ።
ያንተ ገንዘቦች ናቸውና ።

፲ ወኵሉ ዘዚአየ ዚአከ ውእቱ ወዘዚአከኒ ዚአየ ውእቱ ።

፲ የኔ ገንዘብ ሐዋርያት ፡ ያንተ ገንዘብ ነቢያት ናቸው ፡ አንድም የኔ ገንዘብ ሐዋርያት ያንተ ገንዘቦችህ ናቸው ወዘዚአከኒ ዚአየ ውእቱ ።
ያንተ ገንዘብ ነቢያትም የኔ ገንዘቦች ናቸው ።
ወተሰባሕኩ ቦሙ ።
በርሳቸው ተገለጽኩ በርሳቸው ሥጋ ከበርኩ ።

፲፩ ወኢይሄሉ እንከ ውስተ ዓለም

፲፩ ከእንግዲህ ወዲህ በዓለም አልኖርም ።
ወእሙንቱሰ ውስተ ዓለም ይሄልዉ ።
እርሳቸው ግን በዓለም ይኖራሉ ።
ወአንሰ ኀቤከ እመጽእ ፡
እኔ ግን ወዳንተ እመጣለሁ ፡
አባ ቅዱስ ዕቀቦሙ በሰምከ ለእለ ወሀብከኒ ፤
ልዩ አባት ፡ ክቡር አባት ፡ አባት የሌለህ አባት በሀብት ስብህ በረድኤት አቅርበህ የሰጠኸኝን ምእመናንን በስምህ ጠብቃቸው ።
ከመ ይኩኑ ፩ደ ብነ ከማነ ከመ ፩ዱ ንሕነ ።
እኛ በባሕርይ አንድ እንደሆነ እርሳቸውም በጸጋ አንድ ይሆኑ ዘንድ ፡

፲፪ አመሰ ሀሎኩ አነ ውስተ ዓሰም ዓቀ ብክዎሙ በሰምከ ለእለ ወሀብከኒ ፡ ዮሐ፡ ፲፰፡፱ መዝ፡ ፶፲፡፲ ።

፲፪ በሀብት ስበህ በረድኤት አቅርበህ የሰጠኸኝን በዚህ ዓለም ሳለሁ በስምህ ጠበቅኋቸው ።
ናሁ ዓቀብክዎሙ ።
አጽንቼ ጠበቅኋቸው ።
ወኢትኃጕለ ፩ሂ እምኔሆሙ ዘእንበለ ወልደ ኃጕል ።
ጥፋት ከሚገባው ከይሁዳ በቀር ከእርሳቸው አንድ ስንኳ የጠፋ የለም ።
ከመ ይትፈጸም ቃለ መጽሐፍ ።
መጽሐፍ ወይጥፋዕ እምድር ዝክሩ ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።

፲፫ ወይእዜሰ ባሕቱ እመጽእ ኀቤከ ።
፲፫ ዛሬ ግን ወዳንተ እመጣለሁ ።
ወለእሉሰ አኃድጎሙ ውስተ ዓለም ።
እርሳቸውን ግን በዓለም እተዋቸዋለሁ ።
ወዘንተ እነግር ውስተ ዓለም
ይኸንንም በዓለም እናገራለሁ
ከመ ይኩን ፍሥሐየ ፍጹመ በላዕሌሆሙ
ደስታዬ በርሳቸው ፍጹም ይሆን ዘንድ ማለት ፈጽሞ
ደስ ይላቸው ዘንድ ።

፲፬ ወአንሰ ፈጺምየ ወሀብክዎሙ ቃለከ ።
፲፬ ሕግህን ፈጽሜ ነገርኳቸው ።
ወዓለምሰ ጸልአሙ ።
ሰው ግን ይጸላቸዋል ።
እስመ ኢኮኑ እሙንቱ እምዓለም ።
እርሳቸው ከዓለም አይደሉምና
በከመ ኢኮንኩ አነ እምዓለም
እኔ ከዓለም ወገን እንዳይደለሁ ከዓለም እንዳልተ
ገኘሁ ።

፲፭ ኢኮ ዘእስእለከ ከመ ትንሥኦሙ እምዓለም።
፲፭ ዛሬስ ከዚህ አኦሮን ሞት ይካስስብናል
እንዳይሉት የምለምንህ በሞት ትወስዳቸው ዘንድ አይ
ደለም ዘእንበለ ዳዕሙ ከመ ትዕቀቦሙ እምእኩይ ።
ከሞት ትጠብቃቸው ዘንድ ነው እንጂ አብ የማያ
ውቅ ሁኖ አይደለም በአብ ለሐዋርያት ለመንገር
ነው ። ዝንቱ ውእቱ ወልድየ ባለ ጊዜ ወልድ ልጅነቱን
የማያውቅ ሁኖ እንዳይደለ በወልድ ለዮሐንስ ለመ
ንገር እንደሆን ።

፲፮ እስመ እሙንቱ ኢኮኑ እምዓለም ።
፲፮ እሳቸው ከዓለም ወገን አይደሉምና ።
በከመ ኢኮንኩ አነ እምዓለም
እኔ ከዓለም እንዳልተገኘሁ ።

፲፯ ቀድሶሙ በጽድቅከ ።
፲፯ በጽኑ ቀጠሮህ አጽናቸው ።
እስመ ጽድቅ ውእቱ ቃልከ ።
ቀጠሮህ ጽኑ ነውና ። አንድም በአካላዊ ቃልህ አከ
ብራቸው ቃልህ አካላዊ ነውና ።

፲፰ በከመ አንተ ፈነውከኒ ውስተ ዓለም ኪያየ።
፲፰ አንተ እኔን ወደዓለም እንደ ላከኸኝ ።
ከማሁ አነኒ ፈነውክዎሙ ውስተ ዓለም ።
እኔም ወደዓለም ላክኋቸው ።

፲፱ ወበእንቲአሆሙ አነ እቄድስ ርእስየ ።
፲፱ ስለርሳቸው ተሰቅዬ ነፍሴን ከሥጋዬ እለያ
ለሁ ። አንድም ስለርሳቸው ራሴን እከብራለሁ።
ከመ ይኩኑ እሙንቱኒ ቅዱሳነ በጽድቅ ።
በውነት ንጹዳን ከቡራን ይሆኑ ዘንድ ።

፳ ወአኮ በእንተ እሉ ባሕቲቶሙ ዘእስእለከ።
፳ የምለምንህ ስለነሱ ብቻ አይደለም ።
አላ በእንተሂ እለ የአምኑ ብየ በቃሎሙ ።
ከርሳቸው ተምረው ስለሚያምኑ እስከ ምጽአት
ድረስ ስለሚነሡ ምእመናንም ነው እንጂ ።

፳፩ ከመ ይኩኑ አሐደ ኵሎሙ ከማነ ከመ
፩ ንሕነ ።

፳፩ ሁሉም አንድ ይሆኑ ዘንድ እኛ በባሕ
ርይ አንድ እንደሆነ
በከመ አንተ አብ ብየ ።
አባት ሆይ አንተ በኔ ህልው እንደሆንከ ።
ወአነሂ ብከ ።
እኔም ባንተ ህልው እንደሆንኩ ።
ከመ ይኩኑ እሙንቱሂ ብነ ከማነ ከመ ፩ ንሕነ ።
እኛ በባሕርይ አንድ እንደሆን እርሳቸው በጸጋ አንድ
ይሆኑ ዘንድ ።
ከመ ይእመን ዓለም ከመ አንተ ፈነውከኒ ።
ባንተ ፈቃድ ሰው እንደሆንኩ ዓለም ያምንዘንድ ።
፳፪ ወአነሂ ወሀብክዎሙ ቃለከ ዘወሀብከኒ ።

፳፪ እኔም የሰጠኸኝን ሰጠኋቸው ማለት
የነገርከኝን ነገርኳቸው ።
ከመ ይኩኑ አሐደ ከማነ በከመ አሐዱ ንሕነ ።
እኛ በባሕርይ አንድ እንደሆን በጸጋ አንድ ይሆኑ
ዘንድ ።

፳፫ ወአነሂ ቦሙ ።
፳፫ እኔም አድሬባቸው እኖራለሁ ።
ወአንተሂ ብየ ።
አንተም በኔ ህልው ሁነህ እንድትኖር ።
ከመ እሙንቱሂ ይኩኑ ፍጹማነ በአሐዱ ።
በአሐዱ ያለውን ፍቅር ብሎታል ሊቁ በፍቅር
አንድ ይሆኑ ዘንድ ።
ከመ ይእመን ዓለም ከመ አንተ ፈነውከኒ ።
አንተ እንደ ላከኸኝ ባንተ ፈቃድ ሰው እንደሆንኩ
ዓለም ያውቅ ዘንድ ።
ወአፍቀርከዎሙ አነ በከመ አንተ ኪያየ አፍቀርከኒ።
እኔን እንደወደድኸኝ ወደድኋቸው ሙት ተሰቀል
እንዳልኸኝ ሙቱ ተሰቀሉ አልኳቸው ።

፳፬ አባ እለሰ ወሀብከኒ እፈቅድ ። ከመ የሀ
ልዉ ኀበ ሀሎኩ አነ ምስሌየ ከመ ይርአዩ ስብ
ሐተ ዘወሀብከኒ ።

፳፬ አባት ሆይ የሰጠኸኝ ምእመናን የሰጠ
ኸኝን ክብር ያዩ ዘንድ ከኔ ጋራ እኔ ካለሁበት ሊኖሩ
እወዳለሁ ። አንድም የሰጠኸኝን ክብር ይወርሱ
ዘንድ ።
እስመ አንተ አፍቀርከኒ እምቅድመ ይትፈጠር ዓለም ።
ዓለም ሳይፈጠር ወደኸኛልና ።

፳፭ አባ ጻድቅ ወዓለምስ ኢያእመረከ ።
፳፭ የባሕርይ አምላክ አባቴ ሰው አላወቀህም
ወእንሰ ባሕቱ አእመርኩከ ።
እኔ ግን አውቄሃለሁ ።
ወእሙንቱስ አእመሩከ ከመ አንተ ፈነውከኒ ።
እርሳቸውም ባንተ ፈቃድ ሰው እንደሆንኩ
ዐውቀዋል ።

፳፮ ወነገርክዎሙ ስመከ ።
፳፮ አባትነትኽን ነገርኳቸው ስምህን አስታ
ወቅኋቸው ።
ወዓዲ እነግሮሙ ።
ዳግመኛም እነግራቸዋለሁ ።
ከመ የሃሉ ኀቤሆሙ ፍቅር ዘአፍቀርከኒ ።
አንተ ያፈቀርከኝ ፍቅር በርሳቸው ጸንቶ ይኖር
ዘንድ ።
ወአነሂ እሄሉ ቦሙ ።
እኔም አድሬባቸው እኖራለሁ ።

ዘከመ ጸለየ ኢየሱስ በጌቴሴማኒ ።

ምዕራፍ ፲፰ ።

፩ ወዘንተ ብሂሎ ወፅአ እግዚእ ኢየሱስ ምስለ
አርዳኢሁ ማዕዶተ ቄድሮስ ፈለገ አርዝ ፪ነገ. ፲፭
፳፫ ፤ ማቴ. ፳፮ ፤ ማቴ ፳፮ ፴፮ ፤ ማር. ፲፬ ፥ ፴፪ ።
ሉቃ. ፳፪ ፥ ፴፱ ።

፩ ማዕዶትና ፈለግ ቄድሮስና አርዝ አንድ
ወገን ነው ። ይህን ተናግሮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስ
ቶስ ወንዙን ተሻግሮ ያለውን ዛፍ አልፎ ወዳሰው
ዱር ገባ ። አንድም ዘይቤውን ለማውጣት ዛፉን
አልፎ ያለውን ወንዝ ተሻግሮ ያለውን ዛፍ አልፎ
ወዳለው ዱር ገባ ። ማቴዎስ ጌቴሴማኒ ፣ ሉቃስ
ደብረ ዘይት ይላል ፣ ከዚህ እንዲህ አለ እንደምን
ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ። አንድ ወገን ነው
እንዳጠናቅር ገብርኤል እንደ ጐንደሮች ጊዮርጊስ
አንድም እንደሉቃስ ዓሥራ አንዱን ይዞ ደብረ
ዘይት ይገባል ስምንቱን በደብረ ዘይት ትቶ እንደ
ማቴዎስ ሦስቱን ባለሟሎቹን አስከትሎ ጌቴሴማኒ
ገብቷል ። መጠነ ሙጋረ እብን ይላል ደንጊያ ወር
ውሮ እስከ ሚያርፍበት ሄዶ ግምባሩን ምድር አስ
ነክቶ ሰግዶ ጸሎቱን ፈጽሞ ተመልሶ ስምንቱን
ከደብረ ዘይት ሦስቱን ባለሟሎቹን ከጌቴሴማኒ ይዞ
እንደ ዮሐንስ ከዚህ ገብቷል ።
ወቦ ህየ ዐጸደ ሐምል ፣
ከዚያ ያታክልት ቦታ አለ ።
ወቦአ እግዚእ ኢየሱስ ውስቴታ ምስለ አርዳኢሁ ።
ጌታም ደቀ መዛሙርቱን አስከትሎ ከዚያ ገባ ።

፪ ወየአምሮ ይሁዳ ዘያገብኦ ለውእቱ መካን ።
፪ የሚያሲዘው ይሁዳ ያንቦታ ያውቀውነበር ።
እስመ ብዙኃ ጊዜ ይትጋባእ እግዚእ ኢየሱስ ህየ
ምስለ አርዳኢሁ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዚያ ሥፍራ ከደቀ መዛ
ሙርቱ ጋራ ብዙ ጊዜ ቆይታ ያደርግ ነበርና ።

ዘከመ አግብአ ይሁዳ ለኢየሱስ ወዘከመ አኀዝዎ
ለኢየሱስ ።

፫ ወነሥኦሙ ይሁዳ ለሠገራት ሰጲራ እምኀበ
ሊቃነ ካህናት ወፈሪሳውያን ፣ ማቴ. ፳፮ ፥ ፵፯ ። ማር.
፲፬ ፥ ፵፫ ሉቃ. ፳፪ ፥ ፵፯ ።
፫ ይሁዳም ከካህናት አለቆችና ከፈሪሳውያን ።
ሰጲራ የሚባል ጭፍራ ተቀብሎ ።
ወነሥአ ረድኤተ ወዓልያኒሆሙ
ብላቴኖቻቸውን ረዳት እኩሎ መጣ ሐተታ እም
ስት ገበያ ሰው ይከተለዋል አግባ መልስ ብሎ ቢጣ
ላንስ ብለው ከጲላጦስ ያመጣሉ ፣ እሱ ከርሳቸው
ተቀብሎ ይዞ ይመጣል ።
ወሖረ ህየ በመሐትው ጽጕ ወፖናት ።
ፋኖስ የጭራሮ መብራት አስይዞ ፣ አንድም ፋኖስ የሚ
ባል ማብሪያ ይዘው ነፋስ የማያስገባ ብርሃን የማይ
ይከለክል ነው ይህን ሁሉ ምን ያሻቸዋል ምልአተ
ወርህ አይደለምን ቢሉ የጨረቃ ብርሃን እንደ ፀሐይ
ብርሃን መልክ ለይቶ አያሳውቅምና ።
አንድም ያለንበት ቦታ ዱር ነው ብርሃን አያስገባምና
ይህ ሁሉ አይደለም መዓልት ብርሃኑዋን እንደ ነሳች
ሌሊትም ብርሃኑዋን ነስታ ነበርና ።
ወበንዋየ ሐቅል ። ሾተል ጐመድ ይዞ ።

፬ ወአእሚሮ እግዚእ ኢየሱስ ኵሎ ዘይበጽሖ
ላዕሌሁ ወፅአ አፍአ ኀቤሆሙ ።

፬ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም የሚመጣበትን
ሁሉ ማለት ሊይዙት እንደመጡ ዐውቆ ካለበት
ቦታ እርሳቸው ወዳሉበት ወጣ ። ሳያውቅ በድንገት
ያዘነው እንዳይሉ እንዳይቀርለት ያውቃልና እንዳ
ልፈራ ለማጠየቅ ። አንድም አፍቅሮ ጸላእት እሾህ
እንዳያወጋቸው ዕንቅፋት እንዳይመታቸው ። አን
ድም ኀድግዎሙ ለእሉ ይሑሩ ለማለት ።
ወይቤሎሙ መነ ተኃሥሡ ።
ማን ትሻላችሁ አላቸው ።
፭ ወአውሥኡ ፣
፭ መለሱ ።
ወይቤሉ ኢየሱስሃ ናዝራዊ ።
የናዝሬቱ ኢየሱስን ነው አሉት
ወይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ አነ ውእቱ ።
ኢየሱስም እኔ ነኝ አላቸው ።
ወሀሎ ይሁዳኒ ዘያገብኦ ይቀውም ምስሌሆሙ ።
ያስያዘው ይሁዳም ከርሳቸው ጋራ ቆሞ ነበር ።

፮ ወሶበ ይቤሎሙ እግዚእ ኢየሱስ ገብኡ ድኅሬሆሙ ወወድቁ ዲበ ምድር ።

፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እኔ ነኝ ባላቸው ጊዜም ወደኋላቸው ተመልሰው ወደቁ ። ወደ ኋላ የወደቁት ድቀት ጽኑ ነው ጽኑ ድቀት እንዳለባቸው ለማጠየቅ ። አንድም ጥፋታቸው በኋላ ዘመን ነውና በሥጋቸው ባርባ ዘመን በጥጦስ በነፍሳቸው በገሃ ነም ። አንድም ወወድቁ ታሕተ ጽላሎቱ ያለው ትን ቢት ሊፈጸም ።

፯ ወእምዝ ካዕበ ተስአሎሙ ወይቤሎሙ መነ ተኀሥሡ ።

፯ ደግሞም ጠየቃቸው እንዲህ ሲል ማን ትሻ ላችሁ ።
ወይቤልዎ ኢየሱስሃ ናዝራዌ ።
የናዝሬቱን ኢየሱስን ነው አሉት ።
፰ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።

፰ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎሙ አኮኑ እቤለክሙ አነ ውእቱ ።
እኔ ነኝ አላልኋችሁምን ።
ወእመሰ ኪያየ ተኀሥሡ ኅድግዎሙ ለእሉ ይሑሩ።
የምትሹ እኔን ከሆነስ እኒህን ተዋቸውና ይሂዱ ።

፱ ከመ ይብጻሕ ቃል ዘይቤ እለሰ ወሀብከኒ ኢተኃጕለ ወኢአሐዱሂ እምኔሆሙ ። ዮሐ. ፲፯፡፲፪።

፱ ከሰጠኸኝ አንዱ ስንኳ አልጠፋም ያለው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።

፲ ወቦ መጥባሕት ለስምዖን ጴጥሮስ ።
፲ ለጴጥሮስ በጉን የበሉበት ሾተል ነበረው ።
ወመልሐ መጥባሕቶ ወዘበጦ ለገብረ ሊቀ ካህናት።
ሾተሉን መዞ የሊቀ ካህናቱን ባሪያ መታው ።
ወመተረ እዝኖ ዘየማን ።
ቀኝ ጆሮውን ቆረጠው ። ንዝብጦሙ ንዝብጦሙ ተባብለዋል በሉቃስ ። አብሮ መብላት አብሮ መጠ ጣት አብሮ ለመሞት እንጂ ነው ። እንበላቸው እን በላቸው ተባብለዋል ቅዱስ ጴጥሮስ ፈጣን ነውና ሾተሉን መዞ መታው ቀኝ ጆሮውን ቆረጠው ። ከመታው አንገቱን አይለውምን ቢሉ የካህን እጅ አያቀናምና ሳንገቱ ያለው ለጆሮው ሆነ አንድም አንገቱን መቶት ቢሆን ይሞታል የጌታም ሞት በርትዕ ነው በተባለ ነበርና ጆሮውንሳ ቢሉ ወእሕ የዎ ይላል ቀጥሎለታል ። ስለምን በጆሮው ምትረትን አዘዘባት ቢሉ ትንቢቱ ምሳሌው ሊፈጸም ትንቢት ወይእቲ እዝን እንተ ኢትሰምዖ ለውእቱ ነቢይ ለት ትቀረጽ ተብሎ ተነግሯል ። ምሳሌም ወለእመ አጥረይከ ገብረ ዕብራዌ ስድስተ ዓመተ ቅንየ ወበ ሳብእ ዓም አግዕዞ በከንቱ ትላለች አሪት ፡ እርሱ ግን የመቤቴ እንጀራዋ ወጡ ጣፍጦኛል የጌታዬ ባሕርይ ተስማምቶኛል ነፃ መውጣቱ ይቅርብኝ ስገዛ እኖራለሁ ቢል ከቤተ መቅደስ ከመድረኩ አስ ተኝቶ ጆሮውን ተልትሎ እፍንጫውኒ ሸንቁሮ እስከ ዕለተ ሞቱ ይግዛው ትላለች ። ጌታም በስድስተኛው ሺህ ከዲያብሎስ ተቀንዮ ነፃ ላወጣችሁ መጥቼ ነበር አይሆንም ካላችሁ በሥጋችሁ ቄሣር በነፍሳችሁ ዲያብሎስ ይሠልጥንባችሁ ለማለት ። ቀኝቱ መሆንዋ ግራይቱ አለመሆንዋ ስለምን ነው ቢሉ ከነገደ ይሁዳ የተወለደ ቀኝ ቀኝ አካሉን ተቀብቶ መንግሥትን ከነገደ ሌዊ የተወለደ ቀኝ ቀኝ አካሉን ተቀብቶ ክህነትን እጅ ያደርግ ነበር መንግሥት ንም ክህነትንም እንዳሳለፈባቸው ለማጠየቅ ።
ወስሙ ለውእቱ ገብር ማልኮስያም ባሪያ ማልኮስ ይባል ነበር ። እግዚእ ወገብር ማለት ነው ፣

፲፩ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ ለጴጥሮስ አግ ብእ ለመጥባሕትከ ውስተ ቤታ ።

፲፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ሾተልክን ወደአፎት ቀጣህን ወደ ትዕግሥት መልስ አለው።
ጽዋዓ ዘወሀበኒ አቡየ ኢየኃድግ ዘእንበለ እስተይ
አባቴ የሰጠኝን ጽዋ ሳልጠጣ አልተወውም ማለት ባባቴ ፈቃድ የሚሆነውን ሞት እሞታለሁ ።

ዘከመ ቆመ ኢየሱስ ማእከለ ዐውድ ።

፲፪ ወአኀዝዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ሰገራተ ስጺራ።
፲፪ ስጺራ የሚባል ጭፍራ ።
ወሊቀ ዓሠርቱ ምእት ።
የመቶ አዝማች ።
ወወዓሊሆሙ ለአይሁድ ።
የአይሁድም ብላቴኖች ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ይዘው ።
ወሐመይዎ ።   አሰሩት ።

፲፫ ወወሰድዎ ኀበ ሐና ቀዲሙ ሉቃ. ፫፡ ፪።
፲፫ አስቀድሞ ከሐና ዘንድ ወሰዱት ።
እስመ ሐሙሁ ውእቱ ለቀያፋ ሊቀ ካህናት ዘዕብሬቱ ይእቲ ዓመት ።
ሹመቱ በዚያ ወራት ለሚሆን ለሊቀ ካህናቱ ለቀ ያፋ አማች ነበርና ። ማቴ አስቀድሞ ከሐና ወሰዱት ይላል ። ከዚህ እንዲህ አለ እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም አስቀድሞ ከቀያፋ ወስደውታል ምንስ እኔ ሹም ብሆን ሽማግሌ ሳለ ክርሉ ውሰዱት ብሏቸዋል ከሐና ወስደውታል የኋለኛውን ዮሐንስ የፊተኛውን ማቴዎስ ይጽፋሉ ። አንድም እንደ ማቴዎስ ነው አስቀድሞ ከሐና ወስደውታል ምንስ እኔ ሽማግሌ ብሆን ሹሙ ሳለ ክርሉ ዘንድ ውሰዱት ብሏቸው ከቀያፋ ወስደውታል የፊተኛውን እንደ ዮሐንስ የኋለኛውን እንደ ማቴዎስ ተናገሩ ። ነገር እንደ ዮሐንስ ነው ። አንድም እንደ ጎንባሲት

ያለች ደጅ አለቻቸው አንድ ጊዜ ባንዱ ሲያገቡት አንድ ጊዜ ባንዱ ሲያወጡት ሲያመላልሱት አድረዋል አንዱ ላንዱ ቅድሙ ነውና ቅድመ ኀበ ቀያፋ ቅድመ ኀበ ሐና አለ ።

፲፬ ወቀያፋሰ ውእቱ ዘአምከሮሙ ለአይሁድ ወይቤሎሙ ይኄይሰነ ንቅትል አሐደ ብእሴ እምይትኀጐል ኵሉ ሕዝብ ዮሐ ፡ ፲፩፡፵፱ ።

፲፬ ያተርካል ቀያፋም ሰው ሁሉ በርሱ አምኖ ሲጎዳ አንድ ሰው ብንገድል ይሻለናል ብሎ አይሁድን የመከራቸው ነው ።

በእንተ ክህደተ ጴጥሮስ ።

፲፭ ወተለውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እምርኁቅ ስምዖን ጴጥሮስ ወካልዕኒ ረድእ ።

፲፭ ዮሐንስና ስምዖን ጴጥሮስ ጌታን ርቀው ተከተሉት ።
ወውእቱስ ረድእ ዘልሙድ በኀበ ሊቀ ካህናት ።
ያም ደቀ መዝሙር ከሊቀ ካህናቱ የለመደ ነው ፤ ባማ ቀረጥ ምክንያት ፡ አንድም ከቤተ ክህነት ከቤተ መንግሥት ይወለዳልና ።
ወቦአ ምስለ እግዚእ ኢየሱስ ውስተ ዐጸደ ሊቀ ካህናት ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ተከትሎ ከሊቀ ካህናቱ ቦታ ገባ ።

፲፮ ወጴጥሮስሰ ቆመ አፍአ ኀበ ኆኅት ። ማቴ፡ ፳፮፡፶፰ ማር፡ ፲፬፡፶፬ ሉቃ፡ ፳፪ ፶፭ ።

፲፮ ጴጥሮስ ግን ተከልክሎ እውጭ ቁሞ ነበር። ወወፅአ ዝኩ ረድዕ ዘልሙድ በኀበ ሊቀ ካህናት ወተናገራ ለአፃዊት ወአብኦ ለስምዖን ጴጥሮስ ፤ ዮሐንስ ወጥቶ ከበረኛዪቱ ተነጋግሮ ጴጥሮስን አስገባው ጠባቂው ወንድ አይደለምን ቢሉ ከጭፍራው ድፋት ያለው ነውና ጩኸት ቢሰማ አስጠብቋት ሂዷል ይህች ልጅ ልጁም እንደሆነች አልታወቀም ።

፲፯ ወትቤሎ ይእቲ ዓመት አፃዊት ለጴጥሮስ አንተኒ እምእርዳኢሁ ለውእቱ ብእሲ ኑንተ ።

፲፯ ያችም ብላቴና ጴጥሮስን አንተም ከዚያ ሰው ደቀ መዛሙርት ወገን ነህ አለችው ።
ወይቤላ ውእቱኒ ኢኮንኩ ።
እርሱም አይደለሁም አላት ።

፲፰ ወሀለዉ ያቀውሙ እግብርቲሆሙ ወወዓልያኒሆሙ ለአይሁድ ወይበቁጹ እፍሐመ ወይስሕኑ
፲፰ ብላቴኖቻቸው ተቀምጠው እሳት እየሞቁ ይሞቁ ነበር ። ወትቀውም ንግሥት በየማንክ እንዲል ።
እስመ ብዙኅ ቍሩ ለይእቲ ሌሊት ።

በዚያ ሌሊት ብርድ ጽንቶ ነበርና ፀአተ ክረምት ነውና። አንድም ወትከውን አሐቲ ዕለት ቍረ ወበረደ ያለው ሊፈጸም ብርድ ጸንቶ ነበር ።
ወይቀውም ጴጥሮስኒ ወይስሕን ምስሌሆሙ ።
ጴጥሮስም ከርሳቸው ጋራ ተቀምጦ ይሞቅ ነበር ።

ዘከመ ተስእልዎ አይሁድ ለኢየሱስ ።

፲፱ ወተስእሎ ሊቀ ካህናት ለእግዚእ ኢየሱስ በእንተ አርዳኢሁ ።

፲፱ ሊቀ ካህናቱ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ስለ ደቀ መዛሙርቱ ማለት ደቀ መዛሙርትህ ምን እያሉ ያስተምራሉ ።
ወበእንተ ትምህርቱ ።
አንተስ ምን ብለህ ታስተምራለህ ብሎ ጠየቀው አንድም ። ሐዋርያት ሰብዓ አርድዕት እያልክ መሾምህ በምን ነገር ነው ብሎ ጠየቀው ።

፳ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፳ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ አንሰ ክሡተ ተናገርኩ ውስተ ዓለም ።
እኔ በዚህ ዓለም ገልጬ አስተማርኩ ።
ወበኵሉ ጊዜ መሐርኩ በምኵራብ ወበቤተ መቅደስ ኀበ ይትጋብኡ ኵሎሙ አይሁድ ።
አይሁድ በሚሰበሰቡበት በምኵራብ በቤተ መቅደስ አስተማርኩ ።
ወአልቦ ዘተናገርኩ ጽሚተ ወኢምንተኒ ።
ምንም ምን ስውሬ የተናገርኩት የለም ።

፳፩ ለምንት እንከ ትሴአለኒ ሊተ ተሰአሎሙ ለእልክቱ እለ ሰምዑኒ ዘተናገርክዎሙ ።

፳፩ የነገርኳቸውን የሰሙትን እሊህን ጠይቃቸው እንጂ እኔን ምን ትጠያቀኛለህ ።
እስመ እሙንቱ የአምሩ ዘተናገርኩ አነ ።
እኔ የተናገርኩትን እርሳቸው ያውቃሉና ።

፳፪ ወዘንተ ብሂሎ ጸፍዖ መልታሕቶ ለእግዚእ ኢየሱስ እምእለ ይቀውሙ ወዓልት ።
፳፪ ይህን በተናገረ ጊዜ ይህን ከተናገረ በኋላ ከቆሙት ብላቴኖች አንዱ ጌታን በጥፊ መታው ፤ መጻጉዕ ነው ።
ወይቤሎ ከመዝኑ ትትዋሥእ ለሊቀ ካህናት ።
ለሊቀ ካህናቱ እንዲህ አኩል ትመልስለታለህን ብሎ ።

፳፫ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ማቴ. ፳፮ ፤ ፷፯ ። ማር. ፲፬ ፤ ፷፭ ። ሉቃ. ፳፪ ፷፫ ።

፳፫ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ እመሰ እኩየ ነበብኩ ስምዓ ኩን ላዕሌየ ። ክፉንስ ተናግሬ እንደሆነ መስክርብኝ ።

ወአስተዋድየኒ በእንተ እኩይ ።
ክፉ ስለተናገርኩ አሳጣኝ አጣላኝ አካሰኝ ።
ወእመሰ ሠናየ ነበብኩ ለምንት እንከ ትዘብጠኒ ።
በጐ ነገር ብናገር ግን ለምን ትመታኛለህ አለው ፣
ጌታ በትሩን ተሰቅቆት አይደለም ከዳኛ ፊት መማታት አይገባም ለማለት ሥርዓት ለማስተማር ነው እንጂ ምንም ቢሆን ነኝ ብሏልና ፣
አንድም ወይቤሎ እመሰ እኩየ ነበብኩ ብለህ መልስ ተንሥእ ወጹር ዓራተከ ብዬ ከደዌህ ባልፈውስህ መስክርብኝ አጣላኝ በእንተ እኩይ ከደዌህ ስላል ፈወስኩህ ፤ ወእመሰ ፤ ከደዌህ ስለፈውስኩህ ግን ለምን ትመታኛለህ የበጐነት ወረታ ክፋት ነውን አለው ። ገጸ መለኮቱን የመታበት እጁ ስሉ ደርቆ ቀርቷል ።

፳፬ ወፈነዎ ሐና ሕሙየ ኀበ ቀያፋ ሊቀ ካህናት
፳፬ እንደታሰረ ወደሊቀ ካህናቱ ወደቀያፋ ላከው
፳፭ ወሀሎ ስምዖን ጴጥሮስ ይቀውም ወይስሕን
፳፭ ጴጥሮስም ቁሞ እሳት ይሞቅ ነበር ።
ወተስእልዎ እለ ይቀውሙ ወዓልት ወይቤልዎ አንተኒ እምአርዳኢሁ ለውእቱ ብእሲ አንተ ።
አንተም ክርሱ ደቀ መዛሙርት ወገን ነህ አሉት።
ወክህደ ወይቤ ኢኮንኩ ።
አይደለሁም ብሎ ካደ ።

፳፮ ወይቤሎ ፩ዱ እምአግብርቲሁ ለሊቀ ካህናት ዘእምአዝማዲሁ ለዝኩ ለዘመተሮ ጴጥሮስ እዝኖ አኮኑ አነ ርኢኩከ ውስተ ገነት ምስሌሁ ።

፳፮ ጴጥሮስ ጆሮውን ከቆረጠው ከሊቀ ካህናቱ ባሪያ ወገን የሚሆን አንዱ ካታክልት ቦታ ከርሱ ጋራ አይቼህ አልነበረምን አለው የማልኩስን በቀል መለስኩ ብሎ ።

፳፯ ወካዕበ ክህደ ጴጥሮስ ።
፳፯ ለቀረበው ካዕበ እያለ ይሄዳል ጴጥሮስ ሁለተኛ ካደ ።
ወበጊሁ ነቀወ ዶርሆ ሶቤሃ ።
ያንጊዜ ዶሮ ጮኸ ፤ የክህደተ ጴጥሮስ መገናኛ እንደምን ነው በመጀመሪያ አንዳንድ ሴት በማለት አራቱ ሁሉ አንድ ናቸው ። በሁለተኛው ማቴዎስና ማርቆስ አንዳንድ ሴት ይላሉ ሉቃስ አንድ ወንድ ፣ ዮሐንስ ብዙ ወንዶች አለ ፣ በሦስተኛው ማቴዎስና ማርቆስ ብዙ ወንዶች ይላሉ ሉቃስና ዮሐንስ አንድ አሉ አይጣላም ቢሉ አይጣላም፣ በመጀመሪያ አራቱ ሁሉ አንዳንድ በማለት አንድ ናቸው ። በሁለተኛው ማቴዎስና ማርቆስ አንዲት ሴት ማለታቸው አንዲት ሴት ለብዙ ወንዶች ነግራለች ሉቃስ አንድ ወንድ ማለቱ ጠያቂውን ሲያይ ዮሐንስ ብዙ ወንዶች ማለቱ መጠየቅ የሁሉ ፈቃድ ከሆነ ብሎ፣በሦስተኛው ማቴዎስና ማርቆስ ብዙ ወንዶች ማለታቸው ፈቃድ የሁሉ ከሆነ ብለው ሉቃስና ዮሐንስ አንድ ወንድ ማለታቸው ጠያቂውን ሲያዩ ነው ።
ዘከመ ቆመ ኢየሱስ ቅድመ ጲላጦስ ።

፳፰ ወወሰድዎ ለእግዚእ ኢየሱስ እምኀበ ቀያፋ ኀበ ዓውድ ። ማቴ፥፳፯፥፪ ማር፥፲፭፥፩ ። ሉቃ፥፳፫፥፲፩ ግብ፥ ፲፥፳፰ ።

፳፰ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስን ከቀያፋ ዘንድ ወደ ዐደባባይ ወሰዱት ።
ወጎህ ውእቱ ።
ማለዳ ነበር ።
ወኢቦኡ አይሁድ ውስተ ዓውደ ምኵናን ።
ካደባባይ አልተገናኙም ነበር
ከመ ኢይርኰሱ አምቅድመ ይብልዑ ፋሥሐ ።
በግዓ ፋሲካውን ሳይበሉ ሥርዓት ማፍረስ እንዳይሆንባቸው ሐተታ ሲያመላልሱት አድረው ነግቶባቸዋል በቀትር በግዓ ፋሲካውን በልተው ወጥተው ሰቅለውታል ዛሬ የጥምቀትን ቍርባን ረፈደ ብለው እንዳይተውት ።

፳፱ ወወፅአ ጲላጦስ አፍአ ኀቤሆሙ ።
፳፱ ጲላጦስ እርሳቸው ወዳሉበት ወጣ ፡
ወይቤሎሙ ምንትኑ ጌጋዩ ለዝብእሲ በዘአምጻእክምዎ ኀቤየ
ወደኔ ባመጣችሁት ገንዘብ ወደኔ ያመጣችሁበት የዚህ ሰው በደሉ ምንድን ነው አላቸው ።

፴ ወአውሥኡ አይሁድ ወይቤልዎ ሶበሰ ኢኮነ ገባሬ እኪት እምኢያግባእናሁ ኀቤከ ።

፴ በደልስ ባልኖረበት ላንተ አሳልፈንም ባል ሰጠነው ነበር አሉት ።

፴፩ ወይቤሎሙ ጲላጦስ ንሥእዎ አንትሙ ወበከመ ሕግክሙ ኰንንዎ ።

፴፩ ጲላጦስም እናንተው ወስዳችሁ እንደ ሕጋችሁ ፍረዱበት ግደሉት አላቸው ። አንተ ትኴንኖ ለእጉከ እንዲል ።
ወይቤልዎ አይሁድ ለነስ ኢይከውነነ ንቅትል ወኢመነሂ ።
እኛስ ማንንም ማን ልንገድል አይቻለንም አሉት።

፴፪ ከመ ይብጻሕ ቃሉ ለእግዚእ ኢየሱስ ዘይቤ እንዘ ይኤምሮሙ በአይ ሞት ሀለዎ ይሙት ማቴ፥ ፳ ፤ ፲፱ ፣

፴፪ በምን ሞት ይሞት ዘንድ አለው ቢሉ በምን ሞት ይሞት ዘንድ እንዳለው ሲያስረዳ ጌታ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ፤ እንዲሉ አደ ረጋቸው ፡ አንድም በምን ሞት ይሞት ዘንድ

አለው ቢሉ በመስቀል ተሰቅሎ ይሞት ዘንድ እን
ዳለው ሲያስረዳ እንዲህ እንዲሉ አደረጋቸው ።
ሐተታ ሰቅለት የሮም ነው አይሁድ በደንጊያ ነው
የሚገሉ ።

፴፫ ወቦአ ካዕበ ጲላጦስ ውስተ ዓውድ ፤
፴፫ ዳግመኛ ጲላጦስ ካደባባይ ወጣ ።
ወጸውዖ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታን ጸራው ።
ወይቤሎ አንተኑ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሥ አንተ ነህን አለው ።

፴፬ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ
፴፬ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ዘእምልብከኑ ትብል ዘንተ ።
ይህን የምትናገር ከራስህ አንቅተህ ነውን ።
ወሚመ ቦኑ ባእድ ዘነገረከ በእንቲአየ ።
ወይም የኔን ነገር የነገረህ ሌላ አለን አለው ።

፴፭ ወአውሥአ ጲላጦስ ።
፴፭ ጲላጦስም መለሰ ።
ወይቤሎ እነሂ አይሁዳዊኑ አነ ።
ከራሴማ አንቅቼ እናገር ዘንድ እኔ አይሁዳዊ ነኝን ።
አኮኑ ሕዝብከ ወሊቃነ ካህናት አግብኡከ ኀቤየ ።
ወገኖችህና የካህናት አለቆች ለኔ አሳልፈው ሰጥ
ተውህ የለምን ።
ምንተኑ እግበረከ ።
ምን ላድርግህ ። አንድም ወገኖችህ ሊቃነ ካህናት
ለኔ አሳልፈው ሰጥተውሀልና ።
ምንተኑ እገብረከ ።
ምን አደርግሃለሁ በደል የሌለብህን አለው ።

፴፮ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፴፮ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ መንግሥትየሰ ኢኮነት እምዝንቱ ዓለም
የኔ መንግሥቴ ከዚህ ዓለም የተገኘች አይደለ
ችም በዚህ ዓለም ብቻ አይደለችም ።
ሶበሰ ኮነት በዝንቱ ዓለም መንግሥትየ እምተ
በአሱ ሊተ ወዓልያንየ ከመ ኢያግብኡኒ አይሁድ
ኀቤከ ።
መንግሥቴስ በዚህ ዓለም ብቻ ብትሆን ። አንድም
ከዚህ ዓለም የተገኘች ብትሆን አይሁድ ላንተ
አሳልፈው እንዳይሰጡኝ ብላቴኖቼ በተጣሉልኝ
ነበር ።
ወይእዜሰ ባሕቱ ኢኮነት መንግሥትየ እምዝንቱ
ዓለም ።
ነገር ግን መንግሥቴ በዚህ ዓለም ብቻ አይደለ
ችም ከዚህ ዓለም የተገኘች አይደለችም ።

፴፯ ወይቤሎ ጲላጦስ እንከሰኬ ንጉሥ አንተ ።
፴፯ ጲላጦስም መንግሥትህ በዚህ ዓለም ብቻ
አይደለችም ከዚህ ዓለም የተገኘች አይደለችም
እንጂ መሆኑን ንጉሥ ነሃ አለው ።
ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታም መለሰ ፤
ወይቤሎ ለሊከ ትቤ ከመ ንጉሥ አነ ፤
እኔ ንጉሥ እንደሆንኩ አንተ ትናገራለህ አለው ።
መሰወር ። አንድም በሦስቱ ዳኞች ልሳን ትጽ
ፈዋለህ ።
ወአንሰ በአንተ ዝንቱ ተወለድኩ ወእንበይነ ዝንቱ
መፃእኩ ውስተ ዓለም ከመ እኩን ሰማዕተ በጽድቅ ።
እኔ በእውነት እመሰክር ዘንድ ተወልጄ ስለዚህ
ወደ ዓለም መጥቻለሁ ።
ወኵሉ ዘእምጽድቅ ውእቱ ይሰምዓኒ ቃልየ ።
ከጽድቅ የተገኘ የጽድቅ ወገን ሁሉ ነገሬን ይቀ
በለኛል ፤

፴፰ ወይቤሎ ጲላጦስ ምንትኑ ውእቱ ጽድቅ ።
፴፰ ጲላጦስም ጽድቁ ምንድ ነው አለው ፤
አንተም ንጉሥ ነኝ ትላለህ እኒያም ንጉሥ ነኝ አለ
ብለው አምጥተውሃል እውነቱ ማናቸው ነው
አለው ። አንድም ወኵሉ ዘእምጽድቅ ይሰምዓኒ
ቃልየ ብሎት ነበርና ነገሩ ቢረቅበት ጽድቁ ምንድ
ነው አለው ።
ወዘንተ ብሂሎ ወፅአ ካዕበ ኀበ አይሁድ ፤
ይህን ተናግሮ ዳግመኛ ወደ አይሁድ ወጣ ።
ወይቤሎሙ አንሰ ኢረከብኩ ጌጋየ ላዕሌሁ ወኢአ
ሐተኒ ።
እኔስ ጥቂት ለንኳን በደል አላገኘሁበትም አላቸው።

፴፱ ወባሕቱ ሀሎ ዘናለምድ ዘአሐዱ ለክሙ
፩ደ እምነ ሙቁሐን ለለፋሲካ ።

፴፱ ባመት አንዳንድ አስር የምንፈታበት ፤
አንድም አሕዱ ለክሙ፡እፈታላችሁ ዘንድ ያለመ
ድነው ሥርዓት አለ ።
ትፈቅዱኑ አንክ ከመ እኅድጎ ወእሕይዎ ለክሙ
ለንጉሠ አይሁድ ።
የአይሁድ ንጉሥ ክርስቶስን ልፈታላችሁ ትወዳ
ላችሁን አላቸው ።

፵ ወከልሑ ካዕበ ኵሎሙ ።
፵ መላው አሰምተው ተናገሩ ።
ወይቤሉ አኮ ዘንተ ዘተሐዩ ወተሐድግ ።
የምትፈታልን ይህን አይደለም ።
አላ በርባንሃ ።
በርባንን ነው እንጂ ።
ወበርባንሰ ሊቀ ፈያት ውእቱ ።
በርባን ግን የወንበዴ አለቃ ነው ።
እንዲህ ሲሆን በደል የሌለበትን ግደል በደል ያለበትን
አትግደል አሉ ለማለት ።

ምዕራፍ ፲፱ ።

፩ ወእምዝ ነሥኦ ጲላጦስ ለእግዚእ ኢየሱስ
ወቀሠፎ ።

፩ ዝ ሲናገረው የመጣው ነው ከዚህ በኋላ
ጲላጦስ ካልቀረሰ በምር ደስ ይበላቸው ብሎ ካደ
ባባይ አውጥቶ ገረፈው ። እንድም ራርተው ይተ
ውታል መስሎት ፣ እንድም መጠ ውኩ ዘባንየ
ለመቅሠፍት ያለው ትንቢት ሊፈጸም ፣ እንድም
ዲያብሎስ የአዳምን ዘባነ ልቡናውን እየገረፈ ገሃነም
አውርዶት ነበርና ለርሱ ካሣ ሊሆን እንድም በጌታ
የግፍ ድርብ ይደረግበታልና በሀገራቸው የሚሰቀል
አይገረፍም እርሱን ግን ገርፈው ይሰቅሉታልና ።

፪ ወጸፈሩ አክሊለ ዘሦክ ።
፪ ጭፍሮች የሾህ አክሊል ጉንጉነው ።
ወአስተቀጸልዎ ላዕለ ርእሱ ።
ከራሱ ላይ ደፉለት እንገሥንህ ብለውታልና ፍና
ተሣልቆ እንድም ወወደዩ ጌራ መድኃኒት ዲበ
ርእሱ ያለው ትንቢት ሊፈጸም ፣ ድርሳነ መድ
ኃኔ ዓለም ሽህ ጥቃቅን ሰብዓ ታላላቅ የብረት
እሾህ ያለው ዘውድ ነው ይላል እንደምን ነው አይ
ጣላም ቢሉ እይጣላም ነገር እንደዚህ ነው ይላል
እንደዚያስ ከሆነ ኢትሰብሩ ዓፅሞ ያለው በፈ
ረሰ ነበር ።
ወአልበስዎ ልብሰ ሜላት ።
ነጭ ግምጃ አለበሱት ።
ማቴዎስ ቀይሀ ይላል ከዚህ እንዲህ አለ እንደምን
ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም መደቡ ነጭ ነው ኋላ
ቀለም አግብተውታል ። እንድም በአንድ ወገን ሲያ
ዩት ነጭ በአንድ ወገን ሲያዩት ቀይ ይሆናል እንደ
ሌታ ቀን ግምጃ ። እንድም እልፎ አልፎ ቀለም
ገብቷል እንደ ሱሲ መጠብር እንደ ቀሽ መሪ
መታጠቂያ እንደ መረሻት ።

፫ ወይመጽኡ ኀቤሁ ወይቤልዎ በሐከ ንጉሠ
አይሁድ ።

፫ ወደርሱ እየመጡ የአይሁድ ንጉሣቸው
ቢሰኛህን ጸበኛህን አያውለው አያሳድረው አለት
ሌላ ቢሰኛ ጸበኛ አለውን አያውለን አያሳድረን
ሲያሰኛቸው ነው ።
ወይጸፍዕዎ ገጾ ።
ፊቱን በጥፊ መቱት ። ወመልታሕቴየ ለጽፍእት ።
ያለው ትንቢት ሊፈጸም ። እንድም ዲያብሎስ
የአዳምን ገጽ ልቡናውን እየጸፋ ገሃነም አውር
ዶት ነበርና ለርሱ ካሣ ሊሆን ።

፬ ወወፅአ ካዕበ ጲላጦስ አፍአ ወይቤሎሙ
ናሁ አውፅአ ለክሙ ከመ ታእምሩ ከመ አልቦ ዘረከ
ብኩ ላዕሌሁ ጌጋየ ወኢአሐተኒ ።

፬ ጲላጦስም ባደባባይ ወጥቶ ጥቂት ስንኳ
ባንድ ወገን ስንኳ ያገኘሁበት በደል እንደሌለ
ታውቁ ዘንድ እነሆ ወደ ዐደባባይ አስመጣላች
ኋለሁ አላቸው ።

፭ ወወፅአ እግዚእ ኢየሱስ አፍአ እንዘ ይት
ቄጸል አክሊለ ዘሦክ ።

፭ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም የእሾህ አክ
ሊል ደፍቶ ።
ወይለብስ ሜላት ።
ነጭ ሐር ለብሶ ወደ ዐደባባይ ወጣ ።
ወይቤሎሙ ጲላጦስ ነዋ ውእቱ ብእሲ ።
ያ ሰው እነሆ አላቸው ።

፮ ወሶበ ርእይዎ ሊቃነ ካህናት ወወዓልያኒ
ሆሙ ለእግዚእ ኢየሱስ ከልሑ ።

፮ ብላቴናዎቻቸውና ሊቃነ ካህናትም ጌታን
ባዩት ጊዜ ጮሁ ።
ወይቤሉ ስቅሎ ።　　　ስቀለው አሉት ።
ወይቤሎሙ ጲላጦስ ንሥእዎ አንትሙ ወለሊከሙ
ስቅልዎ ጲላጦስም እናንተ ወስዳችሁ ስቀሉት ።
አንሰ ኢረከብኩ ላዕሌሁ ጌጋየ ።
እኔስ የሚሰቀልበት በደል ነውር አላገኘሁበትም
አላቸው ።

፯ ወአውሥኡ አይሁድ ወይቤልዎ ንሕነሰ
ሕግ ብነ ።

፯ አይሁድም መለሱለት አሉትም እኛስ
ሥርዓት አለን ።
ወበከመ ሕግነ ርቱዕ ይሙት ።
እንደ ሥርዓታችን ሞት ይገባዋል ።
እስመ ወልደ እግዚአብሔር ረሰየ ርእሶ ።
የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ ብሏልና አሉት ምን ይዘው
እንዲህ አሉ ቢሉ በወልደ ሰሎሚት ልማድ አባቱ ፣
ግብጻዊ ነው እናቱ ዕብራዊት ናት የእናቱን
ዘመዶች እናቱን ተከትሎ ወጣ ፣ በም
ድረ በዳ በገዳም ሳሉ ካንዱ ጋራ ተጣሉ
በግብጽማ ሳላችሁ ያባቴ ባሮች አልነበራችሁምን
አለው ። እስራኤል ይኸን ሰምተው ሁለት መቶ
ካሥራ አምስት ዘመን የገዙን አልበቃቸው ብሎ እየ
ተከተሉ እየመጡ ይሰድቡን ጀመር ብለው አዘኑ
ሙሴ ወደ እግዚአብሔር አመለከተ እስራኤል የኔ
ባሮች ናቸው እስራኤልን ባሪያዬ ማለት አምላክ
ነኝ ማለት አይደለምን ። ዘፀአት ይሀን ሲናገር
የሰማው አስቀድሞ ድንጊያ ይጣልበት ከዚህ በኋላ
ግደሉት ብሎ ገድለውታል ።

፰ ወሰሚዖ ጲላጦስ ዘንተ ነገረ ፈርሀ ፈድፋደ ።
፰ ጲላጦስ ይህን ነገር ሰምቶ ፈጽሞ ፈራ።
ወቦአ ካዕበ ኀበ ዐውድ ።
ሁለተኛ ወደ ዐደባባይ ወጣ ።

፱ ወይቤሎ እግዚእ ኢየሱስ እምአይቴ አንተ።
፱ ትውልድህ ነገድህ ከወዴት ነህ አለው ።
ወኢተሰጥዎ እግዚእ ኢየሱስ ወኢምንተኒ ።
ጌታ ግን አልመለሰለትም ። እንዳልፈራ ለማጠየቅ እንዳለፈው ጨርሶ ።

፲ ወይቤሎ ጲላጦስ ሊተኒ ኢትነብበኒሁ ።
፲ ጲላጦስም አለው ለኔም አትመልስልኝ ።
ኢተአምርሁ ከመ ብውህ ሊተ እቅትልከኒ ወብውህ ሊተ አሕዩከኒ ።
ብስቅልህስ ባድንህስ እንዲቻለኝ አታውቅምን አለው ።

፲፩ ወአውሥአ እግዚእ ኢየሱስ ።
፲፩ ጌታም መለሰ ።
ወይቤሎ ኢኮንከ ብውሐ ላዕሌየ እመ ኢተውህበ ለከ እምሰማይ ።
ከሰማይ ካልተሰጠህ ማለት መለኮቴ በሥጋ ካልተሰጠህ ፡ አንድም ሥልጣኑ ካባቴ ካልተሰጠህ በኔ ሥሉጥ አይደለህም አንድም ምንም ምን ሥልጣን የለህም አለው ።
ወበእንተዝ ዘአግብአኒ ኀቤከ ዘየዓቢ ጌጋይ ላዕሌሁ ።
ስለዚህ ለአንተ አሳልፎ በሰጠኝ በይሁዳ ጽኑ ፍዳ አለበት ።

፲፪ ወበእንተዝ ፈቀደ ጲላጦስ ከመ ይኅድጎ ወያሕይዎ ።
፲፪ ዘየአቢ ጌጋይ ላዕሌሁ ስላለው ጲላጦስ ሊያድነው ወደደ ።
ወከልሑ አይሁድ ወይቤሉ እመ አሕየውኮ ለዝንቱ ኢኮንከ አርኮ ለቄሣር ።
ይህን ካዳንከው የቄሣር ፈቃደኛው አይደለህም
ብለው አይሁድ አሰምተው ተናገሩ ።
እስመ ኵሉ ዘያነግሥ ርእሶ ዓላዊ ነጋሢ ውእቱ።
ራሱን ንጉሥ ነኝ የሚል ሁሉ ወሬኛ ንጉሥ ነውና።

፲፫ ወሰሚዖ ጲላጦስ ዘንተ ነገረ አውፅኦ ለእግዚእ ኢየሱስ አፍአ ።
፲፫ የቄሣር ፈቃደኛው አይደለህም ያሉትን ጲላጦስ ሰምቶ ጌታን ወደ ውጭ አወጣው ።
ወነበረ ዲበ መንበር ውስተ መካን ዘስሙ ሊቶስጥሮስ በዕብራይስጥ ይብልዎ ገቦታ ።
በዕብራይስጥ ገቦታ የሚባል ንጽፍ ደንጊያ ባለበት ቦታ ወንበር አዘርግቶ ተቀመጠ ።

፲፬ ወዓርብ ፋሲካ ።
፲፬ ፋሲካቸው ዓርብ ነበረ ። አንድም ወዓርበ ይላል ፋሲካቸው አለፈ ተከተተ ።
ወውእቱ ጊዜ ቀትር ዘስሱ ሰዓት ።
ያውም ድልድል ቀትር ነበር ።
ወይቤሎሙ ጲላጦስ ለአይሁድ ነዋ ንጉሥክሙ ።
ጲላጦስ አይሁድን እነሆ ንጉሣችሁ አላቸው ።

፲፭ ወከልሑ አይሁድ ወይቤሉ አእትቶ ወስቅሎ ።
፲፭ በሞት አርቀው ስቀለው ብለው አሰምተው ተናገሩ ።
ወይቤሎሙ ጲላጦስ ለንጉሥክሙኑ እሰቅሎ ።
ጲላጦስም ንጉሣችሁን ልስቀለውን አላቸው ።
ወአውሥኡ ሊቃነ ካህናት ።
የካህናት አለቆችም መለሱ ።
ወይቤሉ አልብነ ንጉሥ ዘእንበለ ቄሣር ።
ቄሣር ነው እንጂ ከቄሣር በቀር ንጉሥ የለንም አሉት ።

፲፮ ወእምዝ ወሀቦሙ ይሰቅልዎ ።
፲፮ ከዚህም በኋላ ስቀሉት ብሎ ሰጣቸው ።
ወተመጠውዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ወአውፅእዎ አፍአ።
ጌታን ተቀብለው ወደ ውጭ ይዘውት ወጡ ።

፲፯ ወወሰድዎ እንዘ ይጸውር መስቀሎ ውስተ መካን ዘስሙ ቀራንዮ ።
፲፯ መስቀሉን ተሸክሞ ቀራንዮ ከሚባል ቦታ ይዘውት ሄዱ ።
ወበዕብራይስጥ ይብልዎ ጎልጎታ ።
የተሰቀለበት ቦታ በዕብራይስጥ ጎልጎታ ይባላል።

፲፰ ኀበ ሰቀልዎ ።
፲፰ ከዚያም ሰቀሉት ።
ወሰቀሉ ምስሌሁ ካልዓነ ክልኤተ ፈያተ ።
ከርሱም ጋራ ሁለት ወንበዴዎች ሰቀሉ ።
አሐደ እምለፌ ወአሐደ እምለፌ ።
አንዱን በቀኝ አንዱን በግራ
ወማእከሎሙ ኢየሱስሃ ።
ጌታንም በመካከላቸው ። አነገሥንህ ብለውታልና ፍና ተሳልቆ ቀኛዝማች ግራዝማች ቀኝ ቢትወደድ ግራ ቢትወደድ ሾምንልህ ለማለት ። አንድም ለማሳሳት በቀኝም በግራም የመጣው ይህ ምንድነው ብሎ ይጠይቃል ወንበዴ ፡ ያሳ የመካከለኛውስ ያስ ከነሀን ልዩ ነው ለማለት ። አንድም ተኍለቈ ምስለ ጊጉያን ያለው ትንቢት ሊፈጸም ይኸንም ከመ ይደምረኒ ምስለ ነፍሰ ጸድቃን ብሎ ተርጕሞታል ምሥጢሩ ግን እኛን ኃጥአንን በግራ ታቆመናለህ ሲያሰኛቸው ነው ።

፲፱ ወጸሐፈ ጲላጦስ መጽሐፈ ወአንበረ ዲበ መስቀሉ ።

፲፱ ጲላጦስም መጻሕፍ ጽፎ ከመስቀሉ ራስ በትርፋ ጠረቀው ።
ወይብል መጽሐፉ ኢየሱስ ናዝራዊ ንጉሦሙ ለአይሁድ ውእቱ ዝንቱ ።
ያብዳቤውም የናዝሬቱ ኢየሱስ የአይሁድ ንጉሣቸው ይህ ነው የሚል ነው ።

፳ ወብዙኃን እምነ አይሁድ አለ አንበብዎ ለይእቲ መጽሐፍ ።

፳ ያችንም ያብዳቤ ከአይሁድ ወገን የተመለከቷት ብዙ ናቸው ።
እስመ ቅሩብ ውእቱ መካን ለሀገር ኀበ ሰቀልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ጌታን የሰቀሉበት ቦታ ለከተማ እቅራቢያ ነበርና።
ወጽሕፈቱ ጽሑፍ ውእቱ በዕብራይስጥ ።
ጽሕፈቱም በዕብራይስጥ ልሳን ነበር ።
ወበጽርዕ ። በጽርዕም ።
ወበሮማይስጥ ።
በሮማይስጥም ። ዕብራዊ ቀያፋ ጽርአዊ ሄሮድስ ሮማዊ ጲላጦስ እሉና ። ምሥጢሩ ግን ወንጌል በሦስቱ ልሳን እንድትጻፍ ያጠይቃል ።

፳፩ ወይቤልዎ ሊቃነ ካህናት ለጲላጦስ ኢትጽሕፍ ንጉሦሙ ለአይሁድ ።

፳፩ የካህናት አለቆች ጲላጦስን የአይሁድ ንጉሣቸው ነው ብለህ አትጻፍ አሉት ።
እላ ለሊሁ ይቤ ንጉሦሙ ለአይሁድ አነ ።
እሱ የአይሁድ ንጉሣቸው ነኝ አለ ብለህ ጻፍ እንጂ ።

፳፪ ወአውሥአ ጲላጦስ ።
፳፪ ጲላጦስም መለሰ ።
ወይቤሎሙ ዘጸሐፍኩ ጸሐፍኩ ።
የጻፍኩትን ጻፍኩ አላቸው ።
ዘፈኖኩ ፈኖኩ እንዲል ። በነገር ሲያኹት ውለው ነበርና ፈንታውን ያሻቸዋል ።

፳፫ ወሐራስ ሶበ ሰቀልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ነሥኡ አልባሲሁ ወተካፈሉ ወረሰይዎ አርባዕተ ክፍለ ።

፳፫ ጭፍሮች ግን ጌታን ከሰቀሉት በኋላ ልብሱን ወስደው ካራት ተካፈሉት ።
ለለአሐዱ እምሐራ ።
ከጭፍራውም ለእንዱም ላንዱ ለእያንዳንዱ ።
ወከዳናሂ አልታሃ ዘአልቦ ርፍአት ዘእምላእሉ እንመቱ ። ሥፍ የሌለበት ሥር ወጥ ቀሚሱን ግን ።

፳፬ ይቤሉ ኢንግምድ ወኢንስጥጥ ።
፳፬ እርስ በእርሳቸው ም አሉ አንቅደደው ።
እላ ንትፋሰስ ለዘረከቦ ይርከቦ ።
ለደረሰው ይደርሰው ዘንድ ዕጣ እንጣጣልበት እንጂ
ከመ ይብጻሕ ቃለ መጽሐፍ ዘይቤ ፡ ተካፈሉ አልባስየ ለርእሶሙ ።
ልብሴን ተካፈሉት ብሎ መጽሐፍ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ። ረሰይዎ አርባዕተ ክፍለ ወተዓፀው ዲበ አራዝየ ። በልብሴ ዕፃ ተጣጣሉበት ብሎ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።
ወተበሀሉ ኢንግምድ ላለው ። ኵፌቱን መጠምጠሚያውን መጐናጸፊያውን ቀሚሱን ልብ አልባውን አርገው ተካፍለዋል ። ቀሚሱን ግን ልብስ ምንንት ብለው ንቀው ትተዋታል ። ንቀዋትስ አይደለም አክብረዋት ነው እንጂ። ሰብአ ሰገል ያመጡለት ሲያድግ የምታድግ አለ እንተ ደም ይውኀዛ የተፈወሱባት ገባሬተ ተእምራት ናት አይንቋትም ። ኵፌቱን መጠምጠሚያውን እንድ ወገን አድርገው ሦስት ዕፃ ይጥላሉ አራተኛ ዕፃውን ይዞ ያቆያል እንደገና አራቱ በርሷ ዕፃ ይጥላሉ ለደረሰው የደረሰች እንደሆነ ያን ላልደረሰው ሰጥቶ እርሷን ይውሰዳል ። ላልደረሰው የደረሰች እንደሆነ የተመቸ ። ለጊዜው እርሱ ሁለት ልብስ አታኑሩ ይላል የአንድ ባሕታዊ ልብስ ላራት ቤት ጭፍራ በቃ ለማለት ። ምሥጢሩ ግን ልብስ የወንጌል ምሳሌ ፡ አራት ዕፃ መጣጣላቸው ወንጌል አራት ወገን ሁና ለመጻፏ አለመቅደዳቸው በምሥጢር እንድ የመሆንዋ ። አንድም መለኮቱን ከትስብእቱ ትስብእቱን ከመለኮቱ ሳንለይ አንመን ሲያሰኛቸው ነው ።
ወከመዝ ገብሩ ሐራ ።
ጭፍሮች እንዲህ አደረጉ ።

፳፭ ወይቀውማ ኀበ መስቀሉ ለእግዚእ ኢየሱስ እሙ ወእኅታ ሬእሙ ።

፳፭ እመቤታችን ስሎሜ ።
ወማርያም እንተ ቀለዮጳ ።
ማርያም ባውፍልያ እንድም እኅታ ለእሙ ማርያም እንተ ቀሌዮጳ ። ሐና ከሞተች በኋላ የቀለዮጳን ሚስት አግብቶ ወልዷታል ።
ወማርያም መግደላዊት ።
ማርያም መግደላዊት ከእግረ መስቀሉ አጠገብ ቁመው ነበር ።

፳፮ ወሶበ ርእዮሙ እግዚእ ኢየሱስ ለእሙ ወለረድኡ ዘያፈቅር ይቀውሙ ።

፳፮ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሚወደውን ደቀ መዝሙሩንና እመቤታችንን ከእግረ መስቀል

ቆመው ባያቸው ጊዜ ።
ወይቤላ ለእሙ አ ብእሲቶ ነዋ ወልድኪ ።
አንች ሆይ ልጅሽ ይርዳሽ ያጥናናሽ አላት ።
ውሉድኪ ሲል ነው ፡ በዮሐንስ እኛን ለርዷ መስጠቱ ነውና ።

፳፯ ወይቤሎ ለውእቱኒ ረድኡ ነያ እምከ ።
፳፯ ደቀ መዝሙሩን እነሆ እናትህ ታጽናህ አለው እምከሙ ሲል ነው በዮሐንስ እርሰዋን ለኛ መስጠቱ ነውና ።
ወእምይእቲ ሰዓት ነሥአ ውእቱ ረድእ ወእእተዋ ቤቶ።
ከዚያም ቀን በኋላ ዮሐንስ ወደቤቱ ይዝዋት ሄደ ።
ከዮሐንስ ቤት ዓሥራእምስት ዓመት ተቀመጠች።

፳፰ ወእምዝ ሶበ ርእየ እግዚእ ኢየሱስ ከመ ተፈጸመ ኵሉ ።
፳፰ ከዚህም በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የተናገረው ትንቢት እንደ ተፈጸመ ባየ ጊዜ ።
ከመ ይብጻሕ ቃለ መጽሐፍ ይቤ ጸማዕኩ ።
መጽሐፍ ወወደዩ ሐሞተ ውስተ መብልዕየ ያለው ትንቢት ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ጸማዕኩ አለ ።

፳፱ ወቦቱ ሀየ ግምዔ ዘምሉእ ብሂዓ ።
መጣጣ የተመላ ማሰሮ ከዚያ አለ ።
ወመልኡ ሰፍነ ወቈጽለ ሁስጱ ወመልኡ ውስቴቱ እምውእቱ ብሂዕ ።
እንዳይነ በጐ ያለ ባዘቶ ውኃ የሚያነሣ ቤታቸውን የሚጠርጉበት ነው ያን ከመጣጣው ነከረው ።
ወአሠሩ በቈጽለ ሁስጱ ዲበ ሕለት ወአስተርከቡ ውስተ አፉሁ ወአፀሩ ።
በስሚዛ ዘንግ አሰረው ካፉ ጠመቈለት ።
ወሰረበ ብሂዓ ኢየሱስ ይቤ ናሁ ተፈጸመ ኵሉ ዘጽሑፍ። ኢየሱስም መጻጻውን በቀመሰ ጊዜ የተጻፈው ሁሉ ደረሰ ተፈጸመ አለ ። በሀገራቸው አራት ነገር ያመጸሉ የስንዴ ቅጥራን የበለስ ቅጥራን አዞ ክል ዝፍተ ወይን ። ሐሞቱን ግን እነሱ አልጨመሩትም ሊሸጠው ገበያ ይዞት ወጥቶ ረከሰበት ሊጥለው ወዶ ቈሞ ሳለ ተቀዶ ገብቷል ።
ወአጽነነ ርእሶ ።
ራሱን ዘለፍ አደረገ ።
ወመጠወ ነፍሶ ወወፅአት መንፈሱ ።
ቅድስት ነፍሱን ከቅድስት ሥጋው በእደ እግዚአ ብሔር ለየ ።
ወአይሁድሰ ። አይሁድ ግን ።
እስመ ዓርብ ውእቱ ።
መሽቷልና ።
ይቤሉ እላንቱ ሥጋት ኢይቢታ ዲበ መላቅሊሆን።
እኒህ ሰዎች እንደተሰቀሉ አይደሩ አሉ ።
በእንተ ሰንበት ።
ስለ ክብረ ሰንበት ።
እስመ ዓባይ ዕለታ ለይእቲ ሰንበት ።
ዕለቲቱ ከብርት ናትና ።
ወሰአልዎ ለጲላጦስ በኀቡእ ከመ ያውርድዎሙ ሰቢሮሙ ቍየጺሆሙ ።
ጭን ጭናቸውን ሰብረው ያወርዷቸው ዘንድ በስውር ጲላጦስን ለመኑት ።

፴፪ ወመጽኡ ሐራ ወሰበሩ ቍይጾ ለቀዳማዊ ።
፴፪ ጭፍሮችም መጥተው የፈያታይ ዘየማንን ጭኑን ሰበሩት ፊቱን ወደርሱ መልሶ ተሰቅሎ ነበርና ቀዳማዊ አለ ።
ወለካልዑኒ ዘተሰቅለ ምስሌሁ ።
ከርሱ ጋራ የተሰቀለውን ፈያታይ ዘፀጋምን ።

፴፫ ወሶበ ሐሩ ኀበ እግዚእ ኢየሱስ ወርእይዎ ወረከብዎ ከመ ሡለጠ መዊተ ።
፴፫ ጭፍሮች ከጌታችን ዘንድ ሄደው ፈጽሞ ሙቶ አገኙት ወኢሰበሩ ቍይጾ ።
ጭኑን አልሰበሩትም ።

፴፬ አላ ፩ዱ እምሐራ ረገዞ ገቦሁ ዘየማን በኲናት ።

፴፬ ከጭፍሮች አንዱ አለን ሞተ ብሎ ቀኝ ጐኑን በጦር ወጋው እንጂ ።
ወሶቤሃ ወፅአ እምኔሁ ደም ወማይ ።
ያንጊዜ ጥሩ ውኃ ትኩስ ደም ፈሰሰ ፡ ሐተታ እንደ ለ ሁኖ ከላይ አንድ ከታች እየራሱ ከላይ አንድ መሆኑ የተዋሕዶ ከታች እየራሱ መሆኑ የተዓቅበ።

፴፭ ወዘርእየ ስምዓ ኮነ ።
፴፭ ያየ ሐራዊ ያየ ወንጌላዊ መሰከረ ።
ወጽድቅ ውእቱ ስምዑ ።
ሀውቆ ያስተምራል ብሎ ምስክርነቱ እውነት ነው ።
ወአእመረ ውእቱ ከመ ጽድቀ ይነግር ።
እውነት እንዲያስተምር አወቀ ።
ከመ አንትሙሂ ትእመኑ ።
እናንተም ታምኑ ዘንድ ።

፴፮ ወዝንቱ ነገር ከመ ይብጻሕ ቃለ መጽሐፍ ዘይቤ ዓፅሞ ኢትስብሩ እምኔሁ ።

፴፮ ይህ ነገር የሆነ መጽሐፍ ዓፅሙን አት ስበሩ ብሎ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ።

፴፯ ወካዕበ ይብል ካልዕኒ መጽሐፍ ሀለዎሙ ይርአይዎ ለዘወግዕዎ ።

፴፯ ዳግመኛም ሌላው መጽሐፍ እጁን እግሩን በቀኖት የቸነከሩትን ጐኑን በጦር ወግተው ያዩት ዘንድ አላቸው ብሎ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ፡ ፩ዱ እምሐራ ረገዞ ገቦሁ ላለው ። አንድም

እጁን እግሩን በቀኖት የቸነከሩት ጐኑን በጦር የወጉት በተአምራት ያዩት ዘንድ አላቸው ብሎ መጽሐፍ የተናገረው ይደርስ ይፈጸም ዘንድ ወፅአ እምኔሁ ደም ወማይ ። የወጋው አንድ ሐራዊ አይ ደለምን ቢሉ ሽ በመከረ አንድ ወረወረ አንዲሉ ፈቃድ የሁሉ ከሆነ ብሎ አንድም መጽሐፍ ስም ካልጠራ ማብዛት ልማድ ነውና ካህናት ኀሉፋነ ፍኖት ከበቱ ፍኖተ እግዚእሙ እንዲል ። አንድም በቀኖት እጁን እግሩን የወጉትን ደርቦ ቈጥሮ ወማ ዕዎ አለ ።

፴፰ ወእምድኅረ ዝንቱ ሰአሎ ለጲላጦስ ዮሴፍ ዘአርማትያስ ።

፴፰ ከዚህ በኋላ የአርማትያስ ሰው የሚሆን ዮሴፍ ጲላጦስን ለመነው ።
እስመ ዝንቱ ረድዑ ውእቱ ለእግዚእ ኢየሱስ።
የጌታ ደቀ መዝሙሩ ነበርና ።
ወኮነ የኀብኦ ለዝንቱ በእንተ ፍርኃቶሙ ለአይ ሁድ ።
አይሁድን ስለ ፈራ ደቀ መዝሙርነቱን ይሰ ውር ነበር ።
ከመ ይንሣእ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
ሰአለ ከመ ይንሣእ ። እንበሳ የገደለው ንጉሥ ያስቀሰው ይታፈራልና ላውርድ ብሎ ለመነ ።
ወአብሖ ጲላጦስ ወሖረ ውእቱኒ ወነሥአ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
አውርድ አለው እሱም ሄዶ የጌታን ሥጋ አወረደ ።

፴፱ ወመጽአ ኒቆዲሞስኒ ዘሖረ ኀቤሁ ለእ ግዚእ ኢየሱስ ቀዲሙ ሌሊተ ።

፴፱ አስቀድሞ በሌሊት ወደጌታ የሄደ ኒቆዲ ሞስም መጣ ።
ወአምጽአ በዘቦቱ ይቀብርዎ ሕውሰ ከርቤ ወዐልወ ።
ገንዘው የሚቀብሩበትን የደቀቀ የጣፈጠ ሽቱአመጣ።
ምእተ ልጥረ ፤
መቶ ምዝን መቶ ግግር ዋግራ ሽቱ የሬት ሽቱ።

፵ ወነሥኡ ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
፵ የጌታን ሥጋ አውርደው ።
ወገነዝዎ በመዋጥሀ ከታን ዘሰንዱናት ምስለ አፈው በከመ ሕገ አይሁድ ሶበ ይገንዙ ወይቀብሩ ። አይሁድ ገንዘው በሚቀብሩበት ጊዜ እንደሚያደ ርጉት ሥርዓት ሽቱ ቀብተው በድርብ በፍታ ገነ ዙት ።

፵፩ ወቦ ሀየ ገነት ውስተ ውእቱ መካን ኀበ ስቀልዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።

፵፩ ጌታ የተሰቀለበት ቦታ የተክል ቦታ ነበር ።

ወውስተ ውእቱ ገነት ዝሀር ሐዲስ ዘአልቦ ዘተ ቀብረ ውስቴቱ ።
ከዚያም ቦታ ሰው ያልተቀበረበት አዲስ ቦታ ነበር።

፵፪ ወሀየ ቀበርዎ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
፵፪ ጌታን ከዚያ ቀበሩት ። እንግዳ ሥር ዓት እሠራላችኋለሁ ለማለት ። አንድም እንደ ኤልሳዕ ግባሬ ተአምራት ነቢይ ከተቀበረበት ቢቀ በር ያ አሥነሣው እንዳይሉ ።
እስመ ተፍጻሜተ ዓርበሙ ውእቱ ለአይሁድ ።
የአይሁድ መከተቻቸው ነበርና ።
ወቅሩብ ውእቱ መቃብር ኀበ ሰቀልዎ ።
መቃብሩ ለተሰቀለበት ቦታ አቅራቢያው ነበር ።
ያሥራሁለቱ ነገደእስራኤል ቦታ በየርስታቸው ነው ገሊላ ከእናቱ ርስት ወስደው እንዳይቀብሩት መሽቶባቸው ከዚያው ቀብረውታል ።

ዘከመ ሖሩ ማርያም መግደላዊት ወጴጥሮስ ወዮሐንስ ውስተ መቃብር ።

## ምዕራፍ ፳ ።

፩ ወበእሑድ ሰንበት መጽአት ማርያም መግ ደላዊት ኀበ መቃብር ። ማቴ፡፳፰፡፩ ማር፡ ፲፮፡፩ ሉቃ፡ ፳፬፡፩ ።

፩ ባንድ ሰንበት አንድም መጀመሪያው ሰን በት ፣ እሑድ ሰንበት በተባለበት ቀን ማርያም መግደላዊት ማለዳ ገሥግሣ ወደ መቃብር መጣች። እንዘ ዓዲሁ ጽልመት ።

ገና ጨለማው ሳይለቅ ገና ጨለማ ሳለ ።
ወረከበት እብነ እቱተ እምእፈ መቃብር ።
ደንጊያውን ከመቃብሩ ተነሥቶ አገኘችው ።

፪ ወሮጸት ወበጽሐት ኀበ ስምዖን ጴጥሮስ ወኀበ ዝኩ ካልዕ ረድእ ።

፪ ከባለሟሉ ከዮሐንስና ከጴጥሮስ ዘንድ ፈጥና ሄደች ።
ወትቤሎሙ ነሥእዎ ለእግዚእየ እምውስተ መቃብር ጌታዬን ከመቃብር አውጥተው ወስደውታል ።
ወኢየአምር ኀበ ወሰድዎ ።
ከወሰዱበት ግን አላውቅም ።

፫ ወወፅኡ ኀቡረ ስምዖን ጴጥሮስ ወዝኩ ካልዕ ረድእ ወሖሩ ኀበ መቃብር ።

፫ ጴጥሮስና ዮሐንስ ወጥተው ወደ መቃብር ሄዱ።

፬ ወእንዘ ይረውጹ ክልኤሆሙ ኀቡረ ።
፬ ሁለቱ ፈጥነው አንድ ሁነው ሲሄዱ በዶሮ ለጴጥሮስ ዝኩ ካልዕ ረድእ በጺሐ ኀበ መቃብር ።

ዮሐንስ ጴጥሮስን ቀድሞት ወደ መቃብር ሄደ
ሕፃን ነውና በፍቅሩ ይናደዳልና ።

፭ ወሶበ ሐወጸ ርእየ መዋጥሐ ንቡረ ።
፭ ዘልቆ በተመለከተ ጊዜ መጐናፀፊያውን
አገኘ ።

ወኢቦአ ባሕቲቱ ።
ነገር ግን አልገባም ። ሕፃን ነውና ቢፈራ ። አን
ድም ስለ ክብረ ጴጥሮስ ። ከኤጲስቆጶስ አስቀ
ድሞ ከመቅደስ እንዳይገባ

፮ ወተለዎ ስምዖን ጴጥሮስ ወበጽሐ ።
፮ ስምዖን ጴጥሮስ ተከትሎት ደረሰ ። አረ
ጋዊ ነውና በኀዘን ተቀጥቅጧልና ።
ወቦአ ውስተ መቃብር ።
ወደ መቃብር ገባ ። ኤጲስቆጶስ ከቄስ አስቀድሞ
መቅደስ እንዲገባ ።
ወረከበ መዋጥሐ ንቡረ ውስተ አሐዱ ገጽ ።
መጐናፀፊያውን ባንድ ወገን አገኘ ።

፯ ወሰበንኒ ዘዲበ ርእሱ እንተ ባሕቲቱ ጥብ
ሉለ ።

፯ ሻሹን እንደተጠመጠመ ለብቻው ።
ወእኮ ምስለ መዋጥሀ ።
ከመጐናፀፊያው ጋራ ሳይቃወስ ።

፰ ወእምዝ ቦአ ዝኩኒ ካልዕ ረድእ ዘበደሮ
በጺሐ ኀበ መቃብር ።

፰ ከዚህ በኋላ ቀድሞ ከመቃብር የደረሰ ዮሐ
ንስም ገባ ቄስ ኤጲስቆጶስን ተከትሎ መቅደስ
እንዲገባ ።
ወርእዩ ወአምኑ
ትንሣኤውን አይተው አመኑ ።

፱ እስመ ዓዲሁ ኢየአምሩ ዘውስተ መጻሕ
ፍት ዘከመ ሀለዎ ይትነሣእ እምነ ምውታን

፱ ከሙታን ተለይቶ ይነሣ ዘንድ እንዳለው
መጻሕፍት የተናገሩትን ገና አላወቁም ነበርና ።

፲ ወአምዝ ሖሩ ፪ኤሆሙ አርዳኢሁ ።
፲ ከዚህ በኋላ ሁለቱ ደቀ መዛሙርቱ ሄዱ።
ወእተው ቤቶሙ ።
ከቤታቸው ገቡ ።
ዘከመ አስተርእያ ኢየሱስ ለማርያም መግደላዊት።

፲፩ ወማርያምሰ ቆመት ኀበ መቃብር አፍአ
ወትበኪ ። ማቴ· ፳፰፥፩ ማር· ፲፮፥፩ ሉቃ ፳፬፥፩

፲፩ ማርያም ግን ከመቃብር አጠገብ ሁና ታለ
ቅስ ነበር ።
ወእንዘ ትበኪ ሐወጸት ውስተ መቃብር ።
እያለቀሰች ወደ መቃብር በተመለከተ ጊዜ ።

፲፪ ወርእየት ክልኤተ መላእክተ በጸዓድው
አልባስ ።

፲፪ ሁለት መላእክት ብሩሀ ብሩሀ ልብስ ለብ
ሰው አየች ።
ወይነብሩ አሐዱ ትርዓስ ወአሐዱ ትርጋፀ ኀበ ነበረ
ሥጋሁ ለእግዚእ ኢየሱስ ።
የጌታችን ሥጋ ካለበት ቦታ አንዱ በራስጌ አንዱ
በግርጌ ተቀምጠው ።

፲፫ ወይቤልዋ እሙንቱ መላእክት ምንት ያበ
ክየኪ አ ብእሲቶ

፲፫ እኒያ መላእክት አንች ሆይ ምን ያስለቅ
ስሻል አሏት ።
ወመነ ተኀሥሢ ።
ማን ትሻለሽ ።
ወትቤሎሙ እስመ ነሥእዎ ለእግዚእየ እምውስተ
መቃብር ።
ጌታዬን ከመቃብር ወስደውታል ።
ወኢየአምር ኀበ ወሰድዎ ።
ከወሰዱበት ግን አላውቅም አለቻቸው ።

፲፬ ወዘንተ ብሂላ ተመይጠት ድኅሬሃ ።
፲፬ ይህን ተናግራ ወደኋላ ተመለሰች ያዘነተኛ
ዓይኑ ባካና ነውና አንድም መላእክት ከወደፊቷ
ሲሰግዱ አይታለች ከወደኋላዋ ጥላውን ጥሎባታል
መለስ ብትል ቁሞ አይታዋለች ።
ወኢያእመረት ከመ እግዚእ ኢየሱስ ውእቱ ።
ጌታ እንደሆነ አላውቀችም ።

፲፭ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ብእሲቶ ምንት
ያበክየኪ ።

፲፭ አንች ሆይ ምን ያስለቅስሻል ።
ወመነ ተኀሥሢ ።
ማነንስ ትሻለሽ አላት ።
ወመሰላ ላቲስ ዓቃቤ ገነት ውእቱ ።
እርሷም አታክልት ጠባቂ መሰሏት ነበር ።
ወትቤሎ እግዚእየ እመኒ አንተ ነሣእኮ ንግረኒ
ኀበ ወሰድኮ ።
ጌታዬ አንተ ወስደኸው እንደሆነ ንገረኝ አለችው ።
ከመ እሑር አነ ወእንሥኦ ኀቤየ ከመ ዕቅብእ ዕፍረተ
ወደኔ እምጥቼ ሽቱ ዕቀባው ዘንድ ።

፲፮ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ለማርያም ።
፲፮ ጌታ ማርያም አላት ።
ወተመይጠት ወትቤሎ በነገረ ዕብራይስጥ ረቡኒ ።
ተመልሳ በዕብራይስጥ ቋንቋ ረቡኒ አለች ።
ዘበትርጓሜሁ ሊቅ ብሂል ወእቱ ።
መምህር ሆይ ማለት ነው ።

፲፯ ወይቤላ እግዚእ ኢየሱስ ኢትልክፍኒ እስመ
ዓዲ ኢዐረጉ ኀበ አቡየ ።

፲፯ የተግሣጽ አነጋገር ወዳባቴ አልወጣሁም ማለት ገና አላመንሽብኝምና አትንኪኝ አላት ። እንድም የመስናበቻው ጊዜ የደረስ መስዓት ቀር ባለች የማርግበት ጊዜ ገና ነውና አትንኪኝ አላት፥ ክህናት ልብስ ተክህኖ ለብሰው ሳሉ ሊነኳቸው እንዳይገባ ለማጠየቅ ።
ወሑሪ ባሕቱ ኀበ አኃውየ ወበሊዮሙ እዓርግ ኀበ እቡየ ወአቡሆሙ ኀበ አምላኪየ ወእምላክክሙ ።
ወደ ወንድሞቼ ሄደሽ ወዳባቴ ወዳባታችሁ ወደ ፈጣሪየ ወደፈጣሪያችሁ ዓርጋለሁ ብለሽ ንገሪያቸው እንጂ አላት አቡየ ብሎ የሱን ልደት ተናገረአቡየ ያለው የርሱ የባሕርይ ነው አቡክሙ ያለው የኛ የጸጋ ነው እምላኪየ አለ በሥጋ ይፈጥረዋል ፣ እምላክክሙ አለ በጥንተ ተፈጥሮ በሐዲስ ተፈጥሮ ይፈጥረናልና።

፲፰ ወሖረት ማርያም መግደላዊት ወአብሠረ ቶሙ ለአርዳኢሁ ።

፲፰ ማርያም መግደላዊትም ሄዳ ለደቀ መዛ ሙርቶቹ ነገረቻቸው ።
ወትቤሎሙ ርኢክዎ ለእግዚእነ ወነገረኒ ዘንተ ።
ጌታችንን አየሁት ይህንም ነገረኝ ብላ ።
ዜነወት ዘንተ ዘከመ ይቤላ ።
ተነሣ ብለሽ ንገሪ እንዳላት ተነሣ ብላ ነገረቻቸው፥ ማቴዎስ ብዙ ሴቶት በአፍአ አንድ መልአክ አዩ ይላል ፡ ማርቆስ ብዙ ሴቶት በውስጥ አንድ መልአክ አዩ ይላል ። ሉቃስ በአፍአ በውስጥ ሳይል ብዙ ሴቶች ሁለት መላእክት አዩ ይላል ። ዮሐንስ አንዲት ሴት በውስጥ ሁለት መላእክት አየች አለ ። እንደምን ነው አይጣላም ቢሉ አይጣላም ማታ ጀምረው ሲመላለሱ አድረዋል እንደመጡ አይተዋል ። ሁለተኛ እንደ ማቴዎስ ባንድ ወገን የሄዱ ብዙ ሴቶች በአፍአ አንድ መልአክ አይተው ሄዱ ። እንደ ማርቆስ ባንድ ወገን የሄዱ ብዙ ሴቶች በውስጥ አንድ መልአክ አይተው ሄዱ ። ሉቃስ በአፍአ በው ስጥ አይልም ባንድ ወገን የመጡ ሴቶች ሁለት መላእክት አይተው ሄዱ ፡ ዮሐንስ አንዲት ሴት በውስጥ ሁለት መላእክት አየች ማለቱ ለመንገር ከበቃች ብሎ ። እንድም እንደ ዮሐንስ ወሮጸት ወበጽሐት ኀበ ስምዖን ጴጥሮስ ወኀበ ዝኩ ካልዕ ረድእ ወትቤሎሙ ነሥእዎ ለእግዚእየ ብላ ተናገረች እንደ ማቴዎስ ባንድ ወገን የመጡ ብዙ ሴቶች በአ ፍአ አንድ መልአክ አይተው ሲሄዱ ጌታን ከመን ገድ አገኙት ። ወቀርባ ወአኀዛ እገሪሁ ወሰገዳ ሎቱ ይላል ። እጁ ነሡት ። ሑራ ንግራሆሙ ለአኃውየ አላቸው እንደ ሉቃስ ኢእምንዎቶ ወእክህድዎን ወመ ሰሎሙ ከመ ዝንጋኤ ይላል አእምሮ የማጣት መስ ሏቸው እንደ ማርቆስ ባንድ ወገን የመጡ ብዙ ሴቶች በውስጥ አንድ አይተው ሲሄዱ በፍቅሩ ትናደዳለ ችና ከመቃብር በአፍአ እያስቀሰች ቀረች ። በውስጥ ሁለት መላእክት አይታለች አንዱን በራሱጌ አንዱን በግርጌ ማቴዎስ ሠርከ ሰንበት ለጸቢሐ እሑድ ማርቆስ ወእንግሃ ሉቃስ አሌ ሳያ ገይሠ ዮሐንስ እንዘ ዓዲሁ ጽልመት ይላል ማታ ጀምረው እስኪነጋ ድረስ ሲመላለሱ አድረዋል ። እንድም ማቴዎስ ሠርከ ሰንበት ሉቃስ አሌሳያ ዮሐንስ ዓዲሁ ጽልመት ይላል ፣ ለመዓልት ሠርክ እንዳ ለው ለሌሊትም ሠርክ አለውና ፣ ማቴዎስ ለጸቢሐ እሑድ ማርቆስ ወሶበ ሠረቀ ፀሐይ ሉቃስ ገይሠ ዮሐንስ በጽባሕ ያለው አንድ ነው ሲነጋ ማለት ነው ።

ዘከመ አስተርአዮሙ ኢየሱስ ለሐዋርያት ።

፲፱ ወመስዮ ውእቱ ዕለት ዘውእቱ እሑድ ሰንበት እንዘ ዕፁው ኆኅት ኀበ ሀለዉ አርዳኢሁ ጉቡአነ በእንተ ፍርሃቶሙ ለአይሁድ ማቴ.፳፰ ፥ ፩ ፤ ማር. ፲፮ ፡ ፩ ፤ ሉቃ. ፳፬ ፥ ፩ ።

፲፱ ያውም ሰንበት የተባለ እሑድ ነው ሲመሽ ደቀ መዛሙርቱ አይሁድን ስለፈሩ በዝግ ቤት ተሰብስበው ሳሉ ።
መጽአ እግዚእ ኢየሱስ ወቆመ ማእከሎሙ ።
ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መጥቶ በዝግ ቤት ገብቶ በመካከላቸው ቆመ ።
ወይቤሎሙ ሰላም ለክሙ ።
እንዴት ሰነበታችሁ አስታረቅኋችሁ አላቸው ።

፳ ወዘንተ ብሂሎ አርአዮሙ እደዊሁ ወእ ገሪሁ ወገቦሁ ።

፳ በዚህ ያልተያየዘ በሉቃስ የተያያዘ ፈርሁ ወደንገፁ ወመሰሎሙ ከመ ዘመንፈስ ይሬእዩ ምትሐት ያዩ መስሏቸው እንዳዩ አድርገው ደነ ገፁ ፈሩምንት ያደነግፁክሙ ወስምንት ሕሊና እኩይ የዓርግ ውስተ ልብክሙ ፡ ርእዩ እደውየ ወእገ ርየ ከመ አነ ውእቱ ወገሥሡኒ ወአእምሩ እስመ ለመንፈስሰ ሥጋ ወዓፅም አልቦቱ ዘከመ ትሬ እዩ ብየ ። በኔ እንደምታዩት ለምትሐት ሥጋ ዓፅም የለውም አላቸው ፡ ይህን ተናግሮ በቀኖት የተወጋውን እጁን እግሩን በጦር የተወጋውን ጐኑን አሳያቸው ።
ወተፈሥሑ አርዳኢሁ ሶበ ርእይዎ ለእግዚእነ ።
ደቀ መዛሙርቱ ጌታን ባዩት ጊዜ ደስ አላቸው ።

፳፩ ወካዕበ ይቤሎሙ እግዚእነ ኢየሱስ ሰላም ለክሙ ።

፳፩ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ፪ኛ እንዴት ሰነበታችሁ መስቀል ቀረባችሁ ፤

